## ሱረቱ አል-ፋቲሃ

## سورة الفاتحة

1. በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡
2. ምስጋና ለአላህ ይገባው የዓለማት ጌታ ለኾነው፤
3. እጅግ በጣም ርኅሩህ በጣም አዛኝ
4. የፍርዱ ቀን ባለቤት ለኾነው፡፡
5. አንተን ብቻ እንግገዛለን፤ አንተንም ብቻ እርዳታን እንለምናለን፡፡
6. ቀጥተኛውን መንገድ ምራን፡፡
7. የእነዚያን በነርሱ ላይ በጎ የዋልክላቸውን በነሱ ላይ ያልተቆጣህባቸውንና ያልተሳሳቱትንም ሰዎች መንገድ (ምራን፤ በሉ)፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ ﴿١﴾

ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٢﴾

ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ ﴿٣﴾

مَٰلِكِ يَوۡمِ ٱلدِّينِ ﴿٤﴾

إِيَّاكَ نَعۡبُدُ وَإِيَّاكَ نَسۡتَعِينُ ﴿٥﴾

ٱهۡدِنَا ٱلصِّرَٰطَ ٱلۡمُسۡتَقِيمَ ﴿٦﴾

صِرَٰطَ ٱلَّذِينَ أَنۡعَمۡتَ عَلَيۡهِمۡ غَيۡرِ ٱلۡمَغۡضُوبِ عَلَيۡهِمۡ وَلَا ٱلضَّآلِّينَ ﴿٧﴾

## ሱረቱ አል-በቀራህ

## سورة البقرة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

1. አ.ለ.መ
2. ይህ መጽሐፍ (ከአላህ ለመኾኑ) ጥርጥር የለበትም፤ ለፈራህያን መሪ ነው፡፡
3. ለነዚያ በሩቁ ነገር የሚያምኑ ሶላትንም ደንቡን ጠብቀው የሚሰግዱ ከሰጠናቸውም ሲሳይ የሚቸሩ ለኾኑት፤
4. ለእነዚያም ወደ አንተ በተወረደውና ከአንተ በፊትም በተወረደው የሚያምኑ በመጨረሻይቱም (ዓለም) እነርሱ የሚያረጋግጡ ለኾኑት (መሪ ነው)፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

الٓمٓ ﴿١﴾

ذَٰلِكَ ٱلۡكِتَٰبُ لَا رَيۡبَۛ فِيهِۛ هُدٗى لِّلۡمُتَّقِينَ ﴿٢﴾

ٱلَّذِينَ يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡغَيۡبِ وَيُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ﴿٣﴾

وَٱلَّذِينَ يُؤۡمِنُونَ بِمَآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ وَمَآ أُنزِلَ مِن قَبۡلِكَ وَبِٱلۡأٓخِرَةِ هُمۡ يُوقِنُونَ ﴿٤﴾

5. እነዚያ ከጌታቸው በመመራት ላይ ናቸው፤ እነዚያም እነሱ ፍላጎታቸውን ያገኙ ናቸው::

أُوْلَٰٓئِكَ عَلَىٰ هُدٗى مِّن رَّبِّهِمۡۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ٥

6. እነዚያ የካዱት (ሰዎች) ብታስፈራራቸውም ባታስፈራራቸውም በነርሱ ላይ እኩል ነው፤ አያምኑም::

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ سَوَآءٌ عَلَيۡهِمۡ ءَأَنذَرۡتَهُمۡ أَمۡ لَمۡ تُنذِرۡهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ٦

7. አላህ በልቦቻቸው ላይ በመስሚያቸውም ላይ አትሞባቸዋል፤ በዓይኖቻቸውም ላይ መሸፈኛ አልለ፤ ለነሱም ታላቅ ቅጣት አላቸው::

خَتَمَ ٱللَّهُ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ وَعَلَىٰ سَمۡعِهِمۡۖ وَعَلَىٰٓ أَبۡصَٰرِهِمۡ غِشَٰوَةٞۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٞ ٧

8. ከሰዎችም «በአላህና በመጨረሻው ቀን አምነናል» የሚሉ አልሉ፤ እነርሱም አማኞች አይደሉም::

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَقُولُ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَبِٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ وَمَا هُم بِمُؤۡمِنِينَ ٨

9. አላህንና እነዚያን ያመኑትን (ሰዎች) ያታልላሉ፤ የማያውቁ ሲኾኑ ነፍሶቻቸውን እንጅ ሌላን አያታልሉም::

يُخَٰدِعُونَ ٱللَّهَ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَمَا يَخۡدَعُونَ إِلَّآ أَنفُسَهُمۡ وَمَا يَشۡعُرُونَ ٩

10. በልቦቻቸው ውስጥ (የንፍቅና) በሽታ አለባቸው:: አላህም በሽታን ጨመረባቸው:: ለነርሱም ይዋሹ በነበሩት ምክንያት አሳማሚ ቅጣት አላቸው::

فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ فَزَادَهُمُ ٱللَّهُ مَرَضٗاۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمُۢ بِمَا كَانُواْ يَكۡذِبُونَ ١٠

11. ለነርሱም «በምድር ላይ አታበላሹ» በተባሉ ጊዜ «እኛ አሳማሪዎች ብቻ ነን» ይላሉ::

وَإِذَا قِيلَ لَهُمۡ لَا تُفۡسِدُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ قَالُوٓاْ إِنَّمَا نَحۡنُ مُصۡلِحُونَ ١١

12. ንቁ እነርሱ አጥፊዎቹ እነሱው ናቸው፤ ግን አያውቁም::

أَلَآ إِنَّهُمۡ هُمُ ٱلۡمُفۡسِدُونَ وَلَٰكِن لَّا يَشۡعُرُونَ ١٢

13. ለነሱም «ሰዎቹ እንዳመኑ እመኑ» በተባሉ ጊዜ «ቂሎቹ እንዳመኑ እናምናለን?» ይላሉ:: አዋጅ ንቁ እነርሱ ቂሎቹ እነርሱው ናቸው፤ ግን አያውቁም::

وَإِذَا قِيلَ لَهُمۡ ءَامِنُواْ كَمَآ ءَامَنَ ٱلنَّاسُ قَالُوٓاْ أَنُؤۡمِنُ كَمَآ ءَامَنَ ٱلسُّفَهَآءُۗ أَلَآ إِنَّهُمۡ هُمُ ٱلسُّفَهَآءُ وَلَٰكِن لَّا يَعۡلَمُونَ ١٣

14. እነዚያንም ያመኑትን በተገናኙ ጊዜ «አምነናል» ይላሉ:: ወደ ሰይጣኖቻቸውም ባገለሉ ጊዜ «እኛ ከናንተ ጋር ነን፤ እኛ (በነሱ) ተሳላቂዎች ብቻ ነን» ይላሉ::

وَإِذَا لَقُواْ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ قَالُوٓاْ ءَامَنَّا وَإِذَا خَلَوۡاْ إِلَىٰ شَيَٰطِينِهِمۡ قَالُوٓاْ إِنَّا مَعَكُمۡ إِنَّمَا نَحۡنُ مُسۡتَهۡزِءُونَ ١٤

15. አላህ በነሱ ይሳለቅባቸዋል፤ በጥመታቸውም ውስጥ የሚዋልሉ ሲኾኑ ያዘገያቸዋል::

ٱللَّهُ يَسۡتَهۡزِئُ بِهِمۡ وَيَمُدُّهُمۡ فِي طُغۡيَٰنِهِمۡ يَعۡمَهُونَ ١٥

16. እነዚህ እነዚያ ስህተትን በቅንነት የገዙ ናቸው፡፡ ንግዳቸውም አላተረፈችም፤ ቀጥተኞችም አልኾኑም፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ ٱشۡتَرَوُاْ ٱلضَّلَٰلَةَ بِٱلۡهُدَىٰ فَمَا رَبِحَت تِّجَٰرَتُهُمۡ وَمَا كَانُواْ مُهۡتَدِينَ ١٦

17. (በንፍቅና) ምሳሌያቸው እንደዚያ እሳትን እንዳነደደ ሰው በዙሪያው ያለውን ሁሉ ባበራች ጊዜም አላህ ብርሃናቸውን እንደወሰደባቸው በጨለማዎችም ውስጥ የማያዩ ኾነው እንደተዋቸው (ሰዎች) ብጤ ነው፡፡

مَثَلُهُمۡ كَمَثَلِ ٱلَّذِي ٱسۡتَوۡقَدَ نَارٗا فَلَمَّآ أَضَآءَتۡ مَا حَوۡلَهُۥ ذَهَبَ ٱللَّهُ بِنُورِهِمۡ وَتَرَكَهُمۡ فِي ظُلُمَٰتٖ لَّا يُبۡصِرُونَ ١٧

18. (እነሱ) ደንቆሮዎች፣ ዲዳዎች፣ ዕውሮች ናቸው፤ ስለዚህ እነርሱ አይመለሱም፡፡

صُمُّۢ بُكۡمٌ عُمۡيٞ فَهُمۡ لَا يَرۡجِعُونَ ١٨

19. ወይም (ምሳሌያቸው) ከሰማይ እንደ ወረደ ዝናም (ባለቤቶች) ነው፤ በርሱ (በደመናው) ውስጥ ጨለማዎች፣ ነጎድጓድም፣ ብልጭታም ያሉበት ሲኾን ከመብረቆቹ ሞትን ለመፍራት ጣቶቻቸውን በጆሮቻቸው ውስጥ እንደሚያደርጉ ብጤ ነው፡፡ አላህም ከሓዲዎችን ከባቢ ነው፡፡

أَوۡ كَصَيِّبٖ مِّنَ ٱلسَّمَآءِ فِيهِ ظُلُمَٰتٞ وَرَعۡدٞ وَبَرۡقٞ يَجۡعَلُونَ أَصَٰبِعَهُمۡ فِيٓ ءَاذَانِهِم مِّنَ ٱلصَّوَٰعِقِ حَذَرَ ٱلۡمَوۡتِۚ وَٱللَّهُ مُحِيطُۢ بِٱلۡكَٰفِرِينَ ١٩

20. ብልጭታው ዓይኖቻቸውን ሊነጥቅ ይቀርባል፡፡ ለነርሱ ባበራላቸው ቁጥር በርሱ ውስጥ ይኼዳሉ፡፡ በነሱም ላይ ባጨለመ ጊዜ ይቆማሉ፡፡ አላህም በሻ ኖሮ መስሚያቸውንና ማየዎቻቸውን በወሰደ ነበር፤ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

يَكَادُ ٱلۡبَرۡقُ يَخۡطَفُ أَبۡصَٰرَهُمۡۖ كُلَّمَآ أَضَآءَ لَهُم مَّشَوۡاْ فِيهِ وَإِذَآ أَظۡلَمَ عَلَيۡهِمۡ قَامُواْۚ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَذَهَبَ بِسَمۡعِهِمۡ وَأَبۡصَٰرِهِمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٢٠

21. እናንተ ሰዎች ሆይ! የፈጠራችሁን እነዚያንም ከናንተ በፊት የነበሩትን (የፈጠረውን) ጌታችሁን ተገዙ፤ (ቅጣትን) ልትጠነቀቁ ይከጀላልና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ٱعۡبُدُواْ رَبَّكُمُ ٱلَّذِي خَلَقَكُمۡ وَٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ٢١

22. (እርሱ) ያ ለናንተ ምድርን ምንጣፍ ሰማይንም ጣራ ያደረገ ነው፤ ከሰማይም (ከደመና) ውሃን ያወረደ በርሱም ከፍሬዎች ለናንተ ሲሳይን ያወጣ ነው፡፡ እናንተም (ፈጣሪነቱን) የምታውቁ ስትኾኑ ለአላህ ባላንጣዎችን አታድርጉ፡፡

ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ فِرَٰشٗا وَٱلسَّمَآءَ بِنَآءٗ وَأَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَخۡرَجَ بِهِۦ مِنَ ٱلثَّمَرَٰتِ رِزۡقٗا لَّكُمۡۖ فَلَا تَجۡعَلُواْ لِلَّهِ أَندَادٗا وَأَنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٢٢

23. በባሪያችንም ላይ ካወረድነው በመጠራጠር ውስጥ ብትኾኑ ከብጤው አንዲትን ምዕራፍ አምጡ፡፡ እውነተኞችም እንደኾናችሁ ከአላህ ሌላ መስካሪዎቻችሁን ጥሩ፡፡

وَإِن كُنتُمۡ فِي رَيۡبٖ مِّمَّا نَزَّلۡنَا عَلَىٰ عَبۡدِنَا فَأۡتُواْ بِسُورَةٖ مِّن مِّثۡلِهِۦ وَٱدۡعُواْ شُهَدَآءَكُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٢٣

24. (ይህንን) ባትሠሩ ፈጽሞም አትሠሩትምና ያችን መቀጣጠያዋ ሰዎችና ድንጋዮች የኾነችውን እሳት ተጠበቁ፤ ለከሓዲዎች ተደግሳለች፡፡

فَإِن لَّمۡ تَفۡعَلُواْ وَلَن تَفۡعَلُواْ فَٱتَّقُواْ ٱلنَّارَ ٱلَّتِي وَقُودُهَا ٱلنَّاسُ وَٱلۡحِجَارَةُۖ أُعِدَّتۡ لِلۡكَٰفِرِينَ ٢٤

25. እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችንም የሠሩትን ለነርሱ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው ገነቶች ያሏቸው መኾኑን አብስራቸው፡፡ ከርሷ ከፍሬ (ዓይነት) ሲሳይን በተመገቡ ቁጥር (ፍሬዎችዋ ስለሚመሳሰሉ) «ይህ ያ ከአሁን በፊት የተገመብነው ነው» ይላሉ፡፡ እርሱንም ተመሳሳይ ኾኖ ተሰጡት፡፡ ለነሱም በውስጧ ንጹህ የተደረጉ ሚስቶች አሏቸው፡፡ እነሱም በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

وَبَشِّرِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ أَنَّ لَهُمۡ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۖ كُلَّمَا رُزِقُواْ مِنۡهَا مِن ثَمَرَةٖ رِّزۡقٗا قَالُواْ هَٰذَا ٱلَّذِي رُزِقۡنَا مِن قَبۡلُۖ وَأُتُواْ بِهِۦ مُتَشَٰبِهٗاۖ وَلَهُمۡ فِيهَآ أَزۡوَٰجٞ مُّطَهَّرَةٞۖ وَهُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٢٥

26. አላህ ማንኛውንም ነገር ትንኝንም ኾነ (በትንሽነት ወይም በትልቅነት) ከበላይዋ የኾነንም ምሳሌ ለማድረግ አያፍርም፡፡ እነዚያ ያመኑትማ፤ እርሱ (ምሳሌው) ከጌታቸው (የተገኘ) እውነት መኾኑን ያውቃሉ፡፡ እነዚያም የካዱትማ «አላህ በዚህ ምንን ምሳሌ ሻ» ይላሉ፡፡ በርሱ (በምሳሌው) ብዙዎችን ያሳስታል በርሱም ብዙዎችን ያቀናል፡፡ በርሱም አመፀኞችን እንጅ ሌላን አያሳስትም፡፡

۞إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَسۡتَحۡيِۦٓ أَن يَضۡرِبَ مَثَلٗا مَّا بَعُوضَةٗ فَمَا فَوۡقَهَاۚ فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ فَيَعۡلَمُونَ أَنَّهُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّهِمۡۖ وَأَمَّا ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَيَقُولُونَ مَاذَآ أَرَادَ ٱللَّهُ بِهَٰذَا مَثَلٗاۘ يُضِلُّ بِهِۦ كَثِيرٗا وَيَهۡدِي بِهِۦ كَثِيرٗاۚ وَمَا يُضِلُّ بِهِۦٓ إِلَّا ٱلۡفَٰسِقِينَ ٢٦

27. እነዚያ የአላህን ቃል ኪዳን ከአጠበቀባቸው በኋላ የሚያፈርሱ እንዲቀጠልም በርሱ ያዘዘውን ነገር የሚቆርጡ በምድርም ላይ የሚያበላሹ እነዚያ እነርሱ ከሳሪዎቹ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ يَنقُضُونَ عَهۡدَ ٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ مِيثَٰقِهِۦ وَيَقۡطَعُونَ مَآ أَمَرَ ٱللَّهُ بِهِۦٓ أَن يُوصَلَ وَيُفۡسِدُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ٢٧

28. ሙታን የነበራችሁ ስትኾኑ ሕያው ያደረጋችሁ ከዚያም የሚገድላችሁ ከዚያም ሕያው የሚያደርጋችሁ ሲኾን ከዚያም ወደርሱ የምትመለሱ ስትኾኑ በአላህ እንዴት ትክዳላችሁ!

كَيۡفَ تَكۡفُرُونَ بِٱللَّهِ وَكُنتُمۡ أَمۡوَٰتٗا فَأَحۡيَٰكُمۡۖ ثُمَّ يُمِيتُكُمۡ ثُمَّ يُحۡيِيكُمۡ ثُمَّ إِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٢٨

29. እርሱ ያ በምድር ያለውን ሁሉ ለእናንተ የፈጠረ ነው፡፡ ከዚያም ወደ ሰማይ አሰበ፤ ሰባት ሰማያትም አደረጋቸው፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي خَلَقَ لَكُم مَّا فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا ثُمَّ ٱسۡتَوَىٰٓ إِلَى ٱلسَّمَآءِ فَسَوَّىٰهُنَّ سَبۡعَ سَمَٰوَٰتٖۚ وَهُوَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ٢٩

30. (ሙሐመድ ሆይ) ጌታህ ለመላእክት፡- «እኔ በምድር ላይ ምትክን አድራጊ ነኝ፤» ባለ ጊዜ (የኾነውን አስታውስ፤ እነርሱም) «እኛ ከማመስገን ጋር የምናጠራህ ላንተም የምንቀድስ ስንኾን በርሷ ውስጥ የሚያጠፋንና ደሞችንም የሚያፈስን ታደርጋለህን?» አሉ፡፡ (አላህ) «እኔ የማታውቁትን ነገር አውቃለሁ» አላቸው፡፡

وَإِذۡ قَالَ رَبُّكَ لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ إِنِّي جَاعِلٞ فِي ٱلۡأَرۡضِ خَلِيفَةٗۖ قَالُوٓاْ أَتَجۡعَلُ فِيهَا مَن يُفۡسِدُ فِيهَا وَيَسۡفِكُ ٱلدِّمَآءَ وَنَحۡنُ نُسَبِّحُ بِحَمۡدِكَ وَنُقَدِّسُ لَكَۖ قَالَ إِنِّيٓ أَعۡلَمُ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ٣٠

31. አደምንም ስሞችን ሁሏንም አስተማረው፡፡ ከዚያም በመላእክት ላይ (ተጠሪዎቹን) አቀረባቸው፡፡ «እውነተኞችም እንደኾናችሁ የነዚህን (ተጠሪዎች) ስሞች ንገሩኝ» አላቸው፡፡

وَعَلَّمَ ءَادَمَ ٱلۡأَسۡمَآءَ كُلَّهَا ثُمَّ عَرَضَهُمۡ عَلَى ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ فَقَالَ أَنۢبِـُٔونِي بِأَسۡمَآءِ هَٰٓؤُلَآءِ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٣١

32. «ጥራት ይገባህ፤ ከአስተማርከን ነገር በስተቀር ለኛ ዕውቀት የለንም፡፡ አንተ ዐዋቂው ጥበበኛው አንተ ብቻ ነህና» (አሉ)፡፡

قَالُواْ سُبۡحَٰنَكَ لَا عِلۡمَ لَنَآ إِلَّا مَا عَلَّمۡتَنَآۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡحَكِيمُ ٣٢

33. ፡-«አደም ሆይ ስሞቻቸውን ንገራቸው» አለው፡፡ ስሞቻቸውን በነገራቸውም ጊዜ «እኔ የሰማያትንና የምድርን ሩቅ ምስጢር ዐውቃለሁ፤ የምትገልጹትንና ያንንም ትደብቁት የነበራችሁትን ዐውቃለሁ አላልኳችሁምን?» አላቸው፡፡

قَالَ يَٰٓـَٔادَمُ أَنۢبِئۡهُم بِأَسۡمَآئِهِمۡۖ فَلَمَّآ أَنۢبَأَهُم بِأَسۡمَآئِهِمۡ قَالَ أَلَمۡ أَقُل لَّكُمۡ إِنِّيٓ أَعۡلَمُ غَيۡبَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَأَعۡلَمُ مَا تُبۡدُونَ وَمَا كُنتُمۡ تَكۡتُمُونَ ٣٣

34. ለመላእክትም «ለአደም ስገዱ» ባልን ጊዜ (አስታውስ) ፡፡ ሁሉም ወዲያውኑ ሰገዱ፤ ኢብሊስ (ዲያብሎስ) ብቻ ሲቀር እምቢ አለ፤ ኮራም ከከሓዲዎቹም ኾነ፡፡

وَإِذۡ قُلۡنَا لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ ٱسۡجُدُواْ لِأٓدَمَ فَسَجَدُوٓاْ إِلَّآ إِبۡلِيسَ أَبَىٰ وَٱسۡتَكۡبَرَ وَكَانَ مِنَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٣٤

35. «አደም ሆይ! አንተ ከነሚስትህ በገነት ተቀመጥ፤ ከርሷም በፈለጋችሁት ስፍራ በሰፊው ተመገቡ፤ ግን ይህችን ዛፍ አትቅረቡ፤ ከበደለኞች ትኾናላችሁና» አልንም፡፡

وَقُلۡنَا يَٰٓـَٔادَمُ ٱسۡكُنۡ أَنتَ وَزَوۡجُكَ ٱلۡجَنَّةَ وَكُلَا مِنۡهَا رَغَدًا حَيۡثُ شِئۡتُمَا وَلَا تَقۡرَبَا هَٰذِهِ ٱلشَّجَرَةَ فَتَكُونَا مِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٣٥

36. ከርሷም ሰይጣን አዳለጣቸው በውስጡም ከነበሩበት (ድሎት) አወጣቸው፡፡ «ከፊላችሁም ለከፊሉ ጠላት ሲኾን ውረዱ፤ ለናንተም በምድር ላይ እስከ ጊዜ (ሞታችሁ) ድረስ መርጊያና መጣቀሚያ አላችሁ» አልናቸው፡፡

فَأَزَلَّهُمَا ٱلشَّيۡطَٰنُ عَنۡهَا فَأَخۡرَجَهُمَا مِمَّا كَانَا فِيهِۖ وَقُلۡنَا ٱهۡبِطُواْ بَعۡضُكُمۡ لِبَعۡضٍ عَدُوّٞۖ وَلَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُسۡتَقَرّٞ وَمَتَٰعٌ إِلَىٰ حِينٖ ٣٦

37. አደምም ከጌታው ቃላትን ተቀበለ፡፡ በርሱ ላይም (ጌታው ጸጸትን በመቀበል) ተመለሰለት፤ እነሆ እርሱ ጸጸትን ተቀባይ አዛኝ ነውና፡፡

فَتَلَقَّىٰٓ ءَادَمُ مِن رَّبِّهِۦ كَلِمَٰتٖ فَتَابَ عَلَيۡهِۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلتَّوَّابُ ٱلرَّحِيمُ ٣٧

38. «ሁላችሁም ኾናችሁ ከርሷ ውረዱ፡፡ ከኔም የኾነ መመሪያ ቢመጣላችሁ ወዲያውኑ መመሪያዬን የተከተለ ሰው በነሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነሱም አያዝኑም» አልናቸው፡፡

قُلۡنَا ٱهۡبِطُواْ مِنۡهَا جَمِيعٗاۖ فَإِمَّا يَأۡتِيَنَّكُم مِّنِّي هُدٗى فَمَن تَبِعَ هُدَايَ فَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ٣٨

39. እነዚያም (በመልክተኞቻችን) የካዱ በአንቀጾቻችንም ያስተባበሉ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٣٩

40. የእስራኤል ልጆች ሆይ! ያችን በናንተ ላይ የለገስኳትን ጸጋዬን አስታውሱ፡፡ በቃል ኪዳኔም ሙሉ፤ በቃል ኪዳናችሁ እሞላለሁና፤ እኔንም ብቻ ፍሩ፡፡

يَٰبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتِيَ ٱلَّتِيٓ أَنۡعَمۡتُ عَلَيۡكُمۡ وَأَوۡفُواْ بِعَهۡدِيٓ أُوفِ بِعَهۡدِكُمۡ وَإِيَّٰيَ فَٱرۡهَبُونِ ٤٠

41. ከናንተ ጋር ያለውን (መጽሐፍ) የሚያረጋግጥ ሆኖ ባወረድኩትም (ቁርኣን) እመኑ፡፡ በርሱም የመጀመሪያ ከሓዲ አትሁኑ፡፡ በአንቀጾቼም ጥቂትን ዋጋ አትለውጡ፡፡ እኔንም ብቻ ተጠንቀቁ፡

وَءَامِنُواْ بِمَآ أَنزَلۡتُ مُصَدِّقٗا لِّمَا مَعَكُمۡ وَلَا تَكُونُوٓاْ أَوَّلَ كَافِرِۭ بِهِۦۖ وَلَا تَشۡتَرُواْ بِـَٔايَٰتِي ثَمَنٗا قَلِيلٗا وَإِيَّٰيَ فَٱتَّقُونِ ٤١

42. እውነቱንም በውሸት አትቀላቅሉ፡፡ እናንተም የምታውቁ ስትሆኑ እውነትን አትደብቁ፡፡

وَلَا تَلۡبِسُواْ ٱلۡحَقَّ بِٱلۡبَٰطِلِ وَتَكۡتُمُواْ ٱلۡحَقَّ وَأَنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٤٢

43. ሶላትንም ደንቡን ጠብቃችሁ ስገዱ፡፡ ዘካንም (ግዴታ ምጽዋትን) ስጡ፡፡ (ለጌታችሁ) ከአጎንባሾች ጋርም አጎንብሱ፡፡

وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُواْ ٱلزَّكَوٰةَ وَٱرۡكَعُواْ مَعَ ٱلرَّٰكِعِينَ ٤٣

44. እናንተ መጽሐፉን የምታነቡ ሆናችሁ ሰዎችን በበጎ ሥራ ታዛላችሁን? ነፍሶቻችሁንም ትረሳላችሁን? (የሥራችሁን መጥፎነት) አታውቁምን?

۞أَتَأۡمُرُونَ ٱلنَّاسَ بِٱلۡبِرِّ وَتَنسَوۡنَ أَنفُسَكُمۡ وَأَنتُمۡ تَتۡلُونَ ٱلۡكِتَٰبَۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ٤٤

45. በመታገስና በሶላትም ተረዱ፡፡ እርሷም (ሶላት) በፈሪዎች ላይ እንጅ በሌላው ላይ በእርግጥ ከባድ ናት፡ :

وَٱسۡتَعِينُواْ بِٱلصَّبۡرِ وَٱلصَّلَوٰةِۚ وَإِنَّهَا لَكَبِيرَةٌ إِلَّا عَلَى ٱلۡخَٰشِعِينَ ٤٥

46. እነዚያ እነርሱ ጌታቸውን የሚገናኙ እነሱም ወደእርሱ ተመላሾች መኾናቸውን የሚያረጋግጡ በኾኑት (ላይ እንጅ ከባድ ናት)፡፡

ٱلَّذِينَ يَظُنُّونَ أَنَّهُم مُّلَٰقُواْ رَبِّهِمۡ وَأَنَّهُمۡ إِلَيۡهِ رَٰجِعُونَ ٤٦

47. የእስራኤል ልጆች ሆይ! ያችን በናንተ ላይ የለገስኳትን ጸጋዬንና እኔም በዓለማት ላይ ያበለጥኳችሁ (አባቶቻችሁን በጊዜያቸው ከነበሩት ዓለማት ያበለጥኩዋቸው) መኾኔን አስታውሱ፡፡

يَٰبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتِيَ ٱلَّتِيٓ أَنۡعَمۡتُ عَلَيۡكُمۡ وَأَنِّي فَضَّلۡتُكُمۡ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ٤٧

48. (ማንኛዋ) ነፍስም ከ(ሌላዋ) ነፍስ ምንንም የማትመነዳበትን፣ ከርሷም ምልጃን የማይቀበሉባትን፣ ከርሷም ቤዛ የማይያዝበትን፣ እነርሱም የማይረዱበትን ቀን ተጠንቀቁ፡፡

وَٱتَّقُواْ يَوۡمٗا لَّا تَجۡزِي نَفۡسٌ عَن نَّفۡسٖ شَيۡـٔٗا وَلَا يُقۡبَلُ مِنۡهَا شَفَٰعَةٞ وَلَا يُؤۡخَذُ مِنۡهَا عَدۡلٞ وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ٤٨

49. ከፈርዖንም ቤተሰቦች (ከጎሶቹና ከሰራዊቱ) ብርቱን ቅጣት የሚያቀምሱዋችሁ ወንዶች ልጆቻችሁን የሚያርዱ ሴቶቻችሁንም የሚተው ሲኾኑ ባዳንናችሁ ጊዜ (የኾነውን አስታውሱ)፡፡ በዚሃችሁም ከጌታችሁ ታላቅ ፈተና አለበት፡፡

وَإِذۡ نَجَّيۡنَٰكُم مِّنۡ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ يَسُومُونَكُمۡ سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِ يُذَبِّحُونَ أَبۡنَآءَكُمۡ وَيَسۡتَحۡيُونَ نِسَآءَكُمۡۚ وَفِي ذَٰلِكُم بَلَآءٞ مِّن رَّبِّكُمۡ عَظِيمٞ ٤٩

50. በናንተም ምክንያት ባሕሩን በከፈልን ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ ወዲያውም አዳንናችሁ፡፡ የፈርዖንንም ቤተሰቦች እናንተ የምትመለከቱ ኾናችሁ አሰጠምናቸው፡፡

وَإِذْ فَرَقْنَا بِكُمُ ٱلْبَحْرَ فَأَنجَيْنَـٰكُمْ وَأَغْرَقْنَآ ءَالَ فِرْعَوْنَ وَأَنتُمْ تَنظُرُونَ ٥٠

51. ሙሳንም አርባን ሌሊት በቀጠርነው ጊዜ (የኾነውን አስታውሱ)፡፡ ከዚያም ከርሱ (መኼድ) በኋላ እናንተ በዳዮች ስትኾኑ ወይፈንን (አምላክ አድርጋችሁ) ያዛችሁ፡፡

وَإِذْ وَٰعَدْنَا مُوسَىٰٓ أَرْبَعِينَ لَيْلَةً ثُمَّ ٱتَّخَذْتُمُ ٱلْعِجْلَ مِنۢ بَعْدِهِۦ وَأَنتُمْ ظَـٰلِمُونَ ٥١

52. ከዚያም ከዚህ በኋላ እናንተ ታመሰግኑ ዘንድ ከናንተ ምሕረት አደረግን፡፡

ثُمَّ عَفَوْنَا عَنكُم مِّنۢ بَعْدِ ذَٰلِكَ لَعَلَّكُمْ تَشْكُرُونَ ٥٢

53. ሙሳንም መጽሐፍንና (እውነትና ውሸትን) መለያንም ትመሩ ዘንድ በሰጠነው ጊዜ (አስታውሱ)፡፡

وَإِذْ ءَاتَيْنَا مُوسَى ٱلْكِتَـٰبَ وَٱلْفُرْقَانَ لَعَلَّكُمْ تَهْتَدُونَ ٥٣

54. ሙሳም ለሕዝቦቹ፡- «ሕዝቦቼ ሆይ! እናንተ ወይፈንን (አምላክ አድርጋችሁ) በመያዛችሁ ነፍሶቻችሁን በደላችሁ፡፡ ወደ ፈጣሪያችሁም ተመለሱ፤ ነፍሶቻችሁንም ግደሉ፤ ይሃችሁ በፈጣሪያችሁ ዘንድ ለናንተ በላጭ ነው» ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ በእናንተም ላይ ጸጸትን በመቀበል ተመለሰላችሁ፡፡ እነሆ እርሱ ጸጸትን ተቀባይ አዛኝ ነውና፡፡

وَإِذْ قَالَ مُوسَىٰ لِقَوْمِهِۦ يَـٰقَوْمِ إِنَّكُمْ ظَلَمْتُمْ أَنفُسَكُم بِٱتِّخَاذِكُمُ ٱلْعِجْلَ فَتُوبُوٓا۟ إِلَىٰ بَارِئِكُمْ فَٱقْتُلُوٓا۟ أَنفُسَكُمْ ذَٰلِكُمْ خَيْرٌ لَّكُمْ عِندَ بَارِئِكُمْ فَتَابَ عَلَيْكُمْ ۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلتَّوَّابُ ٱلرَّحِيمُ ٥٤

55. «ሙሳ ሆይ! አላህን በግልጽ እስከምናይ ድረስ ላንተ በፍጹም አናምንልህም» በላችሁም ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ እናንተም እየተመለከታችሁ መብረቅ ያዘቻችሁ፡፡

وَإِذْ قُلْتُمْ يَـٰمُوسَىٰ لَن نُّؤْمِنَ لَكَ حَتَّىٰ نَرَى ٱللَّهَ جَهْرَةً فَأَخَذَتْكُمُ ٱلصَّـٰعِقَةُ وَأَنتُمْ تَنظُرُونَ ٥٥

56. ከዚያም ታመሰግኑ ዘንድ ከሞታችሁ በኋላ አስነሳናችሁ፡፡

ثُمَّ بَعَثْنَـٰكُم مِّنۢ بَعْدِ مَوْتِكُمْ لَعَلَّكُمْ تَشْكُرُونَ ٥٦

57. በናንተም ላይ ደመናን አጠለልን፡፡ በናተም ላይ (እንደ ነጭ ማር ያለ) መንናን እና ድርጭትን አወረድን፡፡ ከሰጠናችሁም ጣፋጮች «ብሉ (አልን)፡፡ » አልበደሉንምም ግን ነፍሶቻቸውን ይበድሉ ነበር፡፡

وَظَلَّلْنَا عَلَيْكُمُ ٱلْغَمَامَ وَأَنزَلْنَا عَلَيْكُمُ ٱلْمَنَّ وَٱلسَّلْوَىٰ ۖ كُلُوا۟ مِن طَيِّبَـٰتِ مَا رَزَقْنَـٰكُمْ ۚ وَمَا ظَلَمُونَا وَلَـٰكِن كَانُوٓا۟ أَنفُسَهُمْ يَظْلِمُونَ ٥٧

58. «ይህችንም ከተማ ግቡ፡፡ ከርሷም በሻችሁት ስፍራ ሰፊን (ምግብ) ተመገቡ፡፡ በሩንም ያጎነበሳችሁ ኾናችሁ ግቡ፤ (ጥያቄያችን የኃጢአታችን መርገፍ ነው) በሉም፡፡ ኃጢአቶቻችሁን ለናንተ እንምራለንና፡፡ በጎ ሠሪዎችንም (ምንዳን) እንጨምርላቸዋለን» ባልን ጊዜ (አስታውሱ)፡፡

وَإِذْ قُلْنَا ٱدْخُلُوا۟ هَـٰذِهِ ٱلْقَرْيَةَ فَكُلُوا۟ مِنْهَا حَيْثُ شِئْتُمْ رَغَدًا وَٱدْخُلُوا۟ ٱلْبَابَ سُجَّدًا وَقُولُوا۟ حِطَّةٌ نَّغْفِرْ لَكُمْ خَطَـٰيَـٰكُمْ ۚ وَسَنَزِيدُ ٱلْمُحْسِنِينَ ٥٨

59. እነዚያም የበደሉት ሰዎች ከዚያ ለነሱ ከተባሉት ሌላ ቃልን ለወጡ፡፡ በነዚያም በበደሉት ላይ ያመጹ በመሆናቸው ምክንያት መቅሠፍትን አወረድንባቸው፡፡

فَبَدَّلَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ قَوۡلًا غَيۡرَ ٱلَّذِي قِيلَ لَهُمۡ فَأَنزَلۡنَا عَلَى ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ رِجۡزٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ بِمَا كَانُواْ يَفۡسُقُونَ ﴿٥٩﴾

60. ሙሳም ለሕዝቦቹ መጠጥን በፈለገ ጊዜ (የኾነውን አስታውሱ)፡፡ «ድንጋዩንም በበትርህ ምታ» አልነው፡፡ (መታውም) ከርሱም ዐሥራሁለት ምንጮች ፈለቁ፡፡ ሰዎቹ ሁሉ መጠጫቸውን በእርግጥ ዐወቁ፡፡ «ከአላህ ሲሳይ ብሉ፤ ጠጡም፤ አመጠኞችም ኾናችሁ በምድር ላይ አታበላሹ» (አልናቸው)፡፡

۞وَإِذِ ٱسۡتَسۡقَىٰ مُوسَىٰ لِقَوۡمِهِۦ فَقُلۡنَا ٱضۡرِب بِّعَصَاكَ ٱلۡحَجَرَۖ فَٱنفَجَرَتۡ مِنۡهُ ٱثۡنَتَا عَشۡرَةَ عَيۡنٗاۖ قَدۡ عَلِمَ كُلُّ أُنَاسٖ مَّشۡرَبَهُمۡۖ كُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ مِن رِّزۡقِ ٱللَّهِ وَلَا تَعۡثَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُفۡسِدِينَ ﴿٦٠﴾

61. ሙሳ ሆይ፡- «በአንድ (ዓይነት) ምግብ ላይ በፍጹም አንታገሥም፤ ስለዚህ ጌታህን ከዚያ ምድር ከምታበቅለው ሁሉ ከቅጠላቅጠል ከዱባዋም ከስንዴዋም ከምስርዋም ከሽንኩርቷም ለኛ ያወጣ ዘንድ ለኛ ለምንልን» ባላችሁም ጊዜ (የኾነውን አስታውሱ፡፡ ሙሳም፡- «ያንን እርሱ ዝቅተኛ የኾነውን በዚያ እርሱ በላጭ በኾነው ነገር ለውጥን ትፈልጋላችሁን? ወደ ከተማ ውረዱ፤ ለናንተም የጠየቃችሁት ነገር አላችሁ» አላቸው፡፡ በነርሱም ላይ ውርደትና ድኽነት ተመታባቸው፡፡ ከአላህም በኾነ ቁጣ ተመለሱ፡፡ ይህ እነርሱ በአላህ ታምራቶች ይክዱና ነቢያትንም ያለ ሕግ ይገድሉ ስለነበሩ ነው፡፡ ይህ በማመጻቸውና ወሰን የሚያልፉ በመኾናቸው ነው፡፡

وَإِذۡ قُلۡتُمۡ يَٰمُوسَىٰ لَن نَّصۡبِرَ عَلَىٰ طَعَامٖ وَٰحِدٖ فَٱدۡعُ لَنَا رَبَّكَ يُخۡرِجۡ لَنَا مِمَّا تُنۢبِتُ ٱلۡأَرۡضُ مِنۢ بَقۡلِهَا وَقِثَّآئِهَا وَفُومِهَا وَعَدَسِهَا وَبَصَلِهَاۖ قَالَ أَتَسۡتَبۡدِلُونَ ٱلَّذِي هُوَ أَدۡنَىٰ بِٱلَّذِي هُوَ خَيۡرٌۚ ٱهۡبِطُواْ مِصۡرٗا فَإِنَّ لَكُم مَّا سَأَلۡتُمۡۗ وَضُرِبَتۡ عَلَيۡهِمُ ٱلذِّلَّةُ وَٱلۡمَسۡكَنَةُ وَبَآءُو بِغَضَبٖ مِّنَ ٱللَّهِۗ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ كَانُواْ يَكۡفُرُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَيَقۡتُلُونَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّۗ ذَٰلِكَ بِمَا عَصَواْ وَّكَانُواْ يَعۡتَدُونَ ﴿٦١﴾

62. እነዚያ ያመኑ እነዚያም ይሁዳውያን የኾኑ፣ ክርስቲያኖችም፣ ሳቢያኖችም (ከእነርሱ) በአላህና በመጨረሻው ቀን ያመነ መልካምንም ሥራ የሠራ ለነርሱ በጌታቸው ዘንድ ምንዳቸው አላቸው፡፡ በነርሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነሱም አያዝኑም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَٱلَّذِينَ هَادُواْ وَٱلنَّصَٰرَىٰ وَٱلصَّٰبِـِٔينَ مَنۡ ءَامَنَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَلَهُمۡ أَجۡرُهُمۡ عِندَ رَبِّهِمۡ وَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ﴿٦٢﴾

63. ከበላያችሁም የጡርን ተራራ ያነሳን ኾነን የጠበቀ ቃልኪዳናችሁን በያዝን ጊዜ (የኾነውን አስታውሱ)፡፡ «ያንን የሰጠናችሁን በኀይል ያዙ፤ በውስጡ ያለውንም ነገር (ከእሳት) ትጠበቁ ዘንድ አስታውሱ» (አልን)፡፡

وَإِذۡ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَكُمۡ وَرَفَعۡنَا فَوۡقَكُمُ ٱلطُّورَ خُذُواْ مَآ ءَاتَيۡنَٰكُم بِقُوَّةٖ وَٱذۡكُرُواْ مَا فِيهِ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ﴿٦٣﴾

64. ከዚያም ከዚህ በኋላ (ኪዳኑን) ተዋችሁ፡፡ በናንተም ላይ የአላህ ችሮታና እዝነቱ ባልነበረ ኖሮ በእርግጥ ከጠፊዎቹ በኾናችሁ ነበር፡፡

ثُمَّ تَوَلَّيۡتُم مِّنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَۖ فَلَوۡلَا فَضۡلُ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَرَحۡمَتُهُۥ لَكُنتُم مِّنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٦٤

65. እነዚያንም ከእናንተ ውስጥ በቅዳሜ ቀን (ዐሣን በማጥመድ) ወሰን ያለፉትንና ለነሱ «ወራዳዎች ስትኾኑ ዝንጀሮዎች ኹኑ» ያልናቸውን በእርግጥ ዐወቃችሁ፡፡

وَلَقَدۡ عَلِمۡتُمُ ٱلَّذِينَ ٱعۡتَدَوۡاْ مِنكُمۡ فِي ٱلسَّبۡتِ فَقُلۡنَا لَهُمۡ كُونُواْ قِرَدَةً خَٰسِـِٔينَ ٦٥

66. (ቅጣቲቱንም) ለነዚያ በስተፊትዋ ለነበሩትና ለነዚያም ከበኋላዋ ላሉት (ሕዝቦች) መቀጣጫ ለፈራህያንም መገሰጫ አደረግናት፡፡

فَجَعَلۡنَٰهَا نَكَٰلٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهَا وَمَا خَلۡفَهَا وَمَوۡعِظَةٗ لِّلۡمُتَّقِينَ ٦٦

67. ሙሳም ለሕዝቦቹ፡- «አላህ ላምን እንድታርዱ ያዛችኋል» ባለ ጊዜ (አስታወሱ)፡፡«መሳለቂያ አድርገህ ትይዘናለህን?» አሉት፡፡ «ከተሳላቂዎች ከመኾን በአላህ እጠበቃለሁ» አላቸው፡፡

وَإِذۡ قَالَ مُوسَىٰ لِقَوۡمِهِۦٓ إِنَّ ٱللَّهَ يَأۡمُرُكُمۡ أَن تَذۡبَحُواْ بَقَرَةٗۖ قَالُوٓاْ أَتَتَّخِذُنَا هُزُوٗاۖ قَالَ أَعُوذُ بِٱللَّهِ أَنۡ أَكُونَ مِنَ ٱلۡجَٰهِلِينَ ٦٧

68. «ለኛ ጌታህን ጠይቅልን፤ እርሷ ምን እንደኾነች (ዕድሜዋን) ያብራራልን» አሉ፡፡ «እርሱ እርሷ ያላረጀች ጥጃም ያልኾነች በዚህ መካከል ልከኛ የኾነች ጊደር ናት ይላችኋል፤ የታዘዛችሁትንም ሥሩ» አላቸው፡፡

قَالُواْ ٱدۡعُ لَنَا رَبَّكَ يُبَيِّن لَّنَا مَا هِيَۚ قَالَ إِنَّهُۥ يَقُولُ إِنَّهَا بَقَرَةٞ لَّا فَارِضٞ وَلَا بِكۡرٌ عَوَانُۢ بَيۡنَ ذَٰلِكَۖ فَٱفۡعَلُواْ مَا تُؤۡمَرُونَ ٦٨

69. «ለኛ ጌታህን ጠይቅልን፤ መልኳ ምን እንደኾነ ለኛ ይግለጽልን» አሉ፡፡ «እርሱ እርሷ መልኳ ደማቅ ተመልካቾችን የምታስደስት ዳለቻ ላም ናት ይላችኋል» አላቸው፡፡

قَالُواْ ٱدۡعُ لَنَا رَبَّكَ يُبَيِّن لَّنَا مَا لَوۡنُهَاۚ قَالَ إِنَّهُۥ يَقُولُ إِنَّهَا بَقَرَةٞ صَفۡرَآءُ فَاقِعٞ لَّوۡنُهَا تَسُرُّ ٱلنَّٰظِرِينَ ٦٩

70. «ለኛ ጌታህን ጠይቅልን፤ እርሷ ምን እንደኾነች ይግለጽልን፤ ከብቶች በኛ ላይ ተመሳሰሉብን፡፡ እኛም አላህ የሻ እንደኾነ በእርግጥ ተመሪዎች ነን» አሉ፡፡

قَالُواْ ٱدۡعُ لَنَا رَبَّكَ يُبَيِّن لَّنَا مَا هِيَ إِنَّ ٱلۡبَقَرَ تَشَٰبَهَ عَلَيۡنَا وَإِنَّآ إِن شَآءَ ٱللَّهُ لَمُهۡتَدُونَ ٧٠

71. «እርሱ እርሷ ያልተገራች ምድርን (በማረስ) የማታስነሳ እርሻንም የማታጠጣ (ከነውር) የተጠበቀች ልዩ ምልክት የሌለባት ናት ይላችኋል» አላቸው፡፡ «አሁን በትክክል መጣህ» አሉ፤ ሊሠሩ ያልተቃረቡም ሲኾኑ አረዷት ፡፡

قَالَ إِنَّهُۥ يَقُولُ إِنَّهَا بَقَرَةٞ لَّا ذَلُولٞ تُثِيرُ ٱلۡأَرۡضَ وَلَا تَسۡقِي ٱلۡحَرۡثَ مُسَلَّمَةٞ لَّا شِيَةَ فِيهَاۚ قَالُواْ ٱلۡـَٰٔنَ جِئۡتَ بِٱلۡحَقِّۚ فَذَبَحُوهَا وَمَا كَادُواْ يَفۡعَلُونَ ٧١

72. ነፍስነም በገደላችሁና በርሷም (ገዳይ) በተከራከራችሁ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ አላህም ትደብቁት የነበራችሁትን ሁሉ ገላጭ ነው፡፡

وَإِذۡ قَتَلۡتُمۡ نَفۡسٗا فَٱدَّٰرَٰٔتُمۡ فِيهَاۖ وَٱللَّهُ مُخۡرِجٞ مَّا كُنتُمۡ تَكۡتُمُونَ ٧٢

73. «(በድኑን) በከፊሏም ምቱት» አልን፤ እንደዚሁ አላህ ሙታንን ያስነሳል፤ ታውቁም ዘንድ ታምራቶችን ያሳያችኋል፡፡

فَقُلْنَا ٱضْرِبُوهُ بِبَعْضِهَا ۚ كَذَٰلِكَ يُحْىِ ٱللَّهُ ٱلْمَوْتَىٰ وَيُرِيكُمْ ءَايَٰتِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَعْقِلُونَ ﴿٧٣﴾

74. ከዚያም ከዚህ በኋላ ልቦቻችሁ ደረቁ፤ እርሷም እንደ ድንጋዮች ወይም በድርቅና ይበልጥ የበረታች ናት፡፡ ከድንጋዮችም ከርሱ ጂረቶች የሚፈሱለት አለለ፡ ፡ ከነርሱም በእርግጥ የሚሰነጠቅና ከርሱ ውሃ (ምንጭ) የሚወጣው አለለ፡፡ ከነርሱም አላህን ከመፍራት የተነሳ ወደ ታች የሚወርድ አለለ፡፡ አላህም ከምትሠሩት ነገር ዘንጊ አይደለም፡፡

ثُمَّ قَسَتْ قُلُوبُكُم مِّنۢ بَعْدِ ذَٰلِكَ فَهِىَ كَٱلْحِجَارَةِ أَوْ أَشَدُّ قَسْوَةً ۚ وَإِنَّ مِنَ ٱلْحِجَارَةِ لَمَا يَتَفَجَّرُ مِنْهُ ٱلْأَنْهَٰرُ ۚ وَإِنَّ مِنْهَا لَمَا يَشَّقَّقُ فَيَخْرُجُ مِنْهُ ٱلْمَآءُ ۚ وَإِنَّ مِنْهَا لَمَا يَهْبِطُ مِنْ خَشْيَةِ ٱللَّهِ ۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعْمَلُونَ ﴿٧٤﴾

75. (አይሁዶች) ከነሱ የኾኑ ጭፍሮች የአላህን ቃል የሚሰሙና ከዚያም ከተረዱት በኋላ እነርሱ እያወቁ የሚለውጡት ሲኾኑ ለናንተ ማመናቸውን ትከጅላላችሁን?

۞ أَفَتَطْمَعُونَ أَن يُؤْمِنُوا۟ لَكُمْ وَقَدْ كَانَ فَرِيقٌ مِّنْهُمْ يَسْمَعُونَ كَلَٰمَ ٱللَّهِ ثُمَّ يُحَرِّفُونَهُۥ مِنۢ بَعْدِ مَا عَقَلُوهُ وَهُمْ يَعْلَمُونَ ﴿٧٥﴾

76. እነዚያንም ያመኑትን ባገኙ ጊዜ «አምነናል» ይላሉ፡፡ ከፊላቸውም ወደ ከፊሉ ባገለለ «ጊዜ አላህ በናንተ ላይ በገለጸላችሁ ነገር እጌታችሁ ዘንድ በርሱ እንዲከራከሩዋችሁ ትነግሩዋቸዋላችሁን? አታውቁምን?» ይላሉ፡፡

وَإِذَا لَقُوا۟ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ قَالُوٓا۟ ءَامَنَّا وَإِذَا خَلَا بَعْضُهُمْ إِلَىٰ بَعْضٍ قَالُوٓا۟ أَتُحَدِّثُونَهُم بِمَا فَتَحَ ٱللَّهُ عَلَيْكُمْ لِيُحَآجُّوكُم بِهِۦ عِندَ رَبِّكُمْ ۚ أَفَلَا تَعْقِلُونَ ﴿٧٦﴾

77. አላህ የሚደብቁትንና የሚገልጹትን የሚያውቅ መኾኑን አያውቁምን?

أَوَلَا يَعْلَمُونَ أَنَّ ٱللَّهَ يَعْلَمُ مَا يُسِرُّونَ وَمَا يُعْلِنُونَ ﴿٧٧﴾

78. ከነሱም መጽሐፉን የማያውቁ መሃይማናን አሉ፡፡ ግን ከንቱ ምኞቶችን (ይመኛሉ)፤ እነርሱም የሚጠራጠሩ እንጂ ሌላ አይደሉም፡፡

وَمِنْهُمْ أُمِّيُّونَ لَا يَعْلَمُونَ ٱلْكِتَٰبَ إِلَّآ أَمَانِىَّ وَإِنْ هُمْ إِلَّا يَظُنُّونَ ﴿٧٨﴾

79. ለነዚያም መጽሐፉን በእጆቻቸው ለሚጽፉና ከዚያም በርሱ ጥቂትን ዋጋ ሊገዙበት «ይህ ከአላህ ዘንድ ነው» ለሚሉ ወዮላቸው፡፡ ለነርሱም ከዚያ እጆቻቸው ከጻፉት ወዮላቸው፡፡ ለነሱም ከዚያ ከሚያፈሩት (ኃጢአት) ወዮላቸው፡፡

فَوَيْلٌ لِّلَّذِينَ يَكْتُبُونَ ٱلْكِتَٰبَ بِأَيْدِيهِمْ ثُمَّ يَقُولُونَ هَٰذَا مِنْ عِندِ ٱللَّهِ لِيَشْتَرُوا۟ بِهِۦ ثَمَنًا قَلِيلًا ۖ فَوَيْلٌ لَّهُم مِّمَّا كَتَبَتْ أَيْدِيهِمْ وَوَيْلٌ لَّهُم مِّمَّا يَكْسِبُونَ ﴿٧٩﴾

80. «እሳትም የተቆጠሩን ቀኖች እንጂ አትነካንም» አሉ፡፡ «አላህ ዘንድ ቃል ኪዳን ይዛችኋልን? (ይህ ከኾነ) አላህም ኪዳኑን አያፈርስም፤ በእውነቱ በአላህ ላይ የማታውቁትን ትናገራላችሁ» በላቸው፡፡

وَقَالُوا۟ لَن تَمَسَّنَا ٱلنَّارُ إِلَّآ أَيَّامًا مَّعْدُودَةً ۚ قُلْ أَتَّخَذْتُمْ عِندَ ٱللَّهِ عَهْدًا فَلَن يُخْلِفَ ٱللَّهُ عَهْدَهُۥٓ ۖ أَمْ تَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعْلَمُونَ ﴿٨٠﴾

81. አይደለም (ትነካችኋለች)፤ መጥፎን (ክሕደትን) የሠራ በርሱም ኃጢአቱ የከበበችው ሰው እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

بَلَىٰۚ مَن كَسَبَ سَيِّئَةٗ وَأَحَٰطَتۡ بِهِۦ خَطِيٓـَٔتُهُۥ فَأُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٨١

82. እነዚያም ያመኑት በጎ ሥራዎችንም የሠሩት እነዚያ የገነት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጧ ዘላለም ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٨٢

83. የእስራኤል ልጆችንም ጥብቅ ኪዳን አላህን እንጂ ሌላን አታምልኩ፤ በወላጆችም በጎን ሥራ (አድርጉ)፤ በዝምድና ባለቤቶችም፣ በየቲሞችም (አባት የሌላቸው ልጆች) በምስኪኖችም (በጎ ዋሉ)፤ ለሰዎችም መልካምን ተናገሩ፤ ሶላትንም ደንቡን ጠብቃችሁ ስገዱ፤ ዘካንም ስጡ በማለት በያዝንባቸው ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ ከዚያም ከናንተ ጥቂቶች ሲቀሩ ሸሻችሁ እናንተም (ኪዳንን) የምትተዉ ናችሁ፡፡

وَإِذۡ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ لَا تَعۡبُدُونَ إِلَّا ٱللَّهَ وَبِٱلۡوَٰلِدَيۡنِ إِحۡسَانٗا وَذِي ٱلۡقُرۡبَىٰ وَٱلۡيَتَٰمَىٰ وَٱلۡمَسَٰكِينِ وَقُولُواْ لِلنَّاسِ حُسۡنٗا وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُواْ ٱلزَّكَوٰةَ ثُمَّ تَوَلَّيۡتُمۡ إِلَّا قَلِيلٗا مِّنكُمۡ وَأَنتُم مُّعۡرِضُونَ ٨٣

84. ደሞቻችሁን አታፍስሱ ነፍሶቻችሁንም (ከፊላችሁን) ከአገሮቻችሁ አታውጡ የምንል ስንኾን የጠበቀ ቃል ኪዳናችሁን በያዝንባችሁ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ ከዚያም (በኪዳኑ) አረጋገጣችሁ፤ እናንተም ትመሰክራላችሁ፡፡

وَإِذۡ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَكُمۡ لَا تَسۡفِكُونَ دِمَآءَكُمۡ وَلَا تُخۡرِجُونَ أَنفُسَكُم مِّن دِيَٰرِكُمۡ ثُمَّ أَقۡرَرۡتُمۡ وَأَنتُمۡ تَشۡهَدُونَ ٨٤

85. ከዚያም እናንተ እነዚያ ነፍሶቻችሁን የምትገድሉ ከናንተም የኾኑ ጭፍሮችን በኃጢአትና በመበደል በነርሱ ላይ የምትረዳዱ ስትኾኑ ከአገሮቻቸው የምታወጡ ምርኮኞችም ኾነው ቢመጡዋችሁ የምትበዡ ናችሁ፡፡ እርሱ (ነገሩ) እነርሱን ማውጣት በእናንተ ላይ የተከለከለ ነው፡፡ በመጽሐፉ ከፊል ታምናላችሁን? በከፊሉም ትክዳላችሁን? ከእናንተም ይህንን የሚሠራ ሰው ቅጣት በቅርቢቱ ሕይወት ውርደት እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ በትንሣኤ ቀንም ወደ ብርቱ ቅጣት ይመለሳሉ፡፡ አላህም ከምትሠሩት ሥራ ሁሉ ዘንጊ አይደለም፡፡

ثُمَّ أَنتُمۡ هَٰٓؤُلَآءِ تَقۡتُلُونَ أَنفُسَكُمۡ وَتُخۡرِجُونَ فَرِيقٗا مِّنكُم مِّن دِيَٰرِهِمۡ تَظَٰهَرُونَ عَلَيۡهِم بِٱلۡإِثۡمِ وَٱلۡعُدۡوَٰنِ وَإِن يَأۡتُوكُمۡ أُسَٰرَىٰ تُفَٰدُوهُمۡ وَهُوَ مُحَرَّمٌ عَلَيۡكُمۡ إِخۡرَاجُهُمۡۚ أَفَتُؤۡمِنُونَ بِبَعۡضِ ٱلۡكِتَٰبِ وَتَكۡفُرُونَ بِبَعۡضٖۚ فَمَا جَزَآءُ مَن يَفۡعَلُ ذَٰلِكَ مِنكُمۡ إِلَّا خِزۡيٞ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَيَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ يُرَدُّونَ إِلَىٰٓ أَشَدِّ ٱلۡعَذَابِۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ٨٥

86. እነዚህ እነዚያ ቅርቢቱን ሕይወት በመጨረሻይቱ አገር የገዙ ናቸው፡፡ ከነሱም ቅጣቱ አይቀልላቸውም፤ እነሱም አይርረዱም፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ ٱشۡتَرَوُاْ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا بِٱلۡأٓخِرَةِۖ فَلَا يُخَفَّفُ عَنۡهُمُ ٱلۡعَذَابُ وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ٨٦

87. ሙሳንም መጽሐፍን በእርግጥ ሰጠነው፡፡ ከበኋላውም መልክተኞችን አስከታተልን፡፡ የመርየምን ልጅ ዒሳንም ግልጽ ታምራቶችን ሰጠነው፡፡ በቅዱሱ መንፈስም አበረታነው፡፡ ነፍሶቻችሁ በማትወደው ነገር መልክተኛ በመጣላችሁ ቁጥር (ከመከተል) ትኮራላችሁን? ከፊሉን አስተባበላችሁ፤ ከፊሉንም ትገድላላችሁ፡፡

وَلَقَدْ ءَاتَيْنَا مُوسَى ٱلْكِتَٰبَ وَقَفَّيْنَا مِنۢ بَعْدِهِۦ بِٱلرُّسُلِ ۖ وَءَاتَيْنَا عِيسَى ٱبْنَ مَرْيَمَ ٱلْبَيِّنَٰتِ وَأَيَّدْنَٰهُ بِرُوحِ ٱلْقُدُسِ ۗ أَفَكُلَّمَا جَآءَكُمْ رَسُولٌۢ بِمَا لَا تَهْوَىٰٓ أَنفُسُكُمُ ٱسْتَكْبَرْتُمْ فَفَرِيقًا كَذَّبْتُمْ وَفَرِيقًا تَقْتُلُونَ ﴿٨٧﴾

88. «ልቦቻችንም ሽፍኖች ናቸው» አሉ፤ አይደለም አላህ በክሕደታቸው ምክንያት ረገማቸው ጥቂትንም ብቻ ያምናሉ፡፡

وَقَالُوا۟ قُلُوبُنَا غُلْفٌۢ ۚ بَل لَّعَنَهُمُ ٱللَّهُ بِكُفْرِهِمْ فَقَلِيلًا مَّا يُؤْمِنُونَ ﴿٨٨﴾

89. ከነሱም ጋር ያለውን (መጽሐፍ) አረጋጋጭ የኾነ መጽሐፍ ከአላህ ዘንድ በመጣላቸው ጊዜ (ከመምጣቱ) በፊት በነዚያ በካዱት ላይ ይረዱበት የነበሩ ሲኾኑ ያወቁት ነገር በመጣላቸው ጊዜ በርሱ ካዱ፡፡ የአላህም ርግማን በከሓዲዎች ላይ ይኹን፡፡

وَلَمَّا جَآءَهُمْ كِتَٰبٌ مِّنْ عِندِ ٱللَّهِ مُصَدِّقٌ لِّمَا مَعَهُمْ وَكَانُوا۟ مِن قَبْلُ يَسْتَفْتِحُونَ عَلَى ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ فَلَمَّا جَآءَهُم مَّا عَرَفُوا۟ كَفَرُوا۟ بِهِۦ ۚ فَلَعْنَةُ ٱللَّهِ عَلَى ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿٨٩﴾

90. ነፍሶቻቸውን በርሱ የሸጡበት ነገር ከፋ! (እርሱም) አላህ ከባሮቹ በሚሻው ሰው ላይ ከችሮታው (ራእይን) ማውረዱን በመመቅኘት አላህ ባወረደው ነገር መካዳቸው ነው፡፡ በቁጣ ላይም ቁጣ (የተረጋገጠባቸው ሲኾኑ) ተመለሱ፡፡ ለከሓዲዎችም አዋራጅ ቅጣት አላቸው፡፡

بِئْسَمَا ٱشْتَرَوْا۟ بِهِۦٓ أَنفُسَهُمْ أَن يَكْفُرُوا۟ بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ بَغْيًا أَن يُنَزِّلَ ٱللَّهُ مِن فَضْلِهِۦ عَلَىٰ مَن يَشَآءُ مِنْ عِبَادِهِۦ ۖ فَبَآءُو بِغَضَبٍ عَلَىٰ غَضَبٍ ۚ وَلِلْكَٰفِرِينَ عَذَابٌ مُّهِينٌ ﴿٩٠﴾

91. አላህም ባወረደው (ሁሉ) ለእነርሱ «እመኑ» በተባሉ ጊዜ «በኛ ላይ በተወረደው (መጽሐፍ ብቻ) እናምናለን» ይላሉ፡፡ ከርሱ ኋላ ባለው (ቁርአን) እርሱ ከነሱ ጋር ላለው (መጽሐፍ) አረጋጋጭ እውተኛ ሲኾን ይክዳሉ፡፡ «አማኞች ከኾናችሁ ከአሁን በፊት የአላህን ነቢያት ለምን ገደላችሁ?» በላቸው፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمْ ءَامِنُوا۟ بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ قَالُوا۟ نُؤْمِنُ بِمَآ أُنزِلَ عَلَيْنَا وَيَكْفُرُونَ بِمَا وَرَآءَهُۥ وَهُوَ ٱلْحَقُّ مُصَدِّقًا لِّمَا مَعَهُمْ ۗ قُلْ فَلِمَ تَقْتُلُونَ أَنۢبِيَآءَ ٱللَّهِ مِن قَبْلُ إِن كُنتُم مُّؤْمِنِينَ ﴿٩١﴾

92. ሙሳም በታምራቶች በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ ከዚያም ከበኋላው እናንተ በዳዮች ስትኾኑ ወይፈንን (አምላክ አድርጋችሁ) ያዛችሁ፡፡

۞ وَلَقَدْ جَآءَكُم مُّوسَىٰ بِٱلْبَيِّنَٰتِ ثُمَّ ٱتَّخَذْتُمُ ٱلْعِجْلَ مِنۢ بَعْدِهِۦ وَأَنتُمْ ظَٰلِمُونَ ﴿٩٢﴾

93. የጡርንም ጋራ ከበላያችሁ ያነሳን ስንኾን (በኦሪት ሕግ እንድትሠሩ) ኪዳናችሁን በያዝን ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ «የሰጠናችሁን በኀይል ያዙ፤ ስሙም፤ » (አልን)፡፡«ሰማን አመጽንም» አሉ፡፡ የወይፈኑንም ውዴታ በክሕደታቸው ምክንያት በልቦቻቸው ውስጥ ተጠጡ፡፡ «አማኞች እንደኾናችሁ እምነታችሁ በርሱ የሚያዛችሁ ነገር ከፋ!» በላቸው፡፡

وَإِذۡ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَكُمۡ وَرَفَعۡنَا فَوۡقَكُمُ ٱلطُّورَ خُذُواْ مَآ ءَاتَيۡنَٰكُم بِقُوَّةٖ وَٱسۡمَعُواْۖ قَالُواْ سَمِعۡنَا وَعَصَيۡنَا وَأُشۡرِبُواْ فِي قُلُوبِهِمُ ٱلۡعِجۡلَ بِكُفۡرِهِمۡۚ قُلۡ بِئۡسَمَا يَأۡمُرُكُم بِهِۦٓ إِيمَٰنُكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ٩٣

94. «የመጨረሻይቱ አገር (ገነት) አላህ ዘንድ ከሰው ሁሉ ሌላ የተለየች ስትኾን ለእናንተ ብቻ እንደኾነች እውነተኞች ከኾናችሁ ሞትን ተመኙ» በላቸው፡፡

قُلۡ إِن كَانَتۡ لَكُمُ ٱلدَّارُ ٱلۡأٓخِرَةُ عِندَ ٱللَّهِ خَالِصَةٗ مِّن دُونِ ٱلنَّاسِ فَتَمَنَّوُاْ ٱلۡمَوۡتَ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٩٤

95. እጆቻቸውም ባሳለፉት (በሠሩት) ምክንያት ምን ጊዜም ፈጽሞ አይመኙትም፤ አላህም በዳዮችን ዐዋቂ ነው፡፡

وَلَن يَتَمَنَّوۡهُ أَبَدَۢا بِمَا قَدَّمَتۡ أَيۡدِيهِمۡۚ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِٱلظَّٰلِمِينَ ٩٥

96. ከሰዎችም ሁሉ ከእነዚያም (ጣዖትን) ከአጋሩት ይበልጥ በሕይወት ላይ የሚጓጉ ኾነው በእርግጥ ታገኛቸዋለህ፡፡ አንዳቸው ሺሕ ዓመት ዕድሜ ቢሰጥ ይወዳል፡፡ እርሱም ዕድሜ መሰጠቱ ከቅጣት የሚያርቀው አይደለም፡፡ አላህም የሚሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

وَلَتَجِدَنَّهُمۡ أَحۡرَصَ ٱلنَّاسِ عَلَىٰ حَيَوٰةٖ وَمِنَ ٱلَّذِينَ أَشۡرَكُواْۚ يَوَدُّ أَحَدُهُمۡ لَوۡ يُعَمَّرُ أَلۡفَ سَنَةٖ وَمَا هُوَ بِمُزَحۡزِحِهِۦ مِنَ ٱلۡعَذَابِ أَن يُعَمَّرَۗ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِمَا يَعۡمَلُونَ ٩٦

97. ለጂብሪል (ለገብርኤል) ጠላት የኾነ ሰው (በቁጭት ይሙት) በላቸው፡፡ እርሱ (ቁርኣኑን) ከበፊቱ ለነበሩት (መጻሕፍት) አረጋጋጭ ለምእመናን መሪና ብስራት ሲኾን በአላህ ፈቃድ በልብህ ላይ አውርዶታልና፡፡

قُلۡ مَن كَانَ عَدُوّٗا لِّجِبۡرِيلَ فَإِنَّهُۥ نَزَّلَهُۥ عَلَىٰ قَلۡبِكَ بِإِذۡنِ ٱللَّهِ مُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ وَهُدٗى وَبُشۡرَىٰ لِلۡمُؤۡمِنِينَ ٩٧

98. ለአላህና ለመላእክቱ ለመልክተኞቹም ለጂብሪልም ለሚካልም (ሚካኤል) ጠላት የኾነ ሰው አላህ ለ(እነዚህ) ከሓዲዎች ጠላት ነው፡፡

مَن كَانَ عَدُوّٗا لِّلَّهِ وَمَلَٰٓئِكَتِهِۦ وَرُسُلِهِۦ وَجِبۡرِيلَ وَمِيكَىٰلَ فَإِنَّ ٱللَّهَ عَدُوّٞ لِّلۡكَٰفِرِينَ ٩٨

99. ወዳንተም ግልጽ የኾኑትን አንቀጾች በእርግጥ አውርደናል፡፡ በርሷም አመጸኞች እንጂ ሌላው አይክድም፤

وَلَقَدۡ أَنزَلۡنَآ إِلَيۡكَ ءَايَٰتِۭ بَيِّنَٰتٖۖ وَمَا يَكۡفُرُ بِهَآ إِلَّا ٱلۡفَٰسِقُونَ ٩٩

100. ቃል ኪዳንንም ቃል በገቡ ቁጥር ከእነርሱ ከፊሉ ይጥለዋልን? (ያፈርሰዋልን?)፤ ይልቁንም አብዛኞቻቸው አያምኑም፡፡

أَوَكُلَّمَا عَٰهَدُواْ عَهۡدٗا نَّبَذَهُۥ فَرِيقٞ مِّنۡهُمۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ١٠٠

101. እነርሱ ጋርም ላለው (መጽሐፍ) አረጋጋጭ የኾነ መልክተኛ ከአላህ ዘንድ በመጣላቸው ጊዜ ከነዚያ መጽሐፍን ከተሰጡት ከፊሉ እነርሱ እንደማያውቁ ኾነው የአላህን መጽሐፍ ከጀርባዎቻቸው ኋላ ጣሉ፡፡

وَلَمَّا جَآءَهُمۡ رَسُولٞ مِّنۡ عِندِ ٱللَّهِ مُصَدِّقٞ لِّمَا مَعَهُمۡ نَبَذَ فَرِيقٞ مِّنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ كِتَٰبَ ٱللَّهِ وَرَآءَ ظُهُورِهِمۡ كَأَنَّهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ﴿١٠١﴾

102. ሰይጣናትም በሱለይማን (ሰሎሞን) ዘመነ መንግስት የሚያነቡትን (ድግምት) ተከተሉ፡፡ ሱለይማንም አልካደም፤ (ድግምተኛ አልነበረም)፤ ግን ሰይጣናት ሰዎችን ድግምትን የሚያስተምሩ ሲኾኑ ካዱ፡፡ ያንንም በባቢል በሁለቱ መላእክት በሃሩትና ማሩት ላይ የተወረደውን ነገር (ያስተምሩዋቸዋል)፡፡ «እኛ መፈተኛ ነንና አትካድ» እስከሚሉም ድረስ አንድንም አያስተምሩም፡፡ ከእነሱም በሰውየውና በሚስቱ መካከል በርሱ የሚለዩበትን ነገር ይማራሉ፡፡ እነርሱም በአላህ ፈቃድ ካልኾነ በርሱ አንድንም ጎጂዎች አይደሉም፡፡ የሚጎዳቸውንና የማይጠቅማቸውንም ይማራሉ፡፡ የገዛውም ሰው ለርሱ በመጨረሻይቱ አገር ምንም እድል የሌለው መኾኑን በእርግጥ ዐወቁ፡፡ ነፍሶቻቸውንም በርሱ የሸጡበት ዋጋ ከፋ! የሚያውቁ በኾኑ ኖሮ (ባልሠሩት ነበር)፡፡

وَٱتَّبَعُواْ مَا تَتۡلُواْ ٱلشَّيَٰطِينُ عَلَىٰ مُلۡكِ سُلَيۡمَٰنَۖ وَمَا كَفَرَ سُلَيۡمَٰنُ وَلَٰكِنَّ ٱلشَّيَٰطِينَ كَفَرُواْ يُعَلِّمُونَ ٱلنَّاسَ ٱلسِّحۡرَ وَمَآ أُنزِلَ عَلَى ٱلۡمَلَكَيۡنِ بِبَابِلَ هَٰرُوتَ وَمَٰرُوتَۚ وَمَا يُعَلِّمَانِ مِنۡ أَحَدٍ حَتَّىٰ يَقُولَآ إِنَّمَا نَحۡنُ فِتۡنَةٞ فَلَا تَكۡفُرۡۖ فَيَتَعَلَّمُونَ مِنۡهُمَا مَا يُفَرِّقُونَ بِهِۦ بَيۡنَ ٱلۡمَرۡءِ وَزَوۡجِهِۦۚ وَمَا هُم بِضَآرِّينَ بِهِۦ مِنۡ أَحَدٍ إِلَّا بِإِذۡنِ ٱللَّهِۚ وَيَتَعَلَّمُونَ مَا يَضُرُّهُمۡ وَلَا يَنفَعُهُمۡۚ وَلَقَدۡ عَلِمُواْ لَمَنِ ٱشۡتَرَىٰهُ مَا لَهُۥ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ مِنۡ خَلَٰقٖۚ وَلَبِئۡسَ مَا شَرَوۡاْ بِهِۦٓ أَنفُسَهُمۡۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ﴿١٠٢﴾

103. እነርሱም (አይሁዶች) ባመኑና በተጠነቀቁ ኖሮ (በተመነዱ ነበር)፡፡ የሚያውቁ ቢኾኑ ከአላህ ዘንድ የኾነው ምንዳ (ነፍሶቻቸውን ከሚሸጡበት) በላጭ ነው፡፤

وَلَوۡ أَنَّهُمۡ ءَامَنُواْ وَٱتَّقَوۡاْ لَمَثُوبَةٞ مِّنۡ عِندِ ٱللَّهِ خَيۡرٞۚ لَّوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ﴿١٠٣﴾

104. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! (ለነቢዩ) ራዒና አትበሉ፡፡ ተመለከትን በሉም፡፡ ስሙም፤ ለከሓዲዎችም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَقُولُواْ رَٰعِنَا وَقُولُواْ ٱنظُرۡنَا وَٱسۡمَعُواْۗ وَلِلۡكَٰفِرِينَ عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿١٠٤﴾

105. እነዚያ ከመጽሐፉ ባለቤቶችና ከአጋሪዎቹም የካዱት በናንተ ላይ ከጌታችሁ የኾነ መልካም ነገር መወረዱን አይወዱም፡፡ አላህም በችሮታው (በነቢይነት) የሚሻውን ይመርጣል፡፡ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

مَّا يَوَدُّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ وَلَا ٱلۡمُشۡرِكِينَ أَن يُنَزَّلَ عَلَيۡكُم مِّنۡ خَيۡرٖ مِّن رَّبِّكُمۡۚ وَٱللَّهُ يَخۡتَصُّ بِرَحۡمَتِهِۦ مَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ ذُو ٱلۡفَضۡلِ ٱلۡعَظِيمِ ﴿١٠٥﴾

106. ከአንቀጽ ብንለውጥ ወይም እርሷን ብናስረሳህ ከርሷ የሚበልጥን ወይም ብጤዋን እናመጣለን፤ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ከሃሊ (ቻይ) መኾኑን አታውቅምን?

۞مَا نَنسَخۡ مِنۡ ءَايَةٍ أَوۡ نُنسِهَا نَأۡتِ بِخَيۡرٖ مِّنۡهَآ أَوۡ مِثۡلِهَآۗ أَلَمۡ تَعۡلَمۡ أَنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ﴿١٠٦﴾

107. አላህ የሰማያትና የምድር ንግሥና ለርሱ ብቻ መኾኑን አታውቅምን? ለእናንተም ከአላህ ሌላ ዘመድና ረዳት ምንም የላችሁም፡፡

أَلَمۡ تَعۡلَمۡ أَنَّ ٱللَّهَ لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۗ وَمَا لَكُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ مِن وَلِيّٖ وَلَا نَصِيرٍ ﴿١٠٧﴾

108. በእውነቱ ከአሁን በፊት ሙሳ እንደተጠየቀ ብጤ መልክተኛችሁን ልትጠይቁ ትፈልጋላችሁን? በእምነትም ክህደትን የሚለውጥ ሰው ትክክለኛውን መንገድ በእርግጥ ተሳሳተ::

أَمْ تُرِيدُونَ أَن تَسْـَٔلُوا۟ رَسُولَكُمْ كَمَا سُئِلَ مُوسَىٰ مِن قَبْلُ ۗ وَمَن يَتَبَدَّلِ ٱلْكُفْرَ بِٱلْإِيمَٰنِ فَقَدْ ضَلَّ سَوَآءَ ٱلسَّبِيلِ ﴿١٠٨﴾

109. ከመጽሐፉ ባለቤቶች ብዙዎች እውነቱ ከተገለጸላቸው በኋላ ከነፍሶቻቸው በኾነው ምቀኝነት ከእምነታችሁ በኋላ ከሓዲዎች አድርገው ሊመልሱዋችሁ ተመኙ:: አላህም ትዕዛዙን እስከሚያመጣ ድረስ ይቅርታ አድርጉ፤ እለፉቸውም:: አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ከሃሊ ነውና::

وَدَّ كَثِيرٌ مِّنْ أَهْلِ ٱلْكِتَٰبِ لَوْ يَرُدُّونَكُم مِّنۢ بَعْدِ إِيمَٰنِكُمْ كُفَّارًا حَسَدًا مِّنْ عِندِ أَنفُسِهِم مِّنۢ بَعْدِ مَا تَبَيَّنَ لَهُمُ ٱلْحَقُّ ۖ فَٱعْفُوا۟ وَٱصْفَحُوا۟ حَتَّىٰ يَأْتِىَ ٱللَّهُ بِأَمْرِهِۦٓ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿١٠٩﴾

110. ሶላትንም አስተካክላችሁ ስገዱ:: ዘካንም ስጡ:: ለነፍሶቻችሁም ከበጎ ሥራ የምታስቀድሙትን አላህ ዘንድ ታገኙታላችሁ:: አላህ የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነውና::

وَأَقِيمُوا۟ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُوا۟ ٱلزَّكَوٰةَ ۚ وَمَا تُقَدِّمُوا۟ لِأَنفُسِكُم مِّنْ خَيْرٍ تَجِدُوهُ عِندَ ٱللَّهِ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ بِمَا تَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ﴿١١٠﴾

111. «ገነትንም አይሁድን ወይም ክርስቲያኖችን የኾነ ሰው እንጂ ሌላ አይገባትም» አሉ:: ይህቺ (ከንቱ) ምኞታቸው ናት:: «እውነተኞች እንደኾናችሁ አስረጃችሁን አምጡ» በላቸው::

وَقَالُوا۟ لَن يَدْخُلَ ٱلْجَنَّةَ إِلَّا مَن كَانَ هُودًا أَوْ نَصَٰرَىٰ ۗ تِلْكَ أَمَانِيُّهُمْ ۗ قُلْ هَاتُوا۟ بُرْهَٰنَكُمْ إِن كُنتُمْ صَٰدِقِينَ ﴿١١١﴾

112. አይደለም (ሌላውም ይገባታል) እርሱ በጎ ሠሪ ኾኖ ፊቱን ለአላህ የሰጠ ሰው ለርሱ በጌታው ዘንድ ምንዳው አለው:: በነሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነሱም አያዝኑም::

بَلَىٰ مَنْ أَسْلَمَ وَجْهَهُۥ لِلَّهِ وَهُوَ مُحْسِنٌ فَلَهُۥٓ أَجْرُهُۥ عِندَ رَبِّهِۦ وَلَا خَوْفٌ عَلَيْهِمْ وَلَا هُمْ يَحْزَنُونَ ﴿١١٢﴾

113. እነርሱ መጽሐፉን የሚያነቡ ሲኾኑ አይሁዶች:- ክርስቲያኖች በምንም ላይ አይደሉም አሉ:: ክርስቲያኖችም:- አይሁዶች በምንም ላይ አይደሉም አሉ:: እንደዚሁ እነዚያ የማያውቁት (አጋሪዎች) የንግግራቸውን ብጤ አሉ:: አላህም በዚያ በርሱ ይለያዩበት በነበሩት ነገር በትንሣኤ ቀን በመካከላቸው ይፈርዳል::

وَقَالَتِ ٱلْيَهُودُ لَيْسَتِ ٱلنَّصَٰرَىٰ عَلَىٰ شَىْءٍ وَقَالَتِ ٱلنَّصَٰرَىٰ لَيْسَتِ ٱلْيَهُودُ عَلَىٰ شَىْءٍ وَهُمْ يَتْلُونَ ٱلْكِتَٰبَ ۗ كَذَٰلِكَ قَالَ ٱلَّذِينَ لَا يَعْلَمُونَ مِثْلَ قَوْلِهِمْ ۚ فَٱللَّهُ يَحْكُمُ بَيْنَهُمْ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ فِيمَا كَانُوا۟ فِيهِ يَخْتَلِفُونَ ﴿١١٣﴾

114. የአላህንም መስጊዶች በውስጣቸው ስሙ እንዳይወሳ ከከለከለና እርሷንም በማበላሸት ከሮጠ ሰው ይበልጥ በዳይ ማነው? እነዚያ ፈሪዎች ኾነው እንጂ ለእነርሱ በቅርቢቱ ዓለም ውርደት አላቸው:: ለነርሱም በመጨረሻይቱ አገር ታላቅ ቅጣት አላቸው::

وَمَنْ أَظْلَمُ مِمَّن مَّنَعَ مَسَٰجِدَ ٱللَّهِ أَن يُذْكَرَ فِيهَا ٱسْمُهُۥ وَسَعَىٰ فِى خَرَابِهَآ ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ مَا كَانَ لَهُمْ أَن يَدْخُلُوهَآ إِلَّا خَآئِفِينَ ۚ لَهُمْ فِى ٱلدُّنْيَا خِزْىٌ وَلَهُمْ فِى ٱلْءَاخِرَةِ عَذَابٌ عَظِيمٌ ﴿١١٤﴾

115. ምሥራቁም ምዕራቡም የአላህ ነው (ፊቶቻችሁን) ወደ የትም ብታዞሩ የአላህ ፊት እዚያ ነው፡፡ አላህ ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَلِلَّهِ ٱلۡمَشۡرِقُ وَٱلۡمَغۡرِبُۚ فَأَيۡنَمَا تُوَلُّواْ فَثَمَّ وَجۡهُ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ وَٰسِعٌ عَلِيمٌ ١١٥

116. አላህም ልጅ አለው አሉ፡፡ (ከሚሉት) ጥራት ተገባው፡፡ አይደለም በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የርሱ ነው፡፡ ሁሉም ለርሱ ታዛዦች ናቸው፡፡

وَقَالُواْ ٱتَّخَذَ ٱللَّهُ وَلَدٗاۗ سُبۡحَٰنَهُۥۖ بَل لَّهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ كُلٌّ لَّهُۥ قَٰنِتُونَ ١١٦

117. ሰማያትንና ምድርን ያለብጤ ፈጣሪ ነው፤ ነገርንም (ማስገኘት) በሻ ጊዜ ለርሱ የሚለው፡- «ኹን ነው፤» ወዲያውም ይኾናል፡፡

بَدِيعُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَإِذَا قَضَىٰٓ أَمۡرٗا فَإِنَّمَا يَقُولُ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ١١٧

118. እነዚያም የማያውቁት (አንተ መልክተኛ ስለመኾንህ) አላህ አያናግረንም ኖሮአልን? ወይም (ለእውነተኛነትህ) ታምር አትመጣልንም ኖሮአልን? አሉ፡፡ እንደዚሁ እነዚያ ከነሱ በፊት የነበሩት እንደ ንግግራቸው ብጤ ብለዋል፡፡ ልቦቻቸው (በክሕደት) ተመሳሰሉ፡፡ ለሚያረጋግጡ ሕዝቦች አንቀጾችን በእርግጥ አብራርተናል፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ لَا يَعۡلَمُونَ لَوۡلَا يُكَلِّمُنَا ٱللَّهُ أَوۡ تَأۡتِينَآ ءَايَةٞۗ كَذَٰلِكَ قَالَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِم مِّثۡلَ قَوۡلِهِمۡۘ تَشَٰبَهَتۡ قُلُوبُهُمۡۗ قَدۡ بَيَّنَّا ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يُوقِنُونَ ١١٨

119. እኛ አብሳሪና አስፈራሪ ኾነህ በውነት ላክንህ፡፡ ከእሳትም ጓዶች አትጠየቅም፡፡

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَٰكَ بِٱلۡحَقِّ بَشِيرٗا وَنَذِيرٗاۖ وَلَا تُسۡـَٔلُ عَنۡ أَصۡحَٰبِ ٱلۡجَحِيمِ ١١٩

120. አይሁዶችና ክርስቲያኖችም ሃይማኖታቸውን እስከምትከተል ድረስ ካንተ ፈጽሞ አይወዱም፡፡ «የአላህ መምራት (ትክክለኛው) መምራት እርሱ ብቻ ነው» በላቸው፡፡ ከዚያም እውቀቱ ከመጣልህ በኋላ ዝንባሌያቸውን ብትከተል ለአንተ ከአላህ (የሚከለክልልህ) ዘመድና ረዳት ምንም የለህም፡፡

وَلَن تَرۡضَىٰ عَنكَ ٱلۡيَهُودُ وَلَا ٱلنَّصَٰرَىٰ حَتَّىٰ تَتَّبِعَ مِلَّتَهُمۡۗ قُلۡ إِنَّ هُدَى ٱللَّهِ هُوَ ٱلۡهُدَىٰۗ وَلَئِنِ ٱتَّبَعۡتَ أَهۡوَآءَهُم بَعۡدَ ٱلَّذِي جَآءَكَ مِنَ ٱلۡعِلۡمِ مَا لَكَ مِنَ ٱللَّهِ مِن وَلِيّٖ وَلَا نَصِيرٍ ١٢٠

121. እነዚያ መጽሐፉን የሰጠናቸው ተገቢ ንባቡን ያነቡታል፡፡ እነዚያ በርሱ ያምናሉ፤ በርሱም የሚክዱ እነዚያ እነርሱ ከሳሪዎቹ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يَتۡلُونَهُۥ حَقَّ تِلَاوَتِهِۦٓ أُوْلَٰٓئِكَ يُؤۡمِنُونَ بِهِۦۗ وَمَن يَكۡفُرۡ بِهِۦ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ١٢١

122. የእስራኤል ልጆች ሆይ! ያችን በናንተ ላይ የለገስኳትን ጸጋዬንና እኔም በዓለማት ላይ ያበለጥኳችሁ መኾኔን አስታውሱ፡፡

يَٰبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتِيَ ٱلَّتِيٓ أَنۡعَمۡتُ عَلَيۡكُمۡ وَأَنِّي فَضَّلۡتُكُمۡ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٢٢

123. (አማኝ) ነፍስም ከ(ከሓዲ) ነፍስ ምንንም የማትጠቅምበትን፣ ከርሷም ቤዛ የማይወሰድበትን፣ ምልጃም ለርሷ የማትጠቅምበትን፣ እነርሱም የማይረዱበትን ቀን ተጠንቀቁ፡፡

وَٱتَّقُواْ يَوۡمٗا لَّا تَجۡزِي نَفۡسٌ عَن نَّفۡسٖ شَيۡـٔٗا وَلَا يُقۡبَلُ مِنۡهَا عَدۡلٞ وَلَا تَنفَعُهَا شَفَٰعَةٞ وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ١٢٣

124. ኢብራሂምንም ጌታው በቃላት (በሕግጋት) በፈተነውና በፈጸማቸው ጊዜ (አስታውስ)፤ «እኔ ለሰዎች መሪ አድራጊህ ነኝ» አለው፡፡ «ከዘሮቼም (አድርግ)» አለ፡፡ ቃል ኪዳኔ በዳዮቹን አያገኝም አለው፡፡

۞وَإِذِ ٱبْتَلَىٰٓ إِبْرَٰهِـۧمَ رَبُّهُۥ بِكَلِمَٰتٍ فَأَتَمَّهُنَّ ۖ قَالَ إِنِّى جَاعِلُكَ لِلنَّاسِ إِمَامًا ۖ قَالَ وَمِن ذُرِّيَّتِى ۖ قَالَ لَا يَنَالُ عَهْدِى ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٢٤﴾

125. ቤቱንም ለሰዎች መመለሻና ጸጥተኛ ባደረግን ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ከኢብራሂምም መቆሚያ መስገጃን አድርጉ፡፡ ወደ ኢብራሂምና ወደ ኢስማዒልም ቤቴን ለዘዋሪዎቹና ለተቀማጮቹም ለአጎንባሾች ሰጋጆቹም አጥሩ ስንል ቃል ኪዳን ያዝን፡፡

وَإِذْ جَعَلْنَا ٱلْبَيْتَ مَثَابَةً لِّلنَّاسِ وَأَمْنًا وَٱتَّخِذُوا۟ مِن مَّقَامِ إِبْرَٰهِـۧمَ مُصَلًّى ۖ وَعَهِدْنَآ إِلَىٰٓ إِبْرَٰهِـۧمَ وَإِسْمَٰعِيلَ أَن طَهِّرَا بَيْتِىَ لِلطَّآئِفِينَ وَٱلْعَٰكِفِينَ وَٱلرُّكَّعِ ٱلسُّجُودِ ﴿١٢٥﴾

126. ኢብራሂም ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ጌታዬ ሆይ! ይህንን ጸጥተኛ አገር አድርግ፡፡ ቤተሰቦቹንም ከነሱ በአላህና በመጨረሻው ቀን ያመነውን ሰው ከፍሬዎች ስጠው፡፡ (አላህም) የካደውንም ሰው፤ (እሰጠዋለሁ)፡፡ ጥቂትም እጠቅመዋለሁ፤ ከዚያም ወደ እሳት ቅጣት አስጠጋዋለሁ፤ ምን ትከፉም መመለሻ! (አለ)፡፡

وَإِذْ قَالَ إِبْرَٰهِـۧمُ رَبِّ ٱجْعَلْ هَٰذَا بَلَدًا ءَامِنًا وَٱرْزُقْ أَهْلَهُۥ مِنَ ٱلثَّمَرَٰتِ مَنْ ءَامَنَ مِنْهُم بِٱللَّهِ وَٱلْيَوْمِ ٱلْءَاخِرِ ۖ قَالَ وَمَن كَفَرَ فَأُمَتِّعُهُۥ قَلِيلًا ثُمَّ أَضْطَرُّهُۥٓ إِلَىٰ عَذَابِ ٱلنَّارِ ۖ وَبِئْسَ ٱلْمَصِيرُ ﴿١٢٦﴾

127. ኢብራሂምና ኢስማኢልም «ጌታችን ሆይ! ከእኛ ተቀበል፡፡ አንተ ሰሚውና ዐዋቂው አንተ ነህና» የሚሉ ሲኾኑ ከቤቱ መሠረቶቹን ከፍ ባደረጉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

وَإِذْ يَرْفَعُ إِبْرَٰهِـۧمُ ٱلْقَوَاعِدَ مِنَ ٱلْبَيْتِ وَإِسْمَٰعِيلُ رَبَّنَا تَقَبَّلْ مِنَّآ ۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلسَّمِيعُ ٱلْعَلِيمُ ﴿١٢٧﴾

128. «ጌታችን ሆይ! ላንተ ታዛዦችም አድርገን፡፡ ከዘሮቻችንም ላንተ ታዛዦች ሕዝቦችን (አድርግ)፡፡ ሕግጋታችንንም አሳየን፤ (አሳውቀን)፡፡ በኛም ላይ ተመለስን፤ አንተ ጸጸትን ተቀባዩ ሩኅሩኅ አንተ ብቻ ነህና፡፡»

رَبَّنَا وَٱجْعَلْنَا مُسْلِمَيْنِ لَكَ وَمِن ذُرِّيَّتِنَآ أُمَّةً مُّسْلِمَةً لَّكَ وَأَرِنَا مَنَاسِكَنَا وَتُبْ عَلَيْنَآ ۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلتَّوَّابُ ٱلرَّحِيمُ ﴿١٢٨﴾

129. «ጌታችን ሆይ! በውስጣቸውም ከነሱው የኾነን መልክተኛ በነርሱ ላይ አንቀጾችህን የሚያነብላቸውን መጽሐፍንና ጥበብንም የሚያስተምራቸውን (ከክህደት) የሚያጠራቸውንም ላክ፤ አንተ አሸናፊው ጥበበኛው አንተ ብቻ ነህና» (የሚሉም ሲኾኑ)፡፡

رَبَّنَا وَٱبْعَثْ فِيهِمْ رَسُولًا مِّنْهُمْ يَتْلُوا۟ عَلَيْهِمْ ءَايَٰتِكَ وَيُعَلِّمُهُمُ ٱلْكِتَٰبَ وَٱلْحِكْمَةَ وَيُزَكِّيهِمْ ۚ إِنَّكَ أَنتَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ﴿١٢٩﴾

130. ከኢብራሂምም ሕግጋት ነፍሱን ያቄለ ሰው ካልኾነ በስተቀር የሚያፈገፍግ ማነው? (የለም)፤ በቅርቢቱም ዓለም በእርግጥ መረጥነው፡፡ በመጨረሻይቱም ዓለም እርሱ ከመልካሞቹ ነው፡፡

وَمَن يَرْغَبُ عَن مِّلَّةِ إِبْرَٰهِـۧمَ إِلَّا مَن سَفِهَ نَفْسَهُۥ ۚ وَلَقَدِ ٱصْطَفَيْنَٰهُ فِى ٱلدُّنْيَا ۖ وَإِنَّهُۥ فِى ٱلْءَاخِرَةِ لَمِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿١٣٠﴾

131. ጌታው ለርሱ ታዘዝ ባለው ጊዜ (መረጠው)፡፡ ለዓለማት ጌታ ታዘዝኩ አለ፡፡

إِذْ قَالَ لَهُۥ رَبُّهُۥٓ أَسْلِمْ ۖ قَالَ أَسْلَمْتُ لِرَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿١٣١﴾

132. በርሷም (በሕግጋቲቱ) ኢብራሂም ልጆቹን አዘዘ፡፡ ያዕቁብም (እንደዚሁ ልጆቹን አዘዘ)፡፡ «ልጆቼ ሆይ! አላህ ለናንተ ሃይማኖትን መረጠ፤ ስለዚህ እናንተ

وَوَصَّىٰ بِهَآ إِبْرَٰهِـۧمُ بَنِيهِ وَيَعْقُوبُ يَٰبَنِىَّ إِنَّ ٱللَّهَ ٱصْطَفَىٰ لَكُمُ ٱلدِّينَ فَلَا تَمُوتُنَّ إِلَّا وَأَنتُم مُّسْلِمُونَ ﴿١٣٢﴾

ሙስሊሞች ኾናችሁ እንጂ አትሙቱ» (አላቸው)፡፡

133. ያዕቁብን ሞት በመጣበት ጊዜ ለልጆቹ ከኔ በኋላ ማንን ትገዛላችሁ ባለ ጊዜ ቀራቢዎች ነበራችሁን? (እነርሱም) አምላክህንና የአባቶችህን የኢብራሂምን የኢስማዒልንና የኢስሐቅንም አምላክ አንድ የኾነውን አምላክ እኛ ለርሱ ፍፁም ታዛዦች ኾነን እናመልካለን አሉ፡፡

أَمْ كُنتُمْ شُهَدَآءَ إِذْ حَضَرَ يَعْقُوبَ ٱلْمَوْتُ إِذْ قَالَ لِبَنِيهِ مَا تَعْبُدُونَ مِنۢ بَعْدِىۖ قَالُوا۟ نَعْبُدُ إِلَـٰهَكَ وَإِلَـٰهَ ءَابَآئِكَ إِبْرَٰهِـۧمَ وَإِسْمَـٰعِيلَ وَإِسْحَـٰقَ إِلَـٰهًا وَٰحِدًا وَنَحْنُ لَهُۥ مُسْلِمُونَ ﴿١٣٣﴾

134. ይህች (የተወሳችው) በእርግጥ ያለፈች ሕዝብ ናት፡፡ ለርሷ የሠራችው (ምንዳ) አላት፡፡ ለናንተም የሠራችሁት (ምንዳ) አላችሁ፡፡ ይሠሩትም ከነበሩት አትጠየቁም፡፡

تِلْكَ أُمَّةٌ قَدْ خَلَتْۖ لَهَا مَا كَسَبَتْ وَلَكُم مَّا كَسَبْتُمْۖ وَلَا تُسْـَٔلُونَ عَمَّا كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ﴿١٣٤﴾

135. «አይሁድን ወይም ክርስቲያኖችን ኹኑ፤ (ቅኑን መንገድ) ትመራላችሁና» አሉም፡፡ «አይደለም የኢብራሂምን ሃይማኖት ቀጥተኛ ሲኾን እንከተላለን፤ ከአጋሪዎችም አልነበረም» በላቸው፡፡

وَقَالُوا۟ كُونُوا۟ هُودًا أَوْ نَصَـٰرَىٰ تَهْتَدُوا۟ۗ قُلْ بَلْ مِلَّةَ إِبْرَٰهِـۧمَ حَنِيفًاۖ وَمَا كَانَ مِنَ ٱلْمُشْرِكِينَ ﴿١٣٥﴾

136. «በአላህና ወደኛ በተወረደው (ቁርኣን) ወደ ኢብራሂምም ወደ ኢስማዒልና ወደ ኢስሐቅም ወደ ያዕቁብና ወደ ነገዶቹም በተወረደው በዚያም ሙሳና ዒሳ በተሰጡት በዚያም ነቢያት ሁሉ ከጌታቸው በተሰጡት ከነርሱ በአንድም መካከል የማንለይ ስንኾን አመንን፤ እኛም ለርሱ (ለአላህ) ታዛዦች ነን» በሉ፡፡

قُولُوٓا۟ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَمَآ أُنزِلَ إِلَيْنَا وَمَآ أُنزِلَ إِلَىٰٓ إِبْرَٰهِـۧمَ وَإِسْمَـٰعِيلَ وَإِسْحَـٰقَ وَيَعْقُوبَ وَٱلْأَسْبَاطِ وَمَآ أُوتِىَ مُوسَىٰ وَعِيسَىٰ وَمَآ أُوتِىَ ٱلنَّبِيُّونَ مِن رَّبِّهِمْ لَا نُفَرِّقُ بَيْنَ أَحَدٍ مِّنْهُمْ وَنَحْنُ لَهُۥ مُسْلِمُونَ ﴿١٣٦﴾

137. በርሱ ባመናችሁበት ብጤ ቢያምኑ በእርግጥ ተመሩ፡፡ ቢዞሩም እነርሱ በጭቅጭቅ ውስጥ ብቻ ናቸው፡፡ እነርሱንም አላህ ይበቃሃል፤ እርሱም ሰሚው ዐዋቂው ነው፡፡

فَإِنْ ءَامَنُوا۟ بِمِثْلِ مَآ ءَامَنتُم بِهِۦ فَقَدِ ٱهْتَدَوا۟ۖ وَّإِن تَوَلَّوْا۟ فَإِنَّمَا هُمْ فِى شِقَاقٍۖ فَسَيَكْفِيكَهُمُ ٱللَّهُۚ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلْعَلِيمُ ﴿١٣٧﴾

138. የአላህን (የተፈጥሮ) መንክር (እምነት) ያዙ፡፡ በመንክርም ከአላህ ይበልጥ ያማረ ማነው? (ማንም የለም) እኛም ለርሱ ብቻ ተገዢዎች ነን (በሉ)፡፡

صِبْغَةَ ٱللَّهِ وَمَنْ أَحْسَنُ مِنَ ٱللَّهِ صِبْغَةًۖ وَنَحْنُ لَهُۥ عَـٰبِدُونَ ﴿١٣٨﴾

139. እርሱ (አላህ) ጌታችንና ጌታችሁ ሲኾን ለኛም ሥራችን ያለን ስንኾን ለናንተም ሥራችሁ ያላችሁ ስትኾኑ እኛም ለርሱ ፍጹም ታዛዦች ስንኾን በአላህ (ሃይማኖት) ትከራከሩናላችሁን? በላቸው፡፡

قُلْ أَتُحَآجُّونَنَا فِى ٱللَّهِ وَهُوَ رَبُّنَا وَرَبُّكُمْ وَلَنَآ أَعْمَـٰلُنَا وَلَكُمْ أَعْمَـٰلُكُمْ وَنَحْنُ لَهُۥ مُخْلِصُونَ ﴿١٣٩﴾

140. ወይም ኢብራሂም ኢስማዒልም ኢስሐቅም ያዕቆብም ነገዶቹም አይሁዶች ወይም ክርስቲያኖች ነበሩ ትላላችሁን? «እናንተ ታውቃላችሁን? ወይንስ አላህ?» በላቸው፡፡ እርሱም ዘንድ ከአላህ የኾነችን ምስክርነት ከደበቀ ሰው ይበልጥ በዳይ ማነው? አላህም ከምትሠሩት ሁሉ ዘንጊ አይደለም፡፡

أَمۡ تَقُولُونَ إِنَّ إِبۡرَٰهِـۧمَ وَإِسۡمَٰعِيلَ وَإِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ وَٱلۡأَسۡبَاطَ كَانُواْ هُودًا أَوۡ نَصَٰرَىٰۗ قُلۡ ءَأَنتُمۡ أَعۡلَمُ أَمِ ٱللَّهُۗ وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّن كَتَمَ شَهَٰدَةً عِندَهُۥ مِنَ ٱللَّهِۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ١٤٠

141. ይህቺ በእርግጥ ያለፈች ሕዝብ ናት፤ ለእርሷ የሠራችው አላት፤ ለናንተም የሠራችሁት አላችሁ፤ ይሠሩትም ከነበሩት አትጠየቁም፡፡

تِلۡكَ أُمَّةٞ قَدۡ خَلَتۡۖ لَهَا مَا كَسَبَتۡ وَلَكُم مَّا كَسَبۡتُمۡۖ وَلَا تُسۡـَٔلُونَ عَمَّا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٤١

142. ከሰዎቹ ቂሎቹ «ከዚያች በርሷ ላይ ከነበሩባት ቂብላቸው ምን አዞራቸው?» ይላሉ፤ «ምሥራቁም ምዕራቡም የአላህ ነው፤ የሻውን ሰው ወደ ቀጥተኛው መንገድ ይመራል» በላቸው፡፡

۞سَيَقُولُ ٱلسُّفَهَآءُ مِنَ ٱلنَّاسِ مَا وَلَّىٰهُمۡ عَن قِبۡلَتِهِمُ ٱلَّتِي كَانُواْ عَلَيۡهَاۚ قُل لِّلَّهِ ٱلۡمَشۡرِقُ وَٱلۡمَغۡرِبُۚ يَهۡدِي مَن يَشَآءُ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ١٤٢

143. እንደዚሁም (እንደመራናችሁ) በሰዎች ላይ መስካሪዎች ልትሆኑና መልክተኛውም በናንተ ላይ መስካሪ ይሆን ዘንድ ምርጥ ሕዝቦች አደረግናችሁ፡፡ ያችንም በርሷ ላይ የነበርክባትን አቅጣጫ መልክተኛውን የሚከተለውን ሰው ወደ ከህደት ከሚመለሰው ሰው ልናውቅ (ልንገልጽ) እንጅ ቂብላ አላደረግናትም፡፡ እርሷም በነዚያ አላህ በመራቸው ሰዎች ላይ በስተቀር በእርግጥ ከባድ ናት፡፡ አላህም እምነታችሁን (ስግደታችሁን) የሚያጠፋ አይደለም፤ አላህ ለሰዎች በጣም ርኅሩኅ አዛኝ ነውና፡፡

وَكَذَٰلِكَ جَعَلۡنَٰكُمۡ أُمَّةٗ وَسَطٗا لِّتَكُونُواْ شُهَدَآءَ عَلَى ٱلنَّاسِ وَيَكُونَ ٱلرَّسُولُ عَلَيۡكُمۡ شَهِيدٗاۗ وَمَا جَعَلۡنَا ٱلۡقِبۡلَةَ ٱلَّتِي كُنتَ عَلَيۡهَآ إِلَّا لِنَعۡلَمَ مَن يَتَّبِعُ ٱلرَّسُولَ مِمَّن يَنقَلِبُ عَلَىٰ عَقِبَيۡهِۚ وَإِن كَانَتۡ لَكَبِيرَةً إِلَّا عَلَى ٱلَّذِينَ هَدَى ٱللَّهُۗ وَمَا كَانَ ٱللَّهُ لِيُضِيعَ إِيمَٰنَكُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِٱلنَّاسِ لَرَءُوفٞ رَّحِيمٞ ١٤٣

144. የፊትህን ወደ ሰማይ መገላበጥ በእርግጥ እናያለን፡፡ ወደምትወዳትም ቂብላ እናዞርሃለን፡፡ ስለዚህ ፊትህን ወደ ተከበረው መስጊድ (ወደ ካዕባ) አግጣጫ አዙር፡፡ የትም ስፍራ ብትኾኑም (ስትሰግዱ) ፊቶቻችሁን ወደርሱ አግጣጫ አዙሩ፡፡ እነዚያም መጽሐፉን የተሰጡት እርሱ ከጌታቸው ሲኾን እውነት መሆኑን ያውቃሉ፡፡ አላህም ከምትሠሩት ሥራ ዘንጊ አይደለም፡፡

قَدۡ نَرَىٰ تَقَلُّبَ وَجۡهِكَ فِي ٱلسَّمَآءِۖ فَلَنُوَلِّيَنَّكَ قِبۡلَةٗ تَرۡضَىٰهَاۚ فَوَلِّ وَجۡهَكَ شَطۡرَ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِۚ وَحَيۡثُ مَا كُنتُمۡ فَوَلُّواْ وُجُوهَكُمۡ شَطۡرَهُۥۗ وَإِنَّ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ لَيَعۡلَمُونَ أَنَّهُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّهِمۡۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا يَعۡمَلُونَ ١٤٤

145. እነዚያንም መጽሐፍን የተሰጡትን በአስረጅ ሁሉ ብትመጣቸው ቂብላህን አይከተሉም፡፡ አንተም ቂብላቸውን ተከታይ አይደለህም፡፡ ከፊላቸውም የከፊሉን ቂብላ ተከታይ አይደሉም፡፡ ከዕውቀትም (ከራዕይ) ከመጣልህ በኋላ ዝንባሌያቸውን ብትከተል አንተ ያን ጊዜ ከበዳዮች ነህ፡፡

وَلَئِنۡ أَتَيۡتَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ بِكُلِّ ءَايَةٖ مَّا تَبِعُواْ قِبۡلَتَكَۚ وَمَآ أَنتَ بِتَابِعٖ قِبۡلَتَهُمۡۚ وَمَا بَعۡضُهُم بِتَابِعٖ قِبۡلَةَ بَعۡضٖۚ وَلَئِنِ ٱتَّبَعۡتَ أَهۡوَآءَهُم مِّنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَكَ مِنَ ٱلۡعِلۡمِ إِنَّكَ إِذٗا لَّمِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٤٥

146. እነዚያ መጽሐፍን የሰጠናቸው ወንዶች ልጆቻቸውን እንደሚያውቁ (ሙሐመድን) ያውቁታል፡፡ ከነሱም የተለዩ ክፍሎች እነርሱ የሚያወቁ ሲኾኑ እውነቱን በእርግጥ ይደብቃሉ፡፡
147. (ይህ) ከጌታህ የኾነ እውነት ነው፤ ከተጠራጣሪዎቹም አትሁን፡፡

ٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يَعۡرِفُونَهُۥ كَمَا يَعۡرِفُونَ أَبۡنَآءَهُمۡۖ وَإِنَّ فَرِيقٗا مِّنۡهُمۡ لَيَكۡتُمُونَ ٱلۡحَقَّ وَهُمۡ يَعۡلَمُونَ ١٤٦

ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ فَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُمۡتَرِينَ ١٤٧

148. ለሁሉም እርሱ (በስግደት ፊቱን) የሚያዞርባት አግጣጫ አለችው፡፡ ወደ መልካም ሥራዎችም ተሽቀዳደሙ፡፡ የትም ስፍራ ብትኾኑ አላህ እናንተን የተሰበሰባችሁ ኾናችሁ ያመጣችኋል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

وَلِكُلّٖ وِجۡهَةٌ هُوَ مُوَلِّيهَاۖ فَٱسۡتَبِقُواْ ٱلۡخَيۡرَٰتِۚ أَيۡنَ مَا تَكُونُواْ يَأۡتِ بِكُمُ ٱللَّهُ جَمِيعًاۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ١٤٨

149. ከየትም (ለጉዞ) ከወጣህበት ስፍራ ፊትህን ወደ ተከበረው መስጊድ አግጣጫ አዙር፡፡ እርሱም ከጌታህ የኾነ እርግጠኛ እውነት ነው፡፡ አላህም ከምትሠሩት ሥራ ዘንጊ አይደለም፡፡

وَمِنۡ حَيۡثُ خَرَجۡتَ فَوَلِّ وَجۡهَكَ شَطۡرَ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِۖ وَإِنَّهُۥ لَلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ١٤٩

150. ከየትም ከወጣህበት ስፍራ ፊትህን ወደ ተከለለው መስጊድ አግጣጫ አዙር፡፡ በየትም ስፍራ ብትኾኑ ለሰዎቹ እነዚያ ከነሱ የበደሉት ሲቀሩ (ሃይማኖታችንን ይክዳሉ ቂብላችንን ይከተላሉ በማለት) በናንተ ላይ መከራከሪያ እንዳይኖራቸው ፊቶቻችሁን ወደ አግጣጫው አዙሩ፡፡ አትፍሩዋቸውም፤ ፍሩኝም፤ (በዚህም ያዘዝኳችሁ መከራከሪያ እንዳይኖራቸው) በናንተም ላይ ጸጋየን እንድሞላላችሁና (ወደ እውነትም) እንድትመሩ ነው፡፡

وَمِنۡ حَيۡثُ خَرَجۡتَ فَوَلِّ وَجۡهَكَ شَطۡرَ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِۚ وَحَيۡثُ مَا كُنتُمۡ فَوَلُّواْ وُجُوهَكُمۡ شَطۡرَهُۥ لِئَلَّا يَكُونَ لِلنَّاسِ عَلَيۡكُمۡ حُجَّةٌ إِلَّا ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنۡهُمۡ فَلَا تَخۡشَوۡهُمۡ وَٱخۡشَوۡنِي وَلِأُتِمَّ نِعۡمَتِي عَلَيۡكُمۡ وَلَعَلَّكُمۡ تَهۡتَدُونَ ١٥٠

151. በውስጣችሁ ከናንተው የኾነን በናንተ ላይ አንቀጾቻችንን የሚያነብላችሁና የሚያጠራችሁ፣ መጽሐፍንና ጥበብንም የሚያስተምራችሁ፣ ታውቁት ያልነበራችሁትንም ነገር የሚያሳውቃችሁ የኾነን መልክተኛ እንደላክን (ጸጋን ሞላንላችሁ)፡፡

كَمَآ أَرۡسَلۡنَا فِيكُمۡ رَسُولٗا مِّنكُمۡ يَتۡلُواْ عَلَيۡكُمۡ ءَايَٰتِنَا وَيُزَكِّيكُمۡ وَيُعَلِّمُكُمُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحِكۡمَةَ وَيُعَلِّمُكُم مَّا لَمۡ تَكُونُواْ تَعۡلَمُونَ ١٥١

152. አስታውሱኝም፤ አስታውሳችኋለሁና ለኔም አመስግኑ፤ አትካዱኝም፡፡
153. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በመታገስና በሶላት ተረዱ፡፡ አላህ (በእርዳታው) ከታጋሾች ጋር ነውና፡፡

فَٱذۡكُرُونِيٓ أَذۡكُرۡكُمۡ وَٱشۡكُرُواْ لِي وَلَا تَكۡفُرُونِ ١٥٢

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱسۡتَعِينُواْ بِٱلصَّبۡرِ وَٱلصَّلَوٰةِۚ إِنَّ ٱللَّهَ مَعَ ٱلصَّٰبِرِينَ ١٥٣

154. በአላህ መንገድ (ለሃይማኖቱ) የሚገደሉትን ሰዎችም «ሙታን ናቸው» አትበሉ፡፡ በእውነቱ ሕያዋን ናቸው፤ ግን አታውቁም፡፡

وَلَا تَقُولُواْ لِمَن يُقۡتَلُ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ أَمۡوَٰتُۢۚ بَلۡ أَحۡيَآءٞ وَلَٰكِن لَّا تَشۡعُرُونَ ١٥٤

155. ከፍርሃትና ከረኃብም በጥቂት ነገር፣ ከገንዘቦችና ከነፍሶችም፣ ከፍራፍሬዎችም በመቀነስ በእርግጥ እንሞክራችኋለን፡፡ ታጋሾችንም (በገነት) አብስር፡፡

وَلَنَبۡلُوَنَّكُم بِشَيۡءٖ مِّنَ ٱلۡخَوۡفِ وَٱلۡجُوعِ وَنَقۡصٖ مِّنَ ٱلۡأَمۡوَٰلِ وَٱلۡأَنفُسِ وَٱلثَّمَرَٰتِۗ وَبَشِّرِ ٱلصَّٰبِرِينَ ١٥٥

156. እነዚያን መከራ፤ በነካቻቸው ጊዜ «እኛ ለአላህ፤ ነን እኛም ወደርሱ ተመላሾች» ነን የሚሉትን (አብስር)::

ٱلَّذِينَ إِذَآ أَصَٰبَتۡهُم مُّصِيبَةٞ قَالُوٓاْ إِنَّا لِلَّهِ وَإِنَّآ إِلَيۡهِ رَٰجِعُونَ ١٥٦

157. እነዚያ በእነርሱ ላይ ከጌታቸው የኾኑ ምሕረቶች ችሮታም አልሉ፡፡ እነርሱም (ወደ እውነት) ተመሪዎቹ እነርሱ ናቸው::

أُوْلَٰٓئِكَ عَلَيۡهِمۡ صَلَوَٰتٞ مِّن رَّبِّهِمۡ وَرَحۡمَةٞۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُهۡتَدُونَ ١٥٧

158. ሶፋና መርዋ ከአላህ (ትዕዛዝ መፈጸሚያ) ምልክቶች ናቸው፡፡ ቤቱን (ካዕባን) በሐጅ ወይም በዑምራህ ሥራ የጎበኘ ሰው በሁለቱ (መካከል) በመመላለሱ በርሱ ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ መልካምንም ሥራ በፈቃደኛነት የሠራ ሰው (አላህ ይመነዳዋል)፤ አላህ አመስጋኝ ዐዋቂ ነውና፡፡

۞إِنَّ ٱلصَّفَا وَٱلۡمَرۡوَةَ مِن شَعَآئِرِ ٱللَّهِۖ فَمَنۡ حَجَّ ٱلۡبَيۡتَ أَوِ ٱعۡتَمَرَ فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡهِ أَن يَطَّوَّفَ بِهِمَاۚ وَمَن تَطَوَّعَ خَيۡرٗا فَإِنَّ ٱللَّهَ شَاكِرٌ عَلِيمٌ ١٥٨

159. እነዚያ ከአንቀጾችና ከቅን መምሪያ ያወረድነውን ለሰዎች በመጽሐፉ ከገለጽነው በኋላ የሚደብቁ፤ እነዚያ አላህ ይረግማቸዋል፤ ረጋሚዎችም ሁሉ ይረግሟቸዋል::

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡتُمُونَ مَآ أَنزَلۡنَا مِنَ ٱلۡبَيِّنَٰتِ وَٱلۡهُدَىٰ مِنۢ بَعۡدِ مَا بَيَّنَّٰهُ لِلنَّاسِ فِي ٱلۡكِتَٰبِ أُوْلَٰٓئِكَ يَلۡعَنُهُمُ ٱللَّهُ وَيَلۡعَنُهُمُ ٱللَّٰعِنُونَ ١٥٩

160. እነዚያ (ከመደበቅ) የተጸጸቱና (ሥራቸውን) ያሳመሩም (የደበቁትን) የገለጹም ብቻ ሲቀሩ፡፡ እነዚህም በነሱ ላይ (ጸጸታቸውን) እቀበላለሁ፤ እኔም ጸጸትን በጣም ተቀባይ አዛኙ ነኝ፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ تَابُواْ وَأَصۡلَحُواْ وَبَيَّنُواْ فَأُوْلَٰٓئِكَ أَتُوبُ عَلَيۡهِمۡ وَأَنَا ٱلتَّوَّابُ ٱلرَّحِيمُ ١٦٠

161. እነዚያ የካዱ እነርሱ ከሐዲዎች ኾነውም የሞቱ እነዚያ በነርሱ ላይ የአላህና የመላእክት የሰዎችም ሁሉ እርግማን አለባቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَمَاتُواْ وَهُمۡ كُفَّارٌ أُوْلَٰٓئِكَ عَلَيۡهِمۡ لَعۡنَةُ ٱللَّهِ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ وَٱلنَّاسِ أَجۡمَعِينَ ١٦١

162. በውስጧ (በርግማንዋ ውስጥ) ሁልጊዜ ዘውታሪዎች ሲኾኑ ቅጣቱ ከነሱ አይቀለልም እነርሱም አይቅቆዩም (ጊዜ አይስሰጡም)፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَا لَا يُخَفَّفُ عَنۡهُمُ ٱلۡعَذَابُ وَلَا هُمۡ يُنظَرُونَ ١٦٢

163. አምላካችሁም አንድ አምላክ ብቻ ነው፤ ከርሱ በቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ (እርሱ) እጅግ በጣም ርኅሩህ አዛኝ ነው፡፡

وَإِلَٰهُكُمۡ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞۖ لَّآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلرَّحۡمَٰنُ ٱلرَّحِيمُ ١٦٣

164. ሰማያትንና ምድርን በመፍጠር ሌሊትንና ቀንንም በማተካካት፣ በዚያቸም ሰዎችን በሚጠቅም ነገር (ተጭና) በባህር ላይ በምትንሻለለው ታንኳ፣ አላህም ከሰማይ ባወረደው ውሃና በርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው በማድረጉ፣ በርሷም ውስጥ ከተንቀሳቃሽ ሁሉ በመበተኑ፣ ነፋሶችንም (በየአግጣጫው) በማገለባበጥ፣ በሰማይና በምድር መካከል በሚነዳውም ደመና ለሚያውቁ ሕዝቦች እርግጠኛ ምልክቶች አሉ፡፡

إِنَّ فِي خَلۡقِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَٱخۡتِلَٰفِ ٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِ وَٱلۡفُلۡكِ ٱلَّتِي تَجۡرِي فِي ٱلۡبَحۡرِ بِمَا يَنفَعُ ٱلنَّاسَ وَمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مِن مَّآءٖ فَأَحۡيَا بِهِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَا وَبَثَّ فِيهَا مِن كُلِّ دَآبَّةٖ وَتَصۡرِيفِ ٱلرِّيَٰحِ وَٱلسَّحَابِ ٱلۡمُسَخَّرِ بَيۡنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ١٦٤

165. ከሰዎችም ከአላህ ሌላ ባለንጣዎችን (ጣዖታትን) አላህን እንደሚወዱ የሚወዷቸው ኾነው የሚይዙ አልሉ፡፡ እነዚያ ያመኑትም አላህን በመውደድ (ከነርሱ) ይበልጥ የበረቱ ናቸው፡፡ እነዚያም የበደሉት ሰዎች ቅጣትን (በትንሣኤ ቀን) ባዩ ጊዜ ኀይል ሁሉ ለአላህ ብቻ መኾኑንና አላህም ቅጣቱ ብርቱ መኾኑን (በአዱኛ ዓለም) ቢያውቁ ኖሮ (ባላንጣዎችን በመያዛቸው በተጸጸቱ ነበር)፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَتَّخِذُ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَندَادًا يُحِبُّونَهُمْ كَحُبِّ ٱللَّهِۖ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَشَدُّ حُبًّا لِّلَّهِۗ وَلَوْ يَرَى ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓاْ إِذْ يَرَوْنَ ٱلْعَذَابَ أَنَّ ٱلْقُوَّةَ لِلَّهِ جَمِيعًا وَأَنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلْعَذَابِ ١٦٥

166. እነዚያ አስከታዮቹ ቅጣትን ያዩ ሲኾኑ ከእነዚያ ከተከታዮች በተጥራሩና በእነርሱም (መካከል) ምክንያቶች በተቆረጡ ጊዜ (የሚኾኑትን ባወቁ ኖሮ በተጸጸቱ ነበር)፡፡

إِذْ تَبَرَّأَ ٱلَّذِينَ ٱتُّبِعُواْ مِنَ ٱلَّذِينَ ٱتَّبَعُواْ وَرَأَوُاْ ٱلْعَذَابَ وَتَقَطَّعَتْ بِهِمُ ٱلْأَسْبَابُ ١٦٦

167. እነዚያም የተከተሉት «ለእኛ (ወደ ቅርቢቱ ዓለም) አንዲት ጊዜ መመለስ በኖረችንና ከእኛ እንደተጥራሩ ከእነርሱ በተጥራራን እንመኛለን» ይላሉ፡ ፡ እንደዚሁ አላህ ሥራዎቻቸውን በነርሱ ላይ ጸጸቶች አድርጎ ያሳያቸዋል፡፡ እነርሱም ከእሳት ወጪዎች አይደሉም፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ ٱتَّبَعُواْ لَوْ أَنَّ لَنَا كَرَّةً فَنَتَبَرَّأَ مِنْهُمْ كَمَا تَبَرَّءُواْ مِنَّاۗ كَذَٰلِكَ يُرِيهِمُ ٱللَّهُ أَعْمَٰلَهُمْ حَسَرَٰتٍ عَلَيْهِمْۖ وَمَا هُم بِخَٰرِجِينَ مِنَ ٱلنَّارِ ١٦٧

168. እናንተ ሰዎች ሆይ! በምድር ካለው ነገር የተፈቀደ ጣፋጭ ሲኾን ብሉ፡፡ የሰይጣንንም እርምጃዎች አትከታተሉ፡፡ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ كُلُواْ مِمَّا فِي ٱلْأَرْضِ حَلَٰلًا طَيِّبًا وَلَا تَتَّبِعُواْ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيْطَٰنِۚ إِنَّهُۥ لَكُمْ عَدُوٌّ مُّبِينٌ ١٦٨

169. (እርሱ) የሚያዛችሁ በኃጢአትና በጸያፍ ነገር በአላህም ላይ የማታውቁትን እንድትናገሩ ብቻ ነው፡፡

إِنَّمَا يَأْمُرُكُم بِٱلسُّوٓءِ وَٱلْفَحْشَآءِ وَأَن تَقُولُواْ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعْلَمُونَ ١٦٩

170. ለእነርሱም «አላህ ያወረደውን ተከተሉ» በተባሉ ጊዜ «አይደለም አባቶቻችንን በርሱ ላይ ያገኘንበትን ነገር እንከተላለን» ይላሉ፡፡ አባቶቻቸው ምንም የማያውቁና (ወደ እውነት) የማይመሩም ቢኾኑ (ይከተሉዋቸዋልን?)

وَإِذَا قِيلَ لَهُمُ ٱتَّبِعُواْ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ قَالُواْ بَلْ نَتَّبِعُ مَآ أَلْفَيْنَا عَلَيْهِ ءَابَآءَنَآۚ أَوَلَوْ كَانَ ءَابَآؤُهُمْ لَا يَعْقِلُونَ شَيْـًٔا وَلَا يَهْتَدُونَ ١٧٠

171. የነዚያም የካዱት (እና ወደ ቅን መንገድ የሚጠራቸው ሰው) ምሳሌ እንደዚያ ድምጽንና ጥሪን በስተቀር ሌላን በማይሰማ (እንስሳ) ላይ እንደሚጮህ ብጤ ነው፡፡ (እነርሱ) ደንቆሮዎች፣ ዲዳዎች፣ ዕውሮች ናቸው፤ ስለዚህ እነርሱ አያውቁም፡፡

وَمَثَلُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ كَمَثَلِ ٱلَّذِي يَنْعِقُ بِمَا لَا يَسْمَعُ إِلَّا دُعَآءً وَنِدَآءًۚ صُمٌّۢ بُكْمٌ عُمْيٌ فَهُمْ لَا يَعْقِلُونَ ١٧١

172. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከነዚያ ከሰጠናችሁ ጣፋጮች ብሉ፡፡ ለአላህም እርሱን ብቻ የምትገዙ እንደኾናችሁ አመስግኑ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُلُواْ مِن طَيِّبَٰتِ مَا رَزَقْنَٰكُمْ وَٱشْكُرُواْ لِلَّهِ إِن كُنتُمْ إِيَّاهُ تَعْبُدُونَ ١٧٢

173. በናንተ ላይ እርም ያደረገው በክትንና ደምን፣ የእሪያ ሥጋንም፣ በእርሱም (ማረድ) ከአላህ ስም ሌላ የተነሳበትን ነገር ብቻ ነው፡፡ ሽፍታና ወሰን አላፊ ሳይኾን (ለሙብላት) የተገደደ ሰውም በርሱ ላይ ኃጢአት የለበትም አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

إِنَّمَا حَرَّمَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡمَيۡتَةَ وَٱلدَّمَ وَلَحۡمَ ٱلۡخِنزِيرِ وَمَآ أُهِلَّ بِهِۦ لِغَيۡرِ ٱللَّهِۖ فَمَنِ ٱضۡطُرَّ غَيۡرَ بَاغٖ وَلَا عَادٖ فَلَآ إِثۡمَ عَلَيۡهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ١٧٣

174. እነዚያ አላህ ከመጽሐፍ ያወረደውን የሚደብቁ በርሱም (በመደበቃቸው) ጥቂትን ዋጋ የሚገዙ እነዚያ በሆዶቻቸው ውስጥ እሳትን እንጂ አይበሉም፡፡ አላህም በትንሣኤ ቀን አያናግራቸውም፤ (ከኃጢአት) አያጠራቸውምም፡፡ ለነርሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡتُمُونَ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَيَشۡتَرُونَ بِهِۦ ثَمَنٗا قَلِيلًا أُوْلَٰٓئِكَ مَا يَأۡكُلُونَ فِي بُطُونِهِمۡ إِلَّا ٱلنَّارَ وَلَا يُكَلِّمُهُمُ ٱللَّهُ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ وَلَا يُزَكِّيهِمۡ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٌ ١٧٤

175. እነዚያ ጥመትን በቅንነት ቅጣትንም በምሕረት የገዙ ናቸው፡፡ በእሳት ላይም ምን ታጋሽ አደረጋቸው!

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ ٱشۡتَرَوُاْ ٱلضَّلَٰلَةَ بِٱلۡهُدَىٰ وَٱلۡعَذَابَ بِٱلۡمَغۡفِرَةِۚ فَمَآ أَصۡبَرَهُمۡ عَلَى ٱلنَّارِ ١٧٥

176. ይህ (ቅጣት) አላህ መጽሐፍን በእውነት ያወረደ በመኾኑ ምክንያት (እና በርሱ በመካዳቸው) ነው፡፡ እነዚያም በመጽሐፉ የተለያዩት (ከእውነት) በራቀ ጭቅጭቅ ውስጥ ናቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ نَزَّلَ ٱلۡكِتَٰبَ بِٱلۡحَقِّۗ وَإِنَّ ٱلَّذِينَ ٱخۡتَلَفُواْ فِي ٱلۡكِتَٰبِ لَفِي شِقَاقِۭ بَعِيدٖ ١٧٦

177. መልካም ሥራ ፊቶቻችሁን ወደ ምሥራቅና ምዕራብ አቅጣጫ ማዞር አይደለም፡፡ ግን መልካም ሥራ በአላህና በመጨረሻው ቀን፣ በመላእክትም፣ በመጻሕፍትም፣ በነቢያትም፣ ያመነ ሰው ገንዘብንም ከመውደዱ ጋር ለዝምድና ባለቤቶችና ለየቲሞች ለምስኪኖችም፣ ለመንገደኞችም፣ ለለማኞችም፣ ለጫንቃዎችም (ማስለቀቅ) የሰጠ ሰውና ሶላትንም ደንቡን ጠብቆ የሰገደ፣ ዘካንም የሰጠ፣ ቃል ኪዳንም በገቡ ጊዜ በኪዳናቸው የሞሉ (ሰዎች ሥራ) ነው፡፡ በችግር በበሽታና በጦር ጊዜም ታጋሾችን (እናወድሳለን)፡፡ እነዚህ እነዚያ እውነትን የያዙ ናቸው፡፡ እነዚያም ተጠንቃቂዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡

۞لَّيۡسَ ٱلۡبِرَّ أَن تُوَلُّواْ وُجُوهَكُمۡ قِبَلَ ٱلۡمَشۡرِقِ وَٱلۡمَغۡرِبِ وَلَٰكِنَّ ٱلۡبِرَّ مَنۡ ءَامَنَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ وَٱلۡكِتَٰبِ وَٱلنَّبِيِّـۧنَ وَءَاتَى ٱلۡمَالَ عَلَىٰ حُبِّهِۦ ذَوِي ٱلۡقُرۡبَىٰ وَٱلۡيَتَٰمَىٰ وَٱلۡمَسَٰكِينَ وَٱبۡنَ ٱلسَّبِيلِ وَٱلسَّآئِلِينَ وَفِي ٱلرِّقَابِ وَأَقَامَ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَى ٱلزَّكَوٰةَ وَٱلۡمُوفُونَ بِعَهۡدِهِمۡ إِذَا عَٰهَدُواْۖ وَٱلصَّٰبِرِينَ فِي ٱلۡبَأۡسَآءِ وَٱلضَّرَّآءِ وَحِينَ ٱلۡبَأۡسِۗ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ صَدَقُواْۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُتَّقُونَ ١٧٧

178. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በተገደሉ ሰዎች ማመሳሰል በናንተ ላይ ተጻፈ፡፡ ነጻ በነጻ ባሪያም በባሪያ ሴትም በሴት (ይገደላሉ)፡፡ ለእርሱም (ለገዳዩ) ከወንድሙ (ደም) ትንሽ ነገር ምሕረት የተደረገለት ሰው (በመሓሪው ላይ ጉማውን) በመልካም መከታተል ወደርሱም (ወደ መሓሪው) ገዳዩ በመልካም አኳኋን መክፈል አለባቸው፡፡ ይህ ከጌታችሁ የኾነ ማቃለልና እዝነት ነው፡፡ ከዚህም በኋላ ሕግን የተላለፈ ሰው ለርሱ አሳማሚ ቅጣት አለው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُتِبَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡقِصَاصُ فِي ٱلۡقَتۡلَىۖ ٱلۡحُرُّ بِٱلۡحُرِّ وَٱلۡعَبۡدُ بِٱلۡعَبۡدِ وَٱلۡأُنثَىٰ بِٱلۡأُنثَىٰۚ فَمَنۡ عُفِيَ لَهُۥ مِنۡ أَخِيهِ شَيۡءٞ فَٱتِّبَاعُۢ بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَأَدَآءٌ إِلَيۡهِ بِإِحۡسَٰنٖۗ ذَٰلِكَ تَخۡفِيفٞ مِّن رَّبِّكُمۡ وَرَحۡمَةٞۗ فَمَنِ ٱعۡتَدَىٰ بَعۡدَ ذَٰلِكَ فَلَهُۥ عَذَابٌ أَلِيمٞ ١٧٨

179. ለእናንተም ባለ አእምሮዎች ሆይ! በማመሳሰል (ሕግ) ውስጥ ሕይወት አላችሁ፡፡ ትጠነቀቁ ዘንድ (ገዳይን መግደል ተደነገገላችሁ)፡፡

وَلَكُمۡ فِي ٱلۡقِصَاصِ حَيَوٰةٞ يَـٰٓأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ١٧٩

180. አንዳችሁን ሞት በመጣበት ጊዜ ሀብትን ቢተው ለወላጆችና ለቅርብ ዘመዶች በበጎ መናዘዝ በናንተ ላይ ተጻፈ፡፡ (ይህ) በጥንቁቆቹ ላይ እርግጠኛ ድንጋጌ ተደነገገ፡፡

كُتِبَ عَلَيۡكُمۡ إِذَا حَضَرَ أَحَدَكُمُ ٱلۡمَوۡتُ إِن تَرَكَ خَيۡرًا ٱلۡوَصِيَّةُ لِلۡوَٰلِدَيۡنِ وَٱلۡأَقۡرَبِينَ بِٱلۡمَعۡرُوفِۖ حَقًّا عَلَى ٱلۡمُتَّقِينَ ١٨٠

181. (ኑዛዜውን) ከሰማውም በኋላ የለወጠው ሰው ኃጢአቱ በነዚያ በሚለውጡት ላይ ብቻ ነው፡፡ አላህ ሰሚ ዐዋቂ ነውና፡፡

فَمَنۢ بَدَّلَهُۥ بَعۡدَمَا سَمِعَهُۥ فَإِنَّمَآ إِثۡمُهُۥ عَلَى ٱلَّذِينَ يُبَدِّلُونَهُۥٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ١٨١

182. ከተናዛዢም በኩል (ከውነት) መዘንበልን ወይም (ከሢሶ በመጨመር) ኃጢአትን ያወቀና በመካከላቸው ያስታረቀ ሰው በእርሱ ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ አላህ በጣም መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

فَمَنۡ خَافَ مِن مُّوصٖ جَنَفًا أَوۡ إِثۡمٗا فَأَصۡلَحَ بَيۡنَهُمۡ فَلَآ إِثۡمَ عَلَيۡهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ١٨٢

183. እናንተ ያመናችሁ ሆይ ጾም በነዚያ ከናንተ በፊት በነበሩት (ሕዝቦች) ላይ እንደ ተጻፈ በናንተም ላይ ተጻፈ (ተደነባ) ልትጠነቀቁ ይከጀላልና፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُتِبَ عَلَيۡكُمُ ٱلصِّيَامُ كَمَا كُتِبَ عَلَى ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ١٨٣

184. የተቆጠሩን ቀኖች (ጹሙ)፡፡ ከእናንተም ውሰጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የኾነ ሰው ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፡፡ በእነዚያም ጾምን በማይችሉት ላይ ቤዛ ድኻን ማብላት አለባቸው፡፡ (ቤዛን በመጨመር) መልካምንም ሥራ የፈቀደ ሰው እርሱ (ፈቅዶ መጨመሩ) ለርሱ በላጭ ነው፡፡ መጾማችሁም ለናንተ የበለጠ ነው፤ የምታውቁ ብትኾኑ (ትመርጡታላችሁ)፡፡

أَيَّامٗا مَّعۡدُودَٰتٖۚ فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوۡ عَلَىٰ سَفَرٖ فَعِدَّةٞ مِّنۡ أَيَّامٍ أُخَرَۚ وَعَلَى ٱلَّذِينَ يُطِيقُونَهُۥ فِدۡيَةٞ طَعَامُ مِسۡكِينٖۖ فَمَن تَطَوَّعَ خَيۡرٗا فَهُوَ خَيۡرٞ لَّهُۥۚ وَأَن تَصُومُواْ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ١٨٤

185. (እንድትጾሙ የተጻፈባችሁ) ያ በርሱ ውስጥ ለሰዎች መሪ ከቅን መንገድና (እውነትን ከውሸት) ከሚለዩም ገላጮች (አንቀጾች) ሲኾን ቁርኣን የተወረደበት የረመዳን ወር ነው፡፡ ከእናንተም ወሩን ያገኘ ሰው ይጹመው፡፡ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የኾነም ሰው ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን (በልኩ) መጾም አለበት፡፡ አላህ በእናንተ ገሩን (ነገር) ይሻል፡፡ በእናንተም ችግሩን አይሻም፡፡ ቁጥሮችንም ልትሞሉ አላህንም ቅኑን መንገድ ስለመራችሁ ታከብሩትና ታመሰግኑት ዘንድ (ይህን ደነገግንላችሁ)፡፡

شَهۡرُ رَمَضَانَ ٱلَّذِيٓ أُنزِلَ فِيهِ ٱلۡقُرۡءَانُ هُدٗى لِّلنَّاسِ وَبَيِّنَٰتٖ مِّنَ ٱلۡهُدَىٰ وَٱلۡفُرۡقَانِۚ فَمَن شَهِدَ مِنكُمُ ٱلشَّهۡرَ فَلۡيَصُمۡهُۖ وَمَن كَانَ مَرِيضًا أَوۡ عَلَىٰ سَفَرٖ فَعِدَّةٞ مِّنۡ أَيَّامٍ أُخَرَۗ يُرِيدُ ٱللَّهُ بِكُمُ ٱلۡيُسۡرَ وَلَا يُرِيدُ بِكُمُ ٱلۡعُسۡرَ وَلِتُكۡمِلُواْ ٱلۡعِدَّةَ وَلِتُكَبِّرُواْ ٱللَّهَ عَلَىٰ مَا هَدَىٰكُمۡ وَلَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ١٨٥

186. ባሮቼም ከእኔ በጠየቁህ ጊዜ (እንዲህ በላቸው):- እኔ ቅርብ ነኝ:: የለማኝን ጸሎት በለመነኝ ጊዜ እቀበለዋለሁ:: ስለዚህ ለኔ ይታዘዙ፤ በኔም ይመኑ፤ እነሱ ሊመሩ ይከጅላልና::

وَإِذَا سَأَلَكَ عِبَادِى عَنِّى فَإِنِّى قَرِيبٌ ۖ أُجِيبُ دَعْوَةَ ٱلدَّاعِ إِذَا دَعَانِ ۖ فَلْيَسْتَجِيبُوا۟ لِى وَلْيُؤْمِنُوا۟ بِى لَعَلَّهُمْ يَرْشُدُونَ ﴿١٨٦﴾

187. በጾም ሌሊት ወደ ሴቶቻችሁ መድረስ ለናንተ ተፈቀደላችሁ:: እነርሱ ለናንተ ልብሶች ናቸው፤ እናንተም ለነርሱ ልብሶች ናችሁ:: አላህ እናንተ ነፍሶቻችሁን የምትበድሉ መኾናችሁን ዐወቀ:: በእናንተም ላይ ተመለሰላችሁ:: ከእናንተም ይቅርታ አደረገ:: አሁን ተገናኙዋቸው:: አላህም ለናንተ የጻፈላችሁን ነገር (ልጅን) ፈልጉ:: ከጎህ የኾነው ነጩ ክርም ከጥቁሩ ክር (ከሌሊት ጨለማ) ለእናንተ እስከሚገለጽላችሁ ድረስ ብሉ፤ ጠጡም:: ከዚያም ጾምን እስከ ሌሊቱ ድረስ ሙሉ:: እናንተም በመስጊዶች ተቀማጮች ስትኾኑ አትገናኙዋቸው:: ይህች የአላህ ሕግጋት ናትና (ለመተላለፍ) አትቅረቧት:: እንደዚሁ አላህ አንቀጾቹን ለሰዎች ያብራራል:: እነርሱ (የተከለከሉትን) ሊጠነቀቁ ይከጅላልና::

أُحِلَّ لَكُمْ لَيْلَةَ ٱلصِّيَامِ ٱلرَّفَثُ إِلَىٰ نِسَآئِكُمْ ۚ هُنَّ لِبَاسٌ لَّكُمْ وَأَنتُمْ لِبَاسٌ لَّهُنَّ ۗ عَلِمَ ٱللَّهُ أَنَّكُمْ كُنتُمْ تَخْتَانُونَ أَنفُسَكُمْ فَتَابَ عَلَيْكُمْ وَعَفَا عَنكُمْ ۖ فَٱلْـَٰٔنَ بَـٰشِرُوهُنَّ وَٱبْتَغُوا۟ مَا كَتَبَ ٱللَّهُ لَكُمْ ۚ وَكُلُوا۟ وَٱشْرَبُوا۟ حَتَّىٰ يَتَبَيَّنَ لَكُمُ ٱلْخَيْطُ ٱلْأَبْيَضُ مِنَ ٱلْخَيْطِ ٱلْأَسْوَدِ مِنَ ٱلْفَجْرِ ۖ ثُمَّ أَتِمُّوا۟ ٱلصِّيَامَ إِلَى ٱلَّيْلِ ۚ وَلَا تُبَـٰشِرُوهُنَّ وَأَنتُمْ عَـٰكِفُونَ فِى ٱلْمَسَـٰجِدِ ۗ تِلْكَ حُدُودُ ٱللَّهِ فَلَا تَقْرَبُوهَا ۗ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ ءَايَـٰتِهِۦ لِلنَّاسِ لَعَلَّهُمْ يَتَّقُونَ ﴿١٨٧﴾

188. ገንዘቦቻችሁንም በመካከላችሁ በከንቱ (ያለ አግባብ) አትብሉ:: እናንተም የምታውቁ ስትኾኑ ከሰዎች ገንዘቦች ከፊልን በኃጢአት ትበሉ ዘንድ ወደ ዳኞች አትጣሏት::

وَلَا تَأْكُلُوٓا۟ أَمْوَٰلَكُم بَيْنَكُم بِٱلْبَـٰطِلِ وَتُدْلُوا۟ بِهَآ إِلَى ٱلْحُكَّامِ لِتَأْكُلُوا۟ فَرِيقًا مِّنْ أَمْوَٰلِ ٱلنَّاسِ بِٱلْإِثْمِ وَأَنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿١٨٨﴾

189. (ሙሐመድ ሆይ!) ከለጋ ጨረቃዎች (መለዋወጥ) ይጠየቁሃል:: እነርሱ ለሰዎች ጥቅም ለሐጅም (ማወቂያ) ጊዜያቶች (ምልክቶች) ናቸው በላቸው:: መልካም ሥራም ቤቶችን ከጀርባዎቻቸው በመምጣታችሁ አይደለም:: ግን የመልካም ሥራ ባለቤት የተጠነቀቀ ሰው ነው:: ቤቶችንም ከደጃፎቻቸው በኩል ግቡ፤ አላህንም ፍሩ ልትድኑ ይከጅላልና (በላቸው)::

۞ يَسْـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلْأَهِلَّةِ ۖ قُلْ هِىَ مَوَٰقِيتُ لِلنَّاسِ وَٱلْحَجِّ ۗ وَلَيْسَ ٱلْبِرُّ بِأَن تَأْتُوا۟ ٱلْبُيُوتَ مِن ظُهُورِهَا وَلَـٰكِنَّ ٱلْبِرَّ مَنِ ٱتَّقَىٰ ۗ وَأْتُوا۟ ٱلْبُيُوتَ مِنْ أَبْوَٰبِهَا ۚ وَٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ لَعَلَّكُمْ تُفْلِحُونَ ﴿١٨٩﴾

190. እነዚያንም የሚጋደሉዋችሁን (ከሓዲዎች) በአላህ መንገድ ተጋደሉ:: ወሰንንም አትለፉ፤ አላህ ወሰን አላፊዎን አይወድምና::

وَقَـٰتِلُوا۟ فِى سَبِيلِ ٱللَّهِ ٱلَّذِينَ يُقَـٰتِلُونَكُمْ وَلَا تَعْتَدُوٓا۟ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلْمُعْتَدِينَ ﴿١٩٠﴾

191. ባገኛችኋቸውም ስፍራ ሁሉ ግደሉዋቸው:: ከአወጧችሁም ስፍራ አውጧቸው:: መከራም ከመግደል ይበልጥ የበረታች ናት:: በተከበረው መስጊድም ዘንድ በርሱ ውስጥ እስከሚጋደሉዋችሁ ድረስ አትጋደሉዋቸው:: ቢጋደሉዋችሁም ግደሉዋቸው፤ የከሓዲዎች ቅጣት እንደዚህ ነው::

وَٱقْتُلُوهُمْ حَيْثُ ثَقِفْتُمُوهُمْ وَأَخْرِجُوهُم مِّنْ حَيْثُ أَخْرَجُوكُمْ ۚ وَٱلْفِتْنَةُ أَشَدُّ مِنَ ٱلْقَتْلِ ۚ وَلَا تُقَـٰتِلُوهُمْ عِندَ ٱلْمَسْجِدِ ٱلْحَرَامِ حَتَّىٰ يُقَـٰتِلُوكُمْ فِيهِ ۖ فَإِن قَـٰتَلُوكُمْ فَٱقْتُلُوهُمْ ۗ كَذَٰلِكَ جَزَآءُ ٱلْكَـٰفِرِينَ ﴿١٩١﴾

192. ቢከለከሉም አላህ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

فَإِنِ ٱنتَهَوۡاْ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿١٩٢﴾

193. ሁከት እስከማይገኝና ሃይማኖት ለአላህ ብቻ እስከሚኾን ድረስ ተጋደሉዋቸው፡፡ ቢከለከሉም ወሰንን ማለፍ፤ በበዳዮች ላይ እንጂ የለም (ወሰን አትለፉባቸው)፡፡

وَقَٰتِلُوهُمۡ حَتَّىٰ لَا تَكُونَ فِتۡنَةٞ وَيَكُونَ ٱلدِّينُ لِلَّهِۖ فَإِنِ ٱنتَهَوۡاْ فَلَا عُدۡوَٰنَ إِلَّا عَلَى ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٩٣﴾

194. የተከበረው ወር በተከበረው ወር አንጻር ነው፡፡ ክብሮችም ሁሉ ተመሳሳዮች ናቸው፡፡ በእናንተም ላይ (በተከበረው ወር) ወሰን ያለፈባችሁን ሰው በናንተ ላይ ወሰን ባለፈው ብጤ በርሱ ላይ ወሰን እለፉበት፡፡ አላህንም ፍሩ አላህ ከሚፈሩት ጋር መኾኑንም ዕወቁ፡፡

ٱلشَّهۡرُ ٱلۡحَرَامُ بِٱلشَّهۡرِ ٱلۡحَرَامِ وَٱلۡحُرُمَٰتُ قِصَاصٞۚ فَمَنِ ٱعۡتَدَىٰ عَلَيۡكُمۡ فَٱعۡتَدُواْ عَلَيۡهِ بِمِثۡلِ مَا ٱعۡتَدَىٰ عَلَيۡكُمۡۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ مَعَ ٱلۡمُتَّقِينَ ﴿١٩٤﴾

195. በአላህም መንገድ ለግሱ፡፡ በእጆቻችሁም (ነፍሶቻችሁን) ወደ ጥፋት አትጣሉ፡፡ በጎ ሥራንም ሥሩ፤ አላህ በጎ ሠሪዎችን ይወዳልና፡፡

وَأَنفِقُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَلَا تُلۡقُواْ بِأَيۡدِيكُمۡ إِلَى ٱلتَّهۡلُكَةِ وَأَحۡسِنُوٓاْۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ﴿١٩٥﴾

196. ሐጅንና ዑምራንም ለአላህ ሙሉ፡፡ ብትታገዱም ከሀድይ (ከመሥዋእት) የተገራውን (መሰዋት) አለባችሁ፡፡ ሀድዩም እስፍራው እስከሚደርስ ድረስ ራሶቻችሁን አትላጩ፡፡ ከናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በራሱ ሁከት ያለበት የኾነ ሰው (ቢላጭ) ከጾም ወይም ከምጽዋት ወይም ከመሥዋዕት ቤዛ አለበት፡፡ ጸጥታም ባገኛችሁ ጊዜ እስከ ሐጅ በዑምራ የተጣቀመ ሰው ከሀድዩ የተገራውን (መሠዋት) አለበት፡፡ ያላገኘም ሰው ሶስትን ቀኖች በሐጅ ወራት፤ ሰባትም በተመለሳችሁ ጊዜ መጾም አለበት፡፡ ይህች ሙሉ ዐሥር (ቀናት) ናት፡፡ ይህም (ሕግ) ቤተሰቦቹ ከቅዱሱ መስጊድ አቅራቢያ ላልኾኑ ነው፡፡ አላህንም ፍሩ፤ አላህም ቅጣተ ብርቱ መኾኑን እወቁ፡፡

وَأَتِمُّواْ ٱلۡحَجَّ وَٱلۡعُمۡرَةَ لِلَّهِۚ فَإِنۡ أُحۡصِرۡتُمۡ فَمَا ٱسۡتَيۡسَرَ مِنَ ٱلۡهَدۡيِۖ وَلَا تَحۡلِقُواْ رُءُوسَكُمۡ حَتَّىٰ يَبۡلُغَ ٱلۡهَدۡيُ مَحِلَّهُۥۚ فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوۡ بِهِۦٓ أَذٗى مِّن رَّأۡسِهِۦ فَفِدۡيَةٞ مِّن صِيَامٍ أَوۡ صَدَقَةٍ أَوۡ نُسُكٖۚ فَإِذَآ أَمِنتُمۡ فَمَن تَمَتَّعَ بِٱلۡعُمۡرَةِ إِلَى ٱلۡحَجِّ فَمَا ٱسۡتَيۡسَرَ مِنَ ٱلۡهَدۡيِۚ فَمَن لَّمۡ يَجِدۡ فَصِيَامُ ثَلَٰثَةِ أَيَّامٖ فِي ٱلۡحَجِّ وَسَبۡعَةٍ إِذَا رَجَعۡتُمۡۗ تِلۡكَ عَشَرَةٞ كَامِلَةٞۗ ذَٰلِكَ لِمَن لَّمۡ يَكُنۡ أَهۡلُهُۥ حَاضِرِي ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ﴿١٩٦﴾

197. ሐጅ (ጊዜያቱ) የታወቁ ወሮች ናቸው፡፡ በእነርሱም ውስጥ ሐጅን (እንዲሠራ) ነፍሱን ያስገደደ ሰው በሐጅ ውስጥ ሴትን መገናኘት ማመጽም ክርክርም የለም፡፡ ከበጎም ሥራ የምትሠሩትን ሁሉ አላህ ያውቀዋል፡፡ ተሰነቁም፤ ከስንቅም ሁሉ በላጩ ጥንቃቄ (አላህን መፍራት) ነው፡፡ የአእምሮዎችም ባለቤቶች ሆይ! ፍሩኝ፡፡

ٱلۡحَجُّ أَشۡهُرٞ مَّعۡلُومَٰتٞۚ فَمَن فَرَضَ فِيهِنَّ ٱلۡحَجَّ فَلَا رَفَثَ وَلَا فُسُوقَ وَلَا جِدَالَ فِي ٱلۡحَجِّۗ وَمَا تَفۡعَلُواْ مِنۡ خَيۡرٖ يَعۡلَمۡهُ ٱللَّهُۗ وَتَزَوَّدُواْ فَإِنَّ خَيۡرَ ٱلزَّادِ ٱلتَّقۡوَىٰۖ وَٱتَّقُونِ يَٰٓأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ ﴿١٩٧﴾

198. (በሐጅ ጊዜ በንግድ ሥራ) ከጌታችሁ ትርፍን በመፈለጋችሁ በናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ ከዐረፋትም በጎረፋችሁ ጊዜ መሽዐረልሐራም ዘንድ አላህን አውሱ፡፡ (ለሐጅ) ስለመራችሁም አውሱት፡፡ ከመምራቱ በፊትም በእርግጥ ከተሳሳቾች ነበራችሁ፡፡

لَيۡسَ عَلَيۡكُمۡ جُنَاحٌ أَن تَبۡتَغُواْ فَضۡلٗا مِّن رَّبِّكُمۡۚ فَإِذَآ أَفَضۡتُم مِّنۡ عَرَفَٰتٖ فَٱذۡكُرُواْ ٱللَّهَ عِندَ ٱلۡمَشۡعَرِ ٱلۡحَرَامِۖ وَٱذۡكُرُوهُ كَمَا هَدَىٰكُمۡ وَإِن كُنتُم مِّن قَبۡلِهِۦ لَمِنَ ٱلضَّآلِّينَ ١٩٨

199. ከዚያም (ቁረይሾች ሆይ!) ሰዎቹ ከጎረፉበት ስፍራ ጉረፉ፤ (ተመለሱ)፡፡ አላህንም ምሕረትን ለምኑ፤ አላህ እጅግ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

ثُمَّ أَفِيضُواْ مِنۡ حَيۡثُ أَفَاضَ ٱلنَّاسُ وَٱسۡتَغۡفِرُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ١٩٩

200. የሐጅ ሥራዎቻችሁንም በፈጸማችሁ ጊዜ አባቶቻችሁን እንደምታወሱ ወይም ይበልጥ የበረታን ማውሳት አላህን አውሱ፡፡ ከሰዎችም ውስጥ፡- «ጌታችን ሆይ! በምድረዓለም መልካም ዕድልን ስጠን» የሚል ሰው አለ፡፡ ለርሱም በመጨረሻይቱ አገር ከዕድል ምንም የለውም፡፡

فَإِذَا قَضَيۡتُم مَّنَٰسِكَكُمۡ فَٱذۡكُرُواْ ٱللَّهَ كَذِكۡرِكُمۡ ءَابَآءَكُمۡ أَوۡ أَشَدَّ ذِكۡرٗاۗ فَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَقُولُ رَبَّنَآ ءَاتِنَا فِي ٱلدُّنۡيَا وَمَا لَهُۥ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ مِنۡ خَلَٰقٖ ٢٠٠

201. ከእነርሱም ውስጥ፡- «ጌታችን ሆይ! በምድረ ዓለም ደግን ነገር (ጸጋን) በመጨረሻይቱም አገር ደግን ነገር (ገነትን) ስጠን፤ የእሳትንም ቅጣት ጠብቀን» የሚሉ ሰዎች አልሉ፡፡

وَمِنۡهُم مَّن يَقُولُ رَبَّنَآ ءَاتِنَا فِي ٱلدُّنۡيَا حَسَنَةٗ وَفِي ٱلۡأٓخِرَةِ حَسَنَةٗ وَقِنَا عَذَابَ ٱلنَّارِ ٢٠١

202. እነዚያከሠሩት በጎ ሥራ ለነርሱ እድል አላቸው፡፡ አላህም ምርመራው ፈጣን ነው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ نَصِيبٞ مِّمَّا كَسَبُواْۚ وَٱللَّهُ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ٢٠٢

203. በተቆጠሩ ቀኖችም ውስጥ (በሚና ጠጠሮችን ስትወረውሩ) አላህን አውሱ፡፡ በሁለት ቀኖችም ውስጥ (በመኼድ) የተቻኮለ ሰው በርሱ ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ የቆየም ሰው በርሱ ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ (ይህም) አላህን ለፈራ ሰው ነው፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ እናንተ ወደርሱ የምትሰበሰቡ መኾናችሁንም ዕወቁ፡፡

۞وَٱذۡكُرُواْ ٱللَّهَ فِيٓ أَيَّامٖ مَّعۡدُودَٰتٖۚ فَمَن تَعَجَّلَ فِي يَوۡمَيۡنِ فَلَآ إِثۡمَ عَلَيۡهِ وَمَن تَأَخَّرَ فَلَآ إِثۡمَ عَلَيۡهِۖ لِمَنِ ٱتَّقَىٰۗ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّكُمۡ إِلَيۡهِ تُحۡشَرُونَ ٢٠٣

204. ከሰዎችም ውስጥ እርሱ ክርክረ ብርቱ ሲኾን በቅርቢቱ ሕይወት ንግግሩ የሚደንቅህና በልቡ ውስጥ ባለው ነገር ላይ አላህን የሚያስመሰክር ሰው አልለ፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يُعۡجِبُكَ قَوۡلُهُۥ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَيُشۡهِدُ ٱللَّهَ عَلَىٰ مَا فِي قَلۡبِهِۦ وَهُوَ أَلَدُّ ٱلۡخِصَامِ ٢٠٤

205. (ካንተ) በዞረም ጊዜ በምድር ላይ በውስጧ ሊያበላሽና አዝመራንና እንስሳዎችን ሊያጠፋ ይሮጣል፡ ፡ አላህም ማበላሸትን አይወድም፡፡

وَإِذَا تَوَلَّىٰ سَعَىٰ فِي ٱلۡأَرۡضِ لِيُفۡسِدَ فِيهَا وَيُهۡلِكَ ٱلۡحَرۡثَ وَٱلنَّسۡلَۚ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ ٱلۡفَسَادَ ٢٠٥

206. ለእርሱ «አላህን ፍራ» በተባለም ጊዜ፤ ትዕቢቱ በኃጢአት (ሥራ) ላይ ትገፈፋዋለች፡፡ ገሀነምም በቂው ናት፤ (እርሷም) በእርግጥ የከፋች ምንጣፍ ናት፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُ ٱتَّقِ ٱللَّهَ أَخَذَتۡهُ ٱلۡعِزَّةُ بِٱلۡإِثۡمِۚ فَحَسۡبُهُۥ جَهَنَّمُۖ وَلَبِئۡسَ ٱلۡمِهَادُ ٢٠٦

207. ከሰዎችም ውስጥ የአላህን ውዴታ ለመፈለግ ነፍሱን የሚሸጥ ሰው አልለ፡፡ አላህም ለባሮቹ በጣም ርኅሩህ ነው፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَشۡرِي نَفۡسَهُ ٱبۡتِغَآءَ مَرۡضَاتِ ٱللَّهِۚ وَٱللَّهُ رَءُوفُۢ بِٱلۡعِبَادِ ٢٠٧

208. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ሁላችሁም በመታዘዝ ውስጥ ግቡ፡፡ የሰይጣንንም እርምጃዎች አትከተሉ፤ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱدۡخُلُواْ فِي ٱلسِّلۡمِ كَآفَّةٗ وَلَا تَتَّبِعُواْ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيۡطَٰنِۚ إِنَّهُۥ لَكُمۡ عَدُوّٞ مُّبِينٞ ٢٠٨

209. ግልጽ ማስረጃዎችም ከመጡላችሁ በኋላ ብትዘነበሉ አላህ አሸናፊ ጥበበኛ መኾኑን እወቁ፡፡

فَإِن زَلَلۡتُم مِّنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَتۡكُمُ ٱلۡبَيِّنَٰتُ فَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٌ ٢٠٩

210. አላህ (ቅጣቱ)ና መላእክቱ ከደመና በኾኑ ጥላዎች ውስጥ ሊመጡዋቸው እንጂ አይጠባበቁም፡፡ ነገሩም ተፈጸመ፤ ነገሮችም ሁሉ ወደ አላህ ይመለሳሉ፡፡

هَلۡ يَنظُرُونَ إِلَّآ أَن يَأۡتِيَهُمُ ٱللَّهُ فِي ظُلَلٖ مِّنَ ٱلۡغَمَامِ وَٱلۡمَلَـٰٓئِكَةُ وَقُضِيَ ٱلۡأَمۡرُۚ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرۡجَعُ ٱلۡأُمُورُ ٢١٠

211. የእስራኤልን ልጆች ከግልጽ ተዓምር ስንትን እደሰጠናቸው ጠይቃቸው፡፡ የአላህንም ጸጋ ከመጣችለት በኋላ የሚለውጥ ሰው አላህ ቅጣተ ብርቱ ነው፡፡

سَلۡ بَنِيٓ إِسۡرَـٰٓءِيلَ كَمۡ ءَاتَيۡنَٰهُم مِّنۡ ءَايَةِۭ بَيِّنَةٖۗ وَمَن يُبَدِّلۡ نِعۡمَةَ ٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَتۡهُ فَإِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٢١١

212. ለእነዚያ ለካዱት ከእነዚያ ካመኑት የሚሳለቁ ሲኾኑ ቅርቢቱ ሕይወት ተሸለመችላቸው፡፡ እነዚያም የተጠነቀቁት በትንሣኤ ቀን ከበላያቸው ናቸው፡፡ አላህም ለሚሻው ሰው ያለ ግምት ይሰጣል፡፡

زُيِّنَ لِلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا وَيَسۡخَرُونَ مِنَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۘ وَٱلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْ فَوۡقَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۗ وَٱللَّهُ يَرۡزُقُ مَن يَشَآءُ بِغَيۡرِ حِسَابٖ ٢١٢

213. ሰዎቹ ሁሉ አንድ ሕዝብ ነበሩ፤ (ተለያዩ)፡፡ አላህም ነቢያትን አብሳሪዎችና አስፈራሪዎች አድርጎ ላከ፡፡ ከእነርሱም ጋር መጻሕፍትን በሰዎቹ መካከል በዚያ በርሱ በተለያዩበት ነገር ይፈርድ ዘንድ በእውነት አወረደ፡፡ በእርሱም (በሃይማኖት) ግልጽ አስረጂዎች ከመጡላቸው በኋላ በመካከላቸው ለኾነው ምቀኝነት እነዚያው የተሰጡት እንጂ አልተለያዩበትም፡፡ አላህም እነዚያን ያመኑትን ሰዎች ለእዚያ ከእውነት በርሱ ለተለያዩበት በፍቃዱ መራቸው፡፡ አላህም የሚሻውን ሰው ወደ ቀጥተኛው መንገድ ይመራል፡፡

كَانَ ٱلنَّاسُ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ فَبَعَثَ ٱللَّهُ ٱلنَّبِيِّـۧنَ مُبَشِّرِينَ وَمُنذِرِينَ وَأَنزَلَ مَعَهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ بِٱلۡحَقِّ لِيَحۡكُمَ بَيۡنَ ٱلنَّاسِ فِيمَا ٱخۡتَلَفُواْ فِيهِۚ وَمَا ٱخۡتَلَفَ فِيهِ إِلَّا ٱلَّذِينَ أُوتُوهُ مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَتۡهُمُ ٱلۡبَيِّنَٰتُ بَغۡيَۢا بَيۡنَهُمۡۖ فَهَدَى ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لِمَا ٱخۡتَلَفُواْ فِيهِ مِنَ ٱلۡحَقِّ بِإِذۡنِهِۦۗ وَٱللَّهُ يَهۡدِي مَن يَشَآءُ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٍ ٢١٣

214. በእውነቱ የእነዚያ ከበፊታችሁ ያለፉት (ምእምናን መከራ) ብጤ ሳይመጣችሁ ገነትን ልትገቡ ታስባላችሁን? መልክተኛውና እነዚያ ከርሱ ጋር ያመኑት «የአላህ እርዳታ መቼ ነው?» እስከሚሉ ድረስ መከራና ጉዳት ነካቻቸው፤ ተርበደበዱም፡፡ ንቁ! የአላህ እርዳታ በእርግጥ ቅርብ ነው (ተባሉም)፡፡

أَمۡ حَسِبۡتُمۡ أَن تَدۡخُلُواْ ٱلۡجَنَّةَ وَلَمَّا يَأۡتِكُم مَّثَلُ ٱلَّذِينَ خَلَوۡاْ مِن قَبۡلِكُمۖ مَّسَّتۡهُمُ ٱلۡبَأۡسَآءُ وَٱلضَّرَّآءُ وَزُلۡزِلُواْ حَتَّىٰ يَقُولَ ٱلرَّسُولُ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَهُۥ مَتَىٰ نَصۡرُ ٱللَّهِۗ أَلَآ إِنَّ نَصۡرَ ٱللَّهِ قَرِيبٞ ٢١٤

215. ምንን (ለማንም) እንደሚለግሱ ይጠይቁሃል:: ከመልካም ነገር የምትለግሱት፤ ለወላጆችና ለቅርብ ዘመዶች፣ ለየቲሞችም፣ ለድሆችም፣ ለመንገደኞችም ነው:: ከበጎ ነገርም ማንኛውንም ብትሠሩ አላህ እርሱን ዐዋቂ ነው በላቸው::

يَسۡـَٔلُونَكَ مَاذَا يُنفِقُونَۖ قُلۡ مَآ أَنفَقۡتُم مِّنۡ خَيۡرٖ فَلِلۡوَٰلِدَيۡنِ وَٱلۡأَقۡرَبِينَ وَٱلۡيَتَٰمَىٰ وَٱلۡمَسَٰكِينِ وَٱبۡنِ ٱلسَّبِيلِۗ وَمَا تَفۡعَلُواْ مِنۡ خَيۡرٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ بِهِۦ عَلِيمٞ ٢١٥

216. መጋደል እርሱ ለእናንተ የተጠላ ሲሆን በእናንተ ላይ ተጻፈ:: አንዳች ነገርን እርሱ ለናንተ የበለጠ ሲሆን የምትጠሉት መኾናችሁ ተረጋገጠ:: አንዳችንም ነገር እርሱ ለናንተ መጥፎ ሲሆን የምትወዱት መሆናችሁ ተረጋገጠ:: አላህም (የሚሻላችሁን) ያውቃል ግን እናንተ አታውቁም::

كُتِبَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡقِتَالُ وَهُوَ كُرۡهٞ لَّكُمۡۖ وَعَسَىٰٓ أَن تَكۡرَهُواْ شَيۡـٔٗا وَهُوَ خَيۡرٞ لَّكُمۡۖ وَعَسَىٰٓ أَن تُحِبُّواْ شَيۡـٔٗا وَهُوَ شَرّٞ لَّكُمۡۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ وَأَنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ٢١٦

217. ከተከበረው ወር (ከረጀብ) በርሱ ውስጥ ከመጋደል ይጠይቁሃል:: በላቸው «በርሱ ውስጥ መጋደል ታላቅ (ኀጢአት) ነው:: ግን ከአላህ መንገድ (ሰዎችን) መከላከል፣ በርሱም መካድ፣ ከተከበረውም መስጊድ (ማገድ) ባለቤቶቹንም ከርሱ ማውጣት አላህ ዘንድ ይበልጥ ታላቅ (ወንጀል) ነው:: ፈተናም (ማጋራት) ከመግደል ይበልጥ ከባድ ነው:: (ከሐዲዎች) ቢችሉ ከሃይማኖታችሁ እስከሚመልሷችሁ ድረስ የሚዋጉዋችሁ ከመሆን አይቦዝኑም:: ከእናንተ ውስጥም ከሃይማኖቱ የሚመለስና እርሱም ከሐዲ ሆኖ የሚሞት ሰው እነዚያ (በጎ) ሥራቸው በቅርቢቱም በመጨረሻይቱም አገር ተበላሸች:: እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው:: እነርሱ በርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው::»

يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلشَّهۡرِ ٱلۡحَرَامِ قِتَالٖ فِيهِۖ قُلۡ قِتَالٞ فِيهِ كَبِيرٞۚ وَصَدٌّ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَكُفۡرُۢ بِهِۦ وَٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِ وَإِخۡرَاجُ أَهۡلِهِۦ مِنۡهُ أَكۡبَرُ عِندَ ٱللَّهِۚ وَٱلۡفِتۡنَةُ أَكۡبَرُ مِنَ ٱلۡقَتۡلِۗ وَلَا يَزَالُونَ يُقَٰتِلُونَكُمۡ حَتَّىٰ يَرُدُّوكُمۡ عَن دِينِكُمۡ إِنِ ٱسۡتَطَٰعُواْۚ وَمَن يَرۡتَدِدۡ مِنكُمۡ عَن دِينِهِۦ فَيَمُتۡ وَهُوَ كَافِرٞ فَأُوْلَٰٓئِكَ حَبِطَتۡ أَعۡمَٰلُهُمۡ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٢١٧

218. እነዚያ ያመኑትና እነዚያም (ከአገራቸው) የተሰደዱት በአላህም መንገድ ላይ የተጋደሉት እነዚያ የአላህን እዝነት ይከጅላሉ:: አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው::

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَٱلَّذِينَ هَاجَرُواْ وَجَٰهَدُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ أُوْلَٰٓئِكَ يَرۡجُونَ رَحۡمَتَ ٱللَّهِۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٢١٨

219. አእምሮን ከሚቃወም መጠጥና ከቁማር ይጠይቁሃል:: «በሁለቱም ውስጥ ታላቅ ኃጢአትና ለሰዎች ጥቅሞች አሉባቸው:: ግን ኃጢአታቸው ከጥቅማቸው በጣም ትልቅ ነው» በላቸው:: ምንን እንደሚመጸውቱም (መጠኑን) ይጠይቁሃል:: «ትርፍን (መጽውቱ)» በላቸው:: እንደዚሁ ታስተነትኑ ዘንድ አላህ ለናንተ አንቀጾችን ይገልጽላችኋል::

۞يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلۡخَمۡرِ وَٱلۡمَيۡسِرِۖ قُلۡ فِيهِمَآ إِثۡمٞ كَبِيرٞ وَمَنَٰفِعُ لِلنَّاسِ وَإِثۡمُهُمَآ أَكۡبَرُ مِن نَّفۡعِهِمَاۗ وَيَسۡـَٔلُونَكَ مَاذَا يُنفِقُونَۖ قُلِ ٱلۡعَفۡوَۗ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمُ ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّكُمۡ تَتَفَكَّرُونَ ٢١٩

220. በቅርቢቱ ዓለምና በመጨረሻይቱ ታስተነትኑ ዘንድ (ይገልጽላችኋል):: ከየቲሞችም ይጠይቁሃል:: «ለእነርሱ (ገንዘባቸውን በማራባት) ማሳመር በላጭ ነው:: ብትቀላቀሏቸውም ወንድሞቻችሁ ናቸው:: አላህም የሚያጠፋውን ከሚያበጀው (ለይቶ) ያውቃል:: አላህም በሻ ኖሮ ባስቸገራችሁ ነበር፤ አላህ አሸናፊ ጥበበኛ ነውና» በላቸው::

فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِۗ وَيَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلۡيَتَٰمَىٰۖ قُلۡ إِصۡلَاحٞ لَّهُمۡ خَيۡرٞۖ وَإِن تُخَالِطُوهُمۡ فَإِخۡوَٰنُكُمۡۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ ٱلۡمُفۡسِدَ مِنَ ٱلۡمُصۡلِحِۚ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَأَعۡنَتَكُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٢٢٠

221. (በአላህ) አጋሪ የሆኑ ሴቶች እስከሚያምኑ ድረስ አታግቡዋቸው፡፡ ከአጋሪይቱ ምንም ብትደንቃችሁም እንኳ ያመነችው ባሪያ በእርግጥ በላጭ ናት፡፡ ለአጋሪዎቹም እስከሚያምኑ ድረስ አትዳሩላቸው፡፡ ከአጋሪው (ጌታ) ምንም ቢደንቃችሁ ምእምኑ ባሪያ በላጭ ነው፡፡ እነዚያ (አጋሪዎች) ወደ እሳት ይጣራሉ፡፡ አላህም በፈቃዱ ወደ ገነትና ወደ ምሕረት ይጠራል፡፡ ሕግጋቱንም ለሰዎች ይገልጻል እነርሱ ሊገሰጹ ይከጀላልና፡፡

وَلَا تَنكِحُواْ ٱلۡمُشۡرِكَٰتِ حَتَّىٰ يُؤۡمِنَّۚ وَلَأَمَةٞ مُّؤۡمِنَةٌ خَيۡرٞ مِّن مُّشۡرِكَةٖ وَلَوۡ أَعۡجَبَتۡكُمۡۗ وَلَا تُنكِحُواْ ٱلۡمُشۡرِكِينَ حَتَّىٰ يُؤۡمِنُواْۚ وَلَعَبۡدٞ مُّؤۡمِنٌ خَيۡرٞ مِّن مُّشۡرِكٖ وَلَوۡ أَعۡجَبَكُمۡۗ أُوْلَٰٓئِكَ يَدۡعُونَ إِلَى ٱلنَّارِۖ وَٱللَّهُ يَدۡعُوٓاْ إِلَى ٱلۡجَنَّةِ وَٱلۡمَغۡفِرَةِ بِإِذۡنِهِۦۖ وَيُبَيِّنُ ءَايَٰتِهِۦ لِلنَّاسِ لَعَلَّهُمۡ يَتَذَكَّرُونَ ٢٢١

222. ከወር አበባም ይጠይቁሃል፡፡ እርሱ አስጠያፊ ነው፡፡ ሴቶችንም በወር አበባ ጊዜ ራቋቸው፡፡ ንጹሕ እስከሚኾኑም ድረስ አትቅረቡዋቸው፡፡ ንጹሕ በኾኑም ጊዜ አላህ ካዘዛችሁ ስፍራ ተገናኙዋቸው፡፡ አላህ (ከኃጢአት) ተመላሾችን ይወዳል፤ ተጥራሪዎችንም ይወዳል በላቸው፡፡

وَيَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلۡمَحِيضِۖ قُلۡ هُوَ أَذٗى فَٱعۡتَزِلُواْ ٱلنِّسَآءَ فِي ٱلۡمَحِيضِ وَلَا تَقۡرَبُوهُنَّ حَتَّىٰ يَطۡهُرۡنَۖ فَإِذَا تَطَهَّرۡنَ فَأۡتُوهُنَّ مِنۡ حَيۡثُ أَمَرَكُمُ ٱللَّهُۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلتَّوَّٰبِينَ وَيُحِبُّ ٱلۡمُتَطَهِّرِينَ ٢٢٢

223. ሴቶቻችሁ ለናንተ እርሻ ናቸው፡፡ እርሻችሁንም በፈለጋችሁት ኹነታ ድረሱ፡፡ ለነፍሶቻችሁም (መልካም ሥራን) አስቀድሙ፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ እናንተም ተገናኝዎቹ መኾናችሁን ዕወቁ፡፡ ምእመናንንም (በገነት) አብስር፡፡

نِسَآؤُكُمۡ حَرۡثٞ لَّكُمۡ فَأۡتُواْ حَرۡثَكُمۡ أَنَّىٰ شِئۡتُمۡۖ وَقَدِّمُواْ لِأَنفُسِكُمۡۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّكُم مُّلَٰقُوهُۗ وَبَشِّرِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٢٢٣

224. መልካም እንዳትሠሩ፣ አላህንም እንዳትፈሩ፣ በሰዎችም መካከል እንዳታስታርቁ አላህን ለመሐላዎቻችሁ ግርዶ አታድርጉ፡፡ አላህም ሰሚ አዋቂ ነው፡፡

وَلَا تَجۡعَلُواْ ٱللَّهَ عُرۡضَةٗ لِّأَيۡمَٰنِكُمۡ أَن تَبَرُّواْ وَتَتَّقُواْ وَتُصۡلِحُواْ بَيۡنَ ٱلنَّاسِۚ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ٢٢٤

225. በመሐላዎቻችሁ በውድቁ (ሳታስቡ በምትምሉት) አላህ አይዛችሁም፡፡ ግን ልቦቻችሁ ባሰቡት ይይዛችኋል፡፡ አላህም በጣም መሐሪ ታጋሽ ነው፡፡

لَّا يُؤَاخِذُكُمُ ٱللَّهُ بِٱللَّغۡوِ فِيٓ أَيۡمَٰنِكُمۡ وَلَٰكِن يُؤَاخِذُكُم بِمَا كَسَبَتۡ قُلُوبُكُمۡۗ وَٱللَّهُ غَفُورٌ حَلِيمٞ ٢٢٥

226. ለእነዚያ ከሴቶቻቸው (ላይቀርቡ) ለሚምሉት አራትን ወሮች መጠበቅ አለባቸው፡፡ (ከመሐላቸው) ቢመለሱም አላህ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

لِّلَّذِينَ يُؤۡلُونَ مِن نِّسَآئِهِمۡ تَرَبُّصُ أَرۡبَعَةِ أَشۡهُرٖۖ فَإِن فَآءُو فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٢٢٦

227. መፍታትንም ቁርጥ አሳብ ቢያደርጉ (ይፍቱ)፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

وَإِنۡ عَزَمُواْ ٱلطَّلَٰقَ فَإِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ٢٢٧

228. የተፈቱ ሴቶችም ነፍሶቻቸውን (ከማግባት) ሦስትን ቁርእ ይጠብቁ፡፡ በአላህና በመጨረሻውም ቀን የሚያምኑ ቢኾኑ አላህ በማሕፀኖቻቸው ውስጥ የፈጠረውን ሊደብቁ ለነርሱ አይፈቀድላቸውም፡፡ ባሎቻቸውም በዚህ ውስጥ እርቅን ቢፈልጉ በመማለሳቸው ተገቢዎች ናቸው፡፡ ለእነርሱም (ለሴቶች) የዚያ በእነርሱ ላይ ያለባቸው (ግዳጅ) ብጤ በመልካም አኗኗር (በባሎቻቸው ላይ መብት) አላቸው፡፡ ለወንዶችም (ጣጣቸውን ስለሚሸከሙ) በእነሱ ላይ ብልጫ አላቸው፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَٱلۡمُطَلَّقَٰتُ يَتَرَبَّصۡنَ بِأَنفُسِهِنَّ ثَلَٰثَةَ قُرُوٓءٖۚ وَلَا يَحِلُّ لَهُنَّ أَن يَكۡتُمۡنَ مَا خَلَقَ ٱللَّهُ فِيٓ أَرۡحَامِهِنَّ إِن كُنَّ يُؤۡمِنَّ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِۚ وَبُعُولَتُهُنَّ أَحَقُّ بِرَدِّهِنَّ فِي ذَٰلِكَ إِنۡ أَرَادُوٓاْ إِصۡلَٰحٗاۚ وَلَهُنَّ مِثۡلُ ٱلَّذِي عَلَيۡهِنَّ بِٱلۡمَعۡرُوفِۚ وَلِلرِّجَالِ عَلَيۡهِنَّ دَرَجَةٞۗ وَٱللَّهُ عَزِيزٌ حَكِيمٌ ٢٢٨

229. ፍች ሁለት ጊዜ ነው፤ (ከዚህ በኋላ) በመልካም መያዝ ወይም በበጎ አኳኋን ማሰናበት ነው፡፡ የአላህንም ሕግጋት አለመጠበቃቸውን ካላወቁ በስተቀር ከሰጣችኋቸው ነገር ምንንም ልትወስዱ ለእናንተ (ለባሎች) አይፈቀድላችሁም፡፡ የአላህንም ሕግጋት አለመጠበቃቸውን ብታውቁ በእርሱ (ነፍሷን) በተበዠችበት ነገር በሁለቱም ላይ ኃጢአት የለም፡፡ ይህች የአላህ ሕግጋት ናት፤ አትተላለፏትም፡፡ የአላህንም ሕግጋት የሚተላለፉ እነዚያ እነርሱ በዳዮች ናቸው፡፡

ٱلطَّلَٰقُ مَرَّتَانِۖ فَإِمۡسَاكُۢ بِمَعۡرُوفٍ أَوۡ تَسۡرِيحُۢ بِإِحۡسَٰنٖۗ وَلَا يَحِلُّ لَكُمۡ أَن تَأۡخُذُواْ مِمَّآ ءَاتَيۡتُمُوهُنَّ شَيۡـًٔا إِلَّآ أَن يَخَافَآ أَلَّا يُقِيمَا حُدُودَ ٱللَّهِۖ فَإِنۡ خِفۡتُمۡ أَلَّا يُقِيمَا حُدُودَ ٱللَّهِ فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡهِمَا فِيمَا ٱفۡتَدَتۡ بِهِۦۗ تِلۡكَ حُدُودُ ٱللَّهِ فَلَا تَعۡتَدُوهَاۚ وَمَن يَتَعَدَّ حُدُودَ ٱللَّهِ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٢٢٩

230. (ሦስተኛ) ቢፈታትም ከዚህ በኋላ ሌላን ባል እስከምታገባ ድረስ ለርሱ አትፈቀድለትም፡፡ (ሁለተኛው ባል) ቢፈታትም የአላህን ሕግጋት መጠበቃቸውን ቢያውቁ በመማለሳቸው በሁለቱም ላይ ኃጢአት የለባቸውም፡፡ ይህችም የአላህ ሕግጋት ናት ለሚያውቁ ሕዝቦች ያብራራታል፡፡

فَإِن طَلَّقَهَا فَلَا تَحِلُّ لَهُۥ مِنۢ بَعۡدُ حَتَّىٰ تَنكِحَ زَوۡجًا غَيۡرَهُۥۗ فَإِن طَلَّقَهَا فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡهِمَآ أَن يَتَرَاجَعَآ إِن ظَنَّآ أَن يُقِيمَا حُدُودَ ٱللَّهِۗ وَتِلۡكَ حُدُودُ ٱللَّهِ يُبَيِّنُهَا لِقَوۡمٖ يَعۡلَمُونَ ٢٣٠

231. ሴቶችን በፈታችሁና (የዒዳ) ጊዜያቸውን በደረሱ ጊዜ በመልካም ያዙዋቸው፤ (ተማለሷቸው) ወይም በመልካም ኹኔታ አሰናብቱዋቸው፡፡ ለመጉዳትም ወሰን ታልፋባቸው ዘንድ አትያዙዋቸው፤ ይህንንም የሚሠራ ሰው ነፍሱን በእርግጥ በደለ፡፡ የአላህንም አንቀጾች ማላገጫ አድርጋችሁ አትያዙ፡፡ የአላህንም ጸጋ በናንተ ላይ ያደረገውን ከመጽሐፍና ከጥበብም በርሱ የሚገስጻችሁ ሲኾን በናንተ ላይ ያወረደውን አስታውሱ፡፡ አላህንም ፍሩ፤ አላህም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ መኾኑን ዕወቁ፡፡

وَإِذَا طَلَّقۡتُمُ ٱلنِّسَآءَ فَبَلَغۡنَ أَجَلَهُنَّ فَأَمۡسِكُوهُنَّ بِمَعۡرُوفٍ أَوۡ سَرِّحُوهُنَّ بِمَعۡرُوفٖۚ وَلَا تُمۡسِكُوهُنَّ ضِرَارٗا لِّتَعۡتَدُواْۚ وَمَن يَفۡعَلۡ ذَٰلِكَ فَقَدۡ ظَلَمَ نَفۡسَهُۥۚ وَلَا تَتَّخِذُوٓاْ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ هُزُوٗاۚ وَٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَمَآ أَنزَلَ عَلَيۡكُم مِّنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَٱلۡحِكۡمَةِ يَعِظُكُم بِهِۦۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ٢٣١

232. ሴቶችንም በፈታችሁና ጊዜያቸውን በደረሱ ጊዜ በመካከላቸው በሕግ በተዋደዱ ጊዜ ባሎቻቸውን ከማግባት አታስተጓጉሏቸው፡፡ ይህ (መከልከል) ከእናንተ በአላህና በመጨረሻው ቀን የሚያምን ሰው በርሱ ይገሰጽበታል፡፡ ይህ ሁኔታችሁ ለእናንተ በላጭ ነው፤ (ከመጠርጠር) አጥሪም ነው፡፡ አላህም ያውቃል፤ እናንተ ግን አታውቁም፡፡

وَإِذَا طَلَّقْتُمُ ٱلنِّسَآءَ فَبَلَغْنَ أَجَلَهُنَّ فَلَا تَعْضُلُوهُنَّ أَن يَنكِحْنَ أَزْوَٰجَهُنَّ إِذَا تَرَٰضَوْاْ بَيْنَهُم بِٱلْمَعْرُوفِ ۗ ذَٰلِكَ يُوعَظُ بِهِۦ مَن كَانَ مِنكُمْ يُؤْمِنُ بِٱللَّهِ وَٱلْيَوْمِ ٱلْءَاخِرِ ۗ ذَٰلِكُمْ أَزْكَىٰ لَكُمْ وَأَطْهَرُ ۚ وَٱللَّهُ يَعْلَمُ وَأَنتُمْ لَا تَعْلَمُونَ ﴿٢٣٢﴾

233. እናቶችም ልጆቻቸውን ሙሉ የኾኑን ሁለት ዓመታት ያጥቡ፡፡ (ይህም) ማጥባትን መሙላት ለሻ ሰው ነው፡፡ ለእርሱም በተወለደለት (አባት) ላይ ምግባቸውና ልብሳቸው በችሎታው ልክ አለበት፡፡ ነፍስ ችሎታዋን እንጂ አትገደድም፡፡ ወላጂት (እናት) በልጅዋ ምክንያት ለርሱ የተወለደለትም (አባት) በልጁ ምክንያት አይጎዳዱ፡፡ በወራሽም ላይ እንደዚሁ ብጤ አለበት፡፡ (ወላጆቹ) ከሁለቱም በኾነ መዋደድና መመካከር (ልጁን ከጡት) መነጠልን ቢፈልጉ በሁለቱም ላይ ኃጢአት የለባቸውም፡፡ ልጆቻችሁንም ለሌሎች አጥቢዎች ማስጠባትን ብትፈልጉ ልትሰጡ የሻችሁትን በመልካም ኹኔታ በሰጣችሁ ጊዜ (በማስጠባታችሁ) በእናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ አላህንም ፍሩ፤ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች መኾኑን ዕወቁ፡፡

۞ وَٱلْوَٰلِدَٰتُ يُرْضِعْنَ أَوْلَٰدَهُنَّ حَوْلَيْنِ كَامِلَيْنِ ۖ لِمَنْ أَرَادَ أَن يُتِمَّ ٱلرَّضَاعَةَ ۚ وَعَلَى ٱلْمَوْلُودِ لَهُۥ رِزْقُهُنَّ وَكِسْوَتُهُنَّ بِٱلْمَعْرُوفِ ۚ لَا تُكَلَّفُ نَفْسٌ إِلَّا وُسْعَهَا ۚ لَا تُضَآرَّ وَٰلِدَةٌۢ بِوَلَدِهَا وَلَا مَوْلُودٌ لَّهُۥ بِوَلَدِهِۦ ۚ وَعَلَى ٱلْوَارِثِ مِثْلُ ذَٰلِكَ ۗ فَإِنْ أَرَادَا فِصَالًا عَن تَرَاضٍ مِّنْهُمَا وَتَشَاوُرٍ فَلَا جُنَاحَ عَلَيْهِمَا ۗ وَإِنْ أَرَدتُّمْ أَن تَسْتَرْضِعُوٓاْ أَوْلَٰدَكُمْ فَلَا جُنَاحَ عَلَيْكُمْ إِذَا سَلَّمْتُم مَّآ ءَاتَيْتُم بِٱلْمَعْرُوفِ ۗ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ بِمَا تَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ﴿٢٣٣﴾

234. እነዚያም ከናንተ ውስጥ የሚሞቱና ሚስቶችን የሚተዉ (ሚስቶቻቸው) በነፍሶቻቸው አራት ወሮች ከዐስር (ቀናት ከጋብቻ) ይታገሱ፡፡ ጊዜያቸውንም በጨረሱ ጊዜ በነፍሶቻቸው በታወቀ ሕግ በሠሩት ነገር በእናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጥ ዐዋቂ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ يُتَوَفَّوْنَ مِنكُمْ وَيَذَرُونَ أَزْوَٰجًا يَتَرَبَّصْنَ بِأَنفُسِهِنَّ أَرْبَعَةَ أَشْهُرٍ وَعَشْرًا ۖ فَإِذَا بَلَغْنَ أَجَلَهُنَّ فَلَا جُنَاحَ عَلَيْكُمْ فِيمَا فَعَلْنَ فِىٓ أَنفُسِهِنَّ بِٱلْمَعْرُوفِ ۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرٌ ﴿٢٣٤﴾

235. ሴቶችንም ከማጨት በርሱ ባሸሞራችሁበት ወይም በነፍሶቻችሁ ውስጥ (ለማግባት) በደበቃችሁት በናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ አላህ እናንተ በእርግጥ የምታስታውሷቸው መኾናችሁን ዐወቀ፡፡ (ስለዚህ ማሸሞርንና ማሰብን ፈቀደላችሁ፡፡) ግን በሕግ የታወቀን ንግግር የምትነጋገሩ ካልኾናችሁ በስተቀር፤ ምስጢርን (ጋብቻን) አትቃጠሩዋቸው፡፡ የተጻፈውም (ዒዳህ) ጊዜውን እስከሚደርስ ድረስ ጋብቻን ለመዋዋል ቁርጥ ሐሳብ አታድርጉ፡፡ አላህም በነፍሶቻችሁ ያለውን ነገር የሚያውቅ መኾኑን ዕወቁ፤ ተጠንቀቁትም፡፡ አላህም መሓሪ ታጋሽ መኾኑን ዕወቁ፡፡

وَلَا جُنَاحَ عَلَيْكُمْ فِيمَا عَرَّضْتُم بِهِۦ مِنْ خِطْبَةِ ٱلنِّسَآءِ أَوْ أَكْنَنتُمْ فِىٓ أَنفُسِكُمْ ۚ عَلِمَ ٱللَّهُ أَنَّكُمْ سَتَذْكُرُونَهُنَّ وَلَٰكِن لَّا تُوَاعِدُوهُنَّ سِرًّا إِلَّآ أَن تَقُولُواْ قَوْلًا مَّعْرُوفًا ۚ وَلَا تَعْزِمُواْ عُقْدَةَ ٱلنِّكَاحِ حَتَّىٰ يَبْلُغَ ٱلْكِتَٰبُ أَجَلَهُۥ ۚ وَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ يَعْلَمُ مَا فِىٓ أَنفُسِكُمْ فَٱحْذَرُوهُ ۚ وَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ غَفُورٌ حَلِيمٌ ﴿٢٣٥﴾

236. ሴቶችን ሳትነኳቸው (ሳትገናኙ)፤ ወይም ለነሱ መህርን ሳትወስኑላቸው ብትፈቷቸው በናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ (ዳረጎት በመስጠት መፍታት ትችላላችሁ፡፡) ጥቀሟቸውም፡፡ በሀብታም ላይ ችሎታው በድኻም ላይ ችሎታው (አቅሙ የሚፈቅደውን መስጠት) አለበት፡፡ መልካም የኾነን መጥቀም በበጎ ሠሪዎች ላይ የተረጋገጠን፤ (ጥቀሟቸው)፡፡

لَّا جُنَاحَ عَلَيۡكُمۡ إِن طَلَّقۡتُمُ ٱلنِّسَآءَ مَا لَمۡ تَمَسُّوهُنَّ أَوۡ تَفۡرِضُواْ لَهُنَّ فَرِيضَةٗۚ وَمَتِّعُوهُنَّ عَلَى ٱلۡمُوسِعِ قَدَرُهُۥ وَعَلَى ٱلۡمُقۡتِرِ قَدَرُهُۥ مَتَٰعَۢا بِٱلۡمَعۡرُوفِۖ حَقًّا عَلَى ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٢٣٦

237. ለእነርሱም መወሰንን በእርግጥ የወሰናችሁላቸው ስትኾኑ ሳትነኳቸው በፊት ብትፈቷቸው ካልማሩዋችሁ ወይም ያ የጋብቻው ውል በእጁ የኾነው (ባልየው) ካልማረ በስተቀር የወሰናችሁት ግማሹ አላቸው፡፡ ምሕረትም ማድረጋችሁ ወደ አላህ ፍራቻ በጣም የቀረበ ነው፡፡ በመካከላችሁም ችሮታን አትርሱ፤ አላህ የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነውና፡፡

وَإِن طَلَّقۡتُمُوهُنَّ مِن قَبۡلِ أَن تَمَسُّوهُنَّ وَقَدۡ فَرَضۡتُمۡ لَهُنَّ فَرِيضَةٗ فَنِصۡفُ مَا فَرَضۡتُمۡ إِلَّآ أَن يَعۡفُونَ أَوۡ يَعۡفُوَاْ ٱلَّذِي بِيَدِهِۦ عُقۡدَةُ ٱلنِّكَاحِۚ وَأَن تَعۡفُوٓاْ أَقۡرَبُ لِلتَّقۡوَىٰۚ وَلَا تَنسَوُاْ ٱلۡفَضۡلَ بَيۡنَكُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٌ ٢٣٧

238. በሶላቶች (በተለይ) በመካከለኛይቱም ሶላት ላይ ተጠባበቁ፡፡ ታዛዦች ኾናችሁም ለአላህ ቁሙ፡፡

حَٰفِظُواْ عَلَى ٱلصَّلَوَٰتِ وَٱلصَّلَوٰةِ ٱلۡوُسۡطَىٰ وَقُومُواْ لِلَّهِ قَٰنِتِينَ ٢٣٨

239. ብትፈሩም እግረኞች ወይም ጋላቢዎች ኾናችሁ (ስገዱ)፡፡ ጸጥተኞችም በኾናችሁ ጊዜ ታውቁት ያልነበራችሁትን እንደ አሳወቃችሁ አላህን አውሱ (ስገዱ)፡፡

فَإِنۡ خِفۡتُمۡ فَرِجَالًا أَوۡ رُكۡبَانٗاۖ فَإِذَآ أَمِنتُمۡ فَٱذۡكُرُواْ ٱللَّهَ كَمَا عَلَّمَكُم مَّا لَمۡ تَكُونُواْ تَعۡلَمُونَ ٢٣٩

240. እነዚያ ከናንተ ውስጥ የሚሞቱ ሚስቶችንም የሚተዉ፤ ለሚስቶቻቸው (ከቤታቸው) የማይወጡ ሲኾኑ ዓመት ድረስ መጠቀምን ኑዛዜን (ይናዘዙ)፡፡ በፈቃዳቸው ቢወጡም በሕግ ከታወቀው ነገር በነፍሶቻቸው በሠሩት በእናንተ (በሟቹ ዘመዶች) ላይ ኃጢአት የለባችሁም አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ يُتَوَفَّوۡنَ مِنكُمۡ وَيَذَرُونَ أَزۡوَٰجٗا وَصِيَّةٗ لِّأَزۡوَٰجِهِم مَّتَٰعًا إِلَى ٱلۡحَوۡلِ غَيۡرَ إِخۡرَاجٖۚ فَإِنۡ خَرَجۡنَ فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡكُمۡ فِي مَا فَعَلۡنَ فِيٓ أَنفُسِهِنَّ مِن مَّعۡرُوفٖۗ وَٱللَّهُ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٢٤٠

241. ለተፈቱ ሴቶችም በችሎታ መጠን ዳረጎት አላቸው፡፡ አላህን በሚፈሩ ላይ ተደንግጓል፡፡

وَلِلۡمُطَلَّقَٰتِ مَتَٰعُۢ بِٱلۡمَعۡرُوفِۖ حَقًّا عَلَى ٱلۡمُتَّقِينَ ٢٤١

242. እንደዚሁ አላህ አንቀጾቹን ታውቁ ዘንድ ለናንተ ያብራራላችኋል፡፡

كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمۡ ءَايَٰتِهِۦ لَعَلَّكُمۡ تَعۡقِلُونَ ٢٤٢

243. ወደ እነዚያ እነርሱ ብዙ ሺሕ ኾነው ሞትን ለመፍራት ከሀገሮቻቸው ወደ ወጡት ሰዎች ዕውቀትህ አልደረሰምን? አላህም ለነርሱ «ሙቱ» አላቸው፤ (ሞቱም)፡፡ ከዚያም ሕያው አደረጋቸው፡፡ አላህም በሰዎች ላይ ባለችሮታ ነው፤ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያመሰግኑም፡፡

۞أَلَمۡ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ خَرَجُواْ مِن دِيَٰرِهِمۡ وَهُمۡ أُلُوفٌ حَذَرَ ٱلۡمَوۡتِ فَقَالَ لَهُمُ ٱللَّهُ مُوتُواْ ثُمَّ أَحۡيَٰهُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَذُو فَضۡلٍ عَلَى ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَشۡكُرُونَ ٢٤٣

244. በአላህም መንገድ (ሃይማኖት) ተጋደሉ፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ መኾኑን ዕወቁ፡፡

وَقَٰتِلُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ٢٤٤

245. ያ ለአላህ መልካም ብድርን የሚያበድርና ለእርሱ (አላህ) ብዙ እጥፎች አድርጎ የሚያነባብርለት ማነው? አላህም ይጨብጣል፤ ይዘረጋልም፤ ወደ እርሱም ትመለሳላችሁ::

مَّن ذَا ٱلَّذِى يُقۡرِضُ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنًا فَيُضَٰعِفَهُۥ لَهُۥٓ أَضۡعَافًا كَثِيرَةً ۚ وَٱللَّهُ يَقۡبِضُ وَيَبۡصُۜطُ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ﴿٢٤٥﴾

246. ከእስራኤል ልጆች ከሙሳ በኋላ ወደ ነበሩት ጭፍሮች ለነቢያቸው (ለሳሙኤል)፡- «ለእኛ ንጉሥን አስነሳልን በአላህ መንገድ እንዋጋለን፤» ባሉ ጊዜ አላየህምን? (አላወቅህምን?)፡-«መዋጋት ቢጻፍባችሁ አትዋጉም ይኾናል» አላቸው:: «ከሀገሮቻችንና ከልጆቻችን የተባረርን ስንኾን በአላህ መንገድ የማንዋጋ ለእኛ ምን አለን?» አሉ:: በእነርሱ ላይ መዋጋት በተጻፈባቸውም ጊዜ ከእነርሱ ጥቂቶች ሲቀሩ አፈገፈጉ:: አላህም በዳዮቹን ዐዋቂ ነው::

أَلَمۡ تَرَ إِلَى ٱلۡمَلَإِ مِنۢ بَنِىٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ مِنۢ بَعۡدِ مُوسَىٰٓ إِذۡ قَالُواْ لِنَبِىٍّ لَّهُمُ ٱبۡعَثۡ لَنَا مَلِكًا نُّقَٰتِلۡ فِى سَبِيلِ ٱللَّهِ ۖ قَالَ هَلۡ عَسَيۡتُمۡ إِن كُتِبَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡقِتَالُ أَلَّا تُقَٰتِلُواْ ۖ قَالُواْ وَمَا لَنَآ أَلَّا نُقَٰتِلَ فِى سَبِيلِ ٱللَّهِ وَقَدۡ أُخۡرِجۡنَا مِن دِيَٰرِنَا وَأَبۡنَآئِنَا ۖ فَلَمَّا كُتِبَ عَلَيۡهِمُ ٱلۡقِتَالُ تَوَلَّوۡاْ إِلَّا قَلِيلًا مِّنۡهُمۡ ۗ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٢٤٦﴾

247. ነቢያቸውም ለእነርሱ፡- «አላህ ጧሉትን (ሳኦልን) ንጉሥ አድርጎ በእርግጥ ላከላችሁ» አላቸው:: (እነርሱም)፡- «እኛ ከእርሱ ይልቅ በንግሥና ተገቢዎች ስንኾን ከሀብትም ስፋትን ያልተሰጠ ሲኾን ለእርሱ በኛ ላይ እንዴት ንግሥና ይኖረዋል?» አሉ:: (ነቢያቸውም)፡-«አላህ በእናንተ ላይ መረጠው:: በዕውቀትና በአካልም ስፋትን ጨመረለት:: አላህም ንግሥናውን ለሚሻው ሰው ይሰጣል:: አላህም ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነው» አላቸው::

وَقَالَ لَهُمۡ نَبِيُّهُمۡ إِنَّ ٱللَّهَ قَدۡ بَعَثَ لَكُمۡ طَالُوتَ مَلِكًا ۚ قَالُوٓاْ أَنَّىٰ يَكُونُ لَهُ ٱلۡمُلۡكُ عَلَيۡنَا وَنَحۡنُ أَحَقُّ بِٱلۡمُلۡكِ مِنۡهُ وَلَمۡ يُؤۡتَ سَعَةً مِّنَ ٱلۡمَالِ ۚ قَالَ إِنَّ ٱللَّهَ ٱصۡطَفَىٰهُ عَلَيۡكُمۡ وَزَادَهُۥ بَسۡطَةً فِى ٱلۡعِلۡمِ وَٱلۡجِسۡمِ ۖ وَٱللَّهُ يُؤۡتِى مُلۡكَهُۥ مَن يَشَآءُ ۚ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٌ ﴿٢٤٧﴾

248. ነቢያቸውም ለእነርሱ፡- «የንግሥናው ምልክት ከጌታችሁ የኾነ እርጋታ የሙሳ ቤተሰብና የሃሩን ቤተሰብ ከተውትም ቅርስ በውስጡ ያለበት መላእክት የሚሸከሙት ኾኖ ሳጥኑ ሊመጣላችሁ ነው:: አማኞች ብትኾኑ በዚህ ለእናንተ እርግጠኛ ምልክት አለለ» አላቸው::

وَقَالَ لَهُمۡ نَبِيُّهُمۡ إِنَّ ءَايَةَ مُلۡكِهِۦٓ أَن يَأۡتِيَكُمُ ٱلتَّابُوتُ فِيهِ سَكِينَةٌ مِّن رَّبِّكُمۡ وَبَقِيَّةٌ مِّمَّا تَرَكَ ءَالُ مُوسَىٰ وَءَالُ هَٰرُونَ تَحۡمِلُهُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ ۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَأٓيَةً لَّكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ﴿٢٤٨﴾

249. ጧሉትም በሠራዊቱ (ታጅቦ) በወጣ ጊዜ:- «አላህ በወንዝ (ውሃ) ፈታኛችሁ ነው ከርሱም የጠጣ ሰው ከእኔ አይደለም። ያልቀመሰውም ሰው በእጁ መዝገንን የዘገነ ሰው ብቻ ሲቀር እርሱ ከኔ ነው» አለ። ከእነርሱም ጥቂቶች ሲቀሩ ከርሱ ጠጡ። እርሱና እነዚያም ከእርሱ ጋር ያመኑት (ወንዙን) ባለፉት ጊዜ:- «ጃሎትንና ሠራዊቱን በመዋጋት ለኛ ዛሬ ችሎታ የለንም» አሉት። እነዚያ እነርሱ አላህን ተገናኝዎች መኾናቸው የሚያረጋግጡት:- «ከጥቂት ጭፍራ በአላህ ፈቃድ ብዙን ጭፍራ ያሸነፈች ብዙ ናት፤ አላህም ከታጋሾች ጋር ነው» አሉ።

فَلَمَّا فَصَلَ طَالُوتُ بِٱلۡجُنُودِ قَالَ إِنَّ ٱللَّهَ مُبۡتَلِيكُم بِنَهَرٖ فَمَن شَرِبَ مِنۡهُ فَلَيۡسَ مِنِّي وَمَن لَّمۡ يَطۡعَمۡهُ فَإِنَّهُۥ مِنِّيٓ إِلَّا مَنِ ٱغۡتَرَفَ غُرۡفَةَۢ بِيَدِهِۦۚ فَشَرِبُواْ مِنۡهُ إِلَّا قَلِيلٗا مِّنۡهُمۡۚ فَلَمَّا جَاوَزَهُۥ هُوَ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَهُۥ قَالُواْ لَا طَاقَةَ لَنَا ٱلۡيَوۡمَ بِجَالُوتَ وَجُنُودِهِۦۚ قَالَ ٱلَّذِينَ يَظُنُّونَ أَنَّهُم مُّلَٰقُواْ ٱللَّهِ كَم مِّن فِئَةٖ قَلِيلَةٍ غَلَبَتۡ فِئَةٗ كَثِيرَةَۢ بِإِذۡنِ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ مَعَ ٱلصَّٰبِرِينَ ٢٤٩

250. ለጃሎትና ለሠራዊቱ በተሰለፉም ጊዜ:- «ጌታችን ሆይ! በእኛ ላይ ትዕግስትን አንቧቧ፤ ጫማዎቻችንንም አደላድል፤ በከሓዲያን ሕዝቦችም ላይ እርዳን» አሉ።

وَلَمَّا بَرَزُواْ لِجَالُوتَ وَجُنُودِهِۦ قَالُواْ رَبَّنَآ أَفۡرِغۡ عَلَيۡنَا صَبۡرٗا وَثَبِّتۡ أَقۡدَامَنَا وَٱنصُرۡنَا عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٢٥٠

251. በአላህም ፈቃድ ድል መቷቸው። ዳውድም ጃሉትን (ዳዊት ጎልያድን) ገደለ። ንግሥናንና ጥበብንም (ነቢይነትን) አላህ ሰጠው። ከሚሻውም ነገር ሁሉ አሳወቀው። አላህም ሰዎችን ከፊላቸውን በከፊሉ መመለሱ ባልነበረ ኖሮ ምድር በተበላሸች ነበር፤ ግን አላህ በዓለማት ላይ የችሮታ ባለቤት ነው።

فَهَزَمُوهُم بِإِذۡنِ ٱللَّهِ وَقَتَلَ دَاوُۥدُ جَالُوتَ وَءَاتَىٰهُ ٱللَّهُ ٱلۡمُلۡكَ وَٱلۡحِكۡمَةَ وَعَلَّمَهُۥ مِمَّا يَشَآءُۗ وَلَوۡلَا دَفۡعُ ٱللَّهِ ٱلنَّاسَ بَعۡضَهُم بِبَعۡضٖ لَّفَسَدَتِ ٱلۡأَرۡضُ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ ذُو فَضۡلٍ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ٢٥١

252. እነዚህ (አንቀጾች) በውነት በአንተ ላይ የምናነባቸው ሲኾኑ የአላህ አንቀጾች ናቸው፤ አንተም በእርግጥ ከመልክተኞቹ ነህ።

تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱللَّهِ نَتۡلُوهَا عَلَيۡكَ بِٱلۡحَقِّۚ وَإِنَّكَ لَمِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ٢٥٢

253. እነዚህን መልክተኞች ከፊላቸውን በከፊሉ ላይ አበለጥን። ከእነርሱ ውስጥ አላህ ያነጋገረው አልለ። ከፊሎቻቸውንም በደረጃዎች ከፍ አደረገ። የመርየምን ልጅ ዒሳንም ግልጽ ታምራቶችን ሰጠነው። በቅዱሱ መንፈስም አበረታነው። አላህም በሻ ኖሮ እነዚያ ከእነርሱ (ከመልክተኞቹ) በኋላ የነበሩት ግልጽ ታምራቶች ከመጡላቸው በኋላ ባልተጋደሉ ነበር። ግን ተለያዩ። ከእነርሱም ውስጥ ያመነ ሰው አልለ። ከነርሱም ውስጥ የካደ ሰው አልለ። አላህም በሻ ኖሮ ባልተዋጉ (ባልተለያዩ) ነበር። ግን አላህ የሚሻውን ይሠራል።

۞تِلۡكَ ٱلرُّسُلُ فَضَّلۡنَا بَعۡضَهُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖۘ مِّنۡهُم مَّن كَلَّمَ ٱللَّهُۖ وَرَفَعَ بَعۡضَهُمۡ دَرَجَٰتٖۚ وَءَاتَيۡنَا عِيسَى ٱبۡنَ مَرۡيَمَ ٱلۡبَيِّنَٰتِ وَأَيَّدۡنَٰهُ بِرُوحِ ٱلۡقُدُسِۗ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَا ٱقۡتَتَلَ ٱلَّذِينَ مِنۢ بَعۡدِهِم مِّنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَتۡهُمُ ٱلۡبَيِّنَٰتُ وَلَٰكِنِ ٱخۡتَلَفُواْ فَمِنۡهُم مَّنۡ ءَامَنَ وَمِنۡهُم مَّن كَفَرَۚ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَا ٱقۡتَتَلُواْ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يَفۡعَلُ مَا يُرِيدُ ٢٥٣

254. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በርሱ ውስጥ ሽያጭ (መበገዘት)፣ ወዳጅነትም፣ ምልጃም የሌለበት ቀን ከመምጣቱ በፊት ከሰጠናችሁ ነገር ለግሱ፡፡ ከሓዲዎችም በዳዮቹ እነርሱ ናቸው፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ أَنفِقُوا۟ مِمَّا رَزَقْنَـٰكُم مِّن قَبْلِ أَن يَأْتِىَ يَوْمٌ لَّا بَيْعٌ فِيهِ وَلَا خُلَّةٌ وَلَا شَفَـٰعَةٌ ۗ وَٱلْكَـٰفِرُونَ هُمُ ٱلظَّـٰلِمُونَ ﴿٢٥٤﴾

255. አላህ ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ ሕያው ራሱን ቻይ ነው፡፡ ማንገላጀትም እንቅልፍም አትይዘውም፡፡ በሰማያት ውስጥና በምድር ውስጥ ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ ነው፡፡ ያ እርሱ ዘንድ በፈቃዱ ቢኾን እንጅ የሚያማልድ ማነው? (ከፍጡሮች) በፊታቸው ያለውንና ከኋላቸው ያለውን ሁሉ ያውቃል፡፡ በሻውም ነገር እንጂ ከዕውቀቱ በምንም ነገር አያካብቡም (አያውቁም)፡፡ መንበሩ ሰማያትንና ምድርን ሰፋ፡፡ ጥበቃቸውም አያቅተውም፡፡ እርሱም የሁሉ በላይ ታላቅ ነው፡፡

ٱللَّهُ لَآ إِلَـٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلْحَىُّ ٱلْقَيُّومُ ۚ لَا تَأْخُذُهُۥ سِنَةٌ وَلَا نَوْمٌ ۚ لَّهُۥ مَا فِى ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۗ مَن ذَا ٱلَّذِى يَشْفَعُ عِندَهُۥٓ إِلَّا بِإِذْنِهِۦ ۚ يَعْلَمُ مَا بَيْنَ أَيْدِيهِمْ وَمَا خَلْفَهُمْ ۖ وَلَا يُحِيطُونَ بِشَىْءٍ مِّنْ عِلْمِهِۦٓ إِلَّا بِمَا شَآءَ ۚ وَسِعَ كُرْسِيُّهُ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ ۖ وَلَا يَـُٔودُهُۥ حِفْظُهُمَا ۚ وَهُوَ ٱلْعَلِىُّ ٱلْعَظِيمُ ﴿٢٥٥﴾

256. በሃይማኖት ማስገደድ የለም፡፡ ቅኑ መንገድ ከጠማማው በእርግጥ ተገለጠ፡፡ በጣዖትም የሚክድና በአላህ የሚያምን ሰው ለርሷ መበጠስ የሌላትን ጠንካራ ዘለበት በእርግጥ ጨበጠ፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

لَآ إِكْرَاهَ فِى ٱلدِّينِ ۖ قَد تَّبَيَّنَ ٱلرُّشْدُ مِنَ ٱلْغَىِّ ۚ فَمَن يَكْفُرْ بِٱلطَّـٰغُوتِ وَيُؤْمِنۢ بِٱللَّهِ فَقَدِ ٱسْتَمْسَكَ بِٱلْعُرْوَةِ ٱلْوُثْقَىٰ لَا ٱنفِصَامَ لَهَا ۗ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٌ ﴿٢٥٦﴾

257. አላህ የእነዚያ ያመኑት ሰዎች ረዳት ነው፡፡ ከጨለማዎች ወደ ብርሃን ያወጣቸዋል፡፡ እነዚያም የካዱት ረዳቶቻቸው ጣዖታት ናቸው፡፡ ከብርሃን ወደ ጨለማዎች ያወጧቸዋል፡፡ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፤ እነርሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

ٱللَّهُ وَلِىُّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ يُخْرِجُهُم مِّنَ ٱلظُّلُمَـٰتِ إِلَى ٱلنُّورِ ۖ وَٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ أَوْلِيَآؤُهُمُ ٱلطَّـٰغُوتُ يُخْرِجُونَهُم مِّنَ ٱلنُّورِ إِلَى ٱلظُّلُمَـٰتِ ۗ أُو۟لَـٰٓئِكَ أَصْحَـٰبُ ٱلنَّارِ ۖ هُمْ فِيهَا خَـٰلِدُونَ ﴿٢٥٧﴾

258. ወደዚያ አላህ ንግሥናን ስለሰጠው ኢብራሂምን በጌታው ነገር ወደ ተከራከረው ሰው አላየህምን ኢብራሂም «ጌታዬ ያ ሕያው የሚያደርግና የሚገድል ነው» ባለ ጊዜ «እኔ ሕያው አደርጋለሁ እገድላለሁም» አለ፡፡ ኢብራሂም፡- «አላህ ፀሐይን ከምሥራቅ በኩል ያመጣል (አንተ) ከምዕራብ በኩል አምጣት» አለው፡፡ ያም የካደው ሰው ዋለለ፤ (መልስ አጣ) አላህም በዳዮች ሕዝቦችን አይመራም፡፡

أَلَمْ تَرَ إِلَى ٱلَّذِى حَآجَّ إِبْرَٰهِـۧمَ فِى رَبِّهِۦٓ أَنْ ءَاتَىٰهُ ٱللَّهُ ٱلْمُلْكَ إِذْ قَالَ إِبْرَٰهِـۧمُ رَبِّىَ ٱلَّذِى يُحْىِۦ وَيُمِيتُ قَالَ أَنَا۠ أُحْىِۦ وَأُمِيتُ ۖ قَالَ إِبْرَٰهِـۧمُ فَإِنَّ ٱللَّهَ يَأْتِى بِٱلشَّمْسِ مِنَ ٱلْمَشْرِقِ فَأْتِ بِهَا مِنَ ٱلْمَغْرِبِ فَبُهِتَ ٱلَّذِى كَفَرَ ۗ وَٱللَّهُ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلظَّـٰلِمِينَ ﴿٢٥٨﴾

259. ወይም ያንን በከተማ ላይ እርሷ በጣራዎችዋ ላይ የወደቀች ስትኾን ያለፈውን ሰው ብጤ (አላየህምን)፡- «ይህችን (ከተማ) ከሞተች በኋላ አላህ እንዴት ሕያው ያደርጋታል» አለ፡፡ አላህም ገደለው መቶ ዓመትን (አቆየውም)፡፡ ከዚያም አስነሳው፡- «ምን ያህል ቆየህ» አለው፡፡ «አንድ ቀን ወይም የቀንን ከፊል ቆየሁ» አለ፡፡ «አይደለም መቶን ዓመት ቆየህ፡፡ ወደ ምግብህና ወደ መጠጥህም ያልተለወጠ ሲኾን ተመልከት፡፡ ወደ አህያህም ተመልከት፡፡ ለሰዎችም አስረጅ እናደርግህ ዘንድ (ይህንን ሠሰራን)፡፡ ወደ ዐፅሞቹም እንዴት እንደምናስነሳት ከዚያም ሥጋን እንደምናለብሳት ተመልከት» አለው፡፡ ለርሱም (በማየት) በተገለጸለት ጊዜ፡- «አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ መኾኑን ዐውቃለሁ» አለ፡፡

أَوۡ كَٱلَّذِي مَرَّ عَلَىٰ قَرۡيَةٖ وَهِيَ خَاوِيَةٌ عَلَىٰ عُرُوشِهَا قَالَ أَنَّىٰ يُحۡيِۦ هَٰذِهِ ٱللَّهُ بَعۡدَ مَوۡتِهَاۖ فَأَمَاتَهُ ٱللَّهُ مِاْئَةَ عَامٖ ثُمَّ بَعَثَهُۥۖ قَالَ كَمۡ لَبِثۡتَۖ قَالَ لَبِثۡتُ يَوۡمًا أَوۡ بَعۡضَ يَوۡمٖۖ قَالَ بَل لَّبِثۡتَ مِاْئَةَ عَامٖ فَٱنظُرۡ إِلَىٰ طَعَامِكَ وَشَرَابِكَ لَمۡ يَتَسَنَّهۡۖ وَٱنظُرۡ إِلَىٰ حِمَارِكَ وَلِنَجۡعَلَكَ ءَايَةٗ لِّلنَّاسِۖ وَٱنظُرۡ إِلَى ٱلۡعِظَامِ كَيۡفَ نُنشِزُهَا ثُمَّ نَكۡسُوهَا لَحۡمٗاۚ فَلَمَّا تَبَيَّنَ لَهُۥ قَالَ أَعۡلَمُ أَنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٢٥٩

260. ኢብራሂምም «ጌታዬ ሆይ! ሙታንን እንዴት ሕያው እንደምታደርግ አሳየኝ» ባለ ጊዜ (አስታውስ፡፡) አላህ ፡- «አላመንክምን» አለው፡፡ «አይደለም (አምኛለሁ)፤ ግን ልቤ እንዲረጋ» ነው አለ፡፡ (አላህም)፡- «ከበራሪዎች (ከወፎች) አራትን ያዝ፡፡ ወደ አንተም ሰብስባቸው፡፡ (ቆራርጣቸውም)፤ ከዚያም በየኮረብታው ሁሉ ላይ ከነርሱ ቁራጭን አድርግ፡፡ ከዚያም ጥራቸው፤ ፈጥነው ይመጡሃልና፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ መኾኑን ዕወቅ» አለው፡፡

وَإِذۡ قَالَ إِبۡرَٰهِـۧمُ رَبِّ أَرِنِي كَيۡفَ تُحۡيِ ٱلۡمَوۡتَىٰۖ قَالَ أَوَ لَمۡ تُؤۡمِنۖ قَالَ بَلَىٰ وَلَٰكِن لِّيَطۡمَئِنَّ قَلۡبِيۖ قَالَ فَخُذۡ أَرۡبَعَةٗ مِّنَ ٱلطَّيۡرِ فَصُرۡهُنَّ إِلَيۡكَ ثُمَّ ٱجۡعَلۡ عَلَىٰ كُلِّ جَبَلٖ مِّنۡهُنَّ جُزۡءٗا ثُمَّ ٱدۡعُهُنَّ يَأۡتِينَكَ سَعۡيٗاۚ وَٱعۡلَمۡ أَنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٢٦٠

261. የእነዚያ ገንዘቦቻቸውን በአላህ መንገድ የሚለግሱ ሰዎች (ልግስና) ምሳሌ በየዘለላው ሁሉ መቶ ቅንጣት ያለባቸውን ሰባት ዘለላዎች እንደ አበቀለች አንዲት ቅንጣት ብጤ ነው፡፡ አላህም ለሚሻው ሰው (ከዚህ በላይ) ያነባብራል፡፡ አላህም ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነው፡፡

مَّثَلُ ٱلَّذِينَ يُنفِقُونَ أَمۡوَٰلَهُمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ كَمَثَلِ حَبَّةٍ أَنۢبَتَتۡ سَبۡعَ سَنَابِلَ فِي كُلِّ سُنۢبُلَةٖ مِّاْئَةُ حَبَّةٖۗ وَٱللَّهُ يُضَٰعِفُ لِمَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٌ ٢٦١

262. እነዚያ ገንዘቦቻቸውን በአላህ መንገድ የሚለግሱ ከዚያም የሰጡትን ነገር መመጻደቅንና ማስከፋትን የማያስከትሉ ለእነርሱ በጌታቸው ዘንድ ምንዳቸው አላቸው፡፡ በእነርሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነርሱም አያዝኑም፡፡

ٱلَّذِينَ يُنفِقُونَ أَمۡوَٰلَهُمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ ثُمَّ لَا يُتۡبِعُونَ مَآ أَنفَقُواْ مَنّٗا وَلَآ أَذٗى لَّهُمۡ أَجۡرُهُمۡ عِندَ رَبِّهِمۡ وَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ٢٦٢

263. መልካም ንግግርና ምሕረት ማድረግ ማስከፋት ከሚከተላት ምጽዋት በላጭ ነው፡፡ አላህም ተብቃቂ ታጋሽ ነው፡፡

۞قَوۡلٞ مَّعۡرُوفٞ وَمَغۡفِرَةٌ خَيۡرٞ مِّن صَدَقَةٖ يَتۡبَعُهَآ أَذٗىۗ وَٱللَّهُ غَنِيٌّ حَلِيمٞ ٢٦٣

264. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እንደዚያ ገንዘቡን ለሰዎች ማሳየት ሲል እንደሚሰጠውና በአላህና በመጨረሻውም ቀን እንደማያምነው ሰው ምጽዋቶቻችሁን በመመጻደቅና በማስከፋት አታበላሹ፡፡ ምሳሌውም በላዩ ዐፈር እንዳለበት ለንጣ ድንጋይ ኃይለኛም ዝናብ እንዳገኘውና ምልጥ አድርጎ እንደተወው ብጤ ነው፡፡ ከሠሩት ነገር በምንም ላይ (ሊጠቀሙ) አይችሉም፡፡ አላህም ከሓዲያንን ሕዝቦች አይመራም፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُبْطِلُواْ صَدَقَـٰتِكُم بِٱلْمَنِّ وَٱلْأَذَىٰ كَٱلَّذِى يُنفِقُ مَالَهُۥ رِئَآءَ ٱلنَّاسِ وَلَا يُؤْمِنُ بِٱللَّهِ وَٱلْيَوْمِ ٱلْـَٔاخِرِ ۖ فَمَثَلُهُۥ كَمَثَلِ صَفْوَانٍ عَلَيْهِ تُرَابٌ فَأَصَابَهُۥ وَابِلٌ فَتَرَكَهُۥ صَلْدًا ۖ لَّا يَقْدِرُونَ عَلَىٰ شَىْءٍ مِّمَّا كَسَبُواْ ۗ وَٱللَّهُ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلْكَـٰفِرِينَ ﴿٢٦٤﴾

265. የእነዚያም የአላህን ውዴታ ለመፈለግና ለነፍሶቻቸው (እምነትን) ለማረጋገጥ ገንዘቦቻቸውን የሚለግሱ ሰዎች ምሳሌ በተስተካከለች ከፍተኛ ስፍራ ላይ እንዳለች አትክልት፣ ብዙ ዝናብ እንደነካት ፍሬዋንም እጥፍ ኾኖ እንደሰጠች፣ ዝናብም ባይነካት ካፊያ እንደሚበቃት ብጤ ነው፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

وَمَثَلُ ٱلَّذِينَ يُنفِقُونَ أَمْوَٰلَهُمُ ٱبْتِغَآءَ مَرْضَاتِ ٱللَّهِ وَتَثْبِيتًا مِّنْ أَنفُسِهِمْ كَمَثَلِ جَنَّةٍۭ بِرَبْوَةٍ أَصَابَهَا وَابِلٌ فَـَٔاتَتْ أُكُلَهَا ضِعْفَيْنِ فَإِن لَّمْ يُصِبْهَا وَابِلٌ فَطَلٌّ ۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ﴿٢٦٥﴾

266. (ከእናንተ) አንዳችሁ ለርሱ ከዘምባባና ከወይኖች በስርዋ ወንዞች የሚፈሱባት አትክልት ልትኖረው፣ በውስጧም ለርሱ ከየፍሬው ሁሉ ሊኖረው እርጅናም ሊነካውና ለርሱ ደካማዎች ዝርያዎች ያሉት ሲኾን በውስጡ እሳት ያለበት ውርጭ ሊያገኛትና ልትቃጠል ይወዳልን እንደዚሁ አላህ አንቀጾችን ለእናንተ ያብራራል፤ ልታስተነትኑ ይከጀላልና፡፡

أَيَوَدُّ أَحَدُكُمْ أَن تَكُونَ لَهُۥ جَنَّةٌ مِّن نَّخِيلٍ وَأَعْنَابٍ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَـٰرُ لَهُۥ فِيهَا مِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِ وَأَصَابَهُ ٱلْكِبَرُ وَلَهُۥ ذُرِّيَّةٌ ضُعَفَآءُ فَأَصَابَهَآ إِعْصَارٌ فِيهِ نَارٌ فَٱحْتَرَقَتْ ۗ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمُ ٱلْـَٔايَـٰتِ لَعَلَّكُمْ تَتَفَكَّرُونَ ﴿٢٦٦﴾

267. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ካፈራችሁትና ከዚያም ለእናንተ ከምድር ካወጣንላችሁ ከመልካሙ ለግሱ፡፡ መጥፎውንም (ለመስጠት) አታስቡ፡፡ በእርሱ ዓይኖቻችሁን ጨፍናችሁ እንጂ የማትወስዱት ስትኾኑ ከእርሱ (ከመጥፎው) ትሰጣላችሁን አላህም ተብቃቂ ምስጉን መኾኑን ዕወቁ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَنفِقُواْ مِن طَيِّبَـٰتِ مَا كَسَبْتُمْ وَمِمَّآ أَخْرَجْنَا لَكُم مِّنَ ٱلْأَرْضِ ۖ وَلَا تَيَمَّمُواْ ٱلْخَبِيثَ مِنْهُ تُنفِقُونَ وَلَسْتُم بِـَٔاخِذِيهِ إِلَّآ أَن تُغْمِضُواْ فِيهِ ۚ وَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ غَنِىٌّ حَمِيدٌ ﴿٢٦٧﴾

268. ሰይጣን (እንዳትለግሱ) ድኽነትን ያስፈራራችኋል፡፡ በመጥፎም ያዛችኋል፡፡ አላህም ከርሱ የኾነን ምሕረትና ችሮታን ይቀጥራችኋል፡፡ አላህም ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነው፡፡

ٱلشَّيْطَـٰنُ يَعِدُكُمُ ٱلْفَقْرَ وَيَأْمُرُكُم بِٱلْفَحْشَآءِ ۖ وَٱللَّهُ يَعِدُكُم مَّغْفِرَةً مِّنْهُ وَفَضْلًا ۗ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٌ ﴿٢٦٨﴾

269. ለሚሻው ሰው ጥበብን ይሰጣል፤ ጥበብንም የሚስሰጥ ሰው ብዙን መልካም ነገር በእርግጥ ተሰጠ፡፡ የአእምሮዎች ባለቤቶች እንጂ (ሌላው) አይገሰጽም፡፡

يُؤْتِى ٱلْحِكْمَةَ مَن يَشَآءُ ۚ وَمَن يُؤْتَ ٱلْحِكْمَةَ فَقَدْ أُوتِىَ خَيْرًا كَثِيرًا ۗ وَمَا يَذَّكَّرُ إِلَّآ أُوْلُواْ ٱلْأَلْبَـٰبِ ﴿٢٦٩﴾

وَمَآ أَنفَقْتُم مِّن نَّفَقَةٍ أَوْ نَذَرْتُم مِّن نَّذْرٍ فَإِنَّ ٱللَّهَ يَعْلَمُهُۥ ۗ وَمَا لِلظَّٰلِمِينَ مِنْ أَنصَارٍ ﴿٢٧٠﴾

270. ከምጽዋትም ማንኛውንም የለገሳችሁትን ወይም ከስለት የተሳላችሁትን አላህ ያውቀዋል፡፡ ለበዳዮችም ከረዳቶች ምንም የላቸውም፡፡

إِن تُبْدُوا۟ ٱلصَّدَقَٰتِ فَنِعِمَّا هِىَ ۖ وَإِن تُخْفُوهَا وَتُؤْتُوهَا ٱلْفُقَرَآءَ فَهُوَ خَيْرٌ لَّكُمْ ۚ وَيُكَفِّرُ عَنكُم مِّن سَيِّـَٔاتِكُمْ ۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرٌ ﴿٢٧١﴾

271. ምጽዋቶችን ብትገልጹ እርሷ ምንኛ መልካም ናት፡፡ ብትደብቋትና ለድኾች ብትሰጧትም እርሱ ለናንተ በላጭ ነው፡፡ ከኃጢአቶቻችሁም ከእናንተ ያብሳል፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

۞ لَّيْسَ عَلَيْكَ هُدَىٰهُمْ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يَهْدِى مَن يَشَآءُ ۗ وَمَا تُنفِقُوا۟ مِنْ خَيْرٍ فَلِأَنفُسِكُمْ ۚ وَمَا تُنفِقُونَ إِلَّا ٱبْتِغَآءَ وَجْهِ ٱللَّهِ ۚ وَمَا تُنفِقُوا۟ مِنْ خَيْرٍ يُوَفَّ إِلَيْكُمْ وَأَنتُمْ لَا تُظْلَمُونَ ﴿٢٧٢﴾

272. እነርሱን ማቅናት በአንተ ላይ የለብህም፡፡ ግን አላህ የሚሻውን ሰው ያቀናል፡፡ ከገንዘብም የምትለግሱት (ምንዳው) ለነፍሶቻችሁ ነው፡፡ የአላህንም ፊት (ውዴታውን) ለመፈለግ እንጂ አትለግሱም፡፡ ከገንዘብም የምትለግሱት ሁሉ (ምንዳው) ወደናንተ ይሞላል፡፡ እናንተም አትበደሉም፡፡

لِلْفُقَرَآءِ ٱلَّذِينَ أُحْصِرُوا۟ فِى سَبِيلِ ٱللَّهِ لَا يَسْتَطِيعُونَ ضَرْبًا فِى ٱلْأَرْضِ يَحْسَبُهُمُ ٱلْجَاهِلُ أَغْنِيَآءَ مِنَ ٱلتَّعَفُّفِ تَعْرِفُهُم بِسِيمَٰهُمْ لَا يَسْـَٔلُونَ ٱلنَّاسَ إِلْحَافًا ۗ وَمَا تُنفِقُوا۟ مِنْ خَيْرٍ فَإِنَّ ٱللَّهَ بِهِۦ عَلِيمٌ ﴿٢٧٣﴾

273. (የምትመጸውቱት) ለእነዚያ በአላህ መንገድ (ለመታገል ሲሉ) ለታገዱት ድኾች ነው፡፡ በምድር መኼድን አይችሉም፡፡ (ልመናን) ከመጥጠበቃቸው (የተነሳ) የማያውቅ ሰው ሀብታሞች ናቸው ብሎ ይጠረጥራቸዋል፡፡ በምልክታቸው ታውቃቸዋለህ፡፡ ሰዎችን በችክታ አይለምኑም፡፡ ከገንዘብም የምትለግሱት አላህ እርሱን ዐዋቂ ነው፡፡

ٱلَّذِينَ يُنفِقُونَ أَمْوَٰلَهُم بِٱلَّيْلِ وَٱلنَّهَارِ سِرًّا وَعَلَانِيَةً فَلَهُمْ أَجْرُهُمْ عِندَ رَبِّهِمْ وَلَا خَوْفٌ عَلَيْهِمْ وَلَا هُمْ يَحْزَنُونَ ﴿٢٧٤﴾

274. እነዚያ ገንዘቦቻቸውን በሌሊትና በቀን በድብቅም በግልጽም የሚለግሱ ለእነርሱ በጌታቸው ዘንድ ምንዳቸው አላቸው፡፡ በእነርሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም እነርሱም አያዝኑም፡፡

ٱلَّذِينَ يَأْكُلُونَ ٱلرِّبَوٰا۟ لَا يَقُومُونَ إِلَّا كَمَا يَقُومُ ٱلَّذِى يَتَخَبَّطُهُ ٱلشَّيْطَٰنُ مِنَ ٱلْمَسِّ ۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمْ قَالُوٓا۟ إِنَّمَا ٱلْبَيْعُ مِثْلُ ٱلرِّبَوٰا۟ ۗ وَأَحَلَّ ٱللَّهُ ٱلْبَيْعَ وَحَرَّمَ ٱلرِّبَوٰا۟ ۚ فَمَن جَآءَهُۥ مَوْعِظَةٌ مِّن رَّبِّهِۦ فَٱنتَهَىٰ فَلَهُۥ مَا سَلَفَ وَأَمْرُهُۥٓ إِلَى ٱللَّهِ ۖ وَمَنْ عَادَ فَأُو۟لَٰٓئِكَ أَصْحَٰبُ ٱلنَّارِ ۖ هُمْ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿٢٧٥﴾

275. እነዚያ አራጣን የሚበሉ ያ ሰይጣን ከመንካቱ የተነሳ የሚጥለው ሰው (ከአውድቁ) እንደሚነሳ ብጤ እንጅ (ከመቃብራቸው) አይነሱም፡፡ ይህ እነርሱ መሸጥ የአራጣ ብጤ ብቻ ነው በማለታቸው ነው፡፡ ግን መሸጥን አላህ ፈቅዷል፡፡ አራጣንም እርም አድርጓል፡፡ ከጌታውም ግሳጼ የመጣለትና የተከለከለ ሰው ለርሱ (ከመከልከሉ በፊት) ያለፈው አለው፡፡ ነገሩም ወደ አላህ ነው፤ (አራጣን ወደ መብላት) የተመለሰም ሰው እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

يَمْحَقُ ٱللَّهُ ٱلرِّبَوٰا۟ وَيُرْبِى ٱلصَّدَقَٰتِ ۗ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ كُلَّ كَفَّارٍ أَثِيمٍ ﴿٢٧٦﴾

276. አላህ አራጣን (በረከቱን) ያጠፋል፡፡ ምጽዋቶችንም ያፋፋል፡፡ አላህም ኃጠኢተኛ ከሓዲን ሁሉ አይወድም፡፡

277. እነዚያ ያመኑ፡፡ መልካም ሥራዎችንም የሠሩ፡፡ ሶላትንም ያስተካከሉ፡፡ ዘካንም የሰጡ ለነርሱ በጌታቸው ዘንድ ምንዳቸው አላቸው፡፡ በእነርሱም ላይ ፍርሃት የለባቸውም እነርሱም አያዝኑም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَوُاْ ٱلزَّكَوٰةَ لَهُمۡ أَجۡرُهُمۡ عِندَ رَبِّهِمۡ وَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ٢٧٧

278. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ ከአራጣም የቀረውን ተዉ፡፡ አማኞች እንደኾናችሁ (ተጠንቀቁ)፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَذَرُواْ مَا بَقِيَ مِنَ ٱلرِّبَوٰٓاْ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ٢٧٨

279. (የታዘዛችሁትን) ባትሠሩም ከአላህና ከመልክተኛው በኾነች ጦር (መወጋታችሁን) ዕወቁ፡፡ ብትጸጸቱም ለእናንተ የገንዘቦቻችሁ ዋናዎች አሏችሁ፡፡ አትበድሉም አትበደሉምም፡፡

فَإِن لَّمۡ تَفۡعَلُواْ فَأۡذَنُواْ بِحَرۡبٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦۖ وَإِن تُبۡتُمۡ فَلَكُمۡ رُءُوسُ أَمۡوَٰلِكُمۡ لَا تَظۡلِمُونَ وَلَا تُظۡلَمُونَ ٢٧٩

280. የድኽነት ባለቤት የኾነም (ባለዕዳ) ሰው ቢኖር እማግኘት ድረስ ማቆየት ነው፡፡ (በመማር) መመጽወታችሁም ለእናንተ በላጭ ነው፡፡ የምታውቁ ብትኾኑ (ትሠሩታላችሁ)፡፡

وَإِن كَانَ ذُو عُسۡرَةٖ فَنَظِرَةٌ إِلَىٰ مَيۡسَرَةٖۚ وَأَن تَصَدَّقُواْ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٢٨٠

281. በእርሱም ውስጥ ወደ አላህ የምትመለሱበትን ከዚያም እነርሱ የማይበደሉ ሲሆኑ ነፍስ ሁሉ የሠራችውን ሥራ የምትሞላበትን ቀን ተጠንቀቁ፡፡

وَٱتَّقُواْ يَوۡمٗا تُرۡجَعُونَ فِيهِ إِلَى ٱللَّهِۖ ثُمَّ تُوَفَّىٰ كُلُّ نَفۡسٖ مَّا كَسَبَتۡ وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ٢٨١

282. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ በዕዳ በተዋዋላችሁ ጊዜ ጻፉት፡፡ ጸሐፊም በመካከላችሁ በትክክል ይጻፍ፡፡ ጸሐፊም አላህ እንደ አሳወቀው መጻፍን እንቢ አይበል፡፡ ይጻፍም፡፡ ያም በርሱ ላይ ዕዳው ያለበት ሰው በቃሉ ያስጽፍ፡፡ አላህንም ጌታውን ይፍራ፡፡ ከእርሱም (ካለበት ዕዳ) ምንንም አያጉድል፡፡ ያም በርሱ ላይ ዕዳው ያለበት ቂል፣ ወይም ደካማ፣ ወይም በቃሉ ማስጻፍን የማይችል ቢኾን ዋቢው በትክክል ያስጽፍለት፡፡ ከወንዶቻችሁም ሁለትን ምስክሮች አስመስክሩ፡፡ ሁለትም ወንዶች ባይኾኑ ከምስክሮች ሲኾኑ ከምትወዱዋቸው የኾኑን አንድ ወንድና አንደኛዋ ስትረሳ አንደኛይቱ ሌላዋን ታስታውሳት ዘንድ ሁለት ሴቶች (ይመስክሩ)፡፡ ምስክሮችም በተጠሩ ጊዜ እንቢ አይበሉ፡፡ (ዕዳው) ትንሽ ወይም ትልቅ ቢኾንም እስከ ጊዜው ድረስ የምትጽፉት ከመኾን አትሰልቹ፡፡ እንዲህ ማድረጋችሁ አላህ ዘንድ በጣም ትክክል ለምስክርነትም አረጋጋጭ ላለመጠራጠራችሁም በጣም ቅርብ ነው፡፡ ግን በመካከላችሁ እጅ በጅ የምትቀባበሏት ንግድ ብትኾን ባትጽፉዋት በናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ በተሻሻጣችሁም ጊዜ አስመስክሩ፡፡ ጸሐፊም ምስክርም (ባለ ጉዳዩ ጋር) አይጎዳዱ፡፡ (ይህንን) ብትሠሩም እርሱ በእናንተ (የሚጠጋ) አመጽ ነው፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ አላህም ያሳውቃችኋል፡፡ አላህም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا تَدَايَنتُم بِدَيۡنٍ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗى فَٱكۡتُبُوهُۚ وَلۡيَكۡتُب بَّيۡنَكُمۡ كَاتِبُۢ بِٱلۡعَدۡلِۚ وَلَا يَأۡبَ كَاتِبٌ أَن يَكۡتُبَ كَمَا عَلَّمَهُ ٱللَّهُۚ فَلۡيَكۡتُبۡ وَلۡيُمۡلِلِ ٱلَّذِي عَلَيۡهِ ٱلۡحَقُّ وَلۡيَتَّقِ ٱللَّهَ رَبَّهُۥ وَلَا يَبۡخَسۡ مِنۡهُ شَيۡـٔٗاۚ فَإِن كَانَ ٱلَّذِي عَلَيۡهِ ٱلۡحَقُّ سَفِيهًا أَوۡ ضَعِيفًا أَوۡ لَا يَسۡتَطِيعُ أَن يُمِلَّ هُوَ فَلۡيُمۡلِلۡ وَلِيُّهُۥ بِٱلۡعَدۡلِۚ وَٱسۡتَشۡهِدُواْ شَهِيدَيۡنِ مِن رِّجَالِكُمۡۖ فَإِن لَّمۡ يَكُونَا رَجُلَيۡنِ فَرَجُلٞ وَٱمۡرَأَتَانِ مِمَّن تَرۡضَوۡنَ مِنَ ٱلشُّهَدَآءِ أَن تَضِلَّ إِحۡدَىٰهُمَا فَتُذَكِّرَ إِحۡدَىٰهُمَا ٱلۡأُخۡرَىٰۚ وَلَا يَأۡبَ ٱلشُّهَدَآءُ إِذَا مَا دُعُواْۚ وَلَا تَسۡـَٔمُوٓاْ أَن تَكۡتُبُوهُ صَغِيرًا أَوۡ كَبِيرًا إِلَىٰٓ أَجَلِهِۦۚ ذَٰلِكُمۡ أَقۡسَطُ عِندَ ٱللَّهِ وَأَقۡوَمُ لِلشَّهَٰدَةِ وَأَدۡنَىٰٓ أَلَّا تَرۡتَابُوٓاْ إِلَّآ أَن تَكُونَ تِجَٰرَةً حَاضِرَةٗ تُدِيرُونَهَا بَيۡنَكُمۡ فَلَيۡسَ عَلَيۡكُمۡ جُنَاحٌ أَلَّا تَكۡتُبُوهَاۗ وَأَشۡهِدُوٓاْ إِذَا تَبَايَعۡتُمۡۚ وَلَا يُضَآرَّ كَاتِبٞ وَلَا شَهِيدٞۚ وَإِن تَفۡعَلُواْ فَإِنَّهُۥ فُسُوقُۢ بِكُمۡۗ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۖ وَيُعَلِّمُكُمُ ٱللَّهُۗ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ٢٨٢

283. በጉዞም ላይ ብትኾኑና ጸሐፊን ባታገኙ የተጨበጡ መተማመኛዎችን ያዙ፡፡ ከፊላችሁም ከፊሉን ቢያምን ያ የታመነው ሰው አደራውን ያድርስ፡፡ አላህንም ጌታውን ይፍራ፡፡ ምስክርነትንም አትደብቁ፡፡ የሚደብቃትም ሰው እርሱ ልቡ ኃጢአተኛ ነው፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

۞وَإِن كُنتُمۡ عَلَىٰ سَفَرٖ وَلَمۡ تَجِدُواْ كَاتِبٗا فَرِهَٰنٞ مَّقۡبُوضَةٞۖ فَإِنۡ أَمِنَ بَعۡضُكُم بَعۡضٗا فَلۡيُؤَدِّ ٱلَّذِي ٱؤۡتُمِنَ أَمَٰنَتَهُۥ وَلۡيَتَّقِ ٱللَّهَ رَبَّهُۥۗ وَلَا تَكۡتُمُواْ ٱلشَّهَٰدَةَۚ وَمَن يَكۡتُمۡهَا فَإِنَّهُۥٓ ءَاثِمٞ قَلۡبُهُۥۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ عَلِيمٞ ٢٨٣

284. በሰማያት ውስጥና በምድርም ውስጥ ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ በነፍሶቻችሁ ውስጥ ያለውን ብትገልጹ ወይም ብትደብቁት አላህ በርሱ ይቆጣጠራችኋል፡፡ ለሚሻውም ሰው ይምራል፡፡ የሚሻውንም ሰው ይቀጣል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

لِّلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۗ وَإِن تُبۡدُواْ مَا فِيٓ أَنفُسِكُمۡ أَوۡ تُخۡفُوهُ يُحَاسِبۡكُم بِهِ ٱللَّهُۖ فَيَغۡفِرُ لِمَن يَشَآءُ وَيُعَذِّبُ مَن يَشَآءُۗ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ٢٨٤

285. መልክተኛው ከጌታው ወደ ርሱ በተወረደው አመነ፡፡ ምእምኖቹም (እንደዚሁ)፡፡ ሁሉም በአላህ፣ በመላዕክቱም፣ በመጻሕፍቱም፣ በመልክተኞቹም ከመልክተኞቹ «በአንድም መካከል አንለይም» (የሚሉ ሲኾኑ) አመኑ፡፡ «ሰማን፤ ታዘዝንም፡፡ ጌታችን ሆይ! ምሕረትህን (እንሻለን)፡፡ መመለሻም ወዳንተ ብቻ ነው» አሉም፡፡

ءَامَنَ ٱلرَّسُولُ بِمَآ أُنزِلَ إِلَيۡهِ مِن رَّبِّهِۦ وَٱلۡمُؤۡمِنُونَۚ كُلٌّ ءَامَنَ بِٱللَّهِ وَمَلَٰٓئِكَتِهِۦ وَكُتُبِهِۦ وَرُسُلِهِۦ لَا نُفَرِّقُ بَيۡنَ أَحَدٖ مِّن رُّسُلِهِۦۚ وَقَالُواْ سَمِعۡنَا وَأَطَعۡنَاۖ غُفۡرَانَكَ رَبَّنَا وَإِلَيۡكَ ٱلۡمَصِيرُ ٢٨٥

286. አላህ ነፍስን ከችሎታዋ በላይ አያስገድዳትም፡፡ ለርስዋ የሠራችው አላት፡፡ በርስዋም ላይ ያፈራችው (ኀጢአት) አለባት፡፡ (በሉ)፡- ጌታችን ሆይ! ብንረሳ ወይም ብንስት አትያዘን፤ (አትቅጣን)፡፡ ጌታችን ሆይ! ከባድ ሸክምን ከእኛ በፊት በነበሩት ላይ እንደጫንከው በእኛ ላይ አትጫንብን፡፡ ጌታችን ሆይ! ለኛም በርሱ ችሎታ የሌለንን ነገር አታሸክመን፡፡ ከእኛም ይቅርታ አድርግ ለእኛም ምሕረት አድርግ፡፡ እዘንልንም፤ ዋቢያችን አንተ ነህና፡፡ በከሓዲዎች ሕዝቦች ላይም እርዳን፡፡

لَا يُكَلِّفُ ٱللَّهُ نَفۡسًا إِلَّا وُسۡعَهَاۚ لَهَا مَا كَسَبَتۡ وَعَلَيۡهَا مَا ٱكۡتَسَبَتۡۗ رَبَّنَا لَا تُؤَاخِذۡنَآ إِن نَّسِينَآ أَوۡ أَخۡطَأۡنَاۚ رَبَّنَا وَلَا تَحۡمِلۡ عَلَيۡنَآ إِصۡرٗا كَمَا حَمَلۡتَهُۥ عَلَى ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِنَاۚ رَبَّنَا وَلَا تُحَمِّلۡنَا مَا لَا طَاقَةَ لَنَا بِهِۦۖ وَٱعۡفُ عَنَّا وَٱغۡفِرۡ لَنَا وَٱرۡحَمۡنَآۚ أَنتَ مَوۡلَىٰنَا فَٱنصُرۡنَا عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٢٨٦

# ሱረቱ አል-ኢምራን

# سورة آل عمران

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ለ.መ (አሊፍ ላም ሚም)፤

الٓمٓ ١

2. አላህ ከርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ (እርሱ) ሕያው ሁሉን ነገር አስተናባሪ ነው፡፡

ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلۡحَيُّ ٱلۡقَيُّومُ ٢

3. ከርሱ በፊት ያሉትን መጻሕፍት የሚያረጋግጥ ሲኾን መጽሐፉን (ቁርኣንን) ባንተ ላይ ከፋፍሎ በእውነት አወረደ፡፡ ተውራትንና ኢንጂልንም አውርዷል፡፡

نَزَّلَ عَلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَ بِٱلۡحَقِّ مُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ وَأَنزَلَ ٱلتَّوۡرَىٰةَ وَٱلۡإِنجِيلَ ٣

4. (ከቁርኣን) በፊት ለሰዎች መሪ አድርጎ (አወረዳቸው)፡፡ ፉርቃንንም አወረደ፡፡ እነዚያ በአላህ ተዓምራቶች የካዱ ለእነርሱ ብርቱ ቅጣት አላቸው፡፡ አላህም አሸናፊ የመበቀል ባለቤት ነው፡፡

مِن قَبۡلُ هُدٗى لِّلنَّاسِ وَأَنزَلَ ٱلۡفُرۡقَانَۗ إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ لَهُمۡ عَذَابٞ شَدِيدٞۗ وَٱللَّهُ عَزِيزٞ ذُو ٱنتِقَامٍ ٤

5. አላህ በምድርም በሰማይም ምንም ነገር በርሱ ላይ አይሰወርም፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَخۡفَىٰ عَلَيۡهِ شَيۡءٞ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فِي ٱلسَّمَآءِ ٥

6. እርሱ ያ በማሕጸኖች ውስጥ እንደሚሻ አድርጎ የሚቀርጻችሁ ነው፡፡ ከእርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي يُصَوِّرُكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡحَامِ كَيۡفَ يَشَآءُۚ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٦

7. እርሱ ያ በአንተ ላይ መጽሐፉን ያወረደ ነው፡፡ ከእርሱ (ከመጽሐፉ) ግልጽ የኾኑ አንቀጾች አልሉ፡፡ እነሱ የመጽሐፉ መሠረቶች ናቸው፡፡ ሌሎችም ተመሳሳዮች አልሉ፡፡ እነዚያማ በልቦቻቸው ውስጥ ጥመት ያለባቸው ሰዎች ማሳሳትን ለመፈለግና ትችቱን ለመፈለግ ከርሱ የተመሳሰለውን ይከታተላሉ፡፡ (ትክክለኛ) ትችቱንም አላህ ብቻ እንጅ ሌላ አያውቀውም፡፡ በዕውቀትም የጠለቁት «በርሱ አምነናል፤ ሁሉም ከጌታችን ዘንድ ነው» ይላሉ፡፡ የአእምሮ ባለቤቶችም እንጅ (ሌላው) አይገሰጽም፡፡

هُوَ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ عَلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَ مِنۡهُ ءَايَٰتٞ مُّحۡكَمَٰتٌ هُنَّ أُمُّ ٱلۡكِتَٰبِ وَأُخَرُ مُتَشَٰبِهَٰتٞۖ فَأَمَّا ٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِمۡ زَيۡغٞ فَيَتَّبِعُونَ مَا تَشَٰبَهَ مِنۡهُ ٱبۡتِغَآءَ ٱلۡفِتۡنَةِ وَٱبۡتِغَآءَ تَأۡوِيلِهِۦۖ وَمَا يَعۡلَمُ تَأۡوِيلَهُۥٓ إِلَّا ٱللَّهُۗ وَٱلرَّٰسِخُونَ فِي ٱلۡعِلۡمِ يَقُولُونَ ءَامَنَّا بِهِۦ كُلّٞ مِّنۡ عِندِ رَبِّنَاۗ وَمَا يَذَّكَّرُ إِلَّآ أُوْلُواْ ٱلۡأَلۡبَٰبِ ٧

8. (እነሱም ይላሉ)፡- «ጌታችን ሆይ! ቅኑን መንገድ ከመራኸን በኋላ ልቦቻችንን አታዘምብልብን፡፡ ከአንተ ዘንድ የኾነን ችሮታም ለኛ ስጠን፡፡ አንተ በጣም ለጋስ ነህና፡፡»

رَبَّنَا لَا تُزِغۡ قُلُوبَنَا بَعۡدَ إِذۡ هَدَيۡتَنَا وَهَبۡ لَنَا مِن لَّدُنكَ رَحۡمَةًۚ إِنَّكَ أَنتَ ٱلۡوَهَّابُ ٨

9. «ጌታችን ሆይ! አንተ በርሱ (ለመምጣቱ) ጥርጥር የሌለበት በኾነ ቀን ሰውን ሁሉ ሰብሳቢ ነህ፡፡ ምንጊዜም አላህ ቀጠሮውን አያፈርስምና፡፡»

رَبَّنَآ إِنَّكَ جَامِعُ ٱلنَّاسِ لِيَوۡمٖ لَّا رَيۡبَ فِيهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُخۡلِفُ ٱلۡمِيعَادَ ٩

10. እነዚያ የካዱት ሰዎች ገንዘቦቻቸውና ልጆቻቸው ከአላህ (ቅጣት) ምንም አያስጥሉዋቸውም፡፡ እነዚያም እነርሱ የእሳት ማገዶዎች ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَن تُغۡنِيَ عَنۡهُمۡ أَمۡوَٰلُهُمۡ وَلَآ أَوۡلَٰدُهُم مِّنَ ٱللَّهِ شَيۡـٔٗاۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمۡ وَقُودُ ٱلنَّارِ ١٠

11. (ልማዳቸው ሁሉ) እንደፈርዖን ቤተሰብና እንደእነዚያ ከበፊታቸው እንደነበሩት ሕዝቦች ልማድ ነው፡፡ በአንቀጾቻችን አስተባበሉ፡፡ አላህም በኃጢአቶቻቸው ያዛቸው፡፡ አላህም ቅጣተብርቱ ነው፡፡

كَدَأۡبِ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ وَٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا فَأَخَذَهُمُ ٱللَّهُ بِذُنُوبِهِمۡۗ وَٱللَّهُ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ١١

12. ለእነዚያ ለካዱት ሰዎች በላቸው፡- «በቅርብ ጊዜ ትሸነፋላችሁ፡፡ ወደ ገሀነምም ትሰበሰባላችሁ፡፡ ምንጣፊቱም ምን ትከፋ!»

قُل لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ سَتُغۡلَبُونَ وَتُحۡشَرُونَ إِلَىٰ جَهَنَّمَۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمِهَادُ ١٢

13. (የበድር ቀን) በተጋጠሙት ሁለት ጭፍሮች ለናንተ በእርግጥ ተዓምር አልለ፡፡ አንደኛዋ ጭፍራ በአላህ መንገድ ትጋደላለች፡፡ ሌላይቱም ከሓዲ ናት፡፡ ከሓዲዎቹ (አማኞቹን) በዓይን አስተያየት እጥፋቸውን ኾነው ያዩዋቸዋል፡፡ አላህም በርዳታው የሚሻውን ሰው ያበረታል፡፡ በዚህ ውስጥ ለማስተዋል ባለቤቶች በእርግጥ መገሰጫ አለበት፡፡

قَدۡ كَانَ لَكُمۡ ءَايَةٞ فِي فِئَتَيۡنِ ٱلۡتَقَتَاۖ فِئَةٞ تُقَٰتِلُ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَأُخۡرَىٰ كَافِرَةٞ يَرَوۡنَهُم مِّثۡلَيۡهِمۡ رَأۡيَ ٱلۡعَيۡنِۚ وَٱللَّهُ يُؤَيِّدُ بِنَصۡرِهِۦ مَن يَشَآءُۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَعِبۡرَةٗ لِّأُوْلِي ٱلۡأَبۡصَٰرِ ١٣

14. ከሴቶች፣ ከወንዶች ልጆችም፣ ከወርቅና ከብር፣ ከተካመቹ ገንዘቦችም፣ ከተሰማሩ ፈረሶችም፣ ከግመል ከከብትና ከፍየልም፣ ከአዝመራም የኾኑ ፍላጎቶችን መውደድ ለሰዎች ተሸለመ፡፡ ይህ ሁሉ የቅርቢቱ ሕይወት መጠቀሚያ ነው፡፡ አላህም እርሱ ዘንድ መልካም መመለሻ (ገነት) አለ፡፡

زُيِّنَ لِلنَّاسِ حُبُّ ٱلشَّهَوَٰتِ مِنَ ٱلنِّسَآءِ وَٱلۡبَنِينَ وَٱلۡقَنَٰطِيرِ ٱلۡمُقَنطَرَةِ مِنَ ٱلذَّهَبِ وَٱلۡفِضَّةِ وَٱلۡخَيۡلِ ٱلۡمُسَوَّمَةِ وَٱلۡأَنۡعَٰمِ وَٱلۡحَرۡثِۗ ذَٰلِكَ مَتَٰعُ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَٱللَّهُ عِندَهُۥ حُسۡنُ ٱلۡمَـَٔابِ ١٤

15. «ከዚህ ሁሉ ነገር የሚበልጥን ልንገራችሁን» በላቸው፡፡ (እርሱም) «ለእነዚያ ለተጠነቀቁት ሰዎች በጌታቸው ዘንድ በሥራቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው ገነቶች በውስጧ ሁልጊዜ ነዋሪዎች ሲኾኑ ንጹሕ የተደረጉ ሚስቶችም፣ ከአላህም የኾነ ውዴታ አላቸው፡፡ አላህም ባሮቹን ተመልካች ነው፡፡»

۞قُلۡ أَؤُنَبِّئُكُم بِخَيۡرٖ مِّن ذَٰلِكُمۡۖ لِلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْ عِندَ رَبِّهِمۡ جَنَّٰتٞ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا وَأَزۡوَٰجٞ مُّطَهَّرَةٞ وَرِضۡوَٰنٞ مِّنَ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِٱلۡعِبَادِ ١٥

16. (እነርሱም) እነዚያ፡- «ጌታችን ሆይ! እኛ አመንን ኀጢአቶቻችንንም ለእኛ ማር፤ የእሳትንም ቅጣት ጠብቀን» የሚሉ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ يَقُولُونَ رَبَّنَآ إِنَّنَآ ءَامَنَّا فَٱغۡفِرۡ لَنَا ذُنُوبَنَا وَقِنَا عَذَابَ ٱلنَّارِ ١٦

17. ታጋሾች እውነተኞችም ታዛዦችም ለጋሶችና በሌሊት መጨረሻዎች ምሕረትን ለማኞች ናቸው፡፡

ٱلصَّٰبِرِينَ وَٱلصَّٰدِقِينَ وَٱلۡقَٰنِتِينَ وَٱلۡمُنفِقِينَ وَٱلۡمُسۡتَغۡفِرِينَ بِٱلۡأَسۡحَارِ ١٧

18. አላህ በማስተካከል የቆመ (አስተናባሪ) ሲኾን ከእርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የሌለ መኾኑን መሰከረ፡፡ መላእክቶችና የዕውቀት ባለቤቶችም (እንደዚሁ መሰከሩ)፡፡ ከእርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

شَهِدَ ٱللَّهُ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ وَأُوْلُواْ ٱلۡعِلۡمِ قَآئِمَۢا بِٱلۡقِسۡطِۚ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ١٨

19. አላህ ዘንድ (የተወደደ) ሃይማኖት ኢስላም ብቻ ነው፡፡ እነዚያም መጽሐፉን የተሰጡት ሰዎች በመካከላቸው ላለው ምቀኝነት ዕውቀቱ ከመጣላቸው በኋላ እንጅ አልተለያዩም፡፡ በአላህም አንቀጾች የሚክድ አላህ ምርመራው ፈጣን ነው፡፡

إِنَّ ٱلدِّينَ عِندَ ٱللَّهِ ٱلۡإِسۡلَٰمُۗ وَمَا ٱخۡتَلَفَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ إِلَّا مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَهُمُ ٱلۡعِلۡمُ بَغۡيَۢا بَيۡنَهُمۡۗ وَمَن يَكۡفُرۡ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ فَإِنَّ ٱللَّهَ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ١٩

20. ቢከራከሩህም፡- «ፊቴን ለአላህ ሰጠሁ፤ የተከተሉኝም ሰዎች (እንደዚሁ ለአላህ ሰጡ)» በላቸው፡፡ ለእነዚያም መጽሐፍን ለተሰጡት ሰዎችና ለመሐይሞቹ፡- «ሰለማችሁን» በላቸው፡፡ ቢሰልሙም በእርግጥ ተመሩ፡፡ እምቢ ቢሉም በአንተ ላይ ያለብህ ማድረስ ብቻ ነው፡፡ አላህም ባሮቹን ተመልካች ነው፡፡

فَإِنۡ حَآجُّوكَ فَقُلۡ أَسۡلَمۡتُ وَجۡهِيَ لِلَّهِ وَمَنِ ٱتَّبَعَنِۗ وَقُل لِّلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡأُمِّيِّـۧنَ ءَأَسۡلَمۡتُمۡۚ فَإِنۡ أَسۡلَمُواْ فَقَدِ ٱهۡتَدَواْۖ وَّإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنَّمَا عَلَيۡكَ ٱلۡبَلَٰغُۗ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِٱلۡعِبَادِ ٢٠

21. እነዚያ በአላህ አንቀጾች የሚክዱ ነቢያትንም ያለ አግባብ የሚገድሉ ከሰዎችም ውስጥ እነዚያን በትክክለኛነት የሚያዙትን የሚገድሉ በአሳማሚ ቅጣት አብስራቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡفُرُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَيَقۡتُلُونَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ بِغَيۡرِ حَقّٖ وَيَقۡتُلُونَ ٱلَّذِينَ يَأۡمُرُونَ بِٱلۡقِسۡطِ مِنَ ٱلنَّاسِ فَبَشِّرۡهُم بِعَذَابٍ أَلِيمٍ ٢١

22. እነዚያ በቅርቢቱና በመጨረሻይቱ ዓለም ሥራዎቻቸው የተበላሹ ናቸው፡፡ ለእነርሱም ምንም ረዳቶች የሏቸውም፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ حَبِطَتۡ أَعۡمَٰلُهُمۡ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ وَمَا لَهُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٢٢

23. ወደ እነዚያ ከመጽሐፉ (ትምህርት) ዕድልን ወደ ተሰጡት ሰዎች አላየህምን ወደ አላህ መጽሐፍ በመካከላቸው ይፈርድ ዘንድ ይጠራሉ፡፡ ከዚያም ከእነሱ ገሚሶቹ እነርሱ (እውነቱን) የተዉ ኾነው ይሸሻሉ፡፡

أَلَمْ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ نَصِيبًا مِّنَ ٱلْكِتَٰبِ يُدْعَوْنَ إِلَىٰ كِتَٰبِ ٱللَّهِ لِيَحْكُمَ بَيْنَهُمْ ثُمَّ يَتَوَلَّىٰ فَرِيقٌ مِّنْهُمْ وَهُم مُّعْرِضُونَ ﴿٢٣﴾

24. ይኸ እነርሱ «እሳት የተቆጠሩ ቀኖችን እንጅ አትነካንም» በማለታቸው ነው፡፡ በሃይማኖታቸውም ይቀጣጥፉት የነበሩት ነገር አታለላቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمْ قَالُوا۟ لَن تَمَسَّنَا ٱلنَّارُ إِلَّآ أَيَّامًا مَّعْدُودَٰتٍ ۖ وَغَرَّهُمْ فِى دِينِهِم مَّا كَانُوا۟ يَفْتَرُونَ ﴿٢٤﴾

25. በርሱ (መምጣት) ጥርጥር የሌለበት በኾነው ቀን በሰበሰብናቸውና ነፍስ ሁሉ የሠራችውን ሥራ በተሞላች ጊዜ እንዴት ይኾናሉ እነርሱም አይበደሉም፡፡

فَكَيْفَ إِذَا جَمَعْنَٰهُمْ لِيَوْمٍ لَّا رَيْبَ فِيهِ وَوُفِّيَتْ كُلُّ نَفْسٍ مَّا كَسَبَتْ وَهُمْ لَا يُظْلَمُونَ ﴿٢٥﴾

26. (ሙሐመድ ሆይ!) በል፡- «የንግስና ባለቤት የኾንክ አላህ ሆይ! ለምትሻው ሰው ንግሥናን ትሰጣለህ፡፡ ከምትሻውም ሰው ንግሥናን ትገፍፋለህ፡፡ የምትሻውንም ሰው ታልቃለህ፡፡ የምትሻውንም ሰው ታዋርዳለህ፡፡ መልካም ነገር ሁሉ በእጅህ (በችሎታህ) ነው፤ አንተ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነህና፡፡»

قُلِ ٱللَّهُمَّ مَٰلِكَ ٱلْمُلْكِ تُؤْتِى ٱلْمُلْكَ مَن تَشَآءُ وَتَنزِعُ ٱلْمُلْكَ مِمَّن تَشَآءُ وَتُعِزُّ مَن تَشَآءُ وَتُذِلُّ مَن تَشَآءُ ۖ بِيَدِكَ ٱلْخَيْرُ ۖ إِنَّكَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٢٦﴾

27. ሌሊቱን በቀን ውስጥ ታስገባለህ፡፡ ቀኑንም በሌሊቱ ውስጥ ታስገባለህ፡፡ ሕያውንም ከሙት ውስጥ ታወጣለህ፡፡ ሙትንም ከሕያው ውስጥ ታወጣለህ፡፡ ለምትሻውም ሰው ያለግምት ትሰጣለህ፡፡

تُولِجُ ٱلَّيْلَ فِى ٱلنَّهَارِ وَتُولِجُ ٱلنَّهَارَ فِى ٱلَّيْلِ ۖ وَتُخْرِجُ ٱلْحَىَّ مِنَ ٱلْمَيِّتِ وَتُخْرِجُ ٱلْمَيِّتَ مِنَ ٱلْحَىِّ ۖ وَتَرْزُقُ مَن تَشَآءُ بِغَيْرِ حِسَابٍ ﴿٢٧﴾

28. ምእምናን ከሓዲዎችን ከምእምናን ሌላ ረዳቶች አድርገው አይያዙ፡፡ ይኼንንም የሚሠራ ሰው ከአላህ (ሃይማኖት) በምንም ውስጥ አይደለም፡፡ ከእነርሱ መጥጠበቅን ብትጠበቁ እንጂ፡፡ አላህም ነፍሱን (ቁጣውን) ያስጠነቅቃችኋል፡፡ መመለሻም ወደ አላህ ብቻ ነው፡፡

لَّا يَتَّخِذِ ٱلْمُؤْمِنُونَ ٱلْكَٰفِرِينَ أَوْلِيَآءَ مِن دُونِ ٱلْمُؤْمِنِينَ ۖ وَمَن يَفْعَلْ ذَٰلِكَ فَلَيْسَ مِنَ ٱللَّهِ فِى شَىْءٍ إِلَّآ أَن تَتَّقُوا۟ مِنْهُمْ تُقَىٰةً ۗ وَيُحَذِّرُكُمُ ٱللَّهُ نَفْسَهُۥ ۗ وَإِلَى ٱللَّهِ ٱلْمَصِيرُ ﴿٢٨﴾

29. «በደረቶቻችሁ ውስጥ ያለውን ነገር ብትደብቁ ወይም ብትገልፁት አላህ ያውቀዋል፡፡ በሰማያት ያለውንና በምድርም ያለውን ሁሉ ያውቃል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው» (በል)፡፡

قُلْ إِن تُخْفُوا۟ مَا فِى صُدُورِكُمْ أَوْ تُبْدُوهُ يَعْلَمْهُ ٱللَّهُ ۗ وَيَعْلَمُ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۗ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٢٩﴾

30. ነፍስ ሁሉ ከመልካም ነገር የሠራችውን የቀረበ ኾኖ የምታገኝበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ ከመጥፎም የሠራችው በርስዋና በርሱ (በኀጢአትዋ) መካከል በጣም የሰፋ ርቀት ቢኖር ትመኛለች፡፡ አላህ ነፍሱን ያስጠነቅቃችኋል፡፡ አላህም ለባሮቹ ሩኅሩኅ ነው፡፡

يَوْمَ تَجِدُ كُلُّ نَفْسٍ مَّا عَمِلَتْ مِنْ خَيْرٍ مُّحْضَرًا وَمَا عَمِلَتْ مِن سُوٓءٍ تَوَدُّ لَوْ أَنَّ بَيْنَهَا وَبَيْنَهُۥٓ أَمَدًۢا بَعِيدًا ۗ وَيُحَذِّرُكُمُ ٱللَّهُ نَفْسَهُۥ ۗ وَٱللَّهُ رَءُوفٌۢ بِٱلْعِبَادِ ﴿٣٠﴾

31. በላቸው፡- «አላህን የምትወዱ እንደኾናችሁ ተከተሉኝ፤ አላህ ይወዳችኋልና፡፡ ኀጢአቶቻችሁንም ለናንተ ይምራልና፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡»

قُلۡ إِن كُنتُمۡ تُحِبُّونَ ٱللَّهَ فَٱتَّبِعُونِي يُحۡبِبۡكُمُ ٱللَّهُ وَيَغۡفِرۡ لَكُمۡ ذُنُوبَكُمۡۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٣١

32. «አላህንና መልክተኛውን ታዘዙ፡፡ ብትሸሹም አላህ ከሓዲዎችን አይወድም» በላቸው፡፡

قُلۡ أَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَٱلرَّسُولَۖ فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٣٢

33. አላህ አደምን፣ ኑሕንም፣ የኢብራሂምንም ቤተሰብ፣ የዒምራንንም ቤተሰብ በዓለማት ላይ መረጠ፡፡

۞إِنَّ ٱللَّهَ ٱصۡطَفَىٰٓ ءَادَمَ وَنُوحٗا وَءَالَ إِبۡرَٰهِيمَ وَءَالَ عِمۡرَٰنَ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ٣٣

34. ከፊልዋ ከከፊሉ የኾነች ዝርያ አድርጎ (መረጣት)፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

ذُرِّيَّةَۢ بَعۡضُهَا مِنۢ بَعۡضٖۗ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٌ ٣٤

35. የዒምራን ባለቤት (ሐና) «ጌታዬ ሆይ! እኔ በሆዴ ውስጥ ያለውን (ፅንስ ከሥራ) ነጻ የተደረገ ሲኾን ለአንተ ተሳልኩ፡፡ ከእኔም ተቀበል አንተ ሰሚው ዐዋቂው ነህና» ባለች ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ قَالَتِ ٱمۡرَأَتُ عِمۡرَٰنَ رَبِّ إِنِّي نَذَرۡتُ لَكَ مَا فِي بَطۡنِي مُحَرَّرٗا فَتَقَبَّلۡ مِنِّيٓۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٣٥

36. በወለደቻትም ጊዜ፡- «ጌታዬ ሆይ! እኔ ሴት ኾና ወለድኋት፡፡» አላህም የወለደችውን ዐዋቂ ነው፡፡ «ወንድም እንደ ሴት አይደለም፡፡ እኔም መርየም ብዬ ስም አወጣሁላት፡፡ እኔም እሷንም ዝርያዋንም ከተረገመው ሰይጣን በአንተ እጠብቃቸዋለሁ» አለች፡፡

فَلَمَّا وَضَعَتۡهَا قَالَتۡ رَبِّ إِنِّي وَضَعۡتُهَآ أُنثَىٰ وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا وَضَعَتۡ وَلَيۡسَ ٱلذَّكَرُ كَٱلۡأُنثَىٰۖ وَإِنِّي سَمَّيۡتُهَا مَرۡيَمَ وَإِنِّيٓ أُعِيذُهَا بِكَ وَذُرِّيَّتَهَا مِنَ ٱلشَّيۡطَٰنِ ٱلرَّجِيمِ ٣٦

37. ጌታዋም በደህና አቀባበል ተቀበላት፡፡ በመልካም አስተዳደግም አፋፋት፡፡ ዘከሪያም አሳደጋት፤ ዘከሪያ በርሷ ላይ በምኹራቧ በገባ ቁጥር እርስዋ ዘንድ ሲሳይን አገኘ፡፡ «መርየም ሆይ! ይህ ለአንቺ ከየት ነው» አላት፡፡ «እርሱ ከአላህ ዘንድ ነው፡፡ አላህ ለሚሻው ሰው ሲሳዩን ያለ ድካም ይሰጣል» አለችው፡፡

فَتَقَبَّلَهَا رَبُّهَا بِقَبُولٍ حَسَنٖ وَأَنۢبَتَهَا نَبَاتًا حَسَنٗا وَكَفَّلَهَا زَكَرِيَّاۖ كُلَّمَا دَخَلَ عَلَيۡهَا زَكَرِيَّا ٱلۡمِحۡرَابَ وَجَدَ عِندَهَا رِزۡقٗاۖ قَالَ يَٰمَرۡيَمُ أَنَّىٰ لَكِ هَٰذَاۖ قَالَتۡ هُوَ مِنۡ عِندِ ٱللَّهِۖ إِنَّ ٱللَّهَ يَرۡزُقُ مَن يَشَآءُ بِغَيۡرِ حِسَابٍ ٣٧

38. እዚያ ዘንድ ዘከሪያ ጌታውን ለመነ፡፡ «ጌታዬ ሆይ! ከአንተ ዘንድ መልካም ዘርን ለኔ ስጠኝ አንተ ጸሎትን ሰሚነህና» አለ፡፡

هُنَالِكَ دَعَا زَكَرِيَّا رَبَّهُۥۖ قَالَ رَبِّ هَبۡ لِي مِن لَّدُنكَ ذُرِّيَّةٗ طَيِّبَةًۖ إِنَّكَ سَمِيعُ ٱلدُّعَآءِ ٣٨

39. እርሱም በጸሎት ማድረሻው ክፍል ቆሞ ሲጸልይ መላእክት ጠራችው፡፡ «አላህ በየሕያ ከአላህ በኾነ ቃል የሚያረጋግጥ ጌታም ድንግልም ከደጋጎቹ ነቢይም ሲኾን ያበስርሃል» በማለት (መላእክት ጠራችው)፡፡

فَنَادَتۡهُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ وَهُوَ قَآئِمٞ يُصَلِّي فِي ٱلۡمِحۡرَابِ أَنَّ ٱللَّهَ يُبَشِّرُكَ بِيَحۡيَىٰ مُصَدِّقَۢا بِكَلِمَةٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَسَيِّدٗا وَحَصُورٗا وَنَبِيّٗا مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ٣٩

40. «ጌታዬ ሆይ! እኔ እርጅና በእርግጥ የደረሰብኝ ስኾን ባልተቤቴም መሐን ስትሆን ለእኔ እንዴት ልጅ ይኖረኛል አለ፡፡ (መልአኩም) እንደዚሁ አላህ የሚሻውን ነገር ይሠራል» አለው፡፡

قَالَ رَبِّ أَنَّىٰ يَكُونُ لِي غُلَٰمٞ وَقَدۡ بَلَغَنِيَ ٱلۡكِبَرُ وَٱمۡرَأَتِي عَاقِرٞۖ قَالَ كَذَٰلِكَ ٱللَّهُ يَفۡعَلُ مَا يَشَآءُ ٤٠

41. «ጌታዬ ሆይ! ለእኔ ምልክትን አድርግልኝ» አለ፡፡ «ምልክትህ ሦስት ቀን በጥቅሻ ቢኾን እንጅ ሰዎችን አለማናገርህ ነው፡፡ ጌታህንም በብዙ አውሳ፡፡ በማታና በጧትም አወድሰው» አለው፡፡

قَالَ رَبِّ ٱجْعَل لِّيٓ ءَايَةٗۖ قَالَ ءَايَتُكَ أَلَّا تُكَلِّمَ ٱلنَّاسَ ثَلَٰثَةَ أَيَّامٍ إِلَّا رَمۡزٗاۗ وَٱذۡكُر رَّبَّكَ كَثِيرٗا وَسَبِّحۡ بِٱلۡعَشِيِّ وَٱلۡإِبۡكَٰرِ ٤١

42. መላእክትም ያሉትን (አስታውስ)፡፡ «መርየም ሆይ! አላህ በእርግጥ መረጠሽ፡፡ አነጻሽም፡፡ በዓለማት ሴቶችም ላይ መረጠሽ፡፡»

وَإِذۡ قَالَتِ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَٰمَرۡيَمُ إِنَّ ٱللَّهَ ٱصۡطَفَىٰكِ وَطَهَّرَكِ وَٱصۡطَفَىٰكِ عَلَىٰ نِسَآءِ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٤٢

43. «መርየም ሆይ! ለጌታሽ ታዘዢ፡፡ ስገጂም፡፡ ከአጎንባሾቹም ጋር አጎንብሺ፡፡»

يَٰمَرۡيَمُ ٱقۡنُتِي لِرَبِّكِ وَٱسۡجُدِي وَٱرۡكَعِي مَعَ ٱلرَّٰكِعِينَ ٤٣

44. ይኸ ወደ አንተ የምናወርደው የኾነ ከሩቅ ወሬዎች ነው፡፡ መርየምንም ማን እንደሚያሳድግ ብርኦቻቸውን (ለዕጣ) በጣሉ ጊዜ እነሱ ዘንድ አልነበርክም፡፡ በሚከራከሩም ጊዜ እነሱ ዘንድ አልነበርክም፡፡

ذَٰلِكَ مِنۡ أَنۢبَآءِ ٱلۡغَيۡبِ نُوحِيهِ إِلَيۡكَۚ وَمَا كُنتَ لَدَيۡهِمۡ إِذۡ يُلۡقُونَ أَقۡلَٰمَهُمۡ أَيُّهُمۡ يَكۡفُلُ مَرۡيَمَ وَمَا كُنتَ لَدَيۡهِمۡ إِذۡ يَخۡتَصِمُونَ ٤٤

45. መላእክት ያሉትን (አስታውስ)፡- «መርየም ሆይ! አላህ ከርሱ በኾነው ቃል ስሙ አልመሲሕ ዒሳ የመርየም ልጅ በዚህ ዓለምና በመጨረሻውም ዓለም የተከበረ ከባለሟሎችም በኾነ (ልጅ) ያበስርሻል፡፡»

إِذۡ قَالَتِ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَٰمَرۡيَمُ إِنَّ ٱللَّهَ يُبَشِّرُكِ بِكَلِمَةٖ مِّنۡهُ ٱسۡمُهُ ٱلۡمَسِيحُ عِيسَى ٱبۡنُ مَرۡيَمَ وَجِيهٗا فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ وَمِنَ ٱلۡمُقَرَّبِينَ ٤٥

46. «በሕፃንነቱና በከፈኒሳነቱ ሰዎቹን ያነጋግራል፡፡ ከመልካሞቹም ነው» (አላት)፡፡

وَيُكَلِّمُ ٱلنَّاسَ فِي ٱلۡمَهۡدِ وَكَهۡلٗا وَمِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ٤٦

47. ፡-ጌታዬ ሆይ! ሰው ያልነካኝ ስኾን ለኔ እንዴት ልጅ ይኖረኛል አለች፡፡ ነገሩ እንዳልሽው ነው፡፡ አላህ የሚሻውን ይፈጥራል፡፡ አንዳችን በሻ ጊዜ ለርሱ ኹን ይለዋል፤ ወዲውኑም ይኾናል አላት፡፡

قَالَتۡ رَبِّ أَنَّىٰ يَكُونُ لِي وَلَدٞ وَلَمۡ يَمۡسَسۡنِي بَشَرٞۖ قَالَ كَذَٰلِكِ ٱللَّهُ يَخۡلُقُ مَا يَشَآءُۚ إِذَا قَضَىٰٓ أَمۡرٗا فَإِنَّمَا يَقُولُ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ٤٧

48. ጽሕፈትንና ጥበብንም ተውራትንና ኢንጂልንም ያስተምረዋል፡፡

وَيُعَلِّمُهُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحِكۡمَةَ وَٱلتَّوۡرَىٰةَ وَٱلۡإِنجِيلَ ٤٨

49. ወደ እስራኤልም ልጆች መልክተኛ ያደርገዋል፡፡ (ይላልም)፡- «እኔ ከጌታዬ ዘንድ በተዓምር ወደ እናንተ መጣሁ፡፡ እኔ ለናንተ ከጭቃ እንደ ወፍ ቅርፅ እፈጥራለሁ፡፡ በርሱም እተነፍስበታለሁ፡፡ በአላህም ፈቃድ ወፍ ይኾናል፡፡ በአላህም ፈቃድ ዕውር ኾኖ የተወለደን፣ ለምጸኛንም አድናለሁ፡፡ ሙታንንም አስነሳለሁ፡፡ የምትበሉትንና በቤታችሁ የምታደልቡትንም ሁሉ እነግራችኋለሁ፡፡ የምታምኑ እንደኾናችሁ ለእናንተ በዚህ ውስጥ በእርግጥ ተዓምር አለበት፡፡»

وَرَسُولًا إِلَىٰ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ أَنِّي قَدۡ جِئۡتُكُم بِـَٔايَةٖ مِّن رَّبِّكُمۡ أَنِّيٓ أَخۡلُقُ لَكُم مِّنَ ٱلطِّينِ كَهَيۡـَٔةِ ٱلطَّيۡرِ فَأَنفُخُ فِيهِ فَيَكُونُ طَيۡرَۢا بِإِذۡنِ ٱللَّهِۖ وَأُبۡرِئُ ٱلۡأَكۡمَهَ وَٱلۡأَبۡرَصَ وَأُحۡيِ ٱلۡمَوۡتَىٰ بِإِذۡنِ ٱللَّهِۖ وَأُنَبِّئُكُم بِمَا تَأۡكُلُونَ وَمَا تَدَّخِرُونَ فِي بُيُوتِكُمۡۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لَّكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ٤٩

50. «ከተውራትም ከእኔ በፊት ያለውን ያረጋገጥሁ ስኾን የዚያንም በእናንተ ላይ እርም የተደረገውን ከፊል ለእናንተ እፈቅድ ዘንድ (መጣኋችሁ) ከጌታችሁም በኾነ ታምር መጣሁዋችሁ፡፡ አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡»

وَمُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيَّ مِنَ ٱلتَّوۡرَىٰةِ وَلِأُحِلَّ لَكُم بَعۡضَ ٱلَّذِي حُرِّمَ عَلَيۡكُمۡۚ وَجِئۡتُكُم بِـَٔايَةٖ مِّن رَّبِّكُمۡ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ٥٠

51. «አላህ ጌታዬና ጌታችሁ ነው፤ ስለዚህ ተገዙት፤ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው» (አላቸው)፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ رَبِّي وَرَبُّكُمۡ فَٱعۡبُدُوهُۚ هَٰذَا صِرَٰطٞ مُّسۡتَقِيمٞ ٥١

52. ዒሳ ከነርሱ ክህደት በተሰማውም ጊዜ፡- «ወደ አላህ (ተጨምረው) ረዳቶቼ እነማን ናቸው» አለ፤ ሐዋርያት፡- «እኛ የአላህ ረዳቶች ነን፤ በአላህ አምነናል፤ እኛም ትክክለኛ ታዛዦች መኾናችንን መስክር» አሉ፡፡

۞فَلَمَّآ أَحَسَّ عِيسَىٰ مِنۡهُمُ ٱلۡكُفۡرَ قَالَ مَنۡ أَنصَارِيٓ إِلَى ٱللَّهِۖ قَالَ ٱلۡحَوَارِيُّونَ نَحۡنُ أَنصَارُ ٱللَّهِ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَٱشۡهَدۡ بِأَنَّا مُسۡلِمُونَ ٥٢

53. «ጌታችን ሆይ! ባወረድኸው አመንን፤ መልክተኛውንም ተከተልን፤ ከመስካሪዎችም ጋር መዝግበን» (አሉ)፡፡

رَبَّنَآ ءَامَنَّا بِمَآ أَنزَلۡتَ وَٱتَّبَعۡنَا ٱلرَّسُولَ فَٱكۡتُبۡنَا مَعَ ٱلشَّٰهِدِينَ ٥٣

54. (አይሁዶችም) አደሙ አላህም አድማቸውን መለሰባቸው፡፡ አላህም ከአድመኞች ሁሉ በላጭ ነው፡፡

وَمَكَرُواْ وَمَكَرَ ٱللَّهُۖ وَٱللَّهُ خَيۡرُ ٱلۡمَٰكِرِينَ ٥٤

55. አላህም ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ዒሳ ሆይ! እኔ ወሳጂህ ወደ እኔም አንሺህ ነኝ፡፡ ከነዚያም ከካዱት ሰዎች አጥሪህ ነኝ እነዚያንም የተከተሉህን እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ ከነዚያ ከካዱት በላይ አድራጊ ነኝ፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደእኔ ነው፡፡ በርሱ ትለያዩበትም በነበራችሁት ነገር በመካከላችሁ እፈርዳለሁ፡፡

إِذۡ قَالَ ٱللَّهُ يَٰعِيسَىٰٓ إِنِّي مُتَوَفِّيكَ وَرَافِعُكَ إِلَيَّ وَمُطَهِّرُكَ مِنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَجَاعِلُ ٱلَّذِينَ ٱتَّبَعُوكَ فَوۡقَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِۖ ثُمَّ إِلَيَّ مَرۡجِعُكُمۡ فَأَحۡكُمُ بَيۡنَكُمۡ فِيمَا كُنتُمۡ فِيهِ تَخۡتَلِفُونَ ٥٥

56. «እነዚያማ የካዱትን ሰዎች በቅርቢቱ ዓለምና በመጨረሻይቱ ዓለም ብርቱን ቅጣት እቀጣቸዋለሁ፡፡ ለእነርሱም ምንም ረዳቶች የሏቸውም፡፡»

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَأُعَذِّبُهُمۡ عَذَابٗا شَدِيدٗا فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ وَمَا لَهُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٥٦

57. እነዚያም ያመኑትማ መልካም ሥራዎችንም የሠሩት ምንዳዎቻቸውን ይሞላላቸዋል፡፡ አላህም በዳዮችን አይወድም፡፡

وَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فَيُوَفِّيهِمۡ أُجُورَهُمۡۗ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ ٱلظَّٰلِمِينَ ٥٧

58. ይህ ከተዓምራቶችና ጥበብን ከያዘው ተግሳጽ ሲኾን በአንተ ላይ እናነበዋለን፡፡

ذَٰلِكَ نَتۡلُوهُ عَلَيۡكَ مِنَ ٱلۡأٓيَٰتِ وَٱلذِّكۡرِ ٱلۡحَكِيمِ ٥٨

59. አላህ ዘንድ የዒሳ ምሳሌ እንደ አዳም ብጤ ነው፡፡ ከዐፈር ፈጠረው፡፡ ከዚያም ለርሱ (ሰው) «ኹን» አለው፤ ኾነም፡፡

إِنَّ مَثَلَ عِيسَىٰ عِندَ ٱللَّهِ كَمَثَلِ ءَادَمَۖ خَلَقَهُۥ مِن تُرَابٖ ثُمَّ قَالَ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ٥٩

60. ይህ ከጌታህ ዘንድ የኾነ እውነት ነው፡፡ ከተጠራጣሪዎቹም አትኹን፡፡

ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ فَلَا تَكُن مِّنَ ٱلۡمُمۡتَرِينَ ٦٠

61. ዕውቀቱም ከመጣልህ በኋላ በርሱ (በዒሳ) የተከራከሩህን ሰዎች «ኑ፤ ልጆቻችንንና ልጆቻችሁን፣ ሴቶቻችንንና ሴቶቻችሁንም፣ ነፍሶቻችንንና ነፍሶቻችሁንም እንጥራ፡፡ ከዚያም አጥብቀን አላህን እንለምን፤ የአላህንም ቁጣ በውሸታሞቹ ላይ እናድርግ» በላቸው፡፡

فَمَنۡ حَآجَّكَ فِيهِ مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَكَ مِنَ ٱلۡعِلۡمِ فَقُلۡ تَعَالَوۡاْ نَدۡعُ أَبۡنَآءَنَا وَأَبۡنَآءَكُمۡ وَنِسَآءَنَا وَنِسَآءَكُمۡ وَأَنفُسَنَا وَأَنفُسَكُمۡ ثُمَّ نَبۡتَهِلۡ فَنَجۡعَل لَّعۡنَتَ ٱللَّهِ عَلَى ٱلۡكَٰذِبِينَ ٦١

62. ይህ እርሱ በእርግጥ እውነተኛ ታሪክ ነው፡፡ አምላክም ከአላህ በስተቀር ምንም የለም፡፡ አላህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَهُوَ ٱلۡقَصَصُ ٱلۡحَقُّۚ وَمَا مِنۡ إِلَٰهٍ إِلَّا ٱللَّهُۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٦٢

63. (ከማመን) እንቢ ቢሉም አላህ አጥፊዎቹን በእርግጥ ዐዋቂ ነው፡፡

فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمُۢ بِٱلۡمُفۡسِدِينَ ٦٣

64. የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! በእኛና በእናንተ መካከል ትክክል ወደ ኾነች ቃል ኑ፡፡ (እርሷም) አላህን እንጅ ሌላን ላንገዛ፣ በርሱም ምንንም ላናጋራ፣ ከፊላችንም ከፊሉን ከአላህ ሌላ አማልክት አድርጎ ላይይዝ ነው፤ በላቸው፡፡ እምቢ ቢሉም፡- እኛ ሙስሊሞች መኾናችንን መስክሩ በሏቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ تَعَالَوۡاْ إِلَىٰ كَلِمَةٖ سَوَآءِۭ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَكُمۡ أَلَّا نَعۡبُدَ إِلَّا ٱللَّهَ وَلَا نُشۡرِكَ بِهِۦ شَيۡـٔٗا وَلَا يَتَّخِذَ بَعۡضُنَا بَعۡضًا أَرۡبَابٗا مِّن دُونِ ٱللَّهِۚ فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَقُولُواْ ٱشۡهَدُواْ بِأَنَّا مُسۡلِمُونَ ٦٤

65. እናንተ የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! በኢብራሂም ለምን ትከራከራላችሁ ተውራትና ኢንጂልም ከርሱ በኋላ እንጅ አልተወረዱም፡፡ ልብ አታደርጉምን በላቸው፡፡

يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لِمَ تُحَآجُّونَ فِيٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَمَآ أُنزِلَتِ ٱلتَّوۡرَىٰةُ وَٱلۡإِنجِيلُ إِلَّا مِنۢ بَعۡدِهِۦٓۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ٦٥

66. ንቁ! እናንተ እነዚያ ለእናንተ በርሱ ዕውቀት ባላችሁ ነገር የተከራከራችሁ ናችሁ፡፡ ታዲያ ለእናንተ በርሱ ዕውቀት በሌላችሁ ነገር ለምን ትከራከራላችሁ አላህም ያውቃል፡፡ እናንተ ግን አታውቁም፡፡

هَٰٓأَنتُمۡ هَٰٓؤُلَآءِ حَٰجَجۡتُمۡ فِيمَا لَكُم بِهِۦ عِلۡمٞ فَلِمَ تُحَآجُّونَ فِيمَا لَيۡسَ لَكُم بِهِۦ عِلۡمٞۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ وَأَنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ٦٦

67. ኢብራሂም ይሁዳዊም ክርስቲያንም አልነበረም፡፡ ግን ወደ ቀጥተኛው ሃይማኖት የተዘነበለ ሙስሊም ነበረ፡፡ ከአጋሪዎችም አልነበረም፡፡

مَا كَانَ إِبۡرَٰهِيمُ يَهُودِيّٗا وَلَا نَصۡرَانِيّٗا وَلَٰكِن كَانَ حَنِيفٗا مُّسۡلِمٗا وَمَا كَانَ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٦٧

68. ከሰው ሁሉ በኢብራሂም ተገቢዎቹ እነዚያ የተከተሉትና ይህ ነቢይ እነዚያም ያመኑት ናቸው፡፡ አላህም የምእምናን ረዳት ነው፡፡

إِنَّ أَوۡلَى ٱلنَّاسِ بِإِبۡرَٰهِيمَ لَلَّذِينَ ٱتَّبَعُوهُ وَهَٰذَا ٱلنَّبِيُّ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۗ وَٱللَّهُ وَلِيُّ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٦٨

69. ከመጽሐፉ ባለቤቶች የኾኑ ጭፍሮች ነፍሶቻቸውን እንጂ የማያሳስቱ ሲኾኑ ሊያሳስቱዋችሁ ተመኙ ግን አያውቁም፡፡

وَدَّت طَّآئِفَةٞ مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ لَوۡ يُضِلُّونَكُمۡ وَمَا يُضِلُّونَ إِلَّآ أَنفُسَهُمۡ وَمَا يَشۡعُرُونَ ٦٩

70. የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! እናንተ የምታውቁ ስትኾኑ በአላህ አንቀጾች ለምን ትክዳላችሁ

يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لِمَ تَكۡفُرُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَأَنتُمۡ تَشۡهَدُونَ ٧٠

71. «የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! እውነቱን በውሸት ለምን ትቀላቅላላችሁ እውነቱንም እናንተ የምታውቁ ስትኾኑ ለምን ትደብቃላችሁ»

يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لِمَ تَلۡبِسُونَ ٱلۡحَقَّ بِٱلۡبَٰطِلِ وَتَكۡتُمُونَ ٱلۡحَقَّ وَأَنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٧١

72. ከመጽሐፉ ባለቤቶች የኾኑ ጭፍሮችም አሉ፡- «በነዚያ በአመኑት ላይ በተወረደው (ቁርኣን) በቀኑ መጀመሪያ ላይ እመኑበት፡፡ በመጨረሻውም ካዱት፡፡ እነርሱ ሊመለሱ ይከጀላልና፡፡»

وَقَالَت طَّآئِفَةٞ مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ ءَامِنُواْ بِٱلَّذِيٓ أُنزِلَ عَلَى ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَجۡهَ ٱلنَّهَارِ وَٱكۡفُرُوٓاْ ءَاخِرَهُۥ لَعَلَّهُمۡ يَرۡجِعُونَ ٧٢

73. እናንተ የተሰጣችሁትን ብጤ አንድም ሰው መሰጠቱን ወይም እጌታችሁ ዘንድ የሚከራከሩዋችሁ መኾንን ሃይማኖታችሁን ለተከተለ ሰው ቢኾን እንጂ አትመኑ (አትግለጹ አሉ)፡፡ «መምሪያው የአላህ መምሪያ ብቻ ነው» በላቸው፡፡ «ችሮታ በአላህ እጅ ነው፡፡ ለሚሻው ይሰጠዋል፡፡ አላህም ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

وَلَا تُؤۡمِنُوٓاْ إِلَّا لِمَن تَبِعَ دِينَكُمۡ قُلۡ إِنَّ ٱلۡهُدَىٰ هُدَى ٱللَّهِ أَن يُؤۡتَىٰٓ أَحَدٞ مِّثۡلَ مَآ أُوتِيتُمۡ أَوۡ يُحَآجُّوكُمۡ عِندَ رَبِّكُمۡۗ قُلۡ إِنَّ ٱلۡفَضۡلَ بِيَدِ ٱللَّهِ يُؤۡتِيهِ مَن يَشَآءُۗ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٞ ٧٣

74. በችሮታው (በነቢይነት) የሚሻውን ይመርጣል፡፡ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

يَخۡتَصُّ بِرَحۡمَتِهِۦ مَن يَشَآءُۗ وَٱللَّهُ ذُو ٱلۡفَضۡلِ ٱلۡعَظِيمِ ٧٤

75. ከመጽሐፉ ሰዎችም በብዙ ገንዘብ ብታምነው ወዳንተ የሚመልስ ሰው አልለ፡፡ ከእነሱም በአንድ ዲናር እንኳ ብታምነው፤ ሁል ጊዜ በርሱ ላይ የምትጠባበቅ ካልኾንክ በስተቀር የማይመልስ ሰው አልለ፡፡ «ይህ በመሃይምናን (በምናደርገው) በእኛ ላይ ምንም መንገድ የለብንም» ስለሚሉ ነው፡፡ እነርሱ እያወቁም በአላህ ላይ ውሸትን ይናገራሉ፡፡

۞وَمِنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ مَنۡ إِن تَأۡمَنۡهُ بِقِنطَارٖ يُؤَدِّهِۦٓ إِلَيۡكَ وَمِنۡهُم مَّنۡ إِن تَأۡمَنۡهُ بِدِينَارٖ لَّا يُؤَدِّهِۦٓ إِلَيۡكَ إِلَّا مَا دُمۡتَ عَلَيۡهِ قَآئِمٗاۗ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَالُواْ لَيۡسَ عَلَيۡنَا فِي ٱلۡأُمِّيِّـۧنَ سَبِيلٞ وَيَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَ وَهُمۡ يَعۡلَمُونَ ٧٥

76. አይደለም (አለባቸው እንጅ)፡፡ በቃል ኪዳኑ የሞላና የተጠነቀቀ ሰው አላህ ጥንቁቆችን ይወዳል፡፡

بَلَىٰۚ مَنۡ أَوۡفَىٰ بِعَهۡدِهِۦ وَٱتَّقَىٰ فَإِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُتَّقِينَ ٧٦

77. እነዚህ በአላህ ቃል ኪዳንና በመሐላዎቻቸው ጥቂትን ዋጋ የሚለውጡ እነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም ምንም ዕድል የላቸውም፡፡ በትንሣኤ ቀንም አላህ አያነጋግራቸውም፡፡ ወደ እነርሱም አይመለከትም አያነጻቸውምም፡፡ ለነሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَشۡتَرُونَ بِعَهۡدِ ٱللَّهِ وَأَيۡمَٰنِهِمۡ ثَمَنٗا قَلِيلًا أُوْلَٰٓئِكَ لَا خَلَٰقَ لَهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ وَلَا يُكَلِّمُهُمُ ٱللَّهُ وَلَا يَنظُرُ إِلَيۡهِمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ وَلَا يُزَكِّيهِمۡ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٧٧

78. ከእነሱም እርሱ ከመጽሐፉ ያይደለ ሲኾን ከመጽሐፉ መኾኑን እንድታስቡ በመጽሐፉ ምላሶቻቸውን የሚያጣምሙ ክፍሎች አሉ፡፡ እርሱ ከአላህ ዘንድ ያልኾነ ሲኾን «እርሱ ከአላህ ዘንድ ነውም» ይላሉ፡፡ እነርሱ የሚያውቁ ሲኾኑም በአላህ ላይ ውሸትን ይናገራሉ፡፡

وَإِنَّ مِنۡهُمۡ لَفَرِيقٗا يَلۡوُۥنَ أَلۡسِنَتَهُم بِٱلۡكِتَٰبِ لِتَحۡسَبُوهُ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَمَا هُوَ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَيَقُولُونَ هُوَ مِنۡ عِندِ ٱللَّهِ وَمَا هُوَ مِنۡ عِندِ ٱللَّهِ وَيَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَ وَهُمۡ يَعۡلَمُونَ ٧٨

79. ለማንም ሰው አላህ መጽሐፍንና ጥበብን ነቢይነትንም ሊሰጠውና ከዚያም ለሰዎች «ከአላህ ሌላ ለእኔ ባሮች ኹኑ» ሊል አይገባውም፡፡ «ግን መጽሐፍን የምታስተምሩ በነበራችሁትና የምታጠኑም በነበራችሁት በዕውቀታችሁ ሠሪዎች ኹኑ» (ይላቸዋል)፡፡

مَا كَانَ لِبَشَرٍ أَن يُؤۡتِيَهُ ٱللَّهُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحُكۡمَ وَٱلنُّبُوَّةَ ثُمَّ يَقُولَ لِلنَّاسِ كُونُواْ عِبَادٗا لِّي مِن دُونِ ٱللَّهِ وَلَٰكِن كُونُواْ رَبَّٰنِيِّـۧنَ بِمَا كُنتُمۡ تُعَلِّمُونَ ٱلۡكِتَٰبَ وَبِمَا كُنتُمۡ تَدۡرُسُونَ ٧٩

80. መላእክትንና ነቢያትንም አማልክቶች አድርጋችሁ እንድትይዙ ሊያዛችሁ (አይገባውም)፡፡ እናንተ ሙስሊሞች ከኾናችሁ በኋላ በክህደት ያዛችኋልን

وَلَا يَأۡمُرَكُمۡ أَن تَتَّخِذُواْ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ وَٱلنَّبِيِّـۧنَ أَرۡبَابًاۗ أَيَأۡمُرُكُم بِٱلۡكُفۡرِ بَعۡدَ إِذۡ أَنتُم مُّسۡلِمُونَ ٨٠

81. አላህ የነቢያትን ቃል ኪዳን ከመጽሐፍና ከጥበብ ሰጥቻችሁ ከዚያም «ከእናንተ ጋር ላለው (መጽሐፍ) የሚያረጋግጥ መልክተኛ ቢመጣላችሁ በርሱ በእርግጥ እንደምታምኑበት በእርግጥም እንድትረዱት ሲል በያዘ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ አረጋገጣችሁን በዚህም ላይ ኪዳኔን ያዛችሁምን» አላቸው፡፡ «አረጋገጥን» አሉ፡፡ «እንግዲያስ መስክሩ፤ እኔም ከእናንተ ጋር ከመስካሪዎቹ ነኝ» አላቸው፡፡

وَإِذۡ أَخَذَ ٱللَّهُ مِيثَٰقَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ لَمَآ ءَاتَيۡتُكُم مِّن كِتَٰبٖ وَحِكۡمَةٖ ثُمَّ جَآءَكُمۡ رَسُولٞ مُّصَدِّقٞ لِّمَا مَعَكُمۡ لَتُؤۡمِنُنَّ بِهِۦ وَلَتَنصُرُنَّهُۥۚ قَالَ ءَأَقۡرَرۡتُمۡ وَأَخَذۡتُمۡ عَلَىٰ ذَٰلِكُمۡ إِصۡرِيۖ قَالُوٓاْ أَقۡرَرۡنَاۚ قَالَ فَٱشۡهَدُواْ وَأَنَا۠ مَعَكُم مِّنَ ٱلشَّٰهِدِينَ ٨١

82. ከዚህም በኋላ የሸሹ ሰዎች እነዚያ እነሱ አመጸኞቹ ናቸው፡፡

فَمَن تَوَلَّىٰ بَعۡدَ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ٨٢

83. በሰማያትና በምድር ያሉ ሁሉ፤ በውድም በግድም ለርሱ የታዘዙ ወደርሱም የሚመለሱ ሲኾኑ (ከሓዲዎች) ከአላህ ሃይማኖት ሌላን ይፈልጋሉን

أَفَغَيۡرَ دِينِ ٱللَّهِ يَبۡغُونَ وَلَهُۥٓ أَسۡلَمَ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ طَوۡعٗا وَكَرۡهٗا وَإِلَيۡهِ يُرۡجَعُونَ ٨٣

قُلۡ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَمَآ أُنزِلَ عَلَيۡنَا وَمَآ أُنزِلَ عَلَىٰٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡمَٰعِيلَ وَإِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ وَٱلۡأَسۡبَاطِ وَمَآ أُوتِيَ مُوسَىٰ وَعِيسَىٰ وَٱلنَّبِيُّونَ مِن رَّبِّهِمۡ لَا نُفَرِّقُ بَيۡنَ أَحَدٖ مِّنۡهُمۡ وَنَحۡنُ لَهُۥ مُسۡلِمُونَ ٨٤

84. «በአላህ አመንን፡፡ በእኛ ላይ በተወረደውም (በቁርኣን)፣ በኢብራሂምና በኢስማዒልም፣ በኢስሓቅም፣ በያዕቆብም፣ በነገዶችም ላይ በተወረደው፤ ለሙሳና ለዒሳም ለነቢያትም ሁሉ ከጌታቸው በተሰጠው (አመንን)፡፡ ከእነርሱ መካከል አንድንም አንለይም፡፡ እኛ ለእርሱ ታዛዦች ነን» በል፡፡

وَمَن يَبۡتَغِ غَيۡرَ ٱلۡإِسۡلَٰمِ دِينٗا فَلَن يُقۡبَلَ مِنۡهُ وَهُوَ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٨٥

85. ከኢስላም ሌላ ሃይማኖትን የሚፈልግ ሰው ፈጽሞ ከርሱ ተቀባይ የለውም፡፡ እርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም ከከሳሪዎቹ ነው፡፡

كَيۡفَ يَهۡدِي ٱللَّهُ قَوۡمٗا كَفَرُواْ بَعۡدَ إِيمَٰنِهِمۡ وَشَهِدُوٓاْ أَنَّ ٱلرَّسُولَ حَقّٞ وَجَآءَهُمُ ٱلۡبَيِّنَٰتُۚ وَٱللَّهُ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٨٦

86. ከእምነታቸውና መልክተኛውም እውነት መኾኑን ከመሰከሩ የተብራሩ አንቀጾችም ከመጡላቸው በኋላ የካዱን ሕዝቦች አላህ እንዴት ያቀናል! አላህ በዳዮችንም ሕዝቦች አያቀናም፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ جَزَآؤُهُمۡ أَنَّ عَلَيۡهِمۡ لَعۡنَةَ ٱللَّهِ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ وَٱلنَّاسِ أَجۡمَعِينَ ٨٧

87. እነዚያ ቅጣታቸው የአላህና የመላእክት የሰዎችም ሁሉ ርግማን በእነሱ ላይ መኾን ነው፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَا لَا يُخَفَّفُ عَنۡهُمُ ٱلۡعَذَابُ وَلَا هُمۡ يُنظَرُونَ ٨٨

88. በውስጧ ዘውታሪዎች ሲኾኑ ቅጣቱም ከነሱ ላይ አይቃለልላቸውም፡፡ እነሱም ቀን አይሰሰጡም፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ تَابُواْ مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ وَأَصۡلَحُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ٨٩

89. እነዚያ ከዚህ በኋላ ንስሓ የገቡና (ሥራቸውን) ያሳመሩ ሲቀሩ፡፡ (እነዚህንስ ይምራቸዋል)፤ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بَعۡدَ إِيمَٰنِهِمۡ ثُمَّ ٱزۡدَادُواْ كُفۡرٗا لَّن تُقۡبَلَ تَوۡبَتُهُمۡ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلضَّآلُّونَ ٩٠

90. እነዚያ ከእምነታቸው በኋላ የካዱ ከዚያም ክህደትን የጨመሩ ጸጸታቸው ፈጽሞ ተቀባይ የላትም፡፡ እነዚያም የተሳሳቱ እነርሱ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَمَاتُواْ وَهُمۡ كُفَّارٞ فَلَن يُقۡبَلَ مِنۡ أَحَدِهِم مِّلۡءُ ٱلۡأَرۡضِ ذَهَبٗا وَلَوِ ٱفۡتَدَىٰ بِهِۦٓۗ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ وَمَا لَهُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٩١

91. እነዚያ የካዱና እነርሱም በክህደታቸው ላይ እንዳሉ የሞቱ ከእነሱ ከአንዳቸው በምድር ሙሉ የኾነ ወርቅ (ቢኖረውና) በርሱ ቢበዥበትም እንኳ ፈጽሞ ተቀባይን አያገኝም፡፡ እነዚያ ለእነርሱ የሚያሰቃይ ቅጣት አላቸው፡፡ ለነርሱም ምንም ረዳቶች የሏቸውም፡ ፡

لَن تَنَالُواْ ٱلۡبِرَّ حَتَّىٰ تُنفِقُواْ مِمَّا تُحِبُّونَۚ وَمَا تُنفِقُواْ مِن شَيۡءٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ بِهِۦ عَلِيمٞ ٩٢

92. የምትወዱትን እስከምትለግሱ ድረስ በጎን ሥራ (ዋጋውን) አታገኙም፡፡ ከምንም ነገር ብትለግሱ አላህ ያውቀዋል፡፡

93. ተውራት ከመወረድዋ በፊት እስራኤል በራሱ ላይ እርም ካደረገው ነገር በስተቀር ምግብ ሁሉ ለእስራኤል ልጆች የተፈቀደ ነበር፡፡ እውነተኞችም እንደኾናችሁ ተውራትን አምጡ አንብቡዋትም በላቸው፡፡

۞ كُلُّ ٱلطَّعَامِ كَانَ حِلّٗا لِّبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ إِلَّا مَا حَرَّمَ إِسۡرَٰٓءِيلُ عَلَىٰ نَفۡسِهِۦ مِن قَبۡلِ أَن تُنَزَّلَ ٱلتَّوۡرَىٰةُۚ قُلۡ فَأۡتُواْ بِٱلتَّوۡرَىٰةِ فَٱتۡلُوهَآ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٩٣

94. ከዚህም በኋላ በአላህ ላይ ውሸትን የቀጣጠፉ ሰዎች እነዚያ እነርሱ በደለኞች ናቸው፡፡

فَمَنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَ مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٩٤

95. «አላህ እውነትን ተናገረ፡፡ የኢብራሂምንም መንገድ ወደ እውነት ያዘነበለ ሲኾን ተከተሉ፡፡ ከአጋሪዎቹም አልነበረም» በላቸው፡፡

قُلۡ صَدَقَ ٱللَّهُۗ فَٱتَّبِعُواْ مِلَّةَ إِبۡرَٰهِيمَ حَنِيفٗاۖ وَمَا كَانَ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٩٥

96. ለሰዎች (መጸለያ) መጀመሪያ የተኖረው ቤት ብሩክና ለዓለማት ሁሉ መመሪያ ሲኾን ያ በበካህ (በመካ) ያለው ነው፡፡

إِنَّ أَوَّلَ بَيۡتٖ وُضِعَ لِلنَّاسِ لَلَّذِي بِبَكَّةَ مُبَارَكٗا وَهُدٗى لِّلۡعَٰلَمِينَ ٩٦

97. በውስጡ ግልጽ የኾኑ ተዓምራቶች የኢብራሒምም መቆሚያ አልለ፡፡ ወደ ውስጡ የገባ ሰው ጸጥተኛ ይኾናል፡፡ ለአላህም በሰዎች ላይ ወደርሱ መኼድን በቻለ ሁሉ ላይ ቤቱን መጎብኘት ግዴታ አለባቸው፡፡ የካደም ሰው አላህ ከዓለማት ሁሉ የተብቃቃ ነው፡፡

فِيهِ ءَايَٰتُۢ بَيِّنَٰتٞ مَّقَامُ إِبۡرَٰهِيمَۖ وَمَن دَخَلَهُۥ كَانَ ءَامِنٗاۗ وَلِلَّهِ عَلَى ٱلنَّاسِ حِجُّ ٱلۡبَيۡتِ مَنِ ٱسۡتَطَاعَ إِلَيۡهِ سَبِيلٗاۚ وَمَن كَفَرَ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَنِيٌّ عَنِ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٩٧

98. «የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! አላህ በምትሠሩት ሁሉ ላይ ዐዋቂ ሲኾን በአላህ ተዓምራት ለምን ትክዳላችሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لِمَ تَكۡفُرُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَٱللَّهُ شَهِيدٌ عَلَىٰ مَا تَعۡمَلُونَ ٩٨

99. «የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! እናንተ መስካሪዎች ኾናችሁ ከአላህ መንገድ መጥመሟን የምትፈልጓት ስትኾኑ ያመነን ሰው ለምን ትከለክላላችሁ አላህም ከምትሰሩት ነገር ሁሉ ዘንጊ አይደለም» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لِمَ تَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ مَنۡ ءَامَنَ تَبۡغُونَهَا عِوَجٗا وَأَنتُمۡ شُهَدَآءُۗ وَمَا ٱللَّهُ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ٩٩

100. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከነዚያ መጽሐፉን ከተሰጡት ሰዎች ከፊሉን ብትታዘዙ ከእምነታችሁ በኋላ ከሓዲዎች አድርገው ይመልሱዋችኋል፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِن تُطِيعُواْ فَرِيقٗا مِّنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ يَرُدُّوكُم بَعۡدَ إِيمَٰنِكُمۡ كَٰفِرِينَ ١٠٠

101. የአላህም አንቀጾች በእናንተ ላይ የሚነበቡ ሲኾኑ መልክተኛውም በውስጣችሁ ያለ ሲኾን እናንተ እንዴት ትክዳላችሁ በአላህም የሚጠበቅ ሰው ወደ ቀጥተኛው መንገድ በእርግጥ ተመራ፡፡

وَكَيۡفَ تَكۡفُرُونَ وَأَنتُمۡ تُتۡلَىٰ عَلَيۡكُمۡ ءَايَٰتُ ٱللَّهِ وَفِيكُمۡ رَسُولُهُۥۗ وَمَن يَعۡتَصِم بِٱللَّهِ فَقَدۡ هُدِيَ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ١٠١

102. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገቢውን መጠንቀቅ ተጠንቀቁት፡፡ እናንተም ሙስሊሞች ኾናችሁ እንጅ አትሙቱ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ حَقَّ تُقَاتِهِۦ وَلَا تَمُوتُنَّ إِلَّا وَأَنتُم مُّسْلِمُونَ ﴿١٠٢﴾

103. የአላህንም (የማመን) ገመድ ሁላችሁም ያዙ፡፡ አትለያዩም፡፡ ጠበኞችም በነበራችሁ ጊዜ በእናንተ ላይ (የዋለውን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ፡፡ በልቦቻችሁም መካከል አስማማ፡፡ በጸጋውም ወንድማማቾች ኾናችሁ፡፡ በእሳት ጉድጓድ አፋፍም ላይ ነበራችሁ፡፡ ከእርስዋም አዳናችሁ፡፡ እንደዚሁ ትመሩ ዘንድ አላህ ለእናንተ አንቀጾቹን ያብራራል፡፡

وَٱعْتَصِمُوا۟ بِحَبْلِ ٱللَّهِ جَمِيعًا وَلَا تَفَرَّقُوا۟ ۚ وَٱذْكُرُوا۟ نِعْمَتَ ٱللَّهِ عَلَيْكُمْ إِذْ كُنتُمْ أَعْدَآءً فَأَلَّفَ بَيْنَ قُلُوبِكُمْ فَأَصْبَحْتُم بِنِعْمَتِهِۦٓ إِخْوَٰنًا وَكُنتُمْ عَلَىٰ شَفَا حُفْرَةٍ مِّنَ ٱلنَّارِ فَأَنقَذَكُم مِّنْهَا ۗ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمْ ءَايَـٰتِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَهْتَدُونَ ﴿١٠٣﴾

104. ከናንተም ወደ በጎ ነገር የሚጠሩ በመልካም ሥራም የሚያዙ ከክፉ ነገርም የሚከለክሉ ሕዝቦች ይኑሩ፡፡ እነዚያም እነሱ የሚድኑ ናቸው፡፡

وَلْتَكُن مِّنكُمْ أُمَّةٌ يَدْعُونَ إِلَى ٱلْخَيْرِ وَيَأْمُرُونَ بِٱلْمَعْرُوفِ وَيَنْهَوْنَ عَنِ ٱلْمُنكَرِ ۚ وَأُو۟لَـٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُفْلِحُونَ ﴿١٠٤﴾

105. እንደነዚያም ግልጽ ተዓምራት ከመጣላቸው በኋላ እንደተለያዩትና እንደ ተጨቃጨቁት አትኹኑ፡፡ እነዚያም ለእነርሱ ታላቅ ቅጣት አላቸው፡፡

وَلَا تَكُونُوا۟ كَٱلَّذِينَ تَفَرَّقُوا۟ وَٱخْتَلَفُوا۟ مِنۢ بَعْدِ مَا جَآءَهُمُ ٱلْبَيِّنَـٰتُ ۚ وَأُو۟لَـٰٓئِكَ لَهُمْ عَذَابٌ عَظِيمٌ ﴿١٠٥﴾

106. ፊቶች የሚያበሩበትን ፊቶችም የሚጠቁሩበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ እነዚያ ፊቶቻቸው የጠቆሩትማ «ከእምነታችሁ በኋላ ካዳችሁን ትክዱት በነበራችሁት ነገር ቅጣቱን ቅመሱ» (ይባላሉ)፡፡

يَوْمَ تَبْيَضُّ وُجُوهٌ وَتَسْوَدُّ وُجُوهٌ ۚ فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ٱسْوَدَّتْ وُجُوهُهُمْ أَكَفَرْتُم بَعْدَ إِيمَـٰنِكُمْ فَذُوقُوا۟ ٱلْعَذَابَ بِمَا كُنتُمْ تَكْفُرُونَ ﴿١٠٦﴾

107. እነዚያም ፊቶቻቸው ያበሩትማ በአላህ ችሮታ (ገነት) ውስጥ ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

وَأَمَّا ٱلَّذِينَ ٱبْيَضَّتْ وُجُوهُهُمْ فَفِى رَحْمَةِ ٱللَّهِ ۖ هُمْ فِيهَا خَـٰلِدُونَ ﴿١٠٧﴾

108. ይህች በአንተ ላይ በእውነት የምናነባት ስትኾን የአላህ ተዓምራት ናት፡፡ አላህም ለዓለማት በደልን የሚሻ አይደለም፡፡

تِلْكَ ءَايَـٰتُ ٱللَّهِ نَتْلُوهَا عَلَيْكَ بِٱلْحَقِّ ۗ وَمَا ٱللَّهُ يُرِيدُ ظُلْمًا لِّلْعَـٰلَمِينَ ﴿١٠٨﴾

109. በሰማያት ያለውና በምድር ያለውም ሁሉ የአላህ ነው፡፡ ነገሮችም ሁሉ ወደ አላህ ብቻ ይመለሳሉ፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۚ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرْجَعُ ٱلْأُمُورُ ﴿١٠٩﴾

110. ለሰዎች ከተገለጸች ሕዝብ ሁሉ በላጭ ኾናችሁ በጽድቅ ነገር ታዛላችሁ፤ ከመጥፎም ነገር ታዛላችሁ፤ በአላህም (አንድነት) ታምናላችሁ፡፡ የመጽሐፉም ሰዎች ባመኑ ኖሮ ለነርሱ የተሻለ በኾነ ነበር፡፡ ከነርሱ አማኞች አሉ፡፡ አብዛኞቻቸው ግን አመጸኞች ናቸው፡፡

كُنتُمۡ خَيۡرَ أُمَّةٍ أُخۡرِجَتۡ لِلنَّاسِ تَأۡمُرُونَ بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَتَنۡهَوۡنَ عَنِ ٱلۡمُنكَرِ وَتُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِۗ وَلَوۡ ءَامَنَ أَهۡلُ ٱلۡكِتَٰبِ لَكَانَ خَيۡرٗا لَّهُمۚ مِّنۡهُمُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ وَأَكۡثَرُهُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ١١٠

111. ማስከፋትን እንጅ ፈጽሞ አይጎዱዋችሁም፡፡ ቢዋጉዋችሁም ጀርባዎችን ያዞሩላችኋል (ይሸሻሉ)፡፡ ከዚያም አይረዱም፡፡

لَن يَضُرُّوكُمۡ إِلَّآ أَذٗىۖ وَإِن يُقَٰتِلُوكُمۡ يُوَلُّوكُمُ ٱلۡأَدۡبَارَ ثُمَّ لَا يُنصَرُونَ ١١١

112. የትም በተገኙበት ስፍራ ከአላህ በኾነ ቃል ኪዳን ከሰዎችም በኾነ ቃል ኪዳን (የተጠበቁ) ካልኾኑ በስተቀር በነርሱ ላይ ውርደት ተመታችባቸው፡፡ ከአላህም በኾነ ቁጣ ተመለሱ፡፡ በእነርሱም ላይ ድኽነት ተመታችባቸው፡፡ ይኽ እነርሱ በአላህ ተዓምራት ይክዱ ስለ ነበሩና ነቢያትንም ያለ ሕግ ይገድሉ ስለነበሩ ነው፡፡ ይህ በማመጻቸውና ወሰንን ይተላለፉ ስለነበሩ ነው፡፡

ضُرِبَتۡ عَلَيۡهِمُ ٱلذِّلَّةُ أَيۡنَ مَا ثُقِفُوٓاْ إِلَّا بِحَبۡلٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَحَبۡلٖ مِّنَ ٱلنَّاسِ وَبَآءُو بِغَضَبٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَضُرِبَتۡ عَلَيۡهِمُ ٱلۡمَسۡكَنَةُۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ كَانُواْ يَكۡفُرُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَيَقۡتُلُونَ ٱلۡأَنۢبِيَآءَ بِغَيۡرِ حَقّٖۚ ذَٰلِكَ بِمَا عَصَواْ وَّكَانُواْ يَعۡتَدُونَ ١١٢

113. (የመጽሐፉ ሰዎች ሁሉ) እኩል አይደሉም፡፡ ከመጽሐፉ ሰዎች ቀጥ ያሉ በሌሊት ሰዓቶች እነርሱ የሚሰግዱ ኾነው የአላህን አንቀጾች የሚያነቡ ሕዝቦች አሉ፡፡

۞لَيۡسُواْ سَوَآءٗۗ مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ أُمَّةٞ قَآئِمَةٞ يَتۡلُونَ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ ءَانَآءَ ٱلَّيۡلِ وَهُمۡ يَسۡجُدُونَ ١١٣

114. በአላህና በመጨረሻው ቀን ያምናሉ፡፡ በጽድቅ ነገርም ያዛሉ፡፡ ከመጥፎ ነገርም ይከለክላሉ፡፡ በበጎ ሥራዎችም ይጣደፋሉ፡፡ እነዚያም ከመልካሞቹ ናቸው፡፡

يُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ وَيَأۡمُرُونَ بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَيَنۡهَوۡنَ عَنِ ٱلۡمُنكَرِ وَيُسَٰرِعُونَ فِي ٱلۡخَيۡرَٰتِۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ مِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ١١٤

115. ከበጎ ሥራ ማንኛውንም ቢሠሩ አይካዱትም፡፡ አላህም ጥንቁቆቹን ዐዋቂ ነው፡፡

وَمَا يَفۡعَلُواْ مِنۡ خَيۡرٖ فَلَن يُكۡفَرُوهُۗ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِٱلۡمُتَّقِينَ ١١٥

116. እነዚያ የካዱት ሰዎች ገንዘቦቻቸውና ልጆቻቸው ከአላህ (ቅጣት) እነርሱን ምንንም አያድኑዋቸውም፡፡ እነዚያም የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በእርስዋ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَن تُغۡنِيَ عَنۡهُمۡ أَمۡوَٰلُهُمۡ وَلَآ أَوۡلَٰدُهُم مِّنَ ٱللَّهِ شَيۡـٔٗاۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ١١٦

117. የዚያ በዚህች በቅርቢቱ ሕይወት የሚለግሱት ነገር ምሳሌ በውስጧ ውርጭ ያለባት ነፋስ ነፍሶቻቸውን የበደሉን ሕዝቦች አዝመራ እንደነካችና እንዳጠፋችው ብጤ ነው፡፡ አላህም አልበደላቸውም ግን ነፍሶቻቸውን ይበድላሉ፡፡

مَثَلُ مَا يُنفِقُونَ فِي هَٰذِهِ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا كَمَثَلِ رِيحٖ فِيهَا صِرٌّ أَصَابَتۡ حَرۡثَ قَوۡمٖ ظَلَمُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ فَأَهۡلَكَتۡهُۚ وَمَا ظَلَمَهُمُ ٱللَّهُ وَلَٰكِنۡ أَنفُسَهُمۡ يَظۡلِمُونَ ١١٧

118. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከእናንተ ሌላ ምስጢረኛን አትያዙ፡፡ ማበላሸትን አይገቱላችሁም፡፡ ጉዳታችሁን ይወዳሉ፡፡ ጥላቻይቱ ከአፎቻቸው በእርግጥ ተገለጸች፡፡ ልቦቻቸውም የሚደብቁት ይበልጥ ትልቅ ነው፡፡ ልብ የምታደርጉ እንደኾናችሁ ለእናንተ ማብራሪያዎችን በእርግጥ ገለጽን፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّخِذُواْ بِطَانَةً مِّن دُونِكُمْ لَا يَأْلُونَكُمْ خَبَالًا وَدُّواْ مَا عَنِتُّمْ قَدْ بَدَتِ ٱلْبَغْضَآءُ مِنْ أَفْوَاهِهِمْ وَمَا تُخْفِي صُدُورُهُمْ أَكْبَرُ ۚ قَدْ بَيَّنَّا لَكُمُ ٱلْـَٔايَـٰتِ ۖ إِن كُنتُمْ تَعْقِلُونَ ﴿١١٨﴾

119. እነሆ እናንተ እነዚያ የምትወዱዋቸው ናችሁ፡፡ (እነሱ) ግን አይወዱዋችሁም፡፡ በመጽሐፉም በሁሉም ታምናላችሁ፡፡ ባገኙዋችሁም ጊዜ «አምነናል» ይላሉ፡፡ ባገለሉም ጊዜ ከቁጭታቸው የተነሳ በእናንተ ላይ ዐጽቆቻቸውን ይነክሳሉ፡፡ «በቁጭታችሁ ሙቱ፤ አላህ ልቦች የቋጠሩትን ዐዋቂ ነውና» በላቸው፡፡

هَـٰٓأَنتُمْ أُوْلَآءِ تُحِبُّونَهُمْ وَلَا يُحِبُّونَكُمْ وَتُؤْمِنُونَ بِٱلْكِتَـٰبِ كُلِّهِۦ وَإِذَا لَقُوكُمْ قَالُوٓاْ ءَامَنَّا وَإِذَا خَلَوْاْ عَضُّواْ عَلَيْكُمُ ٱلْأَنَامِلَ مِنَ ٱلْغَيْظِ ۚ قُلْ مُوتُواْ بِغَيْظِكُمْ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ﴿١١٩﴾

120. ደግ ነገር ብትነካችሁ ታስከፋቸዋለች፡፡ መጥፎም ነገር ብታገኛችሁ በእርሷ ይደሰታሉ፡፡ ብትታገሱና ብትጠነቀቁም ተንኮላቸው ምንም አይጎዳችሁም፡፡ አላህ በሚሠሩት ሁሉ (በዕውቀቱ) ከባቢ ነውና፡፡

إِن تَمْسَسْكُمْ حَسَنَةٌ تَسُؤْهُمْ وَإِن تُصِبْكُمْ سَيِّئَةٌ يَفْرَحُواْ بِهَا ۖ وَإِن تَصْبِرُواْ وَتَتَّقُواْ لَا يَضُرُّكُمْ كَيْدُهُمْ شَيْـًٔا ۗ إِنَّ ٱللَّهَ بِمَا يَعْمَلُونَ مُحِيطٌ ﴿١٢٠﴾

121. ለምእምኖቹም ለውጊያ ሥራዎችን የምታዘጋጅ ኾነህ ከቤተሰብህ በማለድክ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

وَإِذْ غَدَوْتَ مِنْ أَهْلِكَ تُبَوِّئُ ٱلْمُؤْمِنِينَ مَقَـٰعِدَ لِلْقِتَالِ ۗ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٌ ﴿١٢١﴾

122. ከእናንተ ሁለት ጭፍሮች አላህ ረዳታቸው ሲኾን ለመፍራት ባሰቡ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ በአላህም ላይ ብቻ ምእምናኖች ይመኩ፡፡

إِذْ هَمَّت طَّآئِفَتَانِ مِنكُمْ أَن تَفْشَلَا وَٱللَّهُ وَلِيُّهُمَا ۗ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلْيَتَوَكَّلِ ٱلْمُؤْمِنُونَ ﴿١٢٢﴾

123. በበድርም እናንተ ጥቂቶች ኾናችሁ ሳለ አላህ በእርግጥ ረዳችሁ፡፡ አላህንም ታመሰግኑ ዘንድ ፍሩት፡፡

وَلَقَدْ نَصَرَكُمُ ٱللَّهُ بِبَدْرٍ وَأَنتُمْ أَذِلَّةٌ ۖ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ لَعَلَّكُمْ تَشْكُرُونَ ﴿١٢٣﴾

124. ለምእምናን «ጌታችሁ በሦስት ሺህ መላእክት የተወረዱ ሲኾኑ ቢረዳችሁ አይበቃችሁምን» በምትል ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذْ تَقُولُ لِلْمُؤْمِنِينَ أَلَن يَكْفِيَكُمْ أَن يُمِدَّكُمْ رَبُّكُم بِثَلَـٰثَةِ ءَالَـٰفٍ مِّنَ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةِ مُنزَلِينَ ﴿١٢٤﴾

125. «አዎን ብትታገሱና ብትጠነቀቁ ከዚህም ፍጥነታቸው (ጠላቶቻችሁ) ቢመጡባችሁ ጌታችሁ ምልክት ባላቸው አምስት ሺህ መላእክት ይረዳችኋል፡፡ »

بَلَىٰٓ ۚ إِن تَصْبِرُواْ وَتَتَّقُواْ وَيَأْتُوكُم مِّن فَوْرِهِمْ هَـٰذَا يُمْدِدْكُمْ رَبُّكُم بِخَمْسَةِ ءَالَـٰفٍ مِّنَ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةِ مُسَوِّمِينَ ﴿١٢٥﴾

126. አላህም (እርዳታውን) ለእናንተ ብስራትና ልቦቻችሁ በእርሱ እንዲረኩ እንጂ አላደረገውም፡፡ ድልም መንሳት አሸናፊ ጥበበኛ ከኾነው አላህ ዘንድ እንጅ ከሌላ አይደለም፡፡

وَمَا جَعَلَهُ ٱللَّهُ إِلَّا بُشْرَىٰ لَكُمْ وَلِتَطْمَئِنَّ قُلُوبُكُم بِهِۦ ۗ وَمَا ٱلنَّصْرُ إِلَّا مِنْ عِندِ ٱللَّهِ ٱلْعَزِيزِ ٱلْحَكِيمِ ﴿١٢٦﴾

127. (ድልን ያጎናጸፋችሁ) ከእነዚያ ከካዱት ከፊልን ሊቆርጥ (ሊያጠፋ) ወይም ሊያዋርዳቸውና ያፈሩ ኾነው እንዲመለሱ ነው፡፡

لِيَقْطَعَ طَرَفًا مِّنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ أَوْ يَكْبِتَهُمْ فَيَنقَلِبُوا۟ خَآئِبِينَ ﴿١٢٧﴾

128. (አላህ) በእነርሱ ላይ ይቅርታ እስኪያደርግ ወይም እነርሱ በዳዮች ናቸውና እስኪቀጣቸው ድረስ ላንተ ከነገሩ ምንም የለህም፡፡

لَيْسَ لَكَ مِنَ ٱلْأَمْرِ شَىْءٌ أَوْ يَتُوبَ عَلَيْهِمْ أَوْ يُعَذِّبَهُمْ فَإِنَّهُمْ ظَٰلِمُونَ ﴿١٢٨﴾

129. በሰማያት ያለው በምድርም ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ ለሚሻው ሰው ይምራል፤ የሚሻውንም ሰው ይቀጣል፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۚ يَغْفِرُ لِمَن يَشَآءُ وَيُعَذِّبُ مَن يَشَآءُ ۚ وَٱللَّهُ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١٢٩﴾

130. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አራጣን የተነባበሩ እጥፎች ሲኾኑ አትብሉ፡፡ ትድኑም ዘንድ አላህን ፍሩ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ لَا تَأْكُلُوا۟ ٱلرِّبَوٰٓا۟ أَضْعَٰفًا مُّضَٰعَفَةً ۖ وَٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ لَعَلَّكُمْ تُفْلِحُونَ ﴿١٣٠﴾

131. ያችንም ለከሓዲዎች የተደገሰችውን እሳት ተጠንቀቁ፡፡

وَٱتَّقُوا۟ ٱلنَّارَ ٱلَّتِىٓ أُعِدَّتْ لِلْكَٰفِرِينَ ﴿١٣١﴾

132. ይታዘንላችሁም ዘንድ አላህንና መልክተኛውን ታዘዙ፡፡

وَأَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَٱلرَّسُولَ لَعَلَّكُمْ تُرْحَمُونَ ﴿١٣٢﴾

133. ከጌታችሁ ወደ ኾነችም ምሕረትና ስፋትዋ እንደ ሰማያትና ምድር ወደ ኾነች ገነት አላህን ለሚፈሩ የተዘጋጀች ስትኾን ተቻኮሉ፡፡

۞ وَسَارِعُوٓا۟ إِلَىٰ مَغْفِرَةٍ مِّن رَّبِّكُمْ وَجَنَّةٍ عَرْضُهَا ٱلسَّمَٰوَٰتُ وَٱلْأَرْضُ أُعِدَّتْ لِلْمُتَّقِينَ ﴿١٣٣﴾

134. ለእነዚያ በድሎትም ኾነ በችግር ለሚለግሱት፣ ቁጭትንም ገቺዎች ከሰዎችም ይቅርታ አድራጊዎች ለኾኑት (ተደግሳለች)፡፡ አላህም በጎ ሠሪዎችን ይወዳል፡፡

ٱلَّذِينَ يُنفِقُونَ فِى ٱلسَّرَّآءِ وَٱلضَّرَّآءِ وَٱلْكَٰظِمِينَ ٱلْغَيْظَ وَٱلْعَافِينَ عَنِ ٱلنَّاسِ ۗ وَٱللَّهُ يُحِبُّ ٱلْمُحْسِنِينَ ﴿١٣٤﴾

135. ለእነዚያም መጥፎ ሥራን በሠሩ ወይም ነፍሶቻቸውን በበደሉ ጊዜ አላህን የሚያስታውሱና ለኀጢአቶቻቸው ምሕረትን የሚለምኑ ለኾኑት ከአላህም ሌላ ኀጢአቶችን የሚምር አንድም የለ፡፡ (በስሕተት) በሠሩትም ላይ እነርሱ የሚያውቁ ሲኾኑ የማይዘወትሩ ለኾኑት (ተደግሳለች)፡፡

وَٱلَّذِينَ إِذَا فَعَلُوا۟ فَٰحِشَةً أَوْ ظَلَمُوٓا۟ أَنفُسَهُمْ ذَكَرُوا۟ ٱللَّهَ فَٱسْتَغْفَرُوا۟ لِذُنُوبِهِمْ وَمَن يَغْفِرُ ٱلذُّنُوبَ إِلَّا ٱللَّهُ وَلَمْ يُصِرُّوا۟ عَلَىٰ مَا فَعَلُوا۟ وَهُمْ يَعْلَمُونَ ﴿١٣٥﴾

136. እነዚያ ምንዳቸው ከጌታቸው ምሕረትና በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ በሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው ገነቶችም ናቸው፡፡ የሠሪዎችም ምንዳ (ገነት) ምንኛ አማረች!፡፡

أُو۟لَٰٓئِكَ جَزَآؤُهُم مَّغْفِرَةٌ مِّن رَّبِّهِمْ وَجَنَّٰتٌ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا ۚ وَنِعْمَ أَجْرُ ٱلْعَٰمِلِينَ ﴿١٣٦﴾

137. ከእናንተ በፊት ድርጊቶች በእርግጥ አልፈዋል፡፡ በምድርም ላይ ኺዱ፡፡ የአስተባባዮችም ፍጻሜ እንዴት እንደነበረ ተመልከቱ፡፡

138. ይህ ለሰዎች ገላጭ፣ ለጥንቁቆች መሪና ገሳጭ ነው፡፡

139. እናንተም የበላዮች ስትኾኑ ምእመናን እንደኾናችሁ አትስነፉ፤ አትዘኑም፡፡

140. ቁስል ቢያገኛችሁ ሰዎቹንም መሰሉ ቁስል አግኝቷቸዋል፡፡ ይኸችንም ቀናት በሰዎች መካከል እናዘዋውራታለን፡፡ (እንድትገሰጹና) አላህም እነዚያን ያመኑትን እንዲያውቅ (እንዲለይ) ከእናንተም ሰማዕታትን እንዲይዝ ነው፡፡ አላህም በዳዮችን አይወድም፡፡

141. አላህም እነዚያን ያመኑትን (ከኀጢአት) ሊያነጻና ከሓዲዎችንም ሊያጠፋ ነው፡፡

142. በእውነቱ አላህ ከናንተ እነዚያን የታገሉትን ሳያውቅ (ሳይለይ) ታጋሾቹንም ሳያውቅ ገነትን ልትገቡ አሰባችሁን

143. (በጦርነት ላይ) መሞትንም ሳታገኙት በፊት በርግጥ የምትመኙት ነበራችሁ፡፡ እናንተም የምትመለከቱ ስትኾኑ በርግጥ አያችሁት (ታዲያ ለምን ሸሻችሁ)

144. ሙሐመድም ከበፊቱ መልክተኞች በእርግጥ ያለፉ የኾነ መልክተኛ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡ ታዲያ ቢሞት ወይም ቢገደል ወደ ኋላችሁ ትገለበጣላችሁን ወደኋላው የሚገለበጥም ሰው አላህን ምንም አይጎዳም፡፡ አላህም አመስጋኞቹን በእርግጥ ይመነዳል፡፡

145. ለማንኛይቱም ነፍስ በአላህ ፍርድ ቢኾን እንጅ ልትሞት አይገባትም፡፡ (ጊዜውም) ተወስኖ ተጽፏል፡፡ የቅርቢቱንም ምንዳ የሚፈልግ ሰው ከእርስዋ እንሰጠዋለን፡፡ የመጨረሻይቱንም ምንዳ የሚፈልግ ሰው ከእርስዋ እንሰጠዋለን፤ አመስጋኞችንም በእርግጥ እንመነዳለን፡፡

146. ከነቢይም ብዙ ሊቃውንት ከርሱ ጋር ኾነው የተዋጉ ብዙ ናቸው፡፡ በአላህም መንገድ ለሚደርስባቸው ነገር አልፈሩም፤ አልደከሙምም፡፡ (ለጠላት) አልተዋረዱምም፡፡ አላህም ትዕግስተኞችን ይወዳል፡፡

قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِكُمۡ سُنَنٞ فَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَٱنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُكَذِّبِينَ ١٣٧

هَٰذَا بَيَانٞ لِّلنَّاسِ وَهُدٗى وَمَوۡعِظَةٞ لِّلۡمُتَّقِينَ ١٣٨

وَلَا تَهِنُواْ وَلَا تَحۡزَنُواْ وَأَنتُمُ ٱلۡأَعۡلَوۡنَ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ١٣٩

إِن يَمۡسَسۡكُمۡ قَرۡحٞ فَقَدۡ مَسَّ ٱلۡقَوۡمَ قَرۡحٞ مِّثۡلُهُۥۚ وَتِلۡكَ ٱلۡأَيَّامُ نُدَاوِلُهَا بَيۡنَ ٱلنَّاسِ وَلِيَعۡلَمَ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَيَتَّخِذَ مِنكُمۡ شُهَدَآءَۗ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٤٠

وَلِيُمَحِّصَ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَيَمۡحَقَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ١٤١

أَمۡ حَسِبۡتُمۡ أَن تَدۡخُلُواْ ٱلۡجَنَّةَ وَلَمَّا يَعۡلَمِ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ جَٰهَدُواْ مِنكُمۡ وَيَعۡلَمَ ٱلصَّٰبِرِينَ ١٤٢

وَلَقَدۡ كُنتُمۡ تَمَنَّوۡنَ ٱلۡمَوۡتَ مِن قَبۡلِ أَن تَلۡقَوۡهُ فَقَدۡ رَأَيۡتُمُوهُ وَأَنتُمۡ تَنظُرُونَ ١٤٣

وَمَا مُحَمَّدٌ إِلَّا رَسُولٞ قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِهِ ٱلرُّسُلُۚ أَفَإِيْن مَّاتَ أَوۡ قُتِلَ ٱنقَلَبۡتُمۡ عَلَىٰٓ أَعۡقَٰبِكُمۡۚ وَمَن يَنقَلِبۡ عَلَىٰ عَقِبَيۡهِ فَلَن يَضُرَّ ٱللَّهَ شَيۡـٔٗاۗ وَسَيَجۡزِي ٱللَّهُ ٱلشَّٰكِرِينَ ١٤٤

وَمَا كَانَ لِنَفۡسٍ أَن تَمُوتَ إِلَّا بِإِذۡنِ ٱللَّهِ كِتَٰبٗا مُّؤَجَّلٗاۗ وَمَن يُرِدۡ ثَوَابَ ٱلدُّنۡيَا نُؤۡتِهِۦ مِنۡهَا وَمَن يُرِدۡ ثَوَابَ ٱلۡأٓخِرَةِ نُؤۡتِهِۦ مِنۡهَاۚ وَسَنَجۡزِي ٱلشَّٰكِرِينَ ١٤٥

وَكَأَيِّن مِّن نَّبِيّٖ قَٰتَلَ مَعَهُۥ رِبِّيُّونَ كَثِيرٞ فَمَا وَهَنُواْ لِمَآ أَصَابَهُمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَمَا ضَعُفُواْ وَمَا ٱسۡتَكَانُواْۗ وَٱللَّهُ يُحِبُّ ٱلصَّٰبِرِينَ ١٤٦

147. ንግግራቸውም «ጌታችን ሆይ! ኃጢአቶቻችንንና በነገራችን ሁሉ ወሰን ማለፋችንን ለእኛ ማር፣ ይዞታችንንም አደላድል፣ በከሓዲዎችም ሕዝቦች ላይ እርዳን» ማለታቸው እንጅ ሌላ አልነበረም፡፡

وَمَا كَانَ قَوۡلَهُمۡ إِلَّآ أَن قَالُواْ رَبَّنَا ٱغۡفِرۡ لَنَا ذُنُوبَنَا وَإِسۡرَافَنَا فِيٓ أَمۡرِنَا وَثَبِّتۡ أَقۡدَامَنَا وَٱنصُرۡنَا عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ١٤٧

148. አላህም የቅርቢቱን ምንዳና የመጨረሻይቱን መልካም ምንዳ ሰጣቸው፡፡ አላህም በጎ አድራጊዎችን ይወዳል፡፡

فَـَٔاتَىٰهُمُ ٱللَّهُ ثَوَابَ ٱلدُّنۡيَا وَحُسۡنَ ثَوَابِ ٱلۡأٓخِرَةِۗ وَٱللَّهُ يُحِبُّ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٤٨

149. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እነዚያን የካዱትን ሰዎች ብትታዘዙ ወደ ኋላችሁ ይመልሱዋችኋል፡፡ ከሳሪዎች ኾናችሁም ትገለበጣላችሁ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِن تُطِيعُواْ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يَرُدُّوكُمۡ عَلَىٰٓ أَعۡقَٰبِكُمۡ فَتَنقَلِبُواْ خَٰسِرِينَ ١٤٩

150. (አይረዷችሁም)፤ ይልቁን አላህ ብቻ ረዳታችሁ ነው፡፡ እርሱም ከረዳቶች ሁሉ በላጭ ነው፡፡

بَلِ ٱللَّهُ مَوۡلَىٰكُمۡۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلنَّٰصِرِينَ ١٥٠

151. በእነዚያ በካዱት ሰዎች ልቦች ውስጥ አላህ በእርሱ አስረጅ ያላወረደበትን ነገር በአላህ በማጋራታቸው ምክንያት ፍርሃትን እንጥላለን፡፡ መኖሪያቸውም እሳት ናት፡፡ የበዳዮችም መኖሪያ ምን ትከፋ!

سَنُلۡقِي فِي قُلُوبِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱلرُّعۡبَ بِمَآ أَشۡرَكُواْ بِٱللَّهِ مَا لَمۡ يُنَزِّلۡ بِهِۦ سُلۡطَٰنٗاۖ وَمَأۡوَىٰهُمُ ٱلنَّارُۖ وَبِئۡسَ مَثۡوَى ٱلظَّٰلِمِينَ ١٥١

152. አላህም በፈቃዱ በምትጨፈጭፏቸው ጊዜ ኪዳኑን በእርግጥ አረጋገጠላችሁ፡፡ የምትወዱትንም ነገር ካሳያችሁ በኋላ በፈራችሁ በትዕዛዙም በተጨቃጨቃችሁና ባመጻችሁ ጊዜ (እርዳታውን ከለከላችሁ)፡፡ ከእናንተ ውስጥ ቅርቢቱን ዓለም የሚሻ አለ፡፡ ከእናንተም የመጨረሻይቱን ዓለም የሚሻ አልለ፡፡ ከዚያም ሊሞክራችሁ ከእነርሱ አዞራችሁ፡፡ በእርግጥም ከእናንተ ይቅርታ አደረገላችሁ፡፡ አላህም በምእምናን ላይ የችሮታ ባለቤት ነው፡፡

وَلَقَدۡ صَدَقَكُمُ ٱللَّهُ وَعۡدَهُۥٓ إِذۡ تَحُسُّونَهُم بِإِذۡنِهِۦۖ حَتَّىٰٓ إِذَا فَشِلۡتُمۡ وَتَنَٰزَعۡتُمۡ فِي ٱلۡأَمۡرِ وَعَصَيۡتُم مِّنۢ بَعۡدِ مَآ أَرَىٰكُم مَّا تُحِبُّونَۚ مِنكُم مَّن يُرِيدُ ٱلدُّنۡيَا وَمِنكُم مَّن يُرِيدُ ٱلۡأٓخِرَةَۚ ثُمَّ صَرَفَكُمۡ عَنۡهُمۡ لِيَبۡتَلِيَكُمۡۖ وَلَقَدۡ عَفَا عَنكُمۡۗ وَٱللَّهُ ذُو فَضۡلٍ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٥٢

153. መልክተኛው ከኋላችሁ የሚጠራችሁ ሲኾን ርቃችሁ በምትሸሹና በአንድም ላይ የማትዞሩ በኾናችሁ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ ባመለጣችሁና በደረሰባችሁም ነገር እንድታዝኑ በሐሳብ ላይ ሐሳብን መነዳችሁ፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

۞إِذۡ تُصۡعِدُونَ وَلَا تَلۡوُۥنَ عَلَىٰٓ أَحَدٖ وَٱلرَّسُولُ يَدۡعُوكُمۡ فِيٓ أُخۡرَىٰكُمۡ فَأَثَٰبَكُمۡ غَمَّۢا بِغَمّٖ لِّكَيۡلَا تَحۡزَنُواْ عَلَىٰ مَا فَاتَكُمۡ وَلَا مَآ أَصَٰبَكُمۡۗ وَٱللَّهُ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١٥٣

154. ከዚያም ከጭንቅ በኋላ ጸጥታን ከእናንተ ከፊሎችን የሚሸፍንን እንቅልፍ በእናንተ ላይ አወረደ፡፡ ከፊሎቹም ነፍሶቻቸው በእርግጥ አሳሰቧቸው፡፡ እውነት ያልኾነውን የመሃይምነትን መጠራጠር በአላህ ይጠራጠራሉ፤ «ከነገሩ ለእኛ ምንም የለንም» ይላሉ፡፡ «ነገሩ ሁሉም ለአላህ ነው» በላቸው፡፡ ለአንተ የማይገልጹትን በነፍሶቻቸው ውስጥ ይደብቃሉ፡፡ «ከነገሩ ለእኛ አንዳች በነበረን ኖሮ እዚህ ባልተገደልን ነበር» ይላሉ፡፡ «በቤታችሁ ውስጥ በኾናችሁም ኖሮ እነዚያ በእነርሱ ላይ መገደል የተጻፈባቸው ወደ መውደቂያቸው በወጡ ነበር» በላቸው፡፡ አላህ (ፍርዱን ሊፈጽምና) በደረቶቻችሁም ውስጥ ያለውን ሊፈትን በልቦቻችሁም ውስጥ ያለውን ነገር ሊገልጽ (ይህን ሠራ)፡፡ አላህም በደረቶች ውስጥ ያለን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

ثُمَّ أَنزَلَ عَلَيۡكُم مِّنۢ بَعۡدِ ٱلۡغَمِّ أَمَنَةٗ نُّعَاسٗا يَغۡشَىٰ طَآئِفَةٗ مِّنكُمۡۖ وَطَآئِفَةٞ قَدۡ أَهَمَّتۡهُمۡ أَنفُسُهُمۡ يَظُنُّونَ بِٱللَّهِ غَيۡرَ ٱلۡحَقِّ ظَنَّ ٱلۡجَٰهِلِيَّةِۖ يَقُولُونَ هَل لَّنَا مِنَ ٱلۡأَمۡرِ مِن شَيۡءٖۗ قُلۡ إِنَّ ٱلۡأَمۡرَ كُلَّهُۥ لِلَّهِۗ يُخۡفُونَ فِيٓ أَنفُسِهِم مَّا لَا يُبۡدُونَ لَكَۖ يَقُولُونَ لَوۡ كَانَ لَنَا مِنَ ٱلۡأَمۡرِ شَيۡءٞ مَّا قُتِلۡنَا هَٰهُنَاۗ قُل لَّوۡ كُنتُمۡ فِي بُيُوتِكُمۡ لَبَرَزَ ٱلَّذِينَ كُتِبَ عَلَيۡهِمُ ٱلۡقَتۡلُ إِلَىٰ مَضَاجِعِهِمۡۖ وَلِيَبۡتَلِيَ ٱللَّهُ مَا فِي صُدُورِكُمۡ وَلِيُمَحِّصَ مَا فِي قُلُوبِكُمۡۚ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ١٥٤

155. እነዚያ ሁለቱ ጭፍሮች በተገናኙ ቀን ከእናንተ የሸሹት ሰዎች በዚያ በሠሩት ከፊል ምክንያት ያሳሳታቸው ሰይጣን ነው፡፡ አላህም ከነሱ በእርግጥ ይቅር አለ፡፡ አላህ መሓሪ በቅጣት የማይቸኩል ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ تَوَلَّوۡاْ مِنكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡتَقَى ٱلۡجَمۡعَانِ إِنَّمَا ٱسۡتَزَلَّهُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ بِبَعۡضِ مَا كَسَبُواْۖ وَلَقَدۡ عَفَا ٱللَّهُ عَنۡهُمۡۗ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٌ حَلِيمٞ ١٥٥

156. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እንደነዚያ እንደ ካዱትና ስለ ወንድሞቻቸው በምድር ላይ በተጓዙ ወይም ዘማቾች በኾኑ ጊዜ «እኛ ዘንድ በነበሩ ኖሮ ባልሞቱም ባልተገደሉም ነበር» እንደሚሉት አትኹኑ፡፡ አላህ ይህንን በልቦቻቸው ውስጥ ጸጸት ያደርግባቸው ዘንድ (ይህንን አሉ)፡፡ አላህም ሕያው ያደርጋል፤ ይገድላልም፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَقَالُواْ لِإِخۡوَٰنِهِمۡ إِذَا ضَرَبُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ أَوۡ كَانُواْ غُزّٗى لَّوۡ كَانُواْ عِندَنَا مَا مَاتُواْ وَمَا قُتِلُواْ لِيَجۡعَلَ ٱللَّهُ ذَٰلِكَ حَسۡرَةٗ فِي قُلُوبِهِمۡۗ وَٱللَّهُ يُحۡيِۦ وَيُمِيتُۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ١٥٦

157. በአላህም መንገድ ብትገደሉ ወይም፤ ብትሞቱ ከአላህ የኾነው ምሕረትና እዝነት (እነርሱ) ከሚሰበስቡት ሀብት በእርግጥ በላጭ ነው፡፡

وَلَئِن قُتِلۡتُمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ أَوۡ مُتُّمۡ لَمَغۡفِرَةٞ مِّنَ ٱللَّهِ وَرَحۡمَةٌ خَيۡرٞ مِّمَّا يَجۡمَعُونَ ١٥٧

158. ብትሞቱም ወይም ብትገደሉ በእርግጥ ወደ አላህ ብቻ ትሰበሰባላችሁ፡፡

وَلَئِن مُّتُّمۡ أَوۡ قُتِلۡتُمۡ لَإِلَى ٱللَّهِ تُحۡشَرُونَ ١٥٨

159. ከአላህም በኾነች ችሮታ ለዘብክላቸው፡፡ ዐመለ መጥፎ ልበ ደረቅም በኾንክ ኖሮ ከዙሪያህ በተበተኑ ነበር፡፡ ከእነርሱም ይቅር በል፡፡ ለእነርሱም ምሕረትን ለምንላቸው፡፡ በነገሩም ሁሉ አማክራቸው፡፡ ቁርጥ ሐሳብም ባደረግህ ጊዜ በአላህ ላይ ተመካ፡፡ አላህ በርሱ ላይ ተመኪዎችን ይወዳልና፡፡

فَبِمَا رَحۡمَةٖ مِّنَ ٱللَّهِ لِنتَ لَهُمۡۖ وَلَوۡ كُنتَ فَظًّا غَلِيظَ ٱلۡقَلۡبِ لَٱنفَضُّواْ مِنۡ حَوۡلِكَۖ فَٱعۡفُ عَنۡهُمۡ وَٱسۡتَغۡفِرۡ لَهُمۡ وَشَاوِرۡهُمۡ فِي ٱلۡأَمۡرِۖ فَإِذَا عَزَمۡتَ فَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُتَوَكِّلِينَ ١٥٩

إِن يَنصُرۡكُمُ ٱللَّهُ فَلَا غَالِبَ لَكُمۡۖ وَإِن يَخۡذُلۡكُمۡ فَمَن ذَا ٱلَّذِي يَنصُرُكُم مِّنۢ بَعۡدِهِۦۗ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلۡيَتَوَكَّلِ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ١٦٠

160. አላህ ቢረዳችሁ ለእናንተ አሸናፊ የለም፡፡ ቢያዋርዳችሁም ያ ከርሱ (ማዋረድ) በኋላ የሚረዳችሁ ማነው በአላህም ላይ ብቻ ምእምናን ይመኩ፡፡

وَمَا كَانَ لِنَبِيٍّ أَن يَغُلَّۚ وَمَن يَغۡلُلۡ يَأۡتِ بِمَا غَلَّ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ ثُمَّ تُوَفَّىٰ كُلُّ نَفۡسٖ مَّا كَسَبَتۡ وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ١٦١

161. ለነቢይም ስለባን መደበቅ አይገባውም፡፡ ስለባንም የሚደብቅ ሰው በትንሣኤ ቀን በደበቀው ነገር (ተሸክሞ) ይመጣል፡፡ ከዚያም ነፍስ ሁሉ የሥራዋን ዋጋ ትሞላለች፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

أَفَمَنِ ٱتَّبَعَ رِضۡوَٰنَ ٱللَّهِ كَمَنۢ بَآءَ بِسَخَطٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَمَأۡوَىٰهُ جَهَنَّمُۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ١٦٢

162. የአላህን ውዴታ የተከተለ ሰው ከአላህ በኾነ ቁጣ እንደ ተመለሰና መኖሪያው ገሀነም እንደ ኾነ ሰው ነውን መመለሻውም ምን ይከፋ!

هُمۡ دَرَجَٰتٌ عِندَ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِمَا يَعۡمَلُونَ ١٦٣

163. እነርሱ አላህ ዘንድ ባለ ደረጃዎች ናቸው፡፡ አላህም የሚሠሩትን ነገር ተመልካች ነው፡፡

لَقَدۡ مَنَّ ٱللَّهُ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ إِذۡ بَعَثَ فِيهِمۡ رَسُولٗا مِّنۡ أَنفُسِهِمۡ يَتۡلُواْ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتِهِۦ وَيُزَكِّيهِمۡ وَيُعَلِّمُهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحِكۡمَةَ وَإِن كَانُواْ مِن قَبۡلُ لَفِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ١٦٤

164. አላህ በምእምናን ላይ ከነሳቸው የኾነን፣ በእነርሱ ላይ አንቀጾቹን የሚያነብ፣ የሚጠራቸውም፣ መጽሐፍንና ጥበብን የሚያስተምራቸውም የኾነን መልእክተኛ በውስጣቸው በላከ ጊዜ፣ በእርግጥ ለገሰላቸው፡፡ እነርሱም ከዚያ በፊት በግልጽ ስህተት ውስጥ ነበሩ፡፡

أَوَلَمَّآ أَصَٰبَتۡكُم مُّصِيبَةٞ قَدۡ أَصَبۡتُم مِّثۡلَيۡهَا قُلۡتُمۡ أَنَّىٰ هَٰذَاۖ قُلۡ هُوَ مِنۡ عِندِ أَنفُسِكُمۡۗ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ١٦٥

165. ሁለት ብጤዎችዋን በእርግጥ ያገኛችሁ የኾነች መከራ (መጠቃት) ባገኘቻችሁ ጊዜ «ይህ ከየት ነው» አላችሁን «እርሱ ከነፍሶቻችሁ ዘንድ ነው፡፡» አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና በላቸው፡፡

وَمَآ أَصَٰبَكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡتَقَى ٱلۡجَمۡعَانِ فَبِإِذۡنِ ٱللَّهِ وَلِيَعۡلَمَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٦٦

166. ሁለቱ ጭፍሮችም በተጋጠሙ ቀን የደረሰባችሁ በአላህ ፈቃድ ነው፡፡ ምእምናንንም (ሊፈትንና) ሊገልጽ ነው፡፡

وَلِيَعۡلَمَ ٱلَّذِينَ نَافَقُواْۚ وَقِيلَ لَهُمۡ تَعَالَوۡاْ قَٰتِلُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ أَوِ ٱدۡفَعُواْۖ قَالُواْ لَوۡ نَعۡلَمُ قِتَالٗا لَّٱتَّبَعۡنَٰكُمۡۗ هُمۡ لِلۡكُفۡرِ يَوۡمَئِذٍ أَقۡرَبُ مِنۡهُمۡ لِلۡإِيمَٰنِۚ يَقُولُونَ بِأَفۡوَٰهِهِم مَّا لَيۡسَ فِي قُلُوبِهِمۡۚ وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا يَكۡتُمُونَ ١٦٧

167. እነዚያንም የነፈቁትንና ለነርሱ «ኑ፤ በአላህ መንገድ ተጋደሉ፤ ወይም ተከላከሉ፤» የተባሉትን ሊገልጽ ነው፡፡ «መዋጋት (መኖሩን) ብናውቅ ኖሮ በተከተልናችሁ ነበር» አሉ፡፡ እነርሱ ያን ጊዜ ከእምነት ይልቅ ወደ ክህደት የቀረቡ ናቸው፡፡ በልቦቻቸው የሌለውን በአፎቻቸው ይናገራሉ፡፡ አላህም የሚደብቁትን ዐዋቂ ነው፡፡

ٱلَّذِينَ قَالُواْ لِإِخۡوَٰنِهِمۡ وَقَعَدُواْ لَوۡ أَطَاعُونَا مَا قُتِلُواْۗ قُلۡ فَٱدۡرَءُواْ عَنۡ أَنفُسِكُمُ ٱلۡمَوۡتَ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ١٦٨

168. እነዚያ (ከትግል) የቀሩ ሲኾኑ ለወንድሞቻቸው፡- «በታዘዙን ኖሮ ባልተገደሉ ነበር» ያሉ ናቸው፡፡ «እውነተኞች እንደኾናችሁ ከነፍሶቻችሁ ላይ ሞትን ገፍትሩ» በላቸው፡፡

169. እነዚያን በአላህ መንገድ የተገደሉትን ሙታን አድርገህ አትገምታቸው:: በእርግጥ እነርሱ እጌታቸው ዘንድ ሕያዋን ናቸው፤ ይመገባሉ::

وَلَا تَحۡسَبَنَّ ٱلَّذِينَ قُتِلُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ أَمۡوَٰتَۢاۚ بَلۡ أَحۡيَآءٌ عِندَ رَبِّهِمۡ يُرۡزَقُونَ ١٦٩

170. አላህ ከችሮታው በሰጣቸው ነገር ተደሳቾች ሲኾኑ (ይመገባሉ):: በነዚያም ከኋላቸው ገና በእነርሱ ባልተከተሉት በእነርሱ ላይ ፍርሃት ባለመኖሩና እነርሱም የማያዝኑ በመኾናቸው ይደሰታሉ::

فَرِحِينَ بِمَآ ءَاتَىٰهُمُ ٱللَّهُ مِن فَضۡلِهِۦ وَيَسۡتَبۡشِرُونَ بِٱلَّذِينَ لَمۡ يَلۡحَقُواْ بِهِم مِّنۡ خَلۡفِهِمۡ أَلَّا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ١٧٠

171. ከአላህ በኾነ ጸጋና ልግስና አላህም የምእምናንን ምንዳ የማያጠፉ በመኾኑ ይደሰታሉ::

۞يَسۡتَبۡشِرُونَ بِنِعۡمَةٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَفَضۡلٖ وَأَنَّ ٱللَّهَ لَا يُضِيعُ أَجۡرَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٧١

172. እነዚያ መቁሰል ካገኛቸው በኋላ ለአላህና ለመልክተኛው የታዘዙት ከእነሱ ለነዚያ በጎ ለሠሩትና ለተጠነቀቁት ታላቅ ምንዳ አላቸው::

ٱلَّذِينَ ٱسۡتَجَابُواْ لِلَّهِ وَٱلرَّسُولِ مِنۢ بَعۡدِ مَآ أَصَابَهُمُ ٱلۡقَرۡحُۚ لِلَّذِينَ أَحۡسَنُواْ مِنۡهُمۡ وَٱتَّقَوۡاْ أَجۡرٌ عَظِيمٌ ١٧٢

173. እነዚያ ሰዎቹ ለእነርሱ:- «ሰዎች ለእናንተ (ጦርን) አከማችተዋልና ፍሩዋቸው» ይሉዋቸውና (ይህም) እምነትን የጨመረላቸው «በቂያችንም አላህ ነው ምን ያምርም መጠጊያ!» ያሉ ናቸው::

ٱلَّذِينَ قَالَ لَهُمُ ٱلنَّاسُ إِنَّ ٱلنَّاسَ قَدۡ جَمَعُواْ لَكُمۡ فَٱخۡشَوۡهُمۡ فَزَادَهُمۡ إِيمَٰنٗا وَقَالُواْ حَسۡبُنَا ٱللَّهُ وَنِعۡمَ ٱلۡوَكِيلُ ١٧٣

174. ከአላህም በኾነ ጸጋና ችሮታ ክፉ ነገር ያልነካቸው ኾነው ተመለሱ:: የአላህንም ውዴታ ተከተሉ፤ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው::

فَٱنقَلَبُواْ بِنِعۡمَةٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَفَضۡلٖ لَّمۡ يَمۡسَسۡهُمۡ سُوٓءٞ وَٱتَّبَعُواْ رِضۡوَٰنَ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ ذُو فَضۡلٍ عَظِيمٍ ١٧٤

175. እንዲህ የሚላችሁ ሰይጣን ብቻ ነው:: ወዳጆቹን ያስፈራራችኋል:: አትፍሩዋቸውም:: ምእምናንም እንደኾናችሁ ፍሩኝ::

إِنَّمَا ذَٰلِكُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ يُخَوِّفُ أَوۡلِيَآءَهُۥ فَلَا تَخَافُوهُمۡ وَخَافُونِ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ١٧٥

176. እነዚያም በክህደት የሚቻኮሉት አያሳዝኑህ:: ከነርሱ ፈጽሞ አላህን በምንም አይጎዱምና:: አላህ በመጨረሻይቱ ዓለም ለእነሱ ዕድልን ላያደርግ ይሻል:: ለእነርሱም ታላቅ ቅጣት አላቸው::

وَلَا يَحۡزُنكَ ٱلَّذِينَ يُسَٰرِعُونَ فِي ٱلۡكُفۡرِۚ إِنَّهُمۡ لَن يَضُرُّواْ ٱللَّهَ شَيۡـٔٗاۗ يُرِيدُ ٱللَّهُ أَلَّا يَجۡعَلَ لَهُمۡ حَظّٗا فِي ٱلۡأٓخِرَةِۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٌ ١٧٦

177. እነዚያ ክህደትን በእምነት የለወጡ አላህን በምንም ነገር ፈጽሞ አይጎዱትም:: ለእነሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው::

إِنَّ ٱلَّذِينَ ٱشۡتَرَوُاْ ٱلۡكُفۡرَ بِٱلۡإِيمَٰنِ لَن يَضُرُّواْ ٱللَّهَ شَيۡـٔٗاۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ١٧٧

178. እነዚያ የካዱት ሰዎች እነርሱን ማዘግየታችንን ለነፍሶቻቸው ደግ ነገር ነው ብለው አያስቡ:: እነርሱን የምናዘገያቸው ኃጢአትን እንዲጨምሩ ብቻ ነው:: ለነሱም አዋራጅ ስቃይ አላቸው::

وَلَا يَحۡسَبَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَنَّمَا نُمۡلِي لَهُمۡ خَيۡرٞ لِّأَنفُسِهِمۡۚ إِنَّمَا نُمۡلِي لَهُمۡ لِيَزۡدَادُوٓاْ إِثۡمٗاۚ وَلَهُمۡ عَذَابٞ مُّهِينٞ ١٧٨

122. እነዚያም ያመኑና በጎ ሥራዎችን የሠሩ በሥራቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች ዘላለም በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ እናገባቸዋለን፡፡ አላህ እውነተኛን ተስፋ ሰጣቸው፡፡ በንግግርም ከአላህ ይበልጥ እውነተኛ ማን ነው

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ سَنُدۡخِلُهُمۡ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۖ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٗاۚ وَمَنۡ أَصۡدَقُ مِنَ ٱللَّهِ قِيلٗا ١٢٢

123. (ነገሩ) በምኞታችሁና በመጽሐፉ ሰዎች ምኞት አይደለም፡፡ መጥፎን የሚሠራ ሰው በእርሱ ይቀጣል፡፡ ለእርሱም ከአላህ ሌላ ጠባቂንም ረዳትንም አያገኝም፡፡

لَّيۡسَ بِأَمَانِيِّكُمۡ وَلَآ أَمَانِيِّ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِۗ مَن يَعۡمَلۡ سُوٓءٗا يُجۡزَ بِهِۦ وَلَا يَجِدۡ لَهُۥ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَلِيّٗا وَلَا نَصِيرٗا ١٢٣

124. ከወንድ ወይም ከሴት እርሱ አማኝ ኾኖ ከበጎ ሥራዎች አንዳችን የሚሠራም ሰው እነዚያ ገነትን ይገባሉ፡፡ በተምር ፍሬ ላይ ያለችን ነጥብ ያክል እንኳ አይበደሉም፡፡

وَمَن يَعۡمَلۡ مِنَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ مِن ذَكَرٍ أَوۡ أُنثَىٰ وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَأُوْلَٰٓئِكَ يَدۡخُلُونَ ٱلۡجَنَّةَ وَلَا يُظۡلَمُونَ نَقِيرٗا ١٢٤

125. እርሱ መልካም ሠሪ ኾኖ ፊቱን ለአላህ ከሰጠና የኢብራሂምንም መንገድ ቀጥተኛ ሲኾን ከተከተለ ሰው ይበልጥ ሃይማኖቱ ያማረ ማን ነው አላህም ኢብራሂምን ፍጹም ወዳጅ አድርጎ ያዘው፡፡

وَمَنۡ أَحۡسَنُ دِينٗا مِّمَّنۡ أَسۡلَمَ وَجۡهَهُۥ لِلَّهِ وَهُوَ مُحۡسِنٞ وَٱتَّبَعَ مِلَّةَ إِبۡرَٰهِيمَ حَنِيفٗاۗ وَٱتَّخَذَ ٱللَّهُ إِبۡرَٰهِيمَ خَلِيلٗا ١٢٥

126. በሰማያት ያለውና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ በዕውቀት ከባቢ ነው፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٖ مُّحِيطٗا ١٢٦

127. በሴቶችም ነገር ያስተቹሃል፡፡ አላህ በእነርሱ ይነግራችኋል፡፡ ያም በመጽሐፉ በእናንተ ላይ የሚነበበው በእነዚያ ለእነርሱ (ከውርስ) የተጻፈላቸውን በማትሰጧቸውና ልታገቧቸው በማትፈልጉት የቲሞች ሴቶች (ይህንን እንዳታደርጉ) ከሕፃናትም ለኾኑት ደካሞች መብታቸውን እንድትሰጡ ለየቲሞችም በትክክል እንድትቆሙ (ይነግራችኋል) በላቸው፡፡ ከበጎም ሥራ ማናቸውንም ብትሠሩ አላህ እርሱን ዐዋቂ ነው፡፡

وَيَسۡتَفۡتُونَكَ فِي ٱلنِّسَآءِۖ قُلِ ٱللَّهُ يُفۡتِيكُمۡ فِيهِنَّ وَمَا يُتۡلَىٰ عَلَيۡكُمۡ فِي ٱلۡكِتَٰبِ فِي يَتَٰمَى ٱلنِّسَآءِ ٱلَّٰتِي لَا تُؤۡتُونَهُنَّ مَا كُتِبَ لَهُنَّ وَتَرۡغَبُونَ أَن تَنكِحُوهُنَّ وَٱلۡمُسۡتَضۡعَفِينَ مِنَ ٱلۡوِلۡدَٰنِ وَأَن تَقُومُواْ لِلۡيَتَٰمَىٰ بِٱلۡقِسۡطِۚ وَمَا تَفۡعَلُواْ مِنۡ خَيۡرٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِهِۦ عَلِيمٗا ١٢٧

128. ሴትም ከባልዋ ጥላቻን ወይም ፊቱን ማዞርን ብታውቅ በመካከላቸው መስማማትን ቢስማሙ በሁለቱ ላይ ኀጢአት የለም፡፡ መታረቅም መልካም ነው፡፡ ነፍሶችም ንፍገት ተጣለባቸው፡፡ መልካምም ብትሠሩ ብትጠነቀቁም አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

وَإِنِ ٱمۡرَأَةٌ خَافَتۡ مِنۢ بَعۡلِهَا نُشُوزًا أَوۡ إِعۡرَاضٗا فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡهِمَآ أَن يُصۡلِحَا بَيۡنَهُمَا صُلۡحٗاۚ وَٱلصُّلۡحُ خَيۡرٞۗ وَأُحۡضِرَتِ ٱلۡأَنفُسُ ٱلشُّحَّۚ وَإِن تُحۡسِنُواْ وَتَتَّقُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِمَا تَعۡمَلُونَ خَبِيرٗا ١٢٨

129. በሴቶችም መካከል ምንም እንኳ ብትጓጉ (በፍቅር) ለማስተካከል አትችሉም፡፡ እንደ ተንጠለጠለችም አድርጋችሁ ትተዋት ዘንድ (ወደምትወዱት) መዘንበልን ሁሉ አትዘንበሉ፡፡ ብታበጁም ብትጠነቀቁም አላህ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلَن تَسۡتَطِيعُوٓاْ أَن تَعۡدِلُواْ بَيۡنَ ٱلنِّسَآءِ وَلَوۡ حَرَصۡتُمۡۖ فَلَا تَمِيلُواْ كُلَّ ٱلۡمَيۡلِ فَتَذَرُوهَا كَٱلۡمُعَلَّقَةِۚ وَإِن تُصۡلِحُواْ وَتَتَّقُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ١٢٩

130. ቢለያዩም አላህ ሁሉንም በችሮታው ያብቃቃቸዋል፡፡ አላህም ችሮታው ሰፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَإِن يَتَفَرَّقَا يُغْنِ ٱللَّهُ كُلًّا مِّن سَعَتِهِۦۚ وَكَانَ ٱللَّهُ وَٰسِعًا حَكِيمًا ﴿١٣٠﴾

131. በሰማያት ያለውና በምድርም ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ እነዚያንም ከበፊታችሁ መጽሐፍን የተሰጡትን እናንተንም አላህን ፍሩ በማለት በእርግጥ አዘዝን፡፡ ብትክዱም በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ (አትጐዱትም)፡፡ አላህም ተብቃቂ ምስጉን ነው፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِۗ وَلَقَدْ وَصَّيْنَا ٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ ٱلْكِتَٰبَ مِن قَبْلِكُمْ وَإِيَّاكُمْ أَنِ ٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَۚ وَإِن تَكْفُرُوا۟ فَإِنَّ لِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ غَنِيًّا حَمِيدًا ﴿١٣١﴾

132. በሰማያት ያለውና በምድርም ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ መመኪያም በአላህ በቃ፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِۚ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ وَكِيلًا ﴿١٣٢﴾

133. ሰዎች ሆይ!(አላህ) ቢሻ ያስወግዳችኋል፡፡ ሌሎችንም ያመጣል፡፡ አላህም በዚህ ላይ ቻይ ነው፡፡

إِن يَشَأْ يُذْهِبْكُمْ أَيُّهَا ٱلنَّاسُ وَيَأْتِ بِـَٔاخَرِينَۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلَىٰ ذَٰلِكَ قَدِيرًا ﴿١٣٣﴾

134. የቅርቢቱን ዓለም ምንዳ የሚፈልግ የኾነ ሰው አላህ ዘንድ የቅርቢቱና የመጨረሻይቱ ምንዳ አልለ፡፡ አላህም ሰሚ ተመልካች ነው፡፡

مَّن كَانَ يُرِيدُ ثَوَابَ ٱلدُّنْيَا فَعِندَ ٱللَّهِ ثَوَابُ ٱلدُّنْيَا وَٱلْـَٔاخِرَةِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ سَمِيعًۢا بَصِيرًا ﴿١٣٤﴾

135. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በትክክል (ፍትሕ) ቀዋሚዎች በነፈሶቻችሁ ወይም በወላጆችና በቅርብ ዘመዶች ላይ ቢኾንም እንኳ ለአላህ መስካሪዎች ኹኑ፡፡ ሀብታም ወይም ድኻ ቢኾን አላህ በእነርሱ (ከእናንተ) ይበልጥ ተገቢ ነው፡፡ እንዳታደሉም ዝንባሌን አትከተሉ፡፡ ብታጠምሙም ወይም (መመስከርን) ብትተው አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

۞ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ كُونُوا۟ قَوَّٰمِينَ بِٱلْقِسْطِ شُهَدَآءَ لِلَّهِ وَلَوْ عَلَىٰٓ أَنفُسِكُمْ أَوِ ٱلْوَٰلِدَيْنِ وَٱلْأَقْرَبِينَۚ إِن يَكُنْ غَنِيًّا أَوْ فَقِيرًا فَٱللَّهُ أَوْلَىٰ بِهِمَاۖ فَلَا تَتَّبِعُوا۟ ٱلْهَوَىٰٓ أَن تَعْدِلُوا۟ۚ وَإِن تَلْوُۥٓا۟ أَوْ تُعْرِضُوا۟ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرًا ﴿١٣٥﴾

136. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በአላህና በመልክተኛው በዚያም በመልክተኛው ላይ ባወረደው መጽሐፍ በዚያም ከበፊቱ ባወረደው መጽሐፍ እመኑ፡፡ በአላህና በመላእክቱም፣ በመጽሐፎቹም፣ በመልክተኞቹም፣ በመጨረሻውም ቀን፣ የካደ ሰው (ከእውነት) የራቀን መሳሳት በእርግጥ ተሳሳተ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ ءَامِنُوا۟ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَٱلْكِتَٰبِ ٱلَّذِى نَزَّلَ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ وَٱلْكِتَٰبِ ٱلَّذِىٓ أَنزَلَ مِن قَبْلُۚ وَمَن يَكْفُرْ بِٱللَّهِ وَمَلَٰٓئِكَتِهِۦ وَكُتُبِهِۦ وَرُسُلِهِۦ وَٱلْيَوْمِ ٱلْـَٔاخِرِ فَقَدْ ضَلَّ ضَلَٰلًۢا بَعِيدًا ﴿١٣٦﴾

137. እነዚያ (በሙሳ) ያመኑና ከዚያም (ወይፈንን በመገዛት) የካዱ ከዚያም (በእርሱ) ያመኑ ከዚያም (በዒሳ) የካዱ ከዚያም (በሙሐመድ) ክሕደትን የጨመሩ አላህ ለእነሱ የሚምራቸውና ቅኑን መንገድ የሚመራቸው አይደለም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ثُمَّ كَفَرُوا۟ ثُمَّ ءَامَنُوا۟ ثُمَّ كَفَرُوا۟ ثُمَّ ٱزْدَادُوا۟ كُفْرًا لَّمْ يَكُنِ ٱللَّهُ لِيَغْفِرَ لَهُمْ وَلَا لِيَهْدِيَهُمْ سَبِيلًۢا ﴿١٣٧﴾

138. መናፍቃንን ለእነርሱ አሳማሚ ቅጣት ያላቸው መኾኑን አብስራቸው፡፡

بَشِّرِ ٱلْمُنَٰفِقِينَ بِأَنَّ لَهُمْ عَذَابًا أَلِيمًا ﴿١٣٨﴾

139. እነዚያ ከምእምናን ሌላ ከሓዲዎችን ወዳጆች አድርገው የሚይዙ እነሱ ዘንድ ልቅናን ይፈልጋሉን ልቅናውም ሁሉ ለአላህ ብቻ ነው።

ٱلَّذِينَ يَتَّخِذُونَ ٱلۡكَٰفِرِينَ أَوۡلِيَآءَ مِن دُونِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۚ أَيَبۡتَغُونَ عِندَهُمُ ٱلۡعِزَّةَ فَإِنَّ ٱلۡعِزَّةَ لِلَّهِ جَمِيعٗا ١٣٩

140. በእናንተም ላይ በመጽሐፉ ውስጥ የአላህን አንቀጾች በርሷ ሲካድባትና በርሷም ሲላገጥባት በሰማችሁ ጊዜ በሌላ ወሬ ውስጥ እስከሚገቡ ድረስ ከእነሱ ጋር አትቀመጡ፡፡ ማለትን በእርግጥ አወረደ፡፡ እናንተ ያንጊዜ ብጤያቸው ናችሁና፡፡ አላህ መናፍቃንን እና ከሓዲዎችን በሙሉ በገሀነም ውስጥ ሰብሳቢ ነውና፡፡

وَقَدۡ نَزَّلَ عَلَيۡكُمۡ فِي ٱلۡكِتَٰبِ أَنۡ إِذَا سَمِعۡتُمۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ يُكۡفَرُ بِهَا وَيُسۡتَهۡزَأُ بِهَا فَلَا تَقۡعُدُواْ مَعَهُمۡ حَتَّىٰ يَخُوضُواْ فِي حَدِيثٍ غَيۡرِهِۦٓ إِنَّكُمۡ إِذٗا مِّثۡلُهُمۡۗ إِنَّ ٱللَّهَ جَامِعُ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ وَٱلۡكَٰفِرِينَ فِي جَهَنَّمَ جَمِيعًا ١٤٠

141. እነዚያ በእናንተ (የጊዜን መዘዋወር) የሚጠባበቁ ናቸው፡፡ ለእናንተም ከአላህ የኾነ አሸናፊነት «ቢኖራችሁ ከእናንተ ጋር አልነበርንምን» ይላሉ፡፡ ለከሓዲዎችም ዕድል ቢኖር «(ከአሁን በፊት) በእናንተ ላይ አልተሾምንምን (እና አልተውናችሁምን) ከምእምናንም (አደጋ) አልከለከልናችሁምን» ይላሉ፡፡ አላህም በትንሣኤ ቀን በመካከላችሁ ይፈርዳል፡፡ አላህም ለከሓዲዎች በምእምናን ላይ መንገድን በፍጹም አያደርግም፡፡

ٱلَّذِينَ يَتَرَبَّصُونَ بِكُمۡ فَإِن كَانَ لَكُمۡ فَتۡحٞ مِّنَ ٱللَّهِ قَالُوٓاْ أَلَمۡ نَكُن مَّعَكُمۡ وَإِن كَانَ لِلۡكَٰفِرِينَ نَصِيبٞ قَالُوٓاْ أَلَمۡ نَسۡتَحۡوِذۡ عَلَيۡكُمۡ وَنَمۡنَعۡكُم مِّنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۚ فَٱللَّهُ يَحۡكُمُ بَيۡنَكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۗ وَلَن يَجۡعَلَ ٱللَّهُ لِلۡكَٰفِرِينَ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ سَبِيلًا ١٤١

142. መናፍቃን አላህን ያታልላሉ፡፡ እርሱም አታላያቸው ነው፡፡ (ይቀጣቸዋል)፡፡ ወደ ሶላትም በቆሙ ጊዜ ታካቾች ስዎችን የሚያሳዩ ኾነው ይቆማሉ፡፡ አላህንም ጥቂትን እንጅ አያወሱም፡፡

إِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ يُخَٰدِعُونَ ٱللَّهَ وَهُوَ خَٰدِعُهُمۡ وَإِذَا قَامُوٓاْ إِلَى ٱلصَّلَوٰةِ قَامُواْ كُسَالَىٰ يُرَآءُونَ ٱلنَّاسَ وَلَا يَذۡكُرُونَ ٱللَّهَ إِلَّا قَلِيلٗا ١٤٢

143. በዚህ መካከል ወላዋዮች ኾነው (ያሳያሉ)፡፡ ወደእነዚህም ወደእነዚያም አይደሉም፡፡ አላህም ያሳሳተውን ሰው ለእርሱ (የቅንነት) መንገድን በፍፁም አታገኝለትም፡፡

مُّذَبۡذَبِينَ بَيۡنَ ذَٰلِكَ لَآ إِلَىٰ هَٰٓؤُلَآءِ وَلَآ إِلَىٰ هَٰٓؤُلَآءِۚ وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَلَن تَجِدَ لَهُۥ سَبِيلٗا ١٤٣

144. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከምእምናን ሌላ ከሓዲዎችን ወዳጆች አድርጋችሁ አትያዙ፤ ለአላህ በናንተ ላይ ግልጽ ማስረጃዎችን ልታደርጉ ትፈልጋላችሁን

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّخِذُواْ ٱلۡكَٰفِرِينَ أَوۡلِيَآءَ مِن دُونِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۚ أَتُرِيدُونَ أَن تَجۡعَلُواْ لِلَّهِ عَلَيۡكُمۡ سُلۡطَٰنٗا مُّبِينًا ١٤٤

145. መናፍቃን በእርግጥ ከእሳት በታችኛው አዘቅት ውስጥ ናቸው፡፡ ለእነሱም ረዳትን አታገኝላቸውም፡፡

إِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ فِي ٱلدَّرۡكِ ٱلۡأَسۡفَلِ مِنَ ٱلنَّارِ وَلَن تَجِدَ لَهُمۡ نَصِيرًا ١٤٥

146. እነዚያ የተመለሱ (ሥራቸውን) ያሳመሩም፣ በአላህም የተጠበቁ፣ ሃይማኖታቸውንም ለአላህ ፍጹም ያደረጉ ሲቀሩ፡፡ እነዚያስ ከምእምናን ጋር ናቸው፡፡ ለምእምናንም አላህ ታላቅን ምንዳ በእርግጥ ይሰጣል፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ تَابُواْ وَأَصۡلَحُواْ وَٱعۡتَصَمُواْ بِٱللَّهِ وَأَخۡلَصُواْ دِينَهُمۡ لِلَّهِ فَأُوْلَٰٓئِكَ مَعَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۖ وَسَوۡفَ يُؤۡتِ ٱللَّهُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ أَجۡرًا عَظِيمٗا ﴿١٤٦﴾

147. ብታመሰግኑና ብታምኑ አላህ እናንተን በመቅጣት ምን ያደርጋል አላህም ወረታን መላሽ ዐዋቂ ነው፡፡

مَّا يَفۡعَلُ ٱللَّهُ بِعَذَابِكُمۡ إِن شَكَرۡتُمۡ وَءَامَنتُمۡۚ وَكَانَ ٱللَّهُ شَاكِرًا عَلِيمٗا ﴿١٤٧﴾

148. አላህ ከንግግር በክፉው መጮህን ከተበደለ ሰው (ጩኸት) በቀር አይወድም፡፡ አላህ ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

۞لَّا يُحِبُّ ٱللَّهُ ٱلۡجَهۡرَ بِٱلسُّوٓءِ مِنَ ٱلۡقَوۡلِ إِلَّا مَن ظُلِمَۚ وَكَانَ ٱللَّهُ سَمِيعًا عَلِيمًا ﴿١٤٨﴾

149. ደግ ነገርን ብትገልጹ ወይም ብትደብቁት ወይም ከመጥፎ ነገር (ከበደል) ይቅርታ ብታደርጉ አላህ ይቅር ባይ ቻያል ነው፡፡

إِن تُبۡدُواْ خَيۡرًا أَوۡ تُخۡفُوهُ أَوۡ تَعۡفُواْ عَن سُوٓءٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ عَفُوّٗا قَدِيرًا ﴿١٤٩﴾

150. እነዚያ በአላህና በመልክተኞቹ የሚክዱ፣ በአላህና በመልክተኞቹም መካከል መለየትን የሚፈልጉ፣ «በከፊሉም እናምናለን በከፊሉም እንክዳለን» የሚሉ፣ በዚህም መካከል መንገድን ሊይዙ የሚፈልጉ፤

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡفُرُونَ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦ وَيُرِيدُونَ أَن يُفَرِّقُواْ بَيۡنَ ٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦ وَيَقُولُونَ نُؤۡمِنُ بِبَعۡضٖ وَنَكۡفُرُ بِبَعۡضٖ وَيُرِيدُونَ أَن يَتَّخِذُواْ بَيۡنَ ذَٰلِكَ سَبِيلًا ﴿١٥٠﴾

151. እነዚያ በውነት ከሓዲዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡ ለከሓዲዎችም አዋራጅን ቅጣት አዘጋጅተናል፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡكَٰفِرُونَ حَقّٗاۚ وَأَعۡتَدۡنَا لِلۡكَٰفِرِينَ عَذَابٗا مُّهِينٗا ﴿١٥١﴾

152. እነዚያም በአላህና በመልክተኞቹ ያመኑ ከነርሱም በአንድም መካከል ያልለዩ እነዚያ ምንዳዎቻቸውን በእርግጥ ይሰጣቸዋል፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦ وَلَمۡ يُفَرِّقُواْ بَيۡنَ أَحَدٖ مِّنۡهُمۡ أُوْلَٰٓئِكَ سَوۡفَ يُؤۡتِيهِمۡ أُجُورَهُمۡۚ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ﴿١٥٢﴾

153. የመጽሐፉ ሰዎች በነሱ ላይ ከሰማይ መጽሐፍን እንድታወርድ ይጠይቁሃል፡፡ ከዚያም የከበደን (ነገር) ሙሳን በእርግጥ ጠይቀዋል፡፡ «አላህንም በግልጽ አሳየን» ብለዋል፡፡ በበደላቸውም መብረቅ ያዘቻቸው፡፡ ከዚያም ተዓምራቶች ከመጡላቸው በኋላ ወይፈኑን (አምላክ አድርገው) ያዙ፡፡ ከዚያም ይቅር አልን፡፡ ሙሳንም ግልጽ ስልጣንን ሰጠነው፡፡

يَسۡـَٔلُكَ أَهۡلُ ٱلۡكِتَٰبِ أَن تُنَزِّلَ عَلَيۡهِمۡ كِتَٰبٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِۚ فَقَدۡ سَأَلُواْ مُوسَىٰٓ أَكۡبَرَ مِن ذَٰلِكَ فَقَالُوٓاْ أَرِنَا ٱللَّهَ جَهۡرَةٗ فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلصَّٰعِقَةُ بِظُلۡمِهِمۡۚ ثُمَّ ٱتَّخَذُواْ ٱلۡعِجۡلَ مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَتۡهُمُ ٱلۡبَيِّنَٰتُ فَعَفَوۡنَا عَن ذَٰلِكَۚ وَءَاتَيۡنَا مُوسَىٰ سُلۡطَٰنٗا مُّبِينٗا ﴿١٥٣﴾

154. በቃል ኪዳናቸውም ምክንያት የጡርን ተራራ ከበላያቸው አነሳን፡፡ ለእነሱም «ደጃፉን አጎንባሾች ኾናችሁ ግቡ» አልን፡፡ ለእነርሱም «በሰንበት ቀን ትዕዛዝን አትተላለፉ» አልን፡፡ ከእነሱም ከባድን ቃል ኪዳን ያዝን፡፡

155. ቃል ኪዳናቸውንም በማፍረሳቸው፣ በአላህም አንቀጾች በመካዳቸው፣ ነቢያትንም ያለ አግባብ በመግደላቸውና «ልቦቻችን ሽፍኖች ናቸው» በማለታቸው ምክንያት (ረገምናቸው)፡፡ በእውነቱ በክህደታቸው ምክንያት አላህ በርሷ (በልቦቻቸው) ላይ አተመ፡፡ ስለዚህ ጥቂትን እንጅ አያምኑም፡፡

156. በመካዳቸውም በመርየም ላይ ከባድ ቅጥፈትን በመናገራቸውም ምክንያት (ረገምናቸው)፡፡

157. «እኛ የአላህን መልክተኛ የመርየምን ልጅ አልመሲሕ ዒሳን ገደልን» በማለታቸውም (ረገምናቸው)፡፡ አልገደሉትም አልሰቀሉትምም፡፡ ግን ለእነሱ (የተገደለው ሰው በዒሳ) ተመሰለ፡፡ እነዚያም በእርሱ ነገር የተለያዩት ከእርሱ (መገደል) በመጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡ ጥርጣሬን ከመከተል በስተቀር በእርሱ ነገር ምንም ዕውቀት የላቸውም፡፡ በእርግጥም አልገደሉትም፡፡

158. ይልቁንስ አላህ (ኢሳን) ወደርሱ አነሳው፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

159. ከመጽሐፉም ሰዎች ከመሞቱ በፊት በእርሱ (በዒሳ) በእርግጥ የሚያምን እንጅ (አንድም) የለም፡፡ በትንሣኤም ቀን በነሱ ላይ መስካሪ ይኾናል፡፡

160. ከእነዚያ ይሁዳውያን ከኾኑትም በተገኘው በደል ሰዎችንም ከአላህ መንገድ በብዙ በመከልከላቸው ምክንያት ለእነሱ ተፈቅደው የነበሩትን ጣፋጮች ምግቦች በእነርሱ ላይ እርም አደረግንባቸው፡፡

161. ከእርሱ በቁርጥ የተከለከሉ ሲኾኑ አራጣንም በመያዛቸውና የሰዎችን ገንዘቦች ያለ አግባብ (በጉቦ) በመብላታቸውም ምክንያት (የተፈቀደላቸውን እርም አደረግንባቸው)፡፡ ከእነሱም ለከሓዲዎቹ አሳማሚን ቅጣት አዘጋጀን፡፡

وَرَفَعۡنَا فَوۡقَهُمُ ٱلطُّورَ بِمِيثَٰقِهِمۡ وَقُلۡنَا لَهُمُ ٱدۡخُلُواْ ٱلۡبَابَ سُجَّدٗا وَقُلۡنَا لَهُمۡ لَا تَعۡدُواْ فِي ٱلسَّبۡتِ وَأَخَذۡنَا مِنۡهُم مِّيثَٰقًا غَلِيظٗا ﴿١٥٤﴾

فَبِمَا نَقۡضِهِم مِّيثَٰقَهُمۡ وَكُفۡرِهِم بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَقَتۡلِهِمُ ٱلۡأَنۢبِيَآءَ بِغَيۡرِ حَقّٖ وَقَوۡلِهِمۡ قُلُوبُنَا غُلۡفُۢۚ بَلۡ طَبَعَ ٱللَّهُ عَلَيۡهَا بِكُفۡرِهِمۡ فَلَا يُؤۡمِنُونَ إِلَّا قَلِيلٗا ﴿١٥٥﴾

وَبِكُفۡرِهِمۡ وَقَوۡلِهِمۡ عَلَىٰ مَرۡيَمَ بُهۡتَٰنًا عَظِيمٗا ﴿١٥٦﴾

وَقَوۡلِهِمۡ إِنَّا قَتَلۡنَا ٱلۡمَسِيحَ عِيسَى ٱبۡنَ مَرۡيَمَ رَسُولَ ٱللَّهِ وَمَا قَتَلُوهُ وَمَا صَلَبُوهُ وَلَٰكِن شُبِّهَ لَهُمۡۚ وَإِنَّ ٱلَّذِينَ ٱخۡتَلَفُواْ فِيهِ لَفِي شَكّٖ مِّنۡهُۚ مَا لَهُم بِهِۦ مِنۡ عِلۡمٍ إِلَّا ٱتِّبَاعَ ٱلظَّنِّۚ وَمَا قَتَلُوهُ يَقِينَۢا ﴿١٥٧﴾

بَل رَّفَعَهُ ٱللَّهُ إِلَيۡهِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَزِيزًا حَكِيمٗا ﴿١٥٨﴾

وَإِن مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ إِلَّا لَيُؤۡمِنَنَّ بِهِۦ قَبۡلَ مَوۡتِهِۦۖ وَيَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ يَكُونُ عَلَيۡهِمۡ شَهِيدٗا ﴿١٥٩﴾

فَبِظُلۡمٖ مِّنَ ٱلَّذِينَ هَادُواْ حَرَّمۡنَا عَلَيۡهِمۡ طَيِّبَٰتٍ أُحِلَّتۡ لَهُمۡ وَبِصَدِّهِمۡ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ كَثِيرٗا ﴿١٦٠﴾

وَأَخۡذِهِمُ ٱلرِّبَوٰاْ وَقَدۡ نُهُواْ عَنۡهُ وَأَكۡلِهِمۡ أَمۡوَٰلَ ٱلنَّاسِ بِٱلۡبَٰطِلِۚ وَأَعۡتَدۡنَا لِلۡكَٰفِرِينَ مِنۡهُمۡ عَذَابًا أَلِيمٗا ﴿١٦١﴾

162. ግን ከነርሱ ውስጥ በዕውቀት የጠለቁትና ምእምናኖቹ በአንተ ላይ በተወረደውና ከአንተም በፊት በተወረደው መጽሐፍ የሚያምኑ ሲኾኑ ሶላትንም ደንቡን ጠብቀው ሰጋጆችን (እናመሰግናለን)፡፡ ዘካንም ሰጪዎቹ በአላህና በመጨረሻዎቹም ቀን አማኞቹ እነዚያ ታላቅ ምንዳን በእርግጥ እንሰጣቸዋለን፡፡

لَّٰكِنِ ٱلرَّٰسِخُونَ فِي ٱلۡعِلۡمِ مِنۡهُمۡ وَٱلۡمُؤۡمِنُونَ يُؤۡمِنُونَ بِمَآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ وَمَآ أُنزِلَ مِن قَبۡلِكَۚ وَٱلۡمُقِيمِينَ ٱلصَّلَوٰةَۚ وَٱلۡمُؤۡتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَٱلۡمُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ أُوْلَٰٓئِكَ سَنُؤۡتِيهِمۡ أَجۡرًا عَظِيمًا ﴿١٦٢﴾

163. እኛ ወደ ኑሕና ከርሱ በኋላ ወደ ነበሩት ነቢያት እንዳወረድን ወደ አንተም አወረድን፡፡ ወደ ኢብራሂምም፣ ወደ ኢስማዒልም፣ ወደ ኢስሓቅም፣ ወደ ያዕቆብም፣ ወደ ነገዶቹም፣ ወደ ዒሳም፣ ወደ አዩብም፣ ወደ ዩኑስም፣ ወደ ሃሩንና፣ ወደ ሱለይማንም አወረድን፡፡ ለዳውድም ዘቡርን ሰጠነው፡፡

۞إِنَّآ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ كَمَآ أَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ نُوحٖ وَٱلنَّبِيِّـۧنَ مِنۢ بَعۡدِهِۦۚ وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡمَٰعِيلَ وَإِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ وَٱلۡأَسۡبَاطِ وَعِيسَىٰ وَأَيُّوبَ وَيُونُسَ وَهَٰرُونَ وَسُلَيۡمَٰنَۚ وَءَاتَيۡنَا دَاوُۥدَ زَبُورٗا ﴿١٦٣﴾

164. ከዚህም በፊት በአንተ ላይ በእርግጥ የተረከናቸውን መልክተኞች ባንተ ላይም ያልተረከናቸውን መልክተኞች (እንደላክን ላክንህ)፡፡ አላህም ሙሳን ማነጋገርን አነጋገረው፡፡

وَرُسُلٗا قَدۡ قَصَصۡنَٰهُمۡ عَلَيۡكَ مِن قَبۡلُ وَرُسُلٗا لَّمۡ نَقۡصُصۡهُمۡ عَلَيۡكَۚ وَكَلَّمَ ٱللَّهُ مُوسَىٰ تَكۡلِيمٗا ﴿١٦٤﴾

165. ከመልክተኞቹ በኋላ ለሰዎች በአላህ ላይ አስረጅ እንዳይኖር አብሳሪዎችና አስፈራሪዎች የኾኑን መልክተኞች (ላክን)፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

رُّسُلٗا مُّبَشِّرِينَ وَمُنذِرِينَ لِئَلَّا يَكُونَ لِلنَّاسِ عَلَى ٱللَّهِ حُجَّةُۢ بَعۡدَ ٱلرُّسُلِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَزِيزًا حَكِيمٗا ﴿١٦٥﴾

166. ግን አላህ ባንተ ላይ ባወረደው ይመሰክራል፡፡ በዕውቀቱ አወረደው፡፡ መላእክቱም ይመሰክራሉ፡፡ መስካሪም በአላህ በቃ፡፡

لَّٰكِنِ ٱللَّهُ يَشۡهَدُ بِمَآ أَنزَلَ إِلَيۡكَۖ أَنزَلَهُۥ بِعِلۡمِهِۦۖ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَشۡهَدُونَۚ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ شَهِيدًا ﴿١٦٦﴾

167. እነዚያ የካዱት ከአላህም መንገድ ያገዱት (ከእውነት) የራቀን መሳሳት በእርግጥ ተሳሳቱ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ قَدۡ ضَلُّواْ ضَلَٰلَۢا بَعِيدًا ﴿١٦٧﴾

168. እነዚያ የካዱ የበደሉም አላህ የሚምራቸውና (ቅን) መንገድን የሚመራቸው አይደለም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَظَلَمُواْ لَمۡ يَكُنِ ٱللَّهُ لِيَغۡفِرَ لَهُمۡ وَلَا لِيَهۡدِيَهُمۡ طَرِيقًا ﴿١٦٨﴾

169. ግን በውስጧ ዘለዓለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ የገሀነምን መንገድ (ይመራቸዋል)፡፡ ይህም በአላህ ላይ ገር ነው፡፡

إِلَّا طَرِيقَ جَهَنَّمَ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۚ وَكَانَ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٗا ﴿١٦٩﴾

170. እናንተ ሰዎች ሆይ! መልክተኛው እውነትን ከጌታችሁ አመጣላችሁ፡፡ እመኑም ለናንተ የተሻለ (ይኾናል)፡፡ ብትክዱም (አትጎዱትም)፡፡ በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነውና፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ قَدۡ جَآءَكُمُ ٱلرَّسُولُ بِٱلۡحَقِّ مِن رَّبِّكُمۡ فَـَٔامِنُواْ خَيۡرٗا لَّكُمۡۚ وَإِن تَكۡفُرُواْ فَإِنَّ لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلِيمًا حَكِيمٗا ﴿١٧٠﴾

يَـٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَـٰبِ لَا تَغۡلُواْ فِي دِينِكُمۡ وَلَا تَقُولُواْ عَلَى ٱللَّهِ إِلَّا ٱلۡحَقَّۚ إِنَّمَا ٱلۡمَسِيحُ عِيسَى ٱبۡنُ مَرۡيَمَ رَسُولُ ٱللَّهِ وَكَلِمَتُهُۥٓ أَلۡقَىٰهَآ إِلَىٰ مَرۡيَمَ وَرُوحٞ مِّنۡهُۖ فَـَٔامِنُواْ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦۖ وَلَا تَقُولُواْ ثَلَٰثَةٌۚ ٱنتَهُواْ خَيۡرٗا لَّكُمۡۚ إِنَّمَا ٱللَّهُ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞۖ سُبۡحَٰنَهُۥٓ أَن يَكُونَ لَهُۥ وَلَدٞۘ لَّهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۗ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ وَكِيلٗا ١٧١

171. እናንተ የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! በሃይማኖታችሁ ወሰንን አትለፉ፡፡ በአላህም ላይ እውነትን እንጅ አትናገሩ፡፡ የመርየም ልጅ አልመሲሕ ዒሳ የአላህ መልክተኛ ወደ መርየም የጣላት «የኹን» ቃሉም ከእርሱ የኾነ መንፈስም ብቻ ነው፡፡ በአላህና በመልክተኞቹም እመኑ፡፡ « (አማልክት) ሦስት ናቸው» አትበሉም፡፡ ተከልከሉ፤ ለእናንተ የተሻለ ይኾናልና፡፡ አላህ አንድ አምላክ ብቻ ነው፡፡ ለእርሱ ልጅ ያለው ከመኾን የጠራ ነው፡፡ በሰማያትና በምድር ያለ ሁሉ የርሱ ነው፡፡ መመኪያም በአላህ በቃ፡፡

لَّن يَسۡتَنكِفَ ٱلۡمَسِيحُ أَن يَكُونَ عَبۡدٗا لِّلَّهِ وَلَا ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ ٱلۡمُقَرَّبُونَۚ وَمَن يَسۡتَنكِفۡ عَنۡ عِبَادَتِهِۦ وَيَسۡتَكۡبِرۡ فَسَيَحۡشُرُهُمۡ إِلَيۡهِ جَمِيعٗا ١٧٢

172. አልመሲሕ (ኢየሱስ) ለአላህ ባሪያ ከመኾን ፈጽሞ አይጠየፍም፡፡ ቀራቢዎች የኾኑት መላእክትም (አይጠየፉም)፡፡ እርሱን ከመገዛት የሚጠየፍና የሚኮራም ሰው (አላህ) ሁሉንም ወደ እርሱ በእርግጥ ይሰበስባቸዋል፡፡

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّـٰلِحَٰتِ فَيُوَفِّيهِمۡ أُجُورَهُمۡ وَيَزِيدُهُم مِّن فَضۡلِهِۦۖ وَأَمَّا ٱلَّذِينَ ٱسۡتَنكَفُواْ وَٱسۡتَكۡبَرُواْ فَيُعَذِّبُهُمۡ عَذَابًا أَلِيمٗا وَلَا يَجِدُونَ لَهُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ وَلِيّٗا وَلَا نَصِيرٗا ١٧٣

173. እነዚያማ ያመኑት መልካሞችንም የሠሩት ምንዳዎቻቸውን ይሞላላቸዋል፡፡ ከችሮታውም ይጨምርላቸዋል፡፡ እነዚያን የተጠየፉትንና የኮሩትንማ አሳማሚን ቅጣት ይቀጣቸዋል፡፡ ከአላህም ሌላ ለእነሱ ዝምድንና ረዳትን አያገኙም፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ قَدۡ جَآءَكُم بُرۡهَٰنٞ مِّن رَّبِّكُمۡ وَأَنزَلۡنَآ إِلَيۡكُمۡ نُورٗا مُّبِينٗا ١٧٤

174. እናንተ ሰዎች ሆይ! ከጌታችሁ ዘንድ በእርግጥ አስረጅ መጣላችሁ፤ ወደእናንተም ገላጭ የኾነን ብርሃን (ቁርኣንን) አወረድን፡፡

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَٱعۡتَصَمُواْ بِهِۦ فَسَيُدۡخِلُهُمۡ فِي رَحۡمَةٖ مِّنۡهُ وَفَضۡلٖ وَيَهۡدِيهِمۡ إِلَيۡهِ صِرَٰطٗا مُّسۡتَقِيمٗا ١٧٥

175. እነዚያማ በአላህ ያመኑ በርሱም የተጠበቁ ከሱ በኾነው እዝነትና ችሮታ ውስጥ በእርግጥ ያስገባቸዋል፡፡ ወደእርሱም ቀጥተኛ መንገድን ይመራቻቸዋል፡፡

يَسۡتَفۡتُونَكَ قُلِ ٱللَّهُ يُفۡتِيكُمۡ فِي ٱلۡكَلَٰلَةِۚ إِنِ ٱمۡرُؤٌاْ هَلَكَ لَيۡسَ لَهُۥ وَلَدٞ وَلَهُۥٓ أُخۡتٞ فَلَهَا نِصۡفُ مَا تَرَكَۚ وَهُوَ يَرِثُهَآ إِن لَّمۡ يَكُن لَّهَا وَلَدٞۚ فَإِن كَانَتَا ٱثۡنَتَيۡنِ فَلَهُمَا ٱلثُّلُثَانِ مِمَّا تَرَكَۚ وَإِن كَانُوٓاْ إِخۡوَةٗ رِّجَالٗا وَنِسَآءٗ فَلِلذَّكَرِ مِثۡلُ حَظِّ ٱلۡأُنثَيَيۡنِۗ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمۡ أَن تَضِلُّواْۗ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمُۢ ١٧٦

176. ይጠይቁሃል በላቸው:- «ወላጅና ልጅ ሳይኖረው በሚወረስ ሰው አላህ ይነግራችኋል፡፡ ለእርሱ ልጅ የሌለው ሰው ቢሞት ለእርሱም እኅት ብትኖረው ለእርስዋ ከተወው ረጅት ግማሹ አላት፡፡ እርሱም ለርሷ ልጅ የሌላት እንደኾነች (በሙሉ) ይወርሳታል፡፡ ሁለት (እኅቶች ወይም ከሁለት በላይ) ቢኾኑም ከተወው ረጅት ከሦስት ሁለት እጁ አላቸው፡፡ ወንድሞች (ና እኅቶች) ወንዶችና ሴቶች ቢኾኑም ለወንዱ የሁለት ሴቶች ድርሻ ብጤ አለው፡፡ አላህ እንዳትሳሳቱ ለእናንተ ያብራራል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡»

# ሱረቱ አል-ማኢዳህ

# سورة المائدة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በቃል ኪዳኖች ሙሉ:: በእናንተ ላይ የሚነበበው ብቻ ሲቀር:: የግመል፣ የከብት፣ የበግና የፍየል እንስሳዎች እናንተ በሐጅ ሥራ ላይ ኾናችሁ ማደንን የተፈቀደ ሳታደርጉ ለእናንተ ተፈቀዱ:: አላህ የሚሻውን ይፈርዳል::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَوۡفُواْ بِٱلۡعُقُودِۚ أُحِلَّتۡ لَكُم بَهِيمَةُ ٱلۡأَنۡعَٰمِ إِلَّا مَا يُتۡلَىٰ عَلَيۡكُمۡ غَيۡرَ مُحِلِّي ٱلصَّيۡدِ وَأَنتُمۡ حُرُمٌۗ إِنَّ ٱللَّهَ يَحۡكُمُ مَا يُرِيدُ ١

2. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! የአላህ (ክልክል ያደረጋቸውን) ምልክቶች የተፈቀዱ አታድርጉ:: የተከበረውንም ወር በመጋደል አትድፈሩ:: ወደ መካ የሚነዱትን መስዋዕትና የሚታበቱባቸውንም ገመዶች ከጌታቸው ችሮታንና ውዴታን ፈልገው ወደ ተከበረው ቤት አሳቢዎችንም ሰዎች (አትንኩ):: ከሐጅም ሥራ በወጣችሁ ጊዜ ዐድኑ:: ከተከበረው መስጊድ ስለከለከሉዋችሁ ሰዎችን መጥላትም (በነሱ ላይ) ወሰን እንድታልፉ አይገፋፋችሁ:: በበጎ ነገርና አላህን በመፍራትም ተረዳዱ:: ግን በኃጢአትና ወሰንን በማለፍ አትረዳዱ:: አላህንም ፍሩ:: አላህ ቅጣተ ብርቱ ነውና::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُحِلُّواْ شَعَٰٓئِرَ ٱللَّهِ وَلَا ٱلشَّهۡرَ ٱلۡحَرَامَ وَلَا ٱلۡهَدۡيَ وَلَا ٱلۡقَلَٰٓئِدَ وَلَآ ءَآمِّينَ ٱلۡبَيۡتَ ٱلۡحَرَامَ يَبۡتَغُونَ فَضۡلٗا مِّن رَّبِّهِمۡ وَرِضۡوَٰنٗاۚ وَإِذَا حَلَلۡتُمۡ فَٱصۡطَادُواْۚ وَلَا يَجۡرِمَنَّكُمۡ شَنَـَٔانُ قَوۡمٍ أَن صَدُّوكُمۡ عَنِ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِ أَن تَعۡتَدُواْۘ وَتَعَاوَنُواْ عَلَى ٱلۡبِرِّ وَٱلتَّقۡوَىٰۖ وَلَا تَعَاوَنُواْ عَلَى ٱلۡإِثۡمِ وَٱلۡعُدۡوَٰنِۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۖ إِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٢

3. በክት፣ ፈሳሽ ደምም፣ የእሪያ (አሣማ) ሥጋም፣ በርሱ ከአላህ (ስም) ሌላ የተነሳበትም፣ የታነቀችም፣ ተደብድባ የተገደለችም፣ ተንከባላ የሞተችም፣ በቀንድ ተውግታ የሞተችም፣ ከርሷ አውሬ የበላላትም (ከእነዚህ በሕይወት ደርሳችሁ) ያረዳችሁት ብቻ ሲቀር ለጣዖታትም የታረደው በአዝላምም ዕድልን መፈለጋችሁ በእናንተ ላይ እርም ተደረገ:: ይህ ድርጊት አመጽ ነው:: ዛሬ እነዚያ የካዱት ከሃይማኖታችሁ ተስፋ ቆረጡ:: ስለዚህ አትፍሩዋቸው:: ፍሩኝም:: ዛሬ ሃይማኖታችሁን ለናንተ ሞላሁላችሁ:: ጸጋዬንም በናንተ ላይ ፈጸምኩ:: ለእናንተም ኢስላምን ከሃይማኖት በኩል ወደድኩ:: በረኃብ ወቅት ወደ ኃጢአት ያዘነበለ ሳይሆን (እርም የኾኑትን ለመብላት) የተገደደ ሰውም (ይብላ):: አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና::

حُرِّمَتۡ عَلَيۡكُمُ ٱلۡمَيۡتَةُ وَٱلدَّمُ وَلَحۡمُ ٱلۡخِنزِيرِ وَمَآ أُهِلَّ لِغَيۡرِ ٱللَّهِ بِهِۦ وَٱلۡمُنۡخَنِقَةُ وَٱلۡمَوۡقُوذَةُ وَٱلۡمُتَرَدِّيَةُ وَٱلنَّطِيحَةُ وَمَآ أَكَلَ ٱلسَّبُعُ إِلَّا مَا ذَكَّيۡتُمۡ وَمَا ذُبِحَ عَلَى ٱلنُّصُبِ وَأَن تَسۡتَقۡسِمُواْ بِٱلۡأَزۡلَٰمِۚ ذَٰلِكُمۡ فِسۡقٌۗ ٱلۡيَوۡمَ يَئِسَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن دِينِكُمۡ فَلَا تَخۡشَوۡهُمۡ وَٱخۡشَوۡنِۚ ٱلۡيَوۡمَ أَكۡمَلۡتُ لَكُمۡ دِينَكُمۡ وَأَتۡمَمۡتُ عَلَيۡكُمۡ نِعۡمَتِي وَرَضِيتُ لَكُمُ ٱلۡإِسۡلَٰمَ دِينٗاۚ فَمَنِ ٱضۡطُرَّ فِي مَخۡمَصَةٍ غَيۡرَ مُتَجَانِفٖ لِّإِثۡمٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٣

4. ለእነርሱ ምን እንደተፈቀደላቸው ይጠይቁሃል:: በላቸው:- «ለእናንተ መልካሞች ሁሉና እነዚያም ከአዳኞች አሰልጣኞች ኾናችሁ ያስተማራችኋቸው (ያደኑት) ተፈቀደላችሁ:: አላህ ከአስተማራችሁ ዕውቀት ታስተምሯቸዋላችሁ:: ለእናንተም ከያዙላችሁ ነገር ብሉ:: በርሱም ላይ የአላህን ስም አውሱ:: አላህንም ፍሩ አላህ ምርመራው ፈጣን ነውና::»

يَسۡـَٔلُونَكَ مَاذَآ أُحِلَّ لَهُمۡۖ قُلۡ أُحِلَّ لَكُمُ ٱلطَّيِّبَٰتُ وَمَا عَلَّمۡتُم مِّنَ ٱلۡجَوَارِحِ مُكَلِّبِينَ تُعَلِّمُونَهُنَّ مِمَّا عَلَّمَكُمُ ٱللَّهُۖ فَكُلُواْ مِمَّآ أَمۡسَكۡنَ عَلَيۡكُمۡ وَٱذۡكُرُواْ ٱسۡمَ ٱللَّهِ عَلَيۡهِۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ٤

5. ዛሬ መልካሞች ሁሉ ለናንተ ተፈቀዱ:: የእነዚያም መጽሐፍን የተሰጡት ሰዎች ምግብ (ያረዱት) ለእናንተ የተፈቀደ ነው:: ምግባችሁም ለነሱ የተፈቀደ ነው:: ከምእመናት ጥብቆቹም ከእነዚያ ከእናንተ በፊት መጽሐፍን ከተሰጡት ሴቶች ጥብቆቹም፤ ዘማዊዎችና (ዝሙተኞች) የምስጢር ወዳጅ ያዢዎች ሳትኾኑ ጥብቆች ኾናችሁ መህሮቻቸውን በሰጣችኋቸው ጊዜ (ልታገቡዋቸው የተፈቀዱ ናቸው):: ከእምነትም የሚመለስ ሰው በእርግጥ ሥራው ተበላሸ:: በመጨረሻም ቀን እርሱ ከከሳሪዎቹ ነው::

ٱلۡيَوۡمَ أُحِلَّ لَكُمُ ٱلطَّيِّبَٰتُۖ وَطَعَامُ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ حِلّٞ لَّكُمۡ وَطَعَامُكُمۡ حِلّٞ لَّهُمۡۖ وَٱلۡمُحۡصَنَٰتُ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ وَٱلۡمُحۡصَنَٰتُ مِنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ مِن قَبۡلِكُمۡ إِذَآ ءَاتَيۡتُمُوهُنَّ أُجُورَهُنَّ مُحۡصِنِينَ غَيۡرَ مُسَٰفِحِينَ وَلَا مُتَّخِذِيٓ أَخۡدَانٖۗ وَمَن يَكۡفُرۡ بِٱلۡإِيمَٰنِ فَقَدۡ حَبِطَ عَمَلُهُۥ وَهُوَ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٥

6. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ወደ ሶላት በቆማችሁ (ለመቆም ባሰባችሁ) ጊዜ ፊቶቻችሁን፣ እጆቻችሁንም እስከ ክርኖች እጠቡ:: ራሶቻችሁንም (በውሃ) አብሱ:: እግሮቻችሁንም እስከ ቁርጭምጭሚቶች (እጠቡ):: (ሴት ጋር በመገናኘት ወይም በሌላ ምክንያት «ጀናባ») ብትኾኑ (ገላችሁን) ታጠቡ:: በሽተኞች ወይም በጉዞ ላይ ብትኾኑም ወይም ከእናንተ አንዳችሁ ከዓይነ ምድር ቢመጣ ወይም ሴቶችን ብትነካኩና ውሃን ባታገኙ ንጹሕን የምድር ገጽ አስቡ :: ከሱም ፊቶቻችሁንና እጆቻችሁን አብሱ:: አላህ በእናንተ ላይ ምንንም ችግር ሊያደርግ አይሻም:: ግን ታመሰግኑ ዘንድ ሊያጠራችሁና ጸጋውን በእናንተ ላይ ሊሞላ ይሻል::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا قُمۡتُمۡ إِلَى ٱلصَّلَوٰةِ فَٱغۡسِلُواْ وُجُوهَكُمۡ وَأَيۡدِيَكُمۡ إِلَى ٱلۡمَرَافِقِ وَٱمۡسَحُواْ بِرُءُوسِكُمۡ وَأَرۡجُلَكُمۡ إِلَى ٱلۡكَعۡبَيۡنِۚ وَإِن كُنتُمۡ جُنُبٗا فَٱطَّهَّرُواْۚ وَإِن كُنتُم مَّرۡضَىٰٓ أَوۡ عَلَىٰ سَفَرٍ أَوۡ جَآءَ أَحَدٞ مِّنكُم مِّنَ ٱلۡغَآئِطِ أَوۡ لَٰمَسۡتُمُ ٱلنِّسَآءَ فَلَمۡ تَجِدُواْ مَآءٗ فَتَيَمَّمُواْ صَعِيدٗا طَيِّبٗا فَٱمۡسَحُواْ بِوُجُوهِكُمۡ وَأَيۡدِيكُم مِّنۡهُۚ مَا يُرِيدُ ٱللَّهُ لِيَجۡعَلَ عَلَيۡكُم مِّنۡ حَرَجٖ وَلَٰكِن يُرِيدُ لِيُطَهِّرَكُمۡ وَلِيُتِمَّ نِعۡمَتَهُۥ عَلَيۡكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ٦

7. በእናንተም ላይ (የለገሰውን) የአላህን ጸጋ ያንንም ሰምተናል ታዘናልም ባላችሁ ጊዜ በርሱ ያጠበቀባችሁን ቃል ኪዳኑን አስታውሱ:: አላህንም ፍሩ:: አላህ በደረቶች ውስጥ ያለውን ሁሉ ዐዋቂ ነውና::

وَٱذۡكُرُواْ نِعۡمَةَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَمِيثَٰقَهُ ٱلَّذِي وَاثَقَكُم بِهِۦٓ إِذۡ قُلۡتُمۡ سَمِعۡنَا وَأَطَعۡنَاۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٧

8. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ለአላህ ቀጥተኞች በትክክል መስካሪዎች ኹኑ:: ሕዝቦችንም መጥላት ባለማስተካከል ላይ አይገፋፋችሁ:: አስተካክሉ:: እርሱ (ማስተካከል) ለአላህ ፍራቻ በጣም የቀረበ ነው:: አላህንም ፍሩ:: አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُونُواْ قَوَّٰمِينَ لِلَّهِ شُهَدَآءَ بِٱلۡقِسۡطِۖ وَلَا يَجۡرِمَنَّكُمۡ شَنَـَٔانُ قَوۡمٍ عَلَىٰٓ أَلَّا تَعۡدِلُواْۚ ٱعۡدِلُواْ هُوَ أَقۡرَبُ لِلتَّقۡوَىٰۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ٨

وَعَدَ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَأَجۡرٌ عَظِيمٞ ٩

9. እነዚያንም ያመኑትንና በጎ ሥራዎችን የሠሩትን አላህ (ገነትን) ተስፋ አደረገላቸው፡፡ ለእነርሱ ምሕረትና ታላቅ ምንዳ አላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَحِيمِ ١٠

10. እነዚያም የካዱና በተአምራቶቻችን ያስተባበሉ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ إِذۡ هَمَّ قَوۡمٌ أَن يَبۡسُطُوٓاْ إِلَيۡكُمۡ أَيۡدِيَهُمۡ فَكَفَّ أَيۡدِيَهُمۡ عَنكُمۡۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلۡيَتَوَكَّلِ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ١١

11. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ሕዝቦች እጆቻቸውን ወደ እናንተ ሊዘረጉ ባሰቡና እጆቻቸውን ከእናንተ ላይ በከለከላችሁ ጊዜ በናንተ ላይ (የዋለላችሁን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ ምእመናንም በአላህ ላይ ይመኩ፡፡

۞وَلَقَدۡ أَخَذَ ٱللَّهُ مِيثَٰقَ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَبَعَثۡنَا مِنۡهُمُ ٱثۡنَيۡ عَشَرَ نَقِيبٗاۖ وَقَالَ ٱللَّهُ إِنِّي مَعَكُمۡۖ لَئِنۡ أَقَمۡتُمُ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَيۡتُمُ ٱلزَّكَوٰةَ وَءَامَنتُم بِرُسُلِي وَعَزَّرۡتُمُوهُمۡ وَأَقۡرَضۡتُمُ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنٗا لَّأُكَفِّرَنَّ عَنكُمۡ سَيِّـَٔاتِكُمۡ وَلَأُدۡخِلَنَّكُمۡ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۚ فَمَن كَفَرَ بَعۡدَ ذَٰلِكَ مِنكُمۡ فَقَدۡ ضَلَّ سَوَآءَ ٱلسَّبِيلِ ١٢

12. አላህም የእስራኤልን ልጆች የጠበቀ ቃል ኪዳን በእርግጥ ያዘባቸው፡፡ ከነርሱም ዐስራ ሁለትን አለቆች አስነሳን፡፡ አላህም አላቸው፤ «እኔ ከናንተ ጋር ነኝ፤ ሶላትን ብታስተካክሉ ግዴታ ምጽዋትንም ብትሰጡ በመልክተኞቼም ብታምኑ ብትረዱዋቸውም ለአላህም መልካም ብድርን ብታበድሩ ኀጢአቶቻችሁን ከናንተ በእርግጥ አብሳለሁ፡፡ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶችም በእርግጥ አገባችኋለሁ፡፡ ከዚህም በኋላ ከእናንተ የካደ ሰው ቀጥተኛውን መንገድ በእርግጥ ተሳሳተ፡፡»

فَبِمَا نَقۡضِهِم مِّيثَٰقَهُمۡ لَعَنَّٰهُمۡ وَجَعَلۡنَا قُلُوبَهُمۡ قَٰسِيَةٗۖ يُحَرِّفُونَ ٱلۡكَلِمَ عَن مَّوَاضِعِهِۦ وَنَسُواْ حَظّٗا مِّمَّا ذُكِّرُواْ بِهِۦۚ وَلَا تَزَالُ تَطَّلِعُ عَلَىٰ خَآئِنَةٖ مِّنۡهُمۡ إِلَّا قَلِيلٗا مِّنۡهُمۡۖ فَٱعۡفُ عَنۡهُمۡ وَٱصۡفَحۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٣

13. ቃል ኪዳናቸውንም በማፍረሳቸው ረገምናቸው፡፡ ልቦቻቸውንም ደረቆች አደረግን፡፡ ቃላትን ከቦታዎቻቸው ይለውጣሉ፡፡ በርሱም ከታዘዙበት ነገር ፈንታን ተው፡፡ ከእነሱም ጥቂቶች ሲቀሩ ከነርሱ የኾነን ክዳት የምታውቅባቸው ከመኾን አትወገድም፡፡ ከእነርሱም ይቅርታ አድርግ እለፋቸውም፡፡ አላህ መልካም ሠሪዎችን ይወዳልና፡፡

وَمِنَ ٱلَّذِينَ قَالُوٓاْ إِنَّا نَصَٰرَىٰٓ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَهُمۡ فَنَسُواْ حَظّٗا مِّمَّا ذُكِّرُواْ بِهِۦ فَأَغۡرَيۡنَا بَيۡنَهُمُ ٱلۡعَدَاوَةَ وَٱلۡبَغۡضَآءَ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ وَسَوۡفَ يُنَبِّئُهُمُ ٱللَّهُ بِمَا كَانُواْ يَصۡنَعُونَ ١٤

14. ከእነዚያም እኛ ክርስቲያኖች ነን ካሉት የጠበቀ ቃል ኪዳናቸውን ያዝን፡፡ በእርሱም ከታዘዙበት ነገር ፈንታን ተውት፡፡ ስለዚህ እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ በመካከላቸው ጠብንና ጥላቻን ጣልንባቸው፡፡ አላህም ይሠሩት የነበሩትን ሁሉ በእርግጥ ይነግራቸዋል፡፡

يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ قَدۡ جَآءَكُمۡ رَسُولُنَا يُبَيِّنُ لَكُمۡ كَثِيرٗا مِّمَّا كُنتُمۡ تُخۡفُونَ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَيَعۡفُواْ عَن كَثِيرٖۚ قَدۡ جَآءَكُم مِّنَ ٱللَّهِ نُورٞ وَكِتَٰبٞ مُّبِينٞ ١٥

15. የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! ከመጽሐፉ ትሸሽጉት ከነበራችሁት ነገር ብዙውን ለእናንተ የሚገልጽ ከብዙውም የሚተው ሲኾን መልክተኛችን (ሙሐመድ) በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ ከአላህ ዘንድ ብርሃንና ገላጭ መጽሐፍ በእርግጥ መጣላችሁ፡፡

16. አላህ ውዴታውን የተከተሉትን ሰዎች የሰላምን መንገዶች በእርሱ ይመራቸዋል፡፡ በፈቃዱም ከጨለማዎች ወደ ብርሃን ያወጣቸዋል፡፡ ወደ ቀጥተኛም መንገድ ይመራቸዋል፡፡

يَهۡدِي بِهِ ٱللَّهُ مَنِ ٱتَّبَعَ رِضۡوَٰنَهُۥ سُبُلَ ٱلسَّلَٰمِ وَيُخۡرِجُهُم مِّنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِ بِإِذۡنِهِۦ وَيَهۡدِيهِمۡ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ﴿١٦﴾

17. እነዚያ አላህ እርሱ የመርየም ልጅ አልመሲሕ ነው ያሉ በእርግጥ ካዱ፡፡ የመርየምን ልጅ አልመሲሕን እናቱንም በምድር ያለንም ሁሉ ለማጥፋት ቢሻ ከአላህ ማዳንን የሚችል ማነው በላቸው፡፡ የሰማያትና የምድር የመካከላቸውም ንግሥና የአላህ ብቻ ነው፡፡ የሚሻውን ይፈጥራል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

لَّقَدۡ كَفَرَ ٱلَّذِينَ قَالُوٓاْ إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡمَسِيحُ ٱبۡنُ مَرۡيَمَۚ قُلۡ فَمَن يَمۡلِكُ مِنَ ٱللَّهِ شَيۡـًٔا إِنۡ أَرَادَ أَن يُهۡلِكَ ٱلۡمَسِيحَ ٱبۡنَ مَرۡيَمَ وَأُمَّهُۥ وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗاۗ وَلِلَّهِ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَاۚ يَخۡلُقُ مَا يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ﴿١٧﴾

18. አይሁዶችና ክርስቲያኖችም «እኛ የአላህ ልጆችና ወዳጆቹ ነን» አሉ፡፡ «ታዲያ በኃጢአቶቻችሁ ለምን ያሰቃያችኋል አይደላችሁም እናንተ ከፈጠራቸው ሰዎች ናችሁ» በላቸው፡፡ ለሚሻው ሰው ይምራል፡፡ የሚሻውንም ሰው ይቀጣል፡፡ የሰማያትና የምድርም በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ንግሥና የአላህ ብቻ ነው፡፡ መመለሻም ወደርሱ ብቻ ነው፡፡

وَقَالَتِ ٱلۡيَهُودُ وَٱلنَّصَٰرَىٰ نَحۡنُ أَبۡنَٰٓؤُاْ ٱللَّهِ وَأَحِبَّٰٓؤُهُۥۚ قُلۡ فَلِمَ يُعَذِّبُكُم بِذُنُوبِكُمۖ بَلۡ أَنتُم بَشَرٞ مِّمَّنۡ خَلَقَۚ يَغۡفِرُ لِمَن يَشَآءُ وَيُعَذِّبُ مَن يَشَآءُۚ وَلِلَّهِ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَاۖ وَإِلَيۡهِ ٱلۡمَصِيرُ ﴿١٨﴾

19. እናንተ የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! «አብሳሪና አስፈራሪ አልመጣልንም» እንዳትሉ ከመልክተኞች በመቋረጥ ጊዜ ላይ ሲኾን (ሕጋችንን) የሚያብራራ ኾኖ መልክተኛችን በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ አብሳሪና አስፈራሪም በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ قَدۡ جَآءَكُمۡ رَسُولُنَا يُبَيِّنُ لَكُمۡ عَلَىٰ فَتۡرَةٖ مِّنَ ٱلرُّسُلِ أَن تَقُولُواْ مَا جَآءَنَا مِنۢ بَشِيرٖ وَلَا نَذِيرٖۖ فَقَدۡ جَآءَكُم بَشِيرٞ وَنَذِيرٞۗ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ﴿١٩﴾

20. ሙሳም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡- «ሕዝቦቼ ሆይ የአላህን ጸጋ በውስጣችሁ ነቢያትን ባደረገና ነገሥታትንም ባደረጋችሁ ከዓለማትም ለአንድም ያልሰጠውን ችሮታ በሰጣችሁ ጊዜ በእናንተ ላይ (ያደረገውን ጸጋ) አስታውሱ፡፡»

وَإِذۡ قَالَ مُوسَىٰ لِقَوۡمِهِۦ يَٰقَوۡمِ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَةَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ إِذۡ جَعَلَ فِيكُمۡ أَنۢبِيَآءَ وَجَعَلَكُم مُّلُوكٗا وَءَاتَىٰكُم مَّا لَمۡ يُؤۡتِ أَحَدٗا مِّنَ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٢٠﴾

21. «ሕዝቦቼ ሆይ! ያችን አላህ ለእናንተ ያደረጋትን የተቀደሰችውን መሬት ግቡ፡፡ ወደ ኋላችሁም አትመለሱ፡፡ ከሳሪዎች ኾናችሁ ትመለሳላችሁና፡፡»

يَٰقَوۡمِ ٱدۡخُلُواْ ٱلۡأَرۡضَ ٱلۡمُقَدَّسَةَ ٱلَّتِي كَتَبَ ٱللَّهُ لَكُمۡ وَلَا تَرۡتَدُّواْ عَلَىٰٓ أَدۡبَارِكُمۡ فَتَنقَلِبُواْ خَٰسِرِينَ ﴿٢١﴾

22. «ሙሳ ሆይ! በርስዋ ውስጥ ኃያላን ሕዝቦች አሉ፡፡ ከርስዋም እስከሚወጡ ድረስ እኛ ፈጽሞ አንገባትም፡፡ ከርስዋም ቢወጡ እኛ ገቢዎች ነን» አሉ፡፡

قَالُواْ يَٰمُوسَىٰٓ إِنَّ فِيهَا قَوۡمٗا جَبَّارِينَ وَإِنَّا لَن نَّدۡخُلَهَا حَتَّىٰ يَخۡرُجُواْ مِنۡهَا فَإِن يَخۡرُجُواْ مِنۡهَا فَإِنَّا دَٰخِلُونَ ﴿٢٢﴾

23. ከእነዚያ (አላህን) ከሚፈሩትና አላህ በእነርሱ ላይ ከለገሰላቸው የኾኑ ሁለት ሰዎች «በእነርሱ (በኀያሎቹ) ላይ በሩን ግቡ፡፡ በገባችሁትም ጊዜ እናንተ አሸናፊዎች ናችሁ፡፡ ምእመናንም እንደ ኾናችሁ በአላህ ላይ ተመኩ» አሉ፡፡

قَالَ رَجُلَانِ مِنَ ٱلَّذِينَ يَخَافُونَ أَنۡعَمَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمَا ٱدۡخُلُواْ عَلَيۡهِمُ ٱلۡبَابَ فَإِذَا دَخَلۡتُمُوهُ فَإِنَّكُمۡ غَٰلِبُونَۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَتَوَكَّلُوٓاْ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ٢٣

24. «ሙሳ ሆይ! በውስጧ እስካሉ ድረስ እኛ ፈጽሞ ምን ጊዜም አንገባትም፡፡ ስለዚህ ኺድ አንተና ጌታህ ተጋደሉም እኛ እዚህ ተቀማጮች ነን» አሉ፡፡

قَالُواْ يَٰمُوسَىٰٓ إِنَّا لَن نَّدۡخُلَهَآ أَبَدٗا مَّا دَامُواْ فِيهَا فَٱذۡهَبۡ أَنتَ وَرَبُّكَ فَقَٰتِلَآ إِنَّا هَٰهُنَا قَٰعِدُونَ ٢٤

25. «ጌታዬ ሆይ እኔ ራሴንና ወንድሜን በቀር (ላስገድድ) አልችልም፡፡ በእኛና በአመጸኞቹም ሕዝቦች መካከል ለይ» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّي لَآ أَمۡلِكُ إِلَّا نَفۡسِي وَأَخِيۖ فَٱفۡرُقۡ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡفَٰسِقِينَ ٢٥

26. እርሷም (የተቀደሰችው መሬት) በእነርሱ ላይ አርባ ዓመት እርም ናት፡፡ በምድረ በዳ ይንከራተታሉ፡፡ «በአመጸኞችም ሕዝቦች ላይ አትዘን» አለው፡፡

قَالَ فَإِنَّهَا مُحَرَّمَةٌ عَلَيۡهِمۡۛ أَرۡبَعِينَ سَنَةٗۛ يَتِيهُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِۚ فَلَا تَأۡسَ عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡفَٰسِقِينَ ٢٦

27. በነርሱም ላይ የአደምን ሁለት ልጆች ወሬ ቁርባንን ባቀረቡና (አላህ) ከአንደኛቸው ተቀብሎ ከሌላው ባልተቀበለ ጊዜ (የኾነውን) በእውነት አንብብላቸው፡፡ «በእርግጥ እገድልሃለሁ» አለው፡፡ (ተገዳዩ) «አላህ የሚቀበለው እኮ ከጥንቁቆቹ ብቻ ነው» አለ፡፡

۞وَٱتۡلُ عَلَيۡهِمۡ نَبَأَ ٱبۡنَيۡ ءَادَمَ بِٱلۡحَقِّ إِذۡ قَرَّبَا قُرۡبَانٗا فَتُقُبِّلَ مِنۡ أَحَدِهِمَا وَلَمۡ يُتَقَبَّلۡ مِنَ ٱلۡأٓخَرِ قَالَ لَأَقۡتُلَنَّكَۖ قَالَ إِنَّمَا يَتَقَبَّلُ ٱللَّهُ مِنَ ٱلۡمُتَّقِينَ ٢٧

28. «ልትገድለኝ እጅህን ወደኔ ብትዘረጋ እኔ ልገድልህ እጄን ወዳንተ የምዘረጋ አይደለሁም፡፡ እኔ የዓለማትን ጌታ አላህን እፈራለሁና» አለ፡፡

لَئِنۢ بَسَطتَ إِلَيَّ يَدَكَ لِتَقۡتُلَنِي مَآ أَنَا۠ بِبَاسِطٖ يَدِيَ إِلَيۡكَ لِأَقۡتُلَكَۖ إِنِّيٓ أَخَافُ ٱللَّهَ رَبَّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٢٨

29. «እኔ በኃጢአቴና በኃጢአትህ ልትመለስና ከእሳት ጓዶች ልትኾን እሻለሁ፤ ይኸም የበደለኞች ቅጣት ነው» (አለ)፡፡

إِنِّيٓ أُرِيدُ أَن تَبُوٓأَ بِإِثۡمِي وَإِثۡمِكَ فَتَكُونَ مِنۡ أَصۡحَٰبِ ٱلنَّارِۚ وَذَٰلِكَ جَزَٰٓؤُاْ ٱلظَّٰلِمِينَ ٢٩

30. ነፍሱም ወንድሙን መግደልን ለርሱ ሸለመችለት፤ (አነሳሳችው፤)፡፡ ገደለውም፡፡ ከከሳሪዎቹም ኾነ፡፡

فَطَوَّعَتۡ لَهُۥ نَفۡسُهُۥ قَتۡلَ أَخِيهِ فَقَتَلَهُۥ فَأَصۡبَحَ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٣٠

31. የወንድሙንም ሬሳ እንዴት እንደሚሸሽግ ያሳየው ዘንድ አላህ መሬትን የሚጭር ቁራን ላከለት፡፡ «ወይ እኔ የወንድሜን ሬሳ እሸሽግ ዘንድ እንደዚህ ቁራ ብጤ መኾን አቃተኝን» አለ፡፡ ከጸጸተኞችም ኾነ፡፡

فَبَعَثَ ٱللَّهُ غُرَابٗا يَبۡحَثُ فِي ٱلۡأَرۡضِ لِيُرِيَهُۥ كَيۡفَ يُوَٰرِي سَوۡءَةَ أَخِيهِۚ قَالَ يَٰوَيۡلَتَىٰٓ أَعَجَزۡتُ أَنۡ أَكُونَ مِثۡلَ هَٰذَا ٱلۡغُرَابِ فَأُوَٰرِيَ سَوۡءَةَ أَخِيۖ فَأَصۡبَحَ مِنَ ٱلنَّٰدِمِينَ ٣١

32. በዚህ ምክንያት በእስራኤል ልጆች ላይ እነሆ ያለ ነፍስ (መግደል) ወይም በምድር ላይ ያለማጥፋት (ካልሆነ በስተቀር) ነፍስን የገደለ ሰው ሰዎቹን ሁሉ እንደገደለ ነው፤ ሕያው ያደረጋትም ሰው ሰዎቹን ሁሉ ሕያው እንዳደረገ ነው ማለትን ጻፍን:: መልክተኞቻችንም በግልጽ ተዓምራት በእርግጥ መጡዋቸው:: ከዚያም ከዚህ በኋላ ከእነሱ ብዙዎቹ በምድር ላይ ወሰንን አላፊዎች ናቸው::

مِنۡ أَجۡلِ ذَٰلِكَ كَتَبۡنَا عَلَىٰ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ أَنَّهُۥ مَن قَتَلَ نَفۡسَۢا بِغَيۡرِ نَفۡسٍ أَوۡ فَسَادٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَكَأَنَّمَا قَتَلَ ٱلنَّاسَ جَمِيعٗا وَمَنۡ أَحۡيَاهَا فَكَأَنَّمَآ أَحۡيَا ٱلنَّاسَ جَمِيعٗاۚ وَلَقَدۡ جَآءَتۡهُمۡ رُسُلُنَا بِٱلۡبَيِّنَٰتِ ثُمَّ إِنَّ كَثِيرٗا مِّنۡهُم بَعۡدَ ذَٰلِكَ فِي ٱلۡأَرۡضِ لَمُسۡرِفُونَ ٣٢

33. የእነዚያ አላህንና መልክተኛውን የሚዋጉ በምድርም ላይ ለማጥፋት የሚተጉ ሰዎች ቅጣት መገደል ወይም መሰቀል ወይም እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን በማፈራረቅ መቆረጥ ወይም ከአገር መባረር ነው:: ይህ በነሱ በቅርቢቱ ዓለም ውርደት ነው:: በመጨረሻይቱም ለእነርሱ ከባድ ቅጣት አላቸው::

إِنَّمَا جَزَٰٓؤُاْ ٱلَّذِينَ يُحَارِبُونَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَيَسۡعَوۡنَ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَسَادًا أَن يُقَتَّلُوٓاْ أَوۡ يُصَلَّبُوٓاْ أَوۡ تُقَطَّعَ أَيۡدِيهِمۡ وَأَرۡجُلُهُم مِّنۡ خِلَٰفٍ أَوۡ يُنفَوۡاْ مِنَ ٱلۡأَرۡضِۚ ذَٰلِكَ لَهُمۡ خِزۡيٞ فِي ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ عَذَابٌ عَظِيمٌ ٣٣

34. እነዚያ በእነርሱ ላይ ከመቻላችሁ (ከመወሰናችሁ) በፊት የተጸጸቱ ሲቀሩ:: አላህም መሓሪ አዛኝ መኾኑን እወቁ::

إِلَّا ٱلَّذِينَ تَابُواْ مِن قَبۡلِ أَن تَقۡدِرُواْ عَلَيۡهِمۡۖ فَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٣٤

35. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ:: ወደርሱም መቃረቢያን (መልካም ሥራን) ፈልጉ:: ትድኑ ዘንድም በእርሱ መንገድ ታገሉ::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱبۡتَغُوٓاْ إِلَيۡهِ ٱلۡوَسِيلَةَ وَجَٰهِدُواْ فِي سَبِيلِهِۦ لَعَلَّكُمۡ تُفۡلِحُونَ ٣٥

36. እነዚያ የካዱት ሰዎች በምድር ላይ ያለው ሁሉ ከእርሱም ጋር ብጤው ከትንሣኤ ቀን ቅጣት በእርሱ ሊበገዙበት ለእነርሱ በኖራቸው ኖሮ ከእነሱ ተቀባይን ባላገኙ ነበር:: ለእነሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው::

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوۡ أَنَّ لَهُم مَّا فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا وَمِثۡلَهُۥ مَعَهُۥ لِيَفۡتَدُواْ بِهِۦ مِنۡ عَذَابِ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ مَا تُقُبِّلَ مِنۡهُمۡۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٣٦

37. ከእሳት ሊወጡ ይፈልጋሉ:: እነርሱም ከርስዋ ወጪዎች አይደሉም:: ለእነርሱም ዘውታሪ ቅጣት አላቸው::

يُرِيدُونَ أَن يَخۡرُجُواْ مِنَ ٱلنَّارِ وَمَا هُم بِخَٰرِجِينَ مِنۡهَاۖ وَلَهُمۡ عَذَابٞ مُّقِيمٞ ٣٧

38. ሰራቂውንና ሰራቂይቱንም በሠሩት ነገር ለቅጣት ከአላህ የኾነን መቀጣጫ እጆቻቸውን ቁረጡ:: አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው::

وَٱلسَّارِقُ وَٱلسَّارِقَةُ فَٱقۡطَعُوٓاْ أَيۡدِيَهُمَا جَزَآءَۢ بِمَا كَسَبَا نَكَٰلٗا مِّنَ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٣٨

39. ከበደሉም በኋላ የተጸጸተና ሥራውን ያሳመረ አላህ ጸጸቱን ከእርሱ ይቀበለዋል:: አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና::

فَمَن تَابَ مِنۢ بَعۡدِ ظُلۡمِهِۦ وَأَصۡلَحَ فَإِنَّ ٱللَّهَ يَتُوبُ عَلَيۡهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ٣٩

40. የሰማያትና የምድር ንግሥና የሱ (የአላህ) ብቻ መኾኑን አላወቅክምን የሚሻውን ሰው ይቀጣል፡፡ ለሚሻውም ሰው ይምራል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

أَلَمْ تَعْلَمْ أَنَّ ٱللَّهَ لَهُۥ مُلْكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ يُعَذِّبُ مَن يَشَآءُ وَيَغْفِرُ لِمَن يَشَآءُ ۗ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٤٠﴾

41. አንተ መልክተኛ ሆይ! እነዚያ በክሕደት የሚቻኮሉት ከእነዚያ ልቦቻቸው ያላመኑ ሲኾኑ በአፎቻቸው «አመንን» ካሉትና ከእነዚያም አይሁድ ከኾኑት ሲኾኑ አያሳዝኑህ፡፡ (እነርሱ) ውሸትን አዳማጮች ናቸው፡፡ ለሌሎች ወዳንተ ላልመጡ ሕዝቦች አዳማጮች ናቸው፡፡ ንግግሮችን ከቦታቸው ሌላ ያጣምማሉ፡፡ «ይህንን (የተጣመመውን) ብትሰሰጡ ያዙት፡፡ ባትሰሰጡትም ተጠንቀቁ» ይላሉ፡፡ አላህም መፈተኑን የሚሻበትን ሰው ለእርሱ ከአላህ (ለመከላከል) ምንንም አትችልም፡፡ እነዚህ እነዚያ አላህ ልቦቻቸውን ማጥራትን ያልሻላቸው ናቸው፡፡ ለእነርሱ በቅርቢቱ ዓለም ውርደት አላቸው፡፡ ለእነርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም ከባድ ቅጣት አላቸው፡፡

۞ يَٰٓأَيُّهَا ٱلرَّسُولُ لَا يَحْزُنكَ ٱلَّذِينَ يُسَٰرِعُونَ فِى ٱلْكُفْرِ مِنَ ٱلَّذِينَ قَالُوٓا۟ ءَامَنَّا بِأَفْوَٰهِهِمْ وَلَمْ تُؤْمِن قُلُوبُهُمْ ۛ وَمِنَ ٱلَّذِينَ هَادُوا۟ ۛ سَمَّٰعُونَ لِلْكَذِبِ سَمَّٰعُونَ لِقَوْمٍ ءَاخَرِينَ لَمْ يَأْتُوكَ ۖ يُحَرِّفُونَ ٱلْكَلِمَ مِنۢ بَعْدِ مَوَاضِعِهِۦ ۖ يَقُولُونَ إِنْ أُوتِيتُمْ هَٰذَا فَخُذُوهُ وَإِن لَّمْ تُؤْتَوْهُ فَٱحْذَرُوا۟ ۚ وَمَن يُرِدِ ٱللَّهُ فِتْنَتَهُۥ فَلَن تَمْلِكَ لَهُۥ مِنَ ٱللَّهِ شَيْـًٔا ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ لَمْ يُرِدِ ٱللَّهُ أَن يُطَهِّرَ قُلُوبَهُمْ ۚ لَهُمْ فِى ٱلدُّنْيَا خِزْىٌ ۖ وَلَهُمْ فِى ٱلْـَٔاخِرَةِ عَذَابٌ عَظِيمٌ ﴿٤١﴾

42. ውሸትን አዳማጮች እርምን በላተኞች ናቸው፡፡ ወደአንተ ቢመጣም በመካከላቸው ፍረድ፡፡ ወይም ተዋቸው፡፡ ብትተዋቸውም ምንም አይጎዱህም፡፡ ብትፈርድም በመካከላቸው በትክክል ፍረድ፡፡ አላህ በትክክል ፈራጆችን ይወዳልና፡፡

سَمَّٰعُونَ لِلْكَذِبِ أَكَّٰلُونَ لِلسُّحْتِ ۚ فَإِن جَآءُوكَ فَٱحْكُم بَيْنَهُمْ أَوْ أَعْرِضْ عَنْهُمْ ۖ وَإِن تُعْرِضْ عَنْهُمْ فَلَن يَضُرُّوكَ شَيْـًٔا ۖ وَإِنْ حَكَمْتَ فَٱحْكُم بَيْنَهُم بِٱلْقِسْطِ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلْمُقْسِطِينَ ﴿٤٢﴾

43. እነርሱም ዘንድ ተውራት እያለች በውስጧ የአላህ ፍርድ ያለባት ስትኾን እንዴት ያስፈርዱሃል! ከዚያም ከዚህ በኋላ እንዴት ይሸሻሉ! እነዚያም በፍጹም ምእምናን አይደሉም፡፡

وَكَيْفَ يُحَكِّمُونَكَ وَعِندَهُمُ ٱلتَّوْرَىٰةُ فِيهَا حُكْمُ ٱللَّهِ ثُمَّ يَتَوَلَّوْنَ مِنۢ بَعْدِ ذَٰلِكَ ۚ وَمَآ أُو۟لَٰٓئِكَ بِٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿٤٣﴾

44. እኛ ተውራትን በውስጥዋ መምሪያና ብርሃን ያለባት ስትኾን አወረድን፡፡ እነዚያ ትዕዛዝን የተቀበሉት ነቢያት በእነዚያ አይሁዳውያን በኾኑት ላይ በርሷ ይፈርዳሉ፡፡ ሊቃውንቱና ዐዋቂዎቹም ከአላህ መጽሐፍ እንዲጠብቁ በተደረጉትና በርሱም ላይ መስካሪዎች በኾኑት (ይፈርዳሉ)፡፡ ሰዎችንም አትፍሩ፡፡ ፍሩኝም፡፡ በአንቀጾቼም አነስተኛን ዋጋ አትለውጡ፡፡ አላህም ባወረደው ነገር ያልፈረደ ሰው እነዚያ ከሓዲዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡

إِنَّآ أَنزَلْنَا ٱلتَّوْرَىٰةَ فِيهَا هُدًى وَنُورٌ ۚ يَحْكُمُ بِهَا ٱلنَّبِيُّونَ ٱلَّذِينَ أَسْلَمُوا۟ لِلَّذِينَ هَادُوا۟ وَٱلرَّبَّٰنِيُّونَ وَٱلْأَحْبَارُ بِمَا ٱسْتُحْفِظُوا۟ مِن كِتَٰبِ ٱللَّهِ وَكَانُوا۟ عَلَيْهِ شُهَدَآءَ ۚ فَلَا تَخْشَوُا۟ ٱلنَّاسَ وَٱخْشَوْنِ وَلَا تَشْتَرُوا۟ بِـَٔايَٰتِى ثَمَنًا قَلِيلًا ۚ وَمَن لَّمْ يَحْكُم بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ فَأُو۟لَٰٓئِكَ هُمُ ٱلْكَٰفِرُونَ ﴿٤٤﴾

45. በእነርሱም ላይ በውስጧ «ነፍስ በነፍስ ዓይንም በዓይን አፍንጫም በአፍንጫ ጆሮም በጆሮ ጥርስም በጥርስ (ይያዛል)፡፡» ቁስሎችንም ማመሳሰል አለባቸው ማለትን ጻፍን፡፡ በእርሱም የመጸወተ (የማረ) ሰው እርሱ ለርሱ (ለሠራው ኃጢአት) ማስተሰሪያ ነው፡፡ አላህም ባወረደው ነገር የማይፈርድ ሰው፤ እነዚያ በደለኞቹ እነርሱ ናቸው፡፡

وَكَتَبۡنَا عَلَيۡهِمۡ فِيهَآ أَنَّ ٱلنَّفۡسَ بِٱلنَّفۡسِ وَٱلۡعَيۡنَ بِٱلۡعَيۡنِ وَٱلۡأَنفَ بِٱلۡأَنفِ وَٱلۡأُذُنَ بِٱلۡأُذُنِ وَٱلسِّنَّ بِٱلسِّنِّ وَٱلۡجُرُوحَ قِصَاصٞۚ فَمَن تَصَدَّقَ بِهِۦ فَهُوَ كَفَّارَةٞ لَّهُۥۚ وَمَن لَّمۡ يَحۡكُم بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٤٥

46. በፈለጎቻቸውም (በነቢያቶቹ ፈለግ) ላይ የመርየምን ልጅ ዒሳን ከተውራት በስተፊቱ ያለውን አረጋጋጭ ሲኾን አስከተልን፡፡ ኢንጂልንም በውስጡ ቀጥታና ብርሃን ያለበት በስተፊቱ ያለችውን ተውራትንም የሚያረጋግጥ ለጥንቁቆችም መሪና ገሳጭ ሲኾን ሰጠነው፡፡

وَقَفَّيۡنَا عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِم بِعِيسَى ٱبۡنِ مَرۡيَمَ مُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ مِنَ ٱلتَّوۡرَىٰةِۖ وَءَاتَيۡنَٰهُ ٱلۡإِنجِيلَ فِيهِ هُدٗى وَنُورٞ وَمُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ مِنَ ٱلتَّوۡرَىٰةِ وَهُدٗى وَمَوۡعِظَةٗ لِّلۡمُتَّقِينَ ٤٦

47. የኢንጅልም ባለቤቶች በውስጡ አላህ ባወረደው ሕግ ይፍረዱ፡፡ አላህም ባወረደው የማይፈርድ ሰው እነዚያ አመጸኞች እነርሱ ናቸው፡፡

وَلۡيَحۡكُمۡ أَهۡلُ ٱلۡإِنجِيلِ بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ فِيهِۚ وَمَن لَّمۡ يَحۡكُم بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ٤٧

48. ወደ አንተም መጽሐፉን ከበፊቱ ያለውን መጽሐፍ አረጋጋጭና በእርሱ ላይ ተጠባባቂ ሲኾን በእውነት አወረድን፡፡ በመካከላቸውም አላህ ባወረደው ሕግ ፍረድ፡፡ እውነቱም ከመጣልህ በኋላ ዝንባሌዎቻቸውን አትከተል፡፡ ከእናንተ ለሁሉም ሕግንና መንገድን አደረግን፡፡ አላህም በሻ ኖሮ አንድ ሕዝብ ባደረጋችሁ ነበር፡፡ ግን በሰጣችሁ ሕግጋት ሊሞክራችሁ (ለያያችሁ)፡፡ በጎ ሥራዎችንም (ለመሥራት) ተሽቀዳደሙ፤ መመለሻችሁ በጠቅላላ ወደ አላህ ነው፡፡ በእርሱም ትለያዩበት የነበራችሁትን ነገር ይነግራችኋል፡፡

وَأَنزَلۡنَآ إِلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَ بِٱلۡحَقِّ مُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَمُهَيۡمِنًا عَلَيۡهِۖ فَٱحۡكُم بَيۡنَهُم بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُۖ وَلَا تَتَّبِعۡ أَهۡوَآءَهُمۡ عَمَّا جَآءَكَ مِنَ ٱلۡحَقِّۚ لِكُلّٖ جَعَلۡنَا مِنكُمۡ شِرۡعَةٗ وَمِنۡهَاجٗاۚ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَجَعَلَكُمۡ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ وَلَٰكِن لِّيَبۡلُوَكُمۡ فِي مَآ ءَاتَىٰكُمۡۖ فَٱسۡتَبِقُواْ ٱلۡخَيۡرَٰتِۚ إِلَى ٱللَّهِ مَرۡجِعُكُمۡ جَمِيعٗا فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ فِيهِ تَخۡتَلِفُونَ ٤٨

49. በመካከላቸውም አላህ ባወረደው ሕግ ፍረድ፡፡ ፍላጎቶቻቸውንም አትከተል፡፡ አላህም ወደ አንተ ካወረደው ከከፊሉ እንዳያሳስቱህ ተጠንቀቃቸው (ማለትን አወረድን)፡፡ ቢዞሩም አላህ የሚሻው በከፊሉ ኃጢአታቸው ሊቀጣቸው መኾኑን ዕወቅ፡፡ ከሰዎቹም ብዙዎቹ አመጸኞች ናቸው፡፡

وَأَنِ ٱحۡكُم بَيۡنَهُم بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ وَلَا تَتَّبِعۡ أَهۡوَآءَهُمۡ وَٱحۡذَرۡهُمۡ أَن يَفۡتِنُوكَ عَنۢ بَعۡضِ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ إِلَيۡكَۖ فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَٱعۡلَمۡ أَنَّمَا يُرِيدُ ٱللَّهُ أَن يُصِيبَهُم بِبَعۡضِ ذُنُوبِهِمۡۗ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِ لَفَٰسِقُونَ ٤٩

50. የማይምንነትን ፍርድ ይፈልጋሉን ለሚያረጋግጡም ሰዎች ከአላህ ይበልጥ ፍርዱ ያማረ ማን ነው

أَفَحُكۡمَ ٱلۡجَٰهِلِيَّةِ يَبۡغُونَۚ وَمَنۡ أَحۡسَنُ مِنَ ٱللَّهِ حُكۡمٗا لِّقَوۡمٖ يُوقِنُونَ ٥٠

51. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አይሁዶችንና ክርስቲያኖችን ረዳቶች አድርጋችሁ አትያዙ:: ከፊላቸው ለከፊሉ ረዳቶች ናቸው:: ከእናንተም ውስጥ ረዳቶች የሚያደርጋቸው ሰው እርሱ ከነርሱ ነው:: አላህ አመጸኞችን ሕዝቦች አያቀናም::

۞يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّخِذُواْ ٱلۡيَهُودَ وَٱلنَّصَـٰرَىٰٓ أَوۡلِيَآءَۘ بَعۡضُهُمۡ أَوۡلِيَآءُ بَعۡضٖۚ وَمَن يَتَوَلَّهُم مِّنكُمۡ فَإِنَّهُۥ مِنۡهُمۡۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلظَّـٰلِمِينَ ﴿٥١﴾

52. እነዚያንም በልቦቻቸው ውስጥ (የንፍቅና) በሽታ ያለባቸውን ሰዎች «የጊዜ መለዋወጥ እንዳያገኘን እንፈራለን የሚሉ» ሲኾኑ በእነርሱ (ለመረዳት) ሲቻኮሉ ታያቸዋለህ፡፡ አላህም ድል መንሳትን ወይም ከእርሱ ዘንድ የኾነን ነገር (ማጋለጥን) ሊያመጣ በነፍሶቻቸው ውስጥ በደበቁትም ነገር ተጸጻቾች ሲሆኑ ተረጋገጡ::

فَتَرَى ٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ يُسَٰرِعُونَ فِيهِمۡ يَقُولُونَ نَخۡشَىٰٓ أَن تُصِيبَنَا دَآئِرَةٞۚ فَعَسَى ٱللَّهُ أَن يَأۡتِيَ بِٱلۡفَتۡحِ أَوۡ أَمۡرٖ مِّنۡ عِندِهِۦ فَيُصۡبِحُواْ عَلَىٰ مَآ أَسَرُّواْ فِيٓ أَنفُسِهِمۡ نَٰدِمِينَ ﴿٥٢﴾

53. እነዚያም ያመኑት ሰዎች፡- «እነዚያ እነርሱ ከእናንተ ጋር ነን ብለው የጠነከረ መሐላቸውን በአላህ የማሉት እነዚህ ናቸውን» ይላሉ:: ሥራዎቻቸው ተበላሹ:: ከሳሪዎችም ኾኑ::

وَيَقُولُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَهَٰٓؤُلَآءِ ٱلَّذِينَ أَقۡسَمُواْ بِٱللَّهِ جَهۡدَ أَيۡمَٰنِهِمۡ إِنَّهُمۡ لَمَعَكُمۡۚ حَبِطَتۡ أَعۡمَٰلُهُمۡ فَأَصۡبَحُواْ خَٰسِرِينَ ﴿٥٣﴾

54. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከእናንተ ውስጥ ከሃይማኖቱ የሚመለስ ሰው አላህ (በእነርሱ ስፍራ) የሚወዳቸውንና የሚወዱትን፣ በምእመናን ላይ ትሑቶች፣ በከሓዲዎች ላይ ኀያላን የኾኑን በአላህ መንገድ የሚታገሉን የወቃሽን ወቀሳ የማይፈሩን ሕዝቦች በእርግጥ ያመጣል፡፡ ይኸ የአላህ ችሮታ ነው፤ ለሚሻው ሰው ይሰጠዋል፤ አላህም ችሮታው ሰፊ ዐዋቂ ነው::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَن يَرۡتَدَّ مِنكُمۡ عَن دِينِهِۦ فَسَوۡفَ يَأۡتِي ٱللَّهُ بِقَوۡمٖ يُحِبُّهُمۡ وَيُحِبُّونَهُۥٓ أَذِلَّةٍ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ أَعِزَّةٍ عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ يُجَٰهِدُونَ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَلَا يَخَافُونَ لَوۡمَةَ لَآئِمٖۚ ذَٰلِكَ فَضۡلُ ٱللَّهِ يُؤۡتِيهِ مَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٌ ﴿٥٤﴾

55. ረዳታችሁ አላህና መልክተኛው እነዚያም ያመኑት ብቻ ናቸው:: (እነርሱ) እነዚያ ሶላትን በደንቡ የሚሰግዱ እነርሱም ያጎነበሱ ኾነው ምጽዋትን የሚሰጡ ናቸው::

إِنَّمَا وَلِيُّكُمُ ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱلَّذِينَ يُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَيُؤۡتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَهُمۡ رَٰكِعُونَ ﴿٥٥﴾

56. አላህንና መልክተኛውን እነዚያንም ያመኑትን የሚወዳጅ ሰው (ከአላህ ጭፍሮች ይኾናል):: የአላህም ጭፍሮች እነርሱ አሸናፊዎች ናቸው::

وَمَن يَتَوَلَّ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ فَإِنَّ حِزۡبَ ٱللَّهِ هُمُ ٱلۡغَٰلِبُونَ ﴿٥٦﴾

57. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከእነዚያ ከበፊታችሁ መጽሐፍን ከተሰጡት እነዚያን ሃይማኖታችሁን ማላገጫና መጫወቻ አድርገው የያዙትን ከሓዲዎችንም ረዳቶች አድርጋችሁ አትያዙ:: ምእምናንም እንደኾናችሁ አላህን ፍሩ::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّخِذُواْ ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُواْ دِينَكُمۡ هُزُوٗا وَلَعِبٗا مِّنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ مِن قَبۡلِكُمۡ وَٱلۡكُفَّارَ أَوۡلِيَآءَۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ﴿٥٧﴾

58. ወደ ሶላትም በጠራችሁ ጊዜ (ጥሪይቱን) መሳለቂያና መጫወቻ አድርገው ይይዟታል:: ይህ እነርሱ የማያውቁ ሕዝቦች በመኾናቸው ነው::

وَإِذَا نَادَيۡتُمۡ إِلَى ٱلصَّلَوٰةِ ٱتَّخَذُوهَا هُزُوٗا وَلَعِبٗاۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَوۡمٞ لَّا يَعۡقِلُونَ ﴿٥٨﴾

59. «የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! በአላህና ወደኛ በተወረደው በፊትም በተወረደው ለማመናችን አብዘኞቻችሁም አመጸኞች ለመኾናችሁ እንጅ (ሌላን ነገር) ከኛ ትጠላላችሁን» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ هَلۡ تَنقِمُونَ مِنَّآ إِلَّآ أَنۡ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَمَآ أُنزِلَ إِلَيۡنَا وَمَآ أُنزِلَ مِن قَبۡلُ وَأَنَّ أَكۡثَرَكُمۡ فَٰسِقُونَ ٥٩

60. «አላህ ዘንድ ቅጣቱ ከዚህ የከፋ ነገር ልንገራችሁን» በላቸው፡፡ (እርሱም) «አላህ የረገመው ሰው በእርሱም ላይ ተቆጣበት፡፡ ከእነርሱም ዝንጀሮዎችንና ከርከሮዎችን ያደረገው ጣዖትንም የተገዛ ሰው (ሃይማኖት) ነው፡፡ እነዚያ በጣም በከፋ ስፍራ ናቸው፡፡» ከቀጥተኛውም መንገድ በጣም የተሳሳቱ ናቸው፡፡

قُلۡ هَلۡ أُنَبِّئُكُم بِشَرّٖ مِّن ذَٰلِكَ مَثُوبَةً عِندَ ٱللَّهِۚ مَن لَّعَنَهُ ٱللَّهُ وَغَضِبَ عَلَيۡهِ وَجَعَلَ مِنۡهُمُ ٱلۡقِرَدَةَ وَٱلۡخَنَازِيرَ وَعَبَدَ ٱلطَّٰغُوتَۚ أُوْلَٰٓئِكَ شَرّٞ مَّكَانٗا وَأَضَلُّ عَن سَوَآءِ ٱلسَّبِيلِ ٦٠

61. በመጡዋችሁም ጊዜ (ወደእናንተ) ከክህደት ጋር በእርግጥ የገቡ እነርሱም ከርሱ ጋር በእርግጥ የወጡ ሲኾኑ «አምነናል» ይላሉ፡፡ አላህም ይደብቁት የነበሩትን ነገር በጣም ዐዋቂ ነው፡፡

وَإِذَا جَآءُوكُمۡ قَالُوٓاْ ءَامَنَّا وَقَد دَّخَلُواْ بِٱلۡكُفۡرِ وَهُمۡ قَدۡ خَرَجُواْ بِهِۦۚ وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا كَانُواْ يَكۡتُمُونَ ٦١

62. ከእነርሱም ብዙዎቹን በኃጢአትና በበደል እርምንም በመብላታቸው የሚጣደፉ ሲኾኑ ታያለህ፡፡ ይሠሩት የነበሩት ነገር በጣም ከፋ!

وَتَرَىٰ كَثِيرٗا مِّنۡهُمۡ يُسَٰرِعُونَ فِي ٱلۡإِثۡمِ وَٱلۡعُدۡوَٰنِ وَأَكۡلِهِمُ ٱلسُّحۡتَۚ لَبِئۡسَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٦٢

63. ቀሳውስቱና ሊቃውንቱ ከኃጢአት ንግግራቸውና እርምን ከመብላታቸው አይከለክሏቸውም ኖሮአልን ይሠሩት የነበሩት ነገር በጣም ከፋ!

لَوۡلَا يَنۡهَىٰهُمُ ٱلرَّبَّٰنِيُّونَ وَٱلۡأَحۡبَارُ عَن قَوۡلِهِمُ ٱلۡإِثۡمَ وَأَكۡلِهِمُ ٱلسُّحۡتَۚ لَبِئۡسَ مَا كَانُواْ يَصۡنَعُونَ ٦٣

64. አይሁዶችም «የአላህ እጅ የታሰረች ናት» አሉ፡፡ እጆቻቸው ይታሰሩ ባሉትም ነገር ይረገሙ፡፡ አይደለም (የአላህ) እጆቹ የተዘረጉ ናቸው፡፡ እንደሚሻ ይለግሳል፡፡ ከጌታህም ወደ አንተ የተወረደው (ቁርአን) ከእነሱ ብዙዎቹን ትዕቢትንና ክህደትን በእርግጥ ይጨምራቸዋል፡፡ በመካከላቸውም ጠብንና ጥላቻን እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ ጣልን፡፡ ለጦር እሳትን ባያያዙ (ባጫሩ) ቁጥር አላህ ያጠፉታል፡፡ በምድርም ውስጥ ለማበላሸት ይሮጣሉ፡፡ አላህም አበላሺዎችን አይወድም፡፡

وَقَالَتِ ٱلۡيَهُودُ يَدُ ٱللَّهِ مَغۡلُولَةٌۚ غُلَّتۡ أَيۡدِيهِمۡ وَلُعِنُواْ بِمَا قَالُواْۘ بَلۡ يَدَاهُ مَبۡسُوطَتَانِ يُنفِقُ كَيۡفَ يَشَآءُۚ وَلَيَزِيدَنَّ كَثِيرٗا مِّنۡهُم مَّآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَ طُغۡيَٰنٗا وَكُفۡرٗاۚ وَأَلۡقَيۡنَا بَيۡنَهُمُ ٱلۡعَدَٰوَةَ وَٱلۡبَغۡضَآءَ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ كُلَّمَآ أَوۡقَدُواْ نَارٗا لِّلۡحَرۡبِ أَطۡفَأَهَا ٱللَّهُۚ وَيَسۡعَوۡنَ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَسَادٗاۚ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ٦٤

65. የመጽሐፉም ባለቤቶች ባመኑና (ከክህደትም) በተጠነቀቁ ኖሮ ከእነሱ ኃጢአቶቻቸውን በእርግጥ ባበስንና የመጠቀሚያ ገነቶችንም በእርግጥ ባገባናቸው ነበር፡፡

وَلَوۡ أَنَّ أَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ ءَامَنُواْ وَٱتَّقَوۡاْ لَكَفَّرۡنَا عَنۡهُمۡ سَيِّـَٔاتِهِمۡ وَلَأَدۡخَلۡنَٰهُمۡ جَنَّٰتِ ٱلنَّعِيمِ ٦٥

66. እነርሱም ተውራትንና ኢንጂልን ከጌታቸውም ወደእነሱ የተወረደውን መጽሐፍ ባቋቋሙ (በሠሩበት) ኖሮ ከበላያቸውና ከእግሮቻቸው ሥር በተመገቡ ነበር፡፡ ከእነሱ ውስጥ ትክክለኞች ሕዝቦች አልሉ፡፡ ከእነሱም ብዙዎቹ የሚሠሩት ነገር ከፋ!

وَلَوۡ أَنَّهُمۡ أَقَامُواْ ٱلتَّوۡرَىٰةَ وَٱلۡإِنجِيلَ وَمَآ أُنزِلَ إِلَيۡهِم مِّن رَّبِّهِمۡ لَأَكَلُواْ مِن فَوۡقِهِمۡ وَمِن تَحۡتِ أَرۡجُلِهِمۚ مِّنۡهُمۡ أُمَّةٞ مُّقۡتَصِدَةٞۖ وَكَثِيرٞ مِّنۡهُمۡ سَآءَ مَا يَعۡمَلُونَ ٦٦

67. አንተ መልክተኛ ሆይ! ከጌታህ ወዳንተ የተወረደውን አድርስ፡፡ ባትሠራም መልክቱን አላደረስክም፡፡ አላህም ከሰዎች ይጠብቅሃል፡፡ አላህ ከሓዲዎችን ሕዝቦች አያቀናምና፡፡

۞يَٰٓأَيُّهَا ٱلرَّسُولُ بَلِّغۡ مَآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَۖ وَإِن لَّمۡ تَفۡعَلۡ فَمَا بَلَّغۡتَ رِسَالَتَهُۥۚ وَٱللَّهُ يَعۡصِمُكَ مِنَ ٱلنَّاسِۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٦٧

68. «እናንተ የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! ተውራትንና ኢንጂልን ከጌታችሁም ወደእናንተ የተወረደውን እስከምታቆሙ (እስከምትሠሩባቸው) ድረስ በምንም ላይ አይደላችሁም» በላቸው፡፡ ከጌታህም ወደ አንተ የተወረደው ቁርኣን ከእነሱ ብዙዎቹን ትዕቢትንና ክህደትን በእርግጥ ይጨምርባቸዋል፡፡ በከሓዲያን ሕዝቦችም ላይ አትዘን፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لَسۡتُمۡ عَلَىٰ شَيۡءٍ حَتَّىٰ تُقِيمُواْ ٱلتَّوۡرَىٰةَ وَٱلۡإِنجِيلَ وَمَآ أُنزِلَ إِلَيۡكُم مِّن رَّبِّكُمۡۗ وَلَيَزِيدَنَّ كَثِيرٗا مِّنۡهُم مَّآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَ طُغۡيَٰنٗا وَكُفۡرٗاۖ فَلَا تَأۡسَ عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٦٨

69. እነዚያ ያመኑና እነዚያም አይሁዳውያን የኾኑ፣ ሳቢያኖችም፣ ክርስቲያኖችም (ከነርሱ) በአላህና በመጨረሻው ቀን ያመነና መልካምን ሥራ የሠራ ሰው በነርሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም፡፡ እነርሱም አያዝኑም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَٱلَّذِينَ هَادُواْ وَٱلصَّٰبِـُٔونَ وَٱلنَّصَٰرَىٰ مَنۡ ءَامَنَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ٦٩

70. የእስራኤልን ልጆች የጠበቀ ቃል ኪዳን በእርግጥ ያዝንባቸው፡፡ ወደእነሱም መልክተኞችን ላክን፡፡ ነፍሶቻቸው በማትወደው ነገር መልእክተኛ በመጣላቸው ቁጥር ከፊሉን አስተባበሉ፤ ከፊሉንም ይገድላሉ፡፡

لَقَدۡ أَخَذۡنَا مِيثَٰقَ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَأَرۡسَلۡنَآ إِلَيۡهِمۡ رُسُلٗاۖ كُلَّمَا جَآءَهُمۡ رَسُولُۢ بِمَا لَا تَهۡوَىٰٓ أَنفُسُهُمۡ فَرِيقٗا كَذَّبُواْ وَفَرِيقٗا يَقۡتُلُونَ ٧٠

71. ፈተናም አለመኖርዋን ጠረጠሩ፡፡ ታወሩም፣ ደነቆሩም፣ ከዚያም አላህ ከነርሱ ላይ ጸጸትን ተቀበለ፡፡ ከዚያም ከእነሱ ብዙዎቹ ታወሩ፣ ደነቆሩም፡፡ አላህም የሚሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

وَحَسِبُوٓاْ أَلَّا تَكُونَ فِتۡنَةٞ فَعَمُواْ وَصَمُّواْ ثُمَّ تَابَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمۡ ثُمَّ عَمُواْ وَصَمُّواْ كَثِيرٞ مِّنۡهُمۡۚ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِمَا يَعۡمَلُونَ ٧١

72. እነዚያ «አላህ እርሱ የመርየም ልጅ አልመሲሕ ነው» ያሉ በእርግጥ ካዱ፡፡ አልመሲህም አለ፡- «የእስራኤል ልጆች ሆይ! ጌታዬንና ጌታችሁን አላህን ተገዙ፡፡» እነሆ! በአላህ የሚያጋራ ሰው አላህ በርሱ ላይ ገነትን በእርግጥ እርም አደረገ፡፡ መኖሪያውም እሳት ናት፡፡ ለበዳዮችም ምንም ረዳቶች የሏቸውም፡፡

لَقَدۡ كَفَرَ ٱلَّذِينَ قَالُوٓاْ إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡمَسِيحُ ٱبۡنُ مَرۡيَمَۖ وَقَالَ ٱلۡمَسِيحُ يَٰبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ رَبِّي وَرَبَّكُمۡۖ إِنَّهُۥ مَن يُشۡرِكۡ بِٱللَّهِ فَقَدۡ حَرَّمَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِ ٱلۡجَنَّةَ وَمَأۡوَىٰهُ ٱلنَّارُۖ وَمَا لِلظَّٰلِمِينَ مِنۡ أَنصَارٖ ٧٢

73. እነዚያ «አላህ የሦስት ሦስተኛ ነው» ያሉ በእርግጥ ካዱ፡፡ ከአምላክም አንድ አምላክ እንጅ ሌላ የለም፡፡ ከሚሉትም ነገር ባይከለከሉ ከነሱ እነዚያን የካዱትን አሳማሚ ቅጣት በእርግጥ ይነካቸዋል፡፡

لَّقَدۡ كَفَرَ ٱلَّذِينَ قَالُوٓاْ إِنَّ ٱللَّهَ ثَالِثُ ثَلَٰثَةٖۘ وَمَا مِنۡ إِلَٰهٍ إِلَّآ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞۚ وَإِن لَّمۡ يَنتَهُواْ عَمَّا يَقُولُونَ لَيَمَسَّنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنۡهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٌ ٧٣

74. ወደ አላህ አይመለሱምና ምሕረትን አይለምኑትምን አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

أَفَلَا يَتُوبُونَ إِلَى ٱللَّهِ وَيَسۡتَغۡفِرُونَهُۥۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٧٤

75. የመርየም ልጅ አልመሲሕ ከበፊቱ መልክተኞች በእርግጥ ያለፉ የኾነ መልክተኛ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡ እናቱም በጣም እውነተኛ ናት፡፡ (ሁለቱም) ምግብን የሚበሉ ነበሩ፤ አንቀጾችን ለነርሱ (ለከሓዲዎች) እንዴት እንደምናብራራ ተመልከት ከዚያም (ከእውነት) እንዴት እንደሚመለሱ ተመልከት፡፡

مَّا ٱلۡمَسِيحُ ٱبۡنُ مَرۡيَمَ إِلَّا رَسُولٞ قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِهِ ٱلرُّسُلُ وَأُمُّهُۥ صِدِّيقَةٞۖ كَانَا يَأۡكُلَانِ ٱلطَّعَامَۗ ٱنظُرۡ كَيۡفَ نُبَيِّنُ لَهُمُ ٱلۡأٓيَٰتِ ثُمَّ ٱنظُرۡ أَنَّىٰ يُؤۡفَكُونَ ٧٥

76. «ከአላህ ሌላ ለእናንተ መጉዳትንና መጥቀምን የማይችልን ትገዛላችሁን» በላቸው፡፡ አላህም እርሱ ሰሚው ዐዋቂ ነው፡፡

قُلۡ أَتَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَمۡلِكُ لَكُمۡ ضَرّٗا وَلَا نَفۡعٗاۚ وَٱللَّهُ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٧٦

77. «እናንተ የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! በሃይማኖታችሁ ከእውነት ሌላ የኾነን (ማለፍ) ወሰንን አትለፉ፡፡ በፊትም በእርግጥ የተሳሳቱትንና ከቀጥተኛው መንገድም (አሁን) የተሳሳቱን ሕዝቦች ከንቱ ዝንባሌዎች አትከተሉ» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ لَا تَغۡلُواْ فِي دِينِكُمۡ غَيۡرَ ٱلۡحَقِّ وَلَا تَتَّبِعُوٓاْ أَهۡوَآءَ قَوۡمٖ قَدۡ ضَلُّواْ مِن قَبۡلُ وَأَضَلُّواْ كَثِيرٗا وَضَلُّواْ عَن سَوَآءِ ٱلسَّبِيلِ ٧٧

78. ከእስራኤል ልጆች እነዚያ የካዱት በዳውድና በመርየም ልጅ በዒሳ ምላስ ተረገሙ፡፡ ይህ ትእዛዝን በመጣሳቸውና ወሰንን የሚያልፉ በመኾናቸው ነው፡፡

لُعِنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنۢ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ عَلَىٰ لِسَانِ دَاوُۥدَ وَعِيسَى ٱبۡنِ مَرۡيَمَۚ ذَٰلِكَ بِمَا عَصَواْ وَّكَانُواْ يَعۡتَدُونَ ٧٨

79. ከሠሩት መጥፎ ነገር አይከላከሉም ነበር፡፡ ይሠሩት የነበሩት ነገር በእርግጥ ከፋ!

كَانُواْ لَا يَتَنَاهَوۡنَ عَن مُّنكَرٖ فَعَلُوهُۚ لَبِئۡسَ مَا كَانُواْ يَفۡعَلُونَ ٧٩

80. ከእነሱ ብዙዎቹን እነዚያን የካዱትን ሲወዳጁ ታያለህ፡፡ በእነሱ ላይ አላህ የተቆጣባቸው በመኾኑ ለእነርሱ ነፍሶቻቸው ያስቀደሙት ሥራ በጣም ከፋ፡፡ እነሱም በቅጣት ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

تَرَىٰ كَثِيرٗا مِّنۡهُمۡ يَتَوَلَّوۡنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْۚ لَبِئۡسَ مَا قَدَّمَتۡ لَهُمۡ أَنفُسُهُمۡ أَن سَخِطَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمۡ وَفِي ٱلۡعَذَابِ هُمۡ خَٰلِدُونَ ٨٠

81. በአላህና በነቢዩ ወደርሱም በተወረደው ቁርኣን የሚያምኑ በኾኑ ኖሮ ወዳጆች አድርገው ባልያዙዋቸው ነበር፡፡ ግን ከነርሱ ብዙዎቹ አመጠኞች ናቸው፡፡

وَلَوۡ كَانُواْ يُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلنَّبِيِّ وَمَآ أُنزِلَ إِلَيۡهِ مَا ٱتَّخَذُوهُمۡ أَوۡلِيَآءَ وَلَٰكِنَّ كَثِيرٗا مِّنۡهُمۡ فَٰسِقُونَ ٨١

82. አይሁዶችንና እነዚያን ያጋሩትን ለእነዚያ ለአመኑት በጠላትነት ከሰዎች ሁሉ ይበልጥ የበረቱ ኾነው በእርግጥ ታገኛለህ፡፡ እነዚያንም «እኛ ክርስቲያኖች ነን» ያሉትን ለእነዚያ ለአመኑት በወዳጅነት በእርግጥ ይበልጥ የቀረቧቸው ኾነው ታገኛለህ፡፡ ይህ ከእነሱ ውስጥ ቀሳውስትና መነኩሳት በመኖራቸውና እነሱም የማይኮሩ በመኾናቸው ነው፡፡

۞لَتَجِدَنَّ أَشَدَّ ٱلنَّاسِ عَدَٰوَةٗ لِّلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱلۡيَهُودَ وَٱلَّذِينَ أَشۡرَكُواْۖ وَلَتَجِدَنَّ أَقۡرَبَهُم مَّوَدَّةٗ لِّلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱلَّذِينَ قَالُوٓاْ إِنَّا نَصَٰرَىٰۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّ مِنۡهُمۡ قِسِّيسِينَ وَرُهۡبَانٗا وَأَنَّهُمۡ لَا يَسۡتَكۡبِرُونَ ٨٢

83. ወደ መልክተኛውም የተወረደውን (ቁርአን) በሰሙ ጊዜ እውነቱን ከማወቃቸው የተነሳ ዓይኖቻቸው እንባን ሲያፈሱ ታያለህ፡፡ «ጌታችን ሆይ! አመንን ከመስካሪዎቹም ጋር ጻፈን » ይላሉ፡፡

وَإِذَا سَمِعُواْ مَآ أُنزِلَ إِلَى ٱلرَّسُولِ تَرَىٰٓ أَعۡيُنَهُمۡ تَفِيضُ مِنَ ٱلدَّمۡعِ مِمَّا عَرَفُواْ مِنَ ٱلۡحَقِّۖ يَقُولُونَ رَبَّنَآ ءَامَنَّا فَٱكۡتُبۡنَا مَعَ ٱلشَّٰهِدِينَ ﴿٨٣﴾

84. «በአላህና ከውነትም በመጣልን ነገር የማናምን ጌታችንም ከመልካም ሰዎች ጋር ሊያስገባን የማንከጅል ለኛ ምን አለን» (ይላሉ)፡፡

وَمَا لَنَا لَا نُؤۡمِنُ بِٱللَّهِ وَمَا جَآءَنَا مِنَ ٱلۡحَقِّ وَنَطۡمَعُ أَن يُدۡخِلَنَا رَبُّنَا مَعَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿٨٤﴾

85. ባሉትም ምክንያት አላህ በስሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ መነዳቸው፡፡ ይህም የበጎ ሠሪዎች ዋጋ ነው፡፡

فَأَثَٰبَهُمُ ٱللَّهُ بِمَا قَالُواْ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَاۚ وَذَٰلِكَ جَزَآءُ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ﴿٨٥﴾

86. እነዚያም የካዱና በአንቀጾቻችን ያስተባበሉ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَحِيمِ ﴿٨٦﴾

87. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህ ለናንተ የፈቀደላችሁን ጣፋጮች እርም አታድርጉ፡፡ ወሰንንም አትለፉ፡፡ አላህ ወሰን አላፊዎችን አይወድምና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُحَرِّمُواْ طَيِّبَٰتِ مَآ أَحَلَّ ٱللَّهُ لَكُمۡ وَلَا تَعۡتَدُوٓاْۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُعۡتَدِينَ ﴿٨٧﴾

88. አላህም ከሰጣችሁ ሲሳይ የተፈቀደ ጣፋጭ ሲኾን ብሉ፡፡ ያንንም እናንተ በርሱ አማኞች የኾናችሁበትን አላህን ፍሩ፡፡

وَكُلُواْ مِمَّا رَزَقَكُمُ ٱللَّهُ حَلَٰلٗا طَيِّبٗاۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ ٱلَّذِيٓ أَنتُم بِهِۦ مُؤۡمِنُونَ ﴿٨٨﴾

89. አላህ በመሐላዎቻችሁ በውድቁ አይዛችሁም፡፡ ግን መሐላዎችን (ባሰባችሁት) ይይዛችኋል፡፡ ማስተሰሪያውም ቤተሰቦቻችሁን ከምትመግቡት ከመካከለኛው (ምግብ) ዐስርን ምስኪኖች ማብላት ወይም እነሱን ማልበስ ወይም ጫንቃን ነጻ ማውጣት ነው፤ (ከተባሉት አንዱን) ያላገኘም ሰው ሦስት ቀኖችን መጾም ነው፤ ይህ በማላችሁ ጊዜ የመሐላዎቻችሁ ማካካሻ ነው፡፡ መሐላዎቻችሁንም ጠብቁ፡፡ እንደዚሁ አላህ ለናንተ አንቀጾችን ያብራራል፡፡ እናንተ ልታመሰግኑ ይከጀላልና፡፡

لَا يُؤَاخِذُكُمُ ٱللَّهُ بِٱللَّغۡوِ فِيٓ أَيۡمَٰنِكُمۡ وَلَٰكِن يُؤَاخِذُكُم بِمَا عَقَّدتُّمُ ٱلۡأَيۡمَٰنَۖ فَكَفَّٰرَتُهُۥٓ إِطۡعَامُ عَشَرَةِ مَسَٰكِينَ مِنۡ أَوۡسَطِ مَا تُطۡعِمُونَ أَهۡلِيكُمۡ أَوۡ كِسۡوَتُهُمۡ أَوۡ تَحۡرِيرُ رَقَبَةٖۖ فَمَن لَّمۡ يَجِدۡ فَصِيَامُ ثَلَٰثَةِ أَيَّامٖۚ ذَٰلِكَ كَفَّٰرَةُ أَيۡمَٰنِكُمۡ إِذَا حَلَفۡتُمۡۚ وَٱحۡفَظُوٓاْ أَيۡمَٰنَكُمۡۚ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمۡ ءَايَٰتِهِۦ لَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ﴿٨٩﴾

90. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! የሚያሰክር መጠጥ ቁማርም ጣዖታትም አዝላምም ከሰይጣን ሥራ የኾኑ እርኩስ ብቻ ናቸው፡፡ (እርኩስን) ራቁትም ልትድኑ ይከጀላልና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِنَّمَا ٱلۡخَمۡرُ وَٱلۡمَيۡسِرُ وَٱلۡأَنصَابُ وَٱلۡأَزۡلَٰمُ رِجۡسٞ مِّنۡ عَمَلِ ٱلشَّيۡطَٰنِ فَٱجۡتَنِبُوهُ لَعَلَّكُمۡ تُفۡلِحُونَ ﴿٩٠﴾

91. ሰይጣን የሚፈልገው በሚያሰክር መጠጥና በቁማር በመካከላችሁ ጠብንና ጥላቻን ሊጥል አላህን ከማውሳትና ከስግደትም ሊያግዳችሁ ብቻ ነው። ታዲያ እናንተ (ከእነዚህ) ተከልካዮች ናችሁን (ተከልከሉ)።

إِنَّمَا يُرِيدُ ٱلشَّيۡطَٰنُ أَن يُوقِعَ بَيۡنَكُمُ ٱلۡعَدَٰوَةَ وَٱلۡبَغۡضَآءَ فِي ٱلۡخَمۡرِ وَٱلۡمَيۡسِرِ وَيَصُدَّكُمۡ عَن ذِكۡرِ ٱللَّهِ وَعَنِ ٱلصَّلَوٰةِۖ فَهَلۡ أَنتُم مُّنتَهُونَ ٩١

92. አላህንም ተገዙ። መልክተኛውንም ታዘዙ። ተጠንቀቁም። ብትሸሹም፤ በመልክተኛችን ላይ ያለበት ግልጽ ማድረስ ብቻ መኾኑን ዕወቁ።

وَأَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُواْ ٱلرَّسُولَ وَٱحۡذَرُواْۚ فَإِن تَوَلَّيۡتُمۡ فَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّمَا عَلَىٰ رَسُولِنَا ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ٩٢

93. በእነዚያ ባመኑትና በጎ ሥራዎችን በሠሩት ላይ (ከህደትን) በተጠነቀቁና ባመኑ መልካም ሥራዎችንም በሠሩ ከዚያም (የሚያሰክርንና ቁማርን) በተጠነቀቁና ባመኑ ከዚያም (ከተከለከለው ሁሉ) በተጠነቀቁና (ሥራን) ባሳመሩ ጊዜ (ከመከልከሉ በፊት) በተመገቡት ነገር ኃጢአት የለባቸውም። አላህም በጎ ሠሪዎችን ይወዳል።

لَيۡسَ عَلَى ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ جُنَاحٞ فِيمَا طَعِمُوٓاْ إِذَا مَا ٱتَّقَواْ وَّءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ ثُمَّ ٱتَّقَواْ وَّءَامَنُواْ ثُمَّ ٱتَّقَواْ وَّأَحۡسَنُواْۚ وَٱللَّهُ يُحِبُّ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٩٣

94. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! (በሐጅ ጊዜ) እጆቻችሁና ጦሮቻችሁ በሚያገኙት ታዳኝ አውሬ አላህ ይሞክራችኋል። በሩቅ ኾኖ የሚፈራውን ሰው አላህ ሊገልጽ (ይሞክራችኋል)። ከዚያም በኋላ ወሰንን ያለፈና ያደነ ሰው ለርሱ አሳማሚ ቅጣት አለው።

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَيَبۡلُوَنَّكُمُ ٱللَّهُ بِشَيۡءٖ مِّنَ ٱلصَّيۡدِ تَنَالُهُۥٓ أَيۡدِيكُمۡ وَرِمَاحُكُمۡ لِيَعۡلَمَ ٱللَّهُ مَن يَخَافُهُۥ بِٱلۡغَيۡبِۚ فَمَنِ ٱعۡتَدَىٰ بَعۡدَ ذَٰلِكَ فَلَهُۥ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٩٤

95. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እናንተ በሐጅ ሥራ ውስጥ ስትኾኑ አውሬን አትግደሉ። ከእናንተም እያወቀ የገደለው ሰው ቅጣቱ ከእናንተ ሁለት የትክክለኛነት ባለቤቶች የሚፈርዱበት የኾነ ወደ ካዕባ ደራሽ መሥዋዕት ሲኾን ከቤት እንስሳዎች የገደለውን ነገር ብጤ መስጠት ወይም ምስኪኖችን ማብላት ወይም የዚህን ልክ መጾም ማካካሻ ነው። (ይኸም) የሥራውን ከባድ ቅጣት እንዲቀምስ ነው። (ሳይከለከል በፊት) ካለፈው ነገር አላህ ይቅርታ አደረገ። (ወደ ጥፋቱም) የተመለሰም ሰው አላህ ከርሱ ይበቀላል። አላህም አሸናፊ የመበቀል ባለቤት ነው።

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَقۡتُلُواْ ٱلصَّيۡدَ وَأَنتُمۡ حُرُمٞۚ وَمَن قَتَلَهُۥ مِنكُم مُّتَعَمِّدٗا فَجَزَآءٞ مِّثۡلُ مَا قَتَلَ مِنَ ٱلنَّعَمِ يَحۡكُمُ بِهِۦ ذَوَا عَدۡلٖ مِّنكُمۡ هَدۡيَۢا بَٰلِغَ ٱلۡكَعۡبَةِ أَوۡ كَفَّٰرَةٞ طَعَامُ مَسَٰكِينَ أَوۡ عَدۡلُ ذَٰلِكَ صِيَامٗا لِّيَذُوقَ وَبَالَ أَمۡرِهِۦۗ عَفَا ٱللَّهُ عَمَّا سَلَفَۚ وَمَنۡ عَادَ فَيَنتَقِمُ ٱللَّهُ مِنۡهُۚ وَٱللَّهُ عَزِيزٞ ذُو ٱنتِقَامٍ ٩٥

96. የባሕር ታዳኝና ምግቡ ለእናንተም ለመንገደኞችም መጠቀሚያ ይኾን ዘንድ ለናንተ ተፈቀደ። በሐጅም ላይ እስካላችሁ ድረስ የየብስ አውሬ በናንተ ላይ እርም ተደረገ። ያንንም ወደርሱ የምትሰበሰቡበትን አላህን ፍሩ።

أُحِلَّ لَكُمۡ صَيۡدُ ٱلۡبَحۡرِ وَطَعَامُهُۥ مَتَٰعٗا لَّكُمۡ وَلِلسَّيَّارَةِۖ وَحُرِّمَ عَلَيۡكُمۡ صَيۡدُ ٱلۡبَرِّ مَا دُمۡتُمۡ حُرُمٗاۗ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ ٱلَّذِيٓ إِلَيۡهِ تُحۡشَرُونَ ٩٦

97. ከዕባን፣ የተከበረውን ቤት፣ ክልክል የኾነውንም ወር፣ መስዋዕቱንና ባለ ምልክቶቹንም መንጋዎች አላህ ለሰዎች መቋቋሚያ አደረገ፡፡ ይህ አላህ በሰማያት ያለውን ሁሉ በምድርም ያለውን ሁሉ የሚያውቅ መኾኑን አላህም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ መኾኑን እንድታውቁ ነው፡፡

۞ جَعَلَ ٱللَّهُ ٱلۡكَعۡبَةَ ٱلۡبَيۡتَ ٱلۡحَرَامَ قِيَٰمٗا لِّلنَّاسِ وَٱلشَّهۡرَ ٱلۡحَرَامَ وَٱلۡهَدۡيَ وَٱلۡقَلَٰٓئِدَۚ ذَٰلِكَ لِتَعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَأَنَّ ٱللَّهَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٌ ٩٧

98. አላህ ቅጣተ ብርቱ መኾኑን አላህም መሓሪ አዛኝ መኾኑን እወቁ፡፡

ٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ وَأَنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٩٨

99. በመልክተኛው ላይ ማድረስ እንጅ ሌላ የለበትም፡፡ አላህም የምትገልጹትን ነገር የምትደብቁትንም ሁሉ ያውቃል፡፡

مَّا عَلَى ٱلرَّسُولِ إِلَّا ٱلۡبَلَٰغُۗ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ مَا تُبۡدُونَ وَمَا تَكۡتُمُونَ ٩٩

100. «የመጥፎው (ገንዘብ) ብዛት ቢያስደንቃችሁም እንኳ መጥፎውና ጥሩው አይስተካከሉም፡፡ ባለልቦች ሆይ! አላህንም ፍሩ፤ እናንተ ልትድኑ ይከጃላልና፤» በላቸው፡፡

قُل لَّا يَسۡتَوِي ٱلۡخَبِيثُ وَٱلطَّيِّبُ وَلَوۡ أَعۡجَبَكَ كَثۡرَةُ ٱلۡخَبِيثِۚ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ يَٰٓأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ لَعَلَّكُمۡ تُفۡلِحُونَ ١٠٠

101. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ለእናንተ ቢገለጹ ከሚያስከፏችሁ ነገሮች አትጠይቁ፡፡ ቁርኣንም በሚወርድበት ጊዜ ከእርሷ ብትጠይቁ ለናንተ ትገለጻለች፤ ከእርሷ አላህ ይቅርታ አደረገ፡፡ አላህም መሓሪ ታጋሽ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَسۡـَٔلُواْ عَنۡ أَشۡيَآءَ إِن تُبۡدَ لَكُمۡ تَسُؤۡكُمۡ وَإِن تَسۡـَٔلُواْ عَنۡهَا حِينَ يُنَزَّلُ ٱلۡقُرۡءَانُ تُبۡدَ لَكُمۡ عَفَا ٱللَّهُ عَنۡهَاۗ وَٱللَّهُ غَفُورٌ حَلِيمٞ ١٠١

102. ከናንተም በፊት ሕዝቦች በእርግጥ ጠየቋት፡፡ ከዚያም በእርሷ (ምክንያት) ከሓዲዎች ኾኑ፡፡

قَدۡ سَأَلَهَا قَوۡمٞ مِّن قَبۡلِكُمۡ ثُمَّ أَصۡبَحُواْ بِهَا كَٰفِرِينَ ١٠٢

103. ከበሒራ ከሳኢባም ከወሲላም ከሓምም አላህ ምንንም (ሕግ) አላደረገም፡፡ ግን እነዚያ የካዱት በአላህ ላይ ውሸትን ይቀጣጥፋሉ፡፡ አብዛኞቻቸውም አያውቁም፡፡

مَا جَعَلَ ٱللَّهُ مِنۢ بَحِيرَةٖ وَلَا سَآئِبَةٖ وَلَا وَصِيلَةٖ وَلَا حَامٖ وَلَٰكِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يَفۡتَرُونَ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَۖ وَأَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡقِلُونَ ١٠٣

104. ለእነርሱም አላህ ወደ አወረደውና ወደ መልክተኛው ኑ በተባሉ ጊዜ «አባቶቻችንን በርሱ ላይ ያገኘንበት ነገር ይበቃናል» ይላሉ፡፡ አባቶቻቸው ምንም የማያውቁና የማይመሩ ቢኾኑም (ይኸንን ማለት ይበቃቸዋልን)

وَإِذَا قِيلَ لَهُمۡ تَعَالَوۡاْ إِلَىٰ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ وَإِلَى ٱلرَّسُولِ قَالُواْ حَسۡبُنَا مَا وَجَدۡنَا عَلَيۡهِ ءَابَآءَنَآۚ أَوَلَوۡ كَانَ ءَابَآؤُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ شَيۡـٔٗا وَلَا يَهۡتَدُونَ ١٠٤

105. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ነፍሶቻችሁን (ከእሳት) ያዙ፤ (ጠብቁ)፡፡ በተመራችሁ ጊዜ የተሳሳተ ሰው አይጎዳችሁም፡፡ የሁላችሁም መመለሻ ወደ አላህ ብቻ ነው፡፡ ትሠሩትም የነበራችሁትን ሁሉ ይነግራችኋል፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ عَلَيۡكُمۡ أَنفُسَكُمۡۖ لَا يَضُرُّكُم مَّن ضَلَّ إِذَا ٱهۡتَدَيۡتُمۡۚ إِلَى ٱللَّهِ مَرۡجِعُكُمۡ جَمِيعٗا فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ١٠٥

106. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አንዳችሁን ሞት በመጣበት ጊዜ በኑዛዜ ወቅት የመካከላችሁ ምስክርነት ከእናንተ ሁለት የትክክለኛነት ባለቤቶች የኾኑ ሰዎች ወይም በምድር ብትጓዙና የሞት አደጋ ብትነካችሁ ከሌሎቻችሁ የኾኑ ሁለት ሌሎች ሰዎች (መመስከር) ነው፡፡ ብትጠራጠሩ ከሶላት (ከዐሱር) በኋላ ታቆሟቸውና (የሚመሰክርለት ሰው) የዝምድና ባለቤት ቢኾንም እንኳ «በርሱ ዋጋን አንገዛም የአላህንም ምስክርነት አንደብቅም፤ ያን ጊዜ (ደብቀን ብንገኝ) እኛ ከኃጢአተኞች ነን» ብለው በአላህ ስም ይምላሉ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ شَهَٰدَةُ بَيۡنِكُمۡ إِذَا حَضَرَ أَحَدَكُمُ ٱلۡمَوۡتُ حِينَ ٱلۡوَصِيَّةِ ٱثۡنَانِ ذَوَا عَدۡلٖ مِّنكُمۡ أَوۡ ءَاخَرَانِ مِنۡ غَيۡرِكُمۡ إِنۡ أَنتُمۡ ضَرَبۡتُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَأَصَٰبَتۡكُم مُّصِيبَةُ ٱلۡمَوۡتِۚ تَحۡبِسُونَهُمَا مِنۢ بَعۡدِ ٱلصَّلَوٰةِ فَيُقۡسِمَانِ بِٱللَّهِ إِنِ ٱرۡتَبۡتُمۡ لَا نَشۡتَرِي بِهِۦ ثَمَنٗا وَلَوۡ كَانَ ذَا قُرۡبَىٰ وَلَا نَكۡتُمُ شَهَٰدَةَ ٱللَّهِ إِنَّآ إِذٗا لَّمِنَ ٱلۡأٓثِمِينَ ١٠٦

107. እነርሱም ኃጢአትን (በውሸት መስከረው) የተገቡ መኾናቸው ቢታወቅ ከእነዚያ (ለሟቹ) ቅርቦች በመኾን (ውርስ) ከተገባቸው የኾኑ ሁለት ሌሎች ሰዎች በስፍራቸው (በምስክሮች ስፍራ) ይቆሙና «ምስክርነታችን ከእነሱ ምስክርነት ይልቅ እውነት ነው ወሰንም አላለፍንም ያን ጊዜ እኛ ከበዳዮች ነን» ሲሉ በአላህ ይምላሉ፡፡

فَإِنۡ عُثِرَ عَلَىٰٓ أَنَّهُمَا ٱسۡتَحَقَّآ إِثۡمٗا فَـَٔاخَرَانِ يَقُومَانِ مَقَامَهُمَا مِنَ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَحَقَّ عَلَيۡهِمُ ٱلۡأَوۡلَيَٰنِ فَيُقۡسِمَانِ بِٱللَّهِ لَشَهَٰدَتُنَآ أَحَقُّ مِن شَهَٰدَتِهِمَا وَمَا ٱعۡتَدَيۡنَآ إِنَّآ إِذٗا لَّمِنَ ٱلظَّـٰلِمِينَ ١٠٧

108. ይህ ምስክርነትን በተገቢዋ ላይ ለማምጣታቸው ወይም ከመሐላዎቻቸው በኋላ የመሐላዎችን (ወደ ወራሾች) መመለስን ለመፍራት በጣም የቀረበ ነው፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ ስሙም፡፡ አላህም አመጸኞች ሕዝቦችን አይመራም፡፡

ذَٰلِكَ أَدۡنَىٰٓ أَن يَأۡتُواْ بِٱلشَّهَٰدَةِ عَلَىٰ وَجۡهِهَآ أَوۡ يَخَافُوٓاْ أَن تُرَدَّ أَيۡمَٰنُۢ بَعۡدَ أَيۡمَٰنِهِمۡۗ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَٱسۡمَعُواْۗ وَٱللَّهُ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡفَٰسِقِينَ ١٠٨

109. አላህ መልክተኞቹን የሚሰበስብበትንና «ምን መልስ ተሰጣችሁ» የሚልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ «ለእኛ ምንም ዕውቀት የለንም አንተ ሩቆችን በጣም ዐዋቂ አንተ ብቻ ነህ» ይላሉ፡፡

۞يَوۡمَ يَجۡمَعُ ٱللَّهُ ٱلرُّسُلَ فَيَقُولُ مَاذَآ أُجِبۡتُمۡۖ قَالُواْ لَا عِلۡمَ لَنَآۖ إِنَّكَ أَنتَ عَلَّـٰمُ ٱلۡغُيُوبِ ١٠٩

110. አላህ በሚል ጊዜ (አስታውስ)፡- «የመርየም ልጅ ዒሳ ሆይ! በአንተና በእናትህ ላይ (የዋልኩላችሁን) ጸጋዬን አስታውስ፡፡ በሕፃንነትና በከፈኒሳነት (የበሰለ ሰው ኾነህ) ሰዎችን የምትናገር ስትኾን በቅዱስ መንፈስ (በገብሬል) ባበረታሁህ ጊዜ፤ ጽሕፈትንና ጥበብንም ተውራትንና ኢንጂልንም ባስተማርኩህ ጊዜ፣ ከጭቃም የወፍ ቅርጽ ብጤ በፈቃዴ በምትሠራና በውስጧ በምትነፋ በፈቃዴም ወፍ በምትኾን ጊዜ፣ ዕውርም ኾኖ የተወለደንና ለምጻምንም በፈቃዴ በምታሽር ጊዜ፣ ሙታንንም በፈቃዴ (ከመቃብራቸው) በምታወጣ ጊዜ፣ የእስራኤልንም ልጆች በተአምራት በመጣህባቸውና ከእነሱ እነዚያ የካዱት ይህ ግልጽ ድግምት እንጅ ሌላ አይደለም ባሉ ጊዜ፣ (ሊገድሉህ ሲያስቡህ) ከአንተ ላይ በከለከልኩልህም ጊዜ (ያደረግሁልህን ውለታ አስታውስ)፡፡»

إِذْ قَالَ ٱللَّهُ يَٰعِيسَى ٱبْنَ مَرْيَمَ ٱذْكُرْ نِعْمَتِى عَلَيْكَ وَعَلَىٰ وَٰلِدَتِكَ إِذْ أَيَّدتُّكَ بِرُوحِ ٱلْقُدُسِ تُكَلِّمُ ٱلنَّاسَ فِى ٱلْمَهْدِ وَكَهْلًا ۖ وَإِذْ عَلَّمْتُكَ ٱلْكِتَٰبَ وَٱلْحِكْمَةَ وَٱلتَّوْرَىٰةَ وَٱلْإِنجِيلَ ۖ وَإِذْ تَخْلُقُ مِنَ ٱلطِّينِ كَهَيْـَٔةِ ٱلطَّيْرِ بِإِذْنِى فَتَنفُخُ فِيهَا فَتَكُونُ طَيْرًۢا بِإِذْنِى ۖ وَتُبْرِئُ ٱلْأَكْمَهَ وَٱلْأَبْرَصَ بِإِذْنِى ۖ وَإِذْ تُخْرِجُ ٱلْمَوْتَىٰ بِإِذْنِى ۖ وَإِذْ كَفَفْتُ بَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ عَنكَ إِذْ جِئْتَهُم بِٱلْبَيِّنَٰتِ فَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ مِنْهُمْ إِنْ هَٰذَآ إِلَّا سِحْرٌ مُّبِينٌ ١١٠

111. ወደ ሐዋርያትም «በኔና በመልክተኛዬ እመኑ» በማለት ባዘዝኩ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «አመንን፤ እኛ ሙስሊሞች መኾናችንን መስክር» አሉ፡፡

وَإِذْ أَوْحَيْتُ إِلَى ٱلْحَوَارِيِّـۧنَ أَنْ ءَامِنُوا۟ بِى وَبِرَسُولِى قَالُوٓا۟ ءَامَنَّا وَٱشْهَدْ بِأَنَّنَا مُسْلِمُونَ ١١١

112. ሐዋርያት፡- «የመርየም ልጅ ዒሳ ሆይ! ጌታህ በእኛ ላይ ከሰማይ ማእድን ሊያወርድልን ይችላልን» ባሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «ምእመናን እንደ ኾናችሁ አላህን ፍሩ» አላቸው፡፡

إِذْ قَالَ ٱلْحَوَارِيُّونَ يَٰعِيسَى ٱبْنَ مَرْيَمَ هَلْ يَسْتَطِيعُ رَبُّكَ أَن يُنَزِّلَ عَلَيْنَا مَآئِدَةً مِّنَ ٱلسَّمَآءِ ۖ قَالَ ٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ إِن كُنتُم مُّؤْمِنِينَ ١١٢

113. «ከእርሷ ልንበላ ልቦቻችንም ሊረኩ እውነት ያልከንም መኾንህን ልናውቅና በእርሷም ላይ ከመስካሪዎች ልንኾን እንፈልጋለን» አሉ፡፡

قَالُوا۟ نُرِيدُ أَن نَّأْكُلَ مِنْهَا وَتَطْمَئِنَّ قُلُوبُنَا وَنَعْلَمَ أَن قَدْ صَدَقْتَنَا وَنَكُونَ عَلَيْهَا مِنَ ٱلشَّٰهِدِينَ ١١٣

114. የመርየም ልጅ ዒሳ አለ፡- «ጌታችን አላህ ሆይ! ለእኛ ለመጀመሪያዎቻችንና ለመጨረሻዎቻችን ባዕል (መደሰቻ) የምትኾንን ከአንተም ተአምር የኾነችን ማእድ ከሰማይ በእኛ ላይ አውርድ፡፡ ስጠንም፡፡ አንተ ከሰጪዎች ሁሉ በላጭ ነህና፡፡»

قَالَ عِيسَى ٱبْنُ مَرْيَمَ ٱللَّهُمَّ رَبَّنَآ أَنزِلْ عَلَيْنَا مَآئِدَةً مِّنَ ٱلسَّمَآءِ تَكُونُ لَنَا عِيدًا لِّأَوَّلِنَا وَءَاخِرِنَا وَءَايَةً مِّنكَ ۖ وَٱرْزُقْنَا وَأَنتَ خَيْرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ١١٤

115. አላህ፡- «እኔ (ማእድዋን) በናንተ ላይ አውራጅዋ ነኝ፡፡ በኋላም ከእናንተ የሚክድ ሰው እኔ ከዓለማት አንድንም የማልቀጣውን ቅጣት እቀጣዋለሁ» አለ፡፡

قَالَ ٱللَّهُ إِنِّى مُنَزِّلُهَا عَلَيْكُمْ ۖ فَمَن يَكْفُرْ بَعْدُ مِنكُمْ فَإِنِّىٓ أُعَذِّبُهُۥ عَذَابًا لَّآ أُعَذِّبُهُۥٓ أَحَدًا مِّنَ ٱلْعَٰلَمِينَ ١١٥

وَإِذۡ قَالَ ٱللَّهُ يَٰعِيسَى ٱبۡنَ مَرۡيَمَ ءَأَنتَ قُلۡتَ لِلنَّاسِ ٱتَّخِذُونِي وَأُمِّيَ إِلَٰهَيۡنِ مِن دُونِ ٱللَّهِۖ قَالَ سُبۡحَٰنَكَ مَا يَكُونُ لِيٓ أَنۡ أَقُولَ مَا لَيۡسَ لِي بِحَقٍّۚ إِن كُنتُ قُلۡتُهُۥ فَقَدۡ عَلِمۡتَهُۥۚ تَعۡلَمُ مَا فِي نَفۡسِي وَلَآ أَعۡلَمُ مَا فِي نَفۡسِكَۚ إِنَّكَ أَنتَ عَلَّٰمُ ٱلۡغُيُوبِ ١١٦

116. አላህም፡- «የመርየም ልጅ ዒሳ ሆይ! አንተ ለሰዎቹ፡- እኔንና እናቴን ከአላህ ሌላ ሁለት አምላኮች አድርጋችሁ ያዙ ብላሃልን» በሚለው ጊዜ (አስታውስ)፡ ፡ «ጥራት ይገባህ፤ ለእኔ ተገቢዬ ያልኾነን ነገር ማለት ለኔ አይገባኝም፡፡ ብዬው እንደ ኾነም በእርግጥ ዐውቀኸዋል፡፡ በነፍሴ ውስጥ ያለውን ሁሉ ታውቃለህ፡ ፡ ግን አንተ ዘንድ ያለውን አላውቅም፡፡ አንተ ሩቆችን ሁሉ በጣም ዐዋቂ አንተ ብቻ ነህና» ይላል፡፡

مَا قُلۡتُ لَهُمۡ إِلَّا مَآ أَمَرۡتَنِي بِهِۦٓ أَنِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ رَبِّي وَرَبَّكُمۡۚ وَكُنتُ عَلَيۡهِمۡ شَهِيدٗا مَّا دُمۡتُ فِيهِمۡۖ فَلَمَّا تَوَفَّيۡتَنِي كُنتَ أَنتَ ٱلرَّقِيبَ عَلَيۡهِمۡۚ وَأَنتَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ شَهِيدٌ ١١٧

117. «በእርሱ ያዘዝከኝን ቃል ጌታዬንና ጌታችሁን አላህን ተገዙ ማለትን እንጂ ለነርሱ ሌላ አላልኩም፡፡ በውስጣቸውም እስካለሁ ድረስ በነርሱ ላይ ተጣባበቂ ነበርኩ፡፡ በተሞላኸኝም ጊዜ (ባነሳኸኝ ጊዜ) አንተ በነሱ ላይ ተጠባባቂ ነበርክ፡፡ አንተም በነገሩ ሁሉ ላይ ዐዋቂ ነህ፡፡»

إِن تُعَذِّبۡهُمۡ فَإِنَّهُمۡ عِبَادُكَۖ وَإِن تَغۡفِرۡ لَهُمۡ فَإِنَّكَ أَنتَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ١١٨

118. «ብትቀጣቸው እነርሱ ባሮችህ ናቸው፡፡ ለነርሱ ብትምርም አንተ አሸናፊው ጥበበኛው ነህ» (ይላል)፡፡

قَالَ ٱللَّهُ هَٰذَا يَوۡمُ يَنفَعُ ٱلصَّٰدِقِينَ صِدۡقُهُمۡۚ لَهُمۡ جَنَّٰتٞ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۖ رَّضِيَ ٱللَّهُ عَنۡهُمۡ وَرَضُواْ عَنۡهُۚ ذَٰلِكَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ١١٩

119. አላህ ይላል፡- «ይህ እውነተኞችን እውነታቸው የሚጠቅምበት ቀን ነው፡፡ ለእነርሱ በሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው በውስጣቸው ሁልጊዜ ዘውታሪዎች ሲኾኑ የሚኖሩባቸው ገነቶች አሉዋቸው፡፡ አላህ ከእነሱ ወደደ፤ እነርሱም ከእርሱ ወደዱ፤ ይህ ታላቅ ዕድል ነው፡፡»

## سورة الأنعام

## ሱረቱ አል-አንዓም

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَجَعَلَ ٱلظُّلُمَٰتِ وَٱلنُّورَۖ ثُمَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِرَبِّهِمۡ يَعۡدِلُونَ ١

1. ምስጋና ለዚያ ሰማያትንና ምድርን ለፈጠረው ጨለማዎችንና ብርሃንንም ላደረገው ለአላህ የተገባ ነው፡፡ ከዚያም እነዚያ የካዱት (ጣዖታትን በጌታቸው) ያስተካክላሉ፡፡

هُوَ ٱلَّذِى خَلَقَكُم مِّن طِينٍ ثُمَّ قَضَىٰٓ أَجَلًاۖ وَأَجَلٌ مُّسَمًّى عِندَهُۥۖ ثُمَّ أَنتُمْ تَمْتَرُونَ ﴿٢﴾

2. እርሱ ያ ከጭቃ የፈጠራችሁ ከዚያም (የሞት) ጊዜን የወሰነ ነው፡፡ እርሱም ዘንድ (ለትንሣኤ) የተወሰነ ጊዜ አልለ፡፡ ከዚያም እናንተ (በመቀስቀሳችሁ) ትጠራጠራላችሁ፡፡

وَهُوَ ٱللَّهُ فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَفِى ٱلْأَرْضِ يَعْلَمُ سِرَّكُمْ وَجَهْرَكُمْ وَيَعْلَمُ مَا تَكْسِبُونَ ﴿٣﴾

3. እርሱም ያ በሰማያትና በምድር (ሊግገዙት የሚገባው) አላህ ነው፡፡ ምስጢራችሁን ግልጻችሁንም ያውቃል፡፡ የምትሠሩትንም ሁሉ ያውቃል፡፡

وَمَا تَأْتِيهِم مِّنْ ءَايَةٍ مِّنْ ءَايَٰتِ رَبِّهِمْ إِلَّا كَانُوا۟ عَنْهَا مُعْرِضِينَ ﴿٤﴾

4. ከጌታቸውም አንቀጾች አንዲትም አንቀጽ አትመጣቸውም ከርሷ የሚሸሹ ቢኾኑ እንጅ፡፡

فَقَدْ كَذَّبُوا۟ بِٱلْحَقِّ لَمَّا جَآءَهُمْ فَسَوْفَ يَأْتِيهِمْ أَنۢبَٰٓؤُا۟ مَا كَانُوا۟ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ﴿٥﴾

5. በእውነቱም (ቁርአን) በመጣላቸው ጊዜ በእርግጥ አስተባበሉ፡፡ በእርሱም ይሳለቁበት የነበሩት ነገር ዜናዎች (ቅጣት) በእርግጥ ይመጣባቸዋል፡፡

أَلَمْ يَرَوْا۟ كَمْ أَهْلَكْنَا مِن قَبْلِهِم مِّن قَرْنٍ مَّكَّنَّٰهُمْ فِى ٱلْأَرْضِ مَا لَمْ نُمَكِّن لَّكُمْ وَأَرْسَلْنَا ٱلسَّمَآءَ عَلَيْهِم مِّدْرَارًا وَجَعَلْنَا ٱلْأَنْهَٰرَ تَجْرِى مِن تَحْتِهِمْ فَأَهْلَكْنَٰهُم بِذُنُوبِهِمْ وَأَنشَأْنَا مِنۢ بَعْدِهِمْ قَرْنًا ءَاخَرِينَ ﴿٦﴾

6. ከበፊታቸው ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙዎችን ማጥፋታችንን አላዩምን ለእናንተ ያላስመቸነውን (ለእነርሱ) በምድር ውስጥ አስመቸናቸው፡፡ በእነርሱም ላይ ዝናምን የተከታተለ ሲኾን ላክን፡፡ ወንዞችንም በሥራቸው እንዲፈሱ አደረግን፡፡ በኃጢአቶቻቸውም አጠፋናቸው፡፡ ከኋላቸውም ሌሎችን የክፍለ ዘመን ሰዎች አስገኘን፡፡

وَلَوْ نَزَّلْنَا عَلَيْكَ كِتَٰبًا فِى قِرْطَاسٍ فَلَمَسُوهُ بِأَيْدِيهِمْ لَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ إِنْ هَٰذَآ إِلَّا سِحْرٌ مُّبِينٌ ﴿٧﴾

7. ባንተም ላይ በወረቀት የተጻፈን መጽሐፍ ባወረድንና በእጆቻቸው በነኩት ኖሮ እነዚያ የካዱት ሰዎች «ይህ ግልጽ ድግምት እንጅ ሌላ አይደለም» ባሉ ነበር፡፡

وَقَالُوا۟ لَوْلَآ أُنزِلَ عَلَيْهِ مَلَكٌۖ وَلَوْ أَنزَلْنَا مَلَكًا لَّقُضِىَ ٱلْأَمْرُ ثُمَّ لَا يُنظَرُونَ ﴿٨﴾

8. «በእርሱም (በሙሐመድ) ላይ መልአክ አይወረድለትም ኖሮአልን» አሉ፡፡ መልአክን ባወረድንም ኖሮ (ባያምኑ በጥፋታቸው) ነገሩ በተፈረደ ነበር፡፡ ከዚያም አይቆዩም ነበር፡፡

وَلَوْ جَعَلْنَٰهُ مَلَكًا لَّجَعَلْنَٰهُ رَجُلًا وَلَلَبَسْنَا عَلَيْهِم مَّا يَلْبِسُونَ ﴿٩﴾

9. (መልክተኛውን) መልአክም ባደረግነው ኖሮ ወንድ (በሰው ምስል) ባደረግነው ነበር፡፡ በእነርሱም ላይ የሚያመሳስሉትን ነገር ባመሳሰልንባቸው ነበር፡፡

وَلَقَدِ ٱسْتُهْزِئَ بِرُسُلٍ مِّن قَبْلِكَ فَحَاقَ بِٱلَّذِينَ سَخِرُوا۟ مِنْهُم مَّا كَانُوا۟ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ﴿١٠﴾

10. ካንተ በፊትም በመልክተኞች በእርግጥ ተላግጧል፡ ፡ በእነዚያም ከእነሱ ባላገጡት ላይ በእርሱ ያላግጡ የነበሩት ነገር (ቅጣት) ወረደባቸው፡፡

قُلْ سِيرُوا۟ فِى ٱلْأَرْضِ ثُمَّ ٱنظُرُوا۟ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلْمُكَذِّبِينَ ﴿١١﴾

11. «በምድር ላይ ኺዱ የአስተባባዮችም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከቱ» በላቸው፡፡

12. «በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የማን ነው» በላቸው፡፡ (ሌላ መልስ የለምና) «የአላህ ነው» በል፡፡ «በነፍሱ ላይ እዝነትን ጻፈ፡፡ በትንሣኤ ቀን በእርሱ ጥርጥር የሌለበት ሲኾን በእርግጥ ይሰበስባችኋል፡፡ እነዚያ ነፍሶቻቸውን ያከሰሩ ናቸው፤ እነርሱም አያምኑም፡፡

قُل لِّمَن مَّا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ قُل لِّلَّهِۚ كَتَبَ عَلَىٰ نَفۡسِهِ ٱلرَّحۡمَةَۚ لَيَجۡمَعَنَّكُمۡ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ لَا رَيۡبَ فِيهِۚ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ فَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿١٢﴾

13. በሌሊትና በቀንም ጸጥ ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ ነው፡፡ እርሱም ሰሚው ዐዋቂ ነው፡፡»

۞وَلَهُۥ مَا سَكَنَ فِي ٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِۚ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿١٣﴾

14. «ሰማያትንና ምድርን ፈጣሪ ከኾነው አላህ እርሱ የሚመግብ የማይመገብም ሲኾን ሌላን አምላክ እይዛለሁን» በላቸው፡፡ «እኔ መጀመሪያ ትእዛዝን ከተቀበለ ሰው ልኾን ታዘዝኩ፡፡ ከአጋሪዎችም ፈጽሞ አትኹን (ተብያለሁ)» በላቸው፡፡

قُلۡ أَغَيۡرَ ٱللَّهِ أَتَّخِذُ وَلِيّٗا فَاطِرِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَهُوَ يُطۡعِمُ وَلَا يُطۡعَمُۗ قُلۡ إِنِّيٓ أُمِرۡتُ أَنۡ أَكُونَ أَوَّلَ مَنۡ أَسۡلَمَۖ وَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ﴿١٤﴾

15. «እኔ በጌታዬ ባምጽ የታላቁን ቀን ቅጣት እፈራለሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنِّيٓ أَخَافُ إِنۡ عَصَيۡتُ رَبِّي عَذَابَ يَوۡمٍ عَظِيمٖ ﴿١٥﴾

16. በዚያ ቀን ከእርሱ ላይ (ቅጣት) የሚመለስለት ሰው (አላህ) በእርግጥ አዘነለት፡፡ ይህም ግልጽ ማግኘት ነው፡፡

مَّن يُصۡرَفۡ عَنۡهُ يَوۡمَئِذٖ فَقَدۡ رَحِمَهُۥۚ وَذَٰلِكَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡمُبِينُ ﴿١٦﴾

17. አላህም በጉዳት ቢነካህ ለእርሱ (ለጉዳቱ) ከእርሱ በቀር ሌላ አስወጋጅ የለም፡፡ በበጎም ነገር ቢነካህ እርሱ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَإِن يَمۡسَسۡكَ ٱللَّهُ بِضُرّٖ فَلَا كَاشِفَ لَهُۥٓ إِلَّا هُوَۖ وَإِن يَمۡسَسۡكَ بِخَيۡرٖ فَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ﴿١٧﴾

18. እርሱም ከባሮቹ በላይ ሲኾን አሸናፊ ነው፡፡ እርሱም ጥበበኛው ውስጥ ዐዋቂው ነው፡፡

وَهُوَ ٱلۡقَاهِرُ فَوۡقَ عِبَادِهِۦۚ وَهُوَ ٱلۡحَكِيمُ ٱلۡخَبِيرُ ﴿١٨﴾

19. «በምስክርነት ከነገሩ ሁሉ ይበልጥ ታላቅ ማነው» በላቸው፡፡ (ሌላ መልስ የለምና) «አላህ ነው፡፡ በእኔና በእናንተ መካከል መስካሪ ነው፡፡ ይህም ቁርኣን እናንተንና የደረሰውን ሰው ሁሉ በርሱ ላስፈራራበት ወደኔ ተወረደ፡፡ ከአላህ ጋር ሌሎች አማልክት መኖራቸውን እናንተ ትመሰክራላችሁን» በላቸው፡፡ «እኔ አልመሰክርም» በላቸው፡፡ «እርሱ አንድ አምላክ ብቻ ነው፡፡ እኔም ከምታጋሩት ነገር ንጹሕ ነኝ» በላቸው፡፡

قُلۡ أَيُّ شَيۡءٍ أَكۡبَرُ شَهَٰدَةٗۖ قُلِ ٱللَّهُۖ شَهِيدُۢ بَيۡنِي وَبَيۡنَكُمۡۚ وَأُوحِيَ إِلَيَّ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانُ لِأُنذِرَكُم بِهِۦ وَمَنۢ بَلَغَۚ أَئِنَّكُمۡ لَتَشۡهَدُونَ أَنَّ مَعَ ٱللَّهِ ءَالِهَةً أُخۡرَىٰۚ قُل لَّآ أَشۡهَدُۚ قُلۡ إِنَّمَا هُوَ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞ وَإِنَّنِي بَرِيٓءٞ مِّمَّا تُشۡرِكُونَ ﴿١٩﴾

20. እነዚያ መጽሐፍን የሰጠናቸው ልጆቻቸውን እንደሚያውቁ (ሙሐመድን) ያውቁታል፡፡ እነዚያ ከእነርሱ ውስጥ ነፍሶቻቸውን ያከሰሩት እነርሱ አያምኑም፡፡

ٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يَعۡرِفُونَهُۥ كَمَا يَعۡرِفُونَ أَبۡنَآءَهُمُۘ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ فَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿٢٠﴾

21. በአላህም ላይ ውሸትን ከቀጣጠፈ ወይም በአንቀጾቹ ካስተባበለ ሰው ይበልጥ በደለኛ ማነው እነሆ በደለኞች አይድኑም፡፡

وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا أَوۡ كَذَّبَ بِـَٔايَٰتِهِۦٓۚ إِنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلظَّٰلِمُونَ ﴿٢١﴾

22. ሁላቸውንም የምንሰበስብበትንና ከዚያም ለእነዚያ (ጣዖታትን) ለአጋሩት እነዚያ (ለአላህ) ተጋሪዎች ናቸው ብላችሁ ታስቧቸው የነበራችሁት ተጋሪዎቻችሁ የት ናቸው የምንልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ نَحۡشُرُهُمۡ جَمِيعٗا ثُمَّ نَقُولُ لِلَّذِينَ أَشۡرَكُوٓاْ أَيۡنَ شُرَكَآؤُكُمُ ٱلَّذِينَ كُنتُمۡ تَزۡعُمُونَ ٢٢

23. ከዚያም መልሳቸው «በጌታችን በአላህ ይኹንብን አጋሪዎች አልነበርንም» ማለት እንጅ ሌላ አትኾንም፡፡

ثُمَّ لَمۡ تَكُن فِتۡنَتُهُمۡ إِلَّآ أَن قَالُواْ وَٱللَّهِ رَبِّنَا مَا كُنَّا مُشۡرِكِينَ ٢٣

24. በነፍሳቸው ላይ እንዴት እንደ ዋሹና ይቀጣጥፉት የነበሩት ነገር ከእነሱ እንዴት እንደ ተሰወረ ተመልከት፡፡

ٱنظُرۡ كَيۡفَ كَذَبُواْ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡۚ وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ٢٤

25. ከእነርሱም ወደ አንተ የሚያዳምጥ ሰው አልለ፡፡ በልቦቻቸውም ላይ እንዳያውቁት ሺፋኖችን በጆሮዎቻቸውም ላይ ድንቁርናን አደረግን፡፡ ተዓምርንም ሁሉ ቢያዩ በርሷ አያምኑም፡፡ በመጡህም ጊዜ የሚከራከሩህ ሲኾኑ እነዚያ የካዱት «ይህ (ቁርኣን) የቀድሞዎቹ ሰዎች ጽሑፍ ተረቶች እንጅ ሌላ አይደለም» ይላሉ፡፡

وَمِنۡهُم مَّن يَسۡتَمِعُ إِلَيۡكَۖ وَجَعَلۡنَا عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ أَكِنَّةً أَن يَفۡقَهُوهُ وَفِيٓ ءَاذَانِهِمۡ وَقۡرٗاۚ وَإِن يَرَوۡاْ كُلَّ ءَايَةٖ لَّا يُؤۡمِنُواْ بِهَاۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءُوكَ يُجَٰدِلُونَكَ يَقُولُ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّآ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٢٥

26. እነርሱም (ሰዎችን) ከእርሱ ይከለክላሉ፡፡ ከእርሱም ይርቃሉ፡፡ ነፍሶቻቸውንም እንጂ ሌላን አያጠፉም፤ ግን አያውቁም፡፡

وَهُمۡ يَنۡهَوۡنَ عَنۡهُ وَيَنۡـَٔوۡنَ عَنۡهُۖ وَإِن يُهۡلِكُونَ إِلَّآ أَنفُسَهُمۡ وَمَا يَشۡعُرُونَ ٢٦

27. በእሳትም ላይ በተቆሙ ጊዜ ምነው (ወደ ምድረ ዓለም) በተመለስን በጌታችንም አንቀጾች ባላስተባበልን ከምእምናንም በኾንን ዋ ምኞታችን! ባሉ ጊዜ ብታይ ኖሮ (የሚያሰደነግጥን ነገር ባየህ ነበር)፡፡

وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذۡ وُقِفُواْ عَلَى ٱلنَّارِ فَقَالُواْ يَٰلَيۡتَنَا نُرَدُّ وَلَا نُكَذِّبَ بِـَٔايَٰتِ رَبِّنَا وَنَكُونَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٢٧

28. ይልቁንም ከዚህ በፊት ይደብቁት የነበሩት ሁሉ ለእነርሱ ተገለጸ፡፡ (ወደምድረ ዓለም) በተመለሱም ኖሮ ከእርሱ ወደ ተከለከሉት ነገር በተመለሱ ነበር፡፡ እነሱም በእርግጥ ውሸታሞች ናቸው፡፡

بَلۡ بَدَا لَهُم مَّا كَانُواْ يُخۡفُونَ مِن قَبۡلُۖ وَلَوۡ رُدُّواْ لَعَادُواْ لِمَا نُهُواْ عَنۡهُ وَإِنَّهُمۡ لَكَٰذِبُونَ ٢٨

29. እርሷም (ሕይወት) «የቅርቢቱ ሕይወታችን እንጅ ሌላ አይደለችም እኛም ተቀስቀቃሾች አይደለንም» አሉ፡፡

وَقَالُوٓاْ إِنۡ هِيَ إِلَّا حَيَاتُنَا ٱلدُّنۡيَا وَمَا نَحۡنُ بِمَبۡعُوثِينَ ٢٩

30. በጌታቸውም ላይ (ለምርመራ) በተቆሙ ጊዜ ብታይ ኖሮ (አስደንጋጭን ነገር ባየህ ነበር)፡፡ «ይህ እውነት አይደለምን» ይላቸዋል፡፡ «በጌታችን ይኹንብን እውነት ነው» ይላሉ፡፡ «ትክዱት በነበራችሁት ምክንያት ቅጣቱን ቅመሱ» ይላቸዋል፡፡

وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذۡ وُقِفُواْ عَلَىٰ رَبِّهِمۡۚ قَالَ أَلَيۡسَ هَٰذَا بِٱلۡحَقِّۚ قَالُواْ بَلَىٰ وَرَبِّنَاۚ قَالَ فَذُوقُواْ ٱلۡعَذَابَ بِمَا كُنتُمۡ تَكۡفُرُونَ ٣٠

31. እነዚያ በአላህ መገናኘት ያስተባበሉ በእርግጥ ከሰሩ፡፡ ሰዓቲቱም በድንገት በመጣቻቸው ጊዜ እነሱ ኃጢአቶቻቸውን በጀርባዎቻቸው ላይ የሚሸከሙ ሲኾኑ «በርሷ (በምድረ ዓለም) ባጓደልነው ነገር ላይ ዋ ቁጪታችን» ይላሉ፡፡ ንቁ! የሚሸከሙት ነገር ከፋ፡፡

قَدْ خَسِرَ ٱلَّذِينَ كَذَّبُوا۟ بِلِقَآءِ ٱللَّهِ ۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَتْهُمُ ٱلسَّاعَةُ بَغْتَةً قَالُوا۟ يَـٰحَسْرَتَنَا عَلَىٰ مَا فَرَّطْنَا فِيهَا وَهُمْ يَحْمِلُونَ أَوْزَارَهُمْ عَلَىٰ ظُهُورِهِمْ ۚ أَلَا سَآءَ مَا يَزِرُونَ ﴿٣١﴾

32. የቅርቢቱም ሕይወት ጨዋታና ላግጣ እንጅ ሌላ አይደለችም፡፡ የመጨረሻይቱም አገር (ገነት) ለእነዚያ ለሚጠነቀቁት በጣም በላጭ ናት፡፡ አታውቁምን

وَمَا ٱلْحَيَوٰةُ ٱلدُّنْيَآ إِلَّا لَعِبٌ وَلَهْوٌ ۖ وَلَلدَّارُ ٱلْـَٔاخِرَةُ خَيْرٌ لِّلَّذِينَ يَتَّقُونَ ۗ أَفَلَا تَعْقِلُونَ ﴿٣٢﴾

33. እነሆ ያ የሚሉህ ነገር እንደሚያሳዝንህ በእርግጥ እናውቃለን፡፡ እነርሱም (በልቦቻቸው) አያስተባብሉህም፡፡ ግን በዳዮቹ በአላህ አንቀጾች ይክዳሉ፡፡

قَدْ نَعْلَمُ إِنَّهُۥ لَيَحْزُنُكَ ٱلَّذِى يَقُولُونَ ۖ فَإِنَّهُمْ لَا يُكَذِّبُونَكَ وَلَـٰكِنَّ ٱلظَّـٰلِمِينَ بِـَٔايَـٰتِ ٱللَّهِ يَجْحَدُونَ ﴿٣٣﴾

34. ከበፊትህም መልክተኞች በእርግጥ ተስተባበሉ፡፡ በተስተባበሉበትም ነገርና በተሰቃዩት ላይ እርዳታችን እስከመጣላቸው ድረስ ታገሱ፡፡ የአላህንም ንግግሮች ለዋጭ የለም፡፡ ከመልክተኞቹም ወሬ (የምትረጋጋበት) በእርግጥ መጣልህ፡፡

وَلَقَدْ كُذِّبَتْ رُسُلٌ مِّن قَبْلِكَ فَصَبَرُوا۟ عَلَىٰ مَا كُذِّبُوا۟ وَأُوذُوا۟ حَتَّىٰٓ أَتَىٰهُمْ نَصْرُنَا ۚ وَلَا مُبَدِّلَ لِكَلِمَـٰتِ ٱللَّهِ ۚ وَلَقَدْ جَآءَكَ مِن نَّبَإِى۟ ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿٣٤﴾

35. (ኢስላምን) መተዋቸውም ባንተ ላይ ከባድ ቢኾንብህ በምድር ውስጥ ቀዳዳን ወይም በሰማይ ውስጥ መሰላልን ልትፈልግና በተአምር ልትመጣቸው ብትችል (አድርግ)፡፡ አላህም በሻ ኖሮ በቅኑ መንገድ ላይ በሰበሰባቸው ነበር፡፡ ከተሳሳቱትም ሰዎች በፍጹም አትኹን፡፡

وَإِن كَانَ كَبُرَ عَلَيْكَ إِعْرَاضُهُمْ فَإِنِ ٱسْتَطَعْتَ أَن تَبْتَغِىَ نَفَقًا فِى ٱلْأَرْضِ أَوْ سُلَّمًا فِى ٱلسَّمَآءِ فَتَأْتِيَهُم بِـَٔايَةٍ ۚ وَلَوْ شَآءَ ٱللَّهُ لَجَمَعَهُمْ عَلَى ٱلْهُدَىٰ ۚ فَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلْجَـٰهِلِينَ ﴿٣٥﴾

36. ጥሪህን የሚቀበሉት እነዚያ የሚሰሙት ብቻ ናቸው፡፡ ሙታንንም አላህ ይቀሰቅሳቸዋል፡፡ ከዚያም ወደርሱ ብቻ ይመለሳሉ፡፡

۞ إِنَّمَا يَسْتَجِيبُ ٱلَّذِينَ يَسْمَعُونَ ۘ وَٱلْمَوْتَىٰ يَبْعَثُهُمُ ٱللَّهُ ثُمَّ إِلَيْهِ يُرْجَعُونَ ﴿٣٦﴾

37. «ከጌታውም በእርሱ ላይ ለምን ተዓምር አልተወረደም» አሉ፡፡ «አላህ ተአምርን በማውረድ ላይ ቻይ ነው» በላቸው፡፡ ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

وَقَالُوا۟ لَوْلَا نُزِّلَ عَلَيْهِ ءَايَةٌ مِّن رَّبِّهِۦ ۚ قُلْ إِنَّ ٱللَّهَ قَادِرٌ عَلَىٰٓ أَن يُنَزِّلَ ءَايَةً وَلَـٰكِنَّ أَكْثَرَهُمْ لَا يَعْلَمُونَ ﴿٣٧﴾

38. ከተንቀሳቃሽም በምድር (የሚኼድ)፣ በሁለት ክንፎቹ የሚበርም በራሪ መሰሎቻችሁ ሕዝቦች እንጅ ሌላ አይደሉም፡፡ በመጽሐፉ ውስጥ ምንንም ነገር አልተውንም ከዚያም ወደ ጌታቸው ይሰበሰባሉ፡፡

وَمَا مِن دَآبَّةٍ فِى ٱلْأَرْضِ وَلَا طَـٰٓئِرٍ يَطِيرُ بِجَنَاحَيْهِ إِلَّآ أُمَمٌ أَمْثَالُكُم ۚ مَّا فَرَّطْنَا فِى ٱلْكِتَـٰبِ مِن شَىْءٍ ۚ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّهِمْ يُحْشَرُونَ ﴿٣٨﴾

39. እነዚያም በአንቀጾቻችን ያስዋሹ ደንቆሮች ድዳዎችም በጨለማዎች ውስጥ ያሉ ናቸው፡፡ አላህ ማጥመሙን የሚሻውን ሰው ያጠመዋል፡፡ መምራቱን የሚሻውንም ሰው በቀጥተኛ መንገድ ላይ ያደርገዋል፡፡

وَٱلَّذِينَ كَذَّبُوا۟ بِـَٔايَـٰتِنَا صُمٌّ وَبُكْمٌ فِى ٱلظُّلُمَـٰتِ ۗ مَن يَشَإِ ٱللَّهُ يُضْلِلْهُ وَمَن يَشَأْ يَجْعَلْهُ عَلَىٰ صِرَٰطٍ مُّسْتَقِيمٍ ﴿٣٩﴾

40. የአላህ ቅጣት ቢመጣባችሁ ወይም ሰዓቲቱ (ትንሣኤ) ብትመጣባችሁ ከአላህ ሌላን ትጠራላችሁን እውነተኞች እንደ ኾናችሁ ንገሩኝ በላቸው፡፡

قُلْ أَرَءَيْتَكُمْ إِنْ أَتَىٰكُمْ عَذَابُ ٱللَّهِ أَوْ أَتَتْكُمُ ٱلسَّاعَةُ أَغَيْرَ ٱللَّهِ تَدْعُونَ إِن كُنتُمْ صَٰدِقِينَ ﴿٤٠﴾

41. አይደለም እርሱን ብቻ ትጠራላችሁ፡፡ ቢሻም ወደርሱ የምትጠሩበትን ነገር ያስወግዳል፡፡ የምታጋሩትንም ነገር ትተዋላችሁ (በላቸው)፡፡

بَلْ إِيَّاهُ تَدْعُونَ فَيَكْشِفُ مَا تَدْعُونَ إِلَيْهِ إِن شَآءَ وَتَنسَوْنَ مَا تُشْرِكُونَ ﴿٤١﴾

42. ከበፊትህም ወደ ነበሩት ሕዝቦች (መልክተኞችን) በእርግጥ ላክን፡፡ እንዲዋደቁም በድህነትና በበሽታ ያዝናቸው፡፡

وَلَقَدْ أَرْسَلْنَآ إِلَىٰٓ أُمَمٍ مِّن قَبْلِكَ فَأَخَذْنَٰهُم بِٱلْبَأْسَآءِ وَٱلضَّرَّآءِ لَعَلَّهُمْ يَتَضَرَّعُونَ ﴿٤٢﴾

43. ታዲያ ቅጣታችን በመጣባቸው ጊዜ አይዋደቁም ኖሯልን ግን ልቦቻቸው ደረቁ፡፡ ይሠሩት የነበሩትንም ነገር ሰይጣን ለነሱ አሳመረላቸው፡፡

فَلَوْلَآ إِذْ جَآءَهُم بَأْسُنَا تَضَرَّعُواْ وَلَٰكِن قَسَتْ قُلُوبُهُمْ وَزَيَّنَ لَهُمُ ٱلشَّيْطَٰنُ مَا كَانُواْ يَعْمَلُونَ ﴿٤٣﴾

44. በርሱም ይገሰጹበት የነበረውን ነገር በተው ጊዜ በእነሱ ላይ የነገርን ሁሉ ደጃፎች ከፈትን (አስመቸናቸው)፡፡ በተሰጡትም ነገር በተደሰቱ ጊዜ በድንገት ያዝናቸው፡፡ ወዲያውኑም እነርሱ ተስፋ ቆራጮች ኾኑ፡፡

فَلَمَّا نَسُواْ مَا ذُكِّرُواْ بِهِۦ فَتَحْنَا عَلَيْهِمْ أَبْوَٰبَ كُلِّ شَىْءٍ حَتَّىٰٓ إِذَا فَرِحُواْ بِمَآ أُوتُوٓاْ أَخَذْنَٰهُم بَغْتَةً فَإِذَا هُم مُّبْلِسُونَ ﴿٤٤﴾

45. የእነዚያም የበደሉት ሕዝቦች መጨረሻ ተቆረጠ፡፡ ምስጋናም ለዓለማት ጌታ ለአላህ ይገባው፡፡

فَقُطِعَ دَابِرُ ٱلْقَوْمِ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ ۚ وَٱلْحَمْدُ لِلَّهِ رَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٤٥﴾

46. ንገሩኝ አላህ መስሚያችሁንና ማያዎቻችሁን ቢወስድ በልቦቻችሁም ላይ ቢያትም ከአላህ ሌላ እሱን የሚያመጣላችሁ አምላክ ማነው በላቸው፡፡ አንቀጾችን እንዴት እንደምናብራራ ከዚያም እነሱ እንዴት እንደሚመለሱ ተመልከት፡፡

قُلْ أَرَءَيْتُمْ إِنْ أَخَذَ ٱللَّهُ سَمْعَكُمْ وَأَبْصَٰرَكُمْ وَخَتَمَ عَلَىٰ قُلُوبِكُم مَّنْ إِلَٰهٌ غَيْرُ ٱللَّهِ يَأْتِيكُم بِهِ ۗ ٱنظُرْ كَيْفَ نُصَرِّفُ ٱلْءَايَٰتِ ثُمَّ هُمْ يَصْدِفُونَ ﴿٤٦﴾

47. «ንገሩኝ የአላህ ቅጣት በድንገት ወይም በግልጽ ቢመጣባችሁ አመጠኞች ሕዝቦች እንጅ ሌላ ይጠፋልን» በላቸው፡፡

قُلْ أَرَءَيْتَكُمْ إِنْ أَتَىٰكُمْ عَذَابُ ٱللَّهِ بَغْتَةً أَوْ جَهْرَةً هَلْ يُهْلَكُ إِلَّا ٱلْقَوْمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ﴿٤٧﴾

48. መልክተኞችንም አብሳሪና አስፈራሪ አድርገን እንጅ አንልክም፡፡ ያመኑና መልካምን የሠሩ ሰዎችም በእነርሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነሱም አያዝኑም፡፡

وَمَا نُرْسِلُ ٱلْمُرْسَلِينَ إِلَّا مُبَشِّرِينَ وَمُنذِرِينَ ۖ فَمَنْ ءَامَنَ وَأَصْلَحَ فَلَا خَوْفٌ عَلَيْهِمْ وَلَا هُمْ يَحْزَنُونَ ﴿٤٨﴾

49. እነዚያም ባንቀጾቻችን ያስዋሹ ያምጹ በነበሩት ምክንያት ቅጣቱ ያገኛቸዋል፡፡

وَٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا يَمَسُّهُمُ ٱلْعَذَابُ بِمَا كَانُواْ يَفْسُقُونَ ﴿٤٩﴾

50. «ለእናንተ የአላህ ግምጃ ቤቶች እኔ ዘንድ ናቸው አልልም፡፡ ሩቅንም አላውቅም፡፡ ለእናንተም እኔ መልአክ ነኝ አልልም፡፡ ወደእኔ የሚወርድልኝን እንጅ ሌላን አልከተልም» በላቸው፡፡ «ዕውርና የሚያይ ይስተካከላሉን አታስተነትኑምን» በላቸው፡፡

قُل لَّآ أَقُولُ لَكُمۡ عِندِى خَزَآئِنُ ٱللَّهِ وَلَآ أَعۡلَمُ ٱلۡغَيۡبَ وَلَآ أَقُولُ لَكُمۡ إِنِّى مَلَكٌۖ إِنۡ أَتَّبِعُ إِلَّا مَا يُوحَىٰٓ إِلَيَّۚ قُلۡ هَلۡ يَسۡتَوِى ٱلۡأَعۡمَىٰ وَٱلۡبَصِيرُۚ أَفَلَا تَتَفَكَّرُونَ ٥٠

51. እነዚያንም ከእርሱ ሌላ ረዳትና አማላጅ የሌላቸው ሲኾኑ ወደ ጌታቸው መሰሰብሰብን የሚፈሩትን ይጠነቀቁ ዘንድ በርሱ (በቁርኣን) አስፈራራ፡፡

وَأَنذِرۡ بِهِ ٱلَّذِينَ يَخَافُونَ أَن يُحۡشَرُوٓاْ إِلَىٰ رَبِّهِمۡ لَيۡسَ لَهُم مِّن دُونِهِۦ وَلِىّٞ وَلَا شَفِيعٞ لَّعَلَّهُمۡ يَتَّقُونَ ٥١

52. እነዚያን ጌታቸውን ፊቱን (ውዴታውን) የሚሹ ኾነው በጧትና በማታ የሚጠሩትን አታባርር፡፡ ታባርራቸውና ከበደለኞችም ትኾን ዘንድ እነሱን መቆጣጠር ባንተ ላይ ምንም የለብህም፡፡ አንተንም መቆጣጠር በነሱ ላይ ምንም የለባቸውም፡፡

وَلَا تَطۡرُدِ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ رَبَّهُم بِٱلۡغَدَوٰةِ وَٱلۡعَشِىِّ يُرِيدُونَ وَجۡهَهُۥۖ مَا عَلَيۡكَ مِنۡ حِسَابِهِم مِّن شَىۡءٖ وَمَا مِنۡ حِسَابِكَ عَلَيۡهِم مِّن شَىۡءٖ فَتَطۡرُدَهُمۡ فَتَكُونَ مِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٥٢

53. እንደዚሁም «ከመካከላችን አላህ የለገሰላቸው እነዚህ ናቸውን» ይሉ ዘንድ ከፊላቸውን በከፊሉ ሞከርን፡፡ አላህ አመስጋኞቹን ዐዋቂ አይደለምን

وَكَذَٰلِكَ فَتَنَّا بَعۡضَهُم بِبَعۡضٖ لِّيَقُولُوٓاْ أَهَٰٓؤُلَآءِ مَنَّ ٱللَّهُ عَلَيۡهِم مِّنۢ بَيۡنِنَآۗ أَلَيۡسَ ٱللَّهُ بِأَعۡلَمَ بِٱلشَّٰكِرِينَ ٥٣

54. እነዚያም በተአምራታችን የሚያምኑት (ወደ አንተ) በመጡ ጊዜ «ሰላም በእናንተ ላይ ይኹን፡፡ ጌታችሁ በነፍሱ ላይ እዝነትን ጻፈ፡፡ እነሆ ከእናንተ ውስጥ በስሕተት ክፉን ሥራ የሠራ ሰው ከዚያም ከእርሱ በኋላ የተጸጸተና ሥራውን ያሳመረ እርሱ (አላህ) መሓሪ አዛኝ ነው» በላቸው፡፡

وَإِذَا جَآءَكَ ٱلَّذِينَ يُؤۡمِنُونَ بِـَٔايَٰتِنَا فَقُلۡ سَلَٰمٌ عَلَيۡكُمۡۖ كَتَبَ رَبُّكُمۡ عَلَىٰ نَفۡسِهِ ٱلرَّحۡمَةَ أَنَّهُۥ مَنۡ عَمِلَ مِنكُمۡ سُوٓءَۢا بِجَهَٰلَةٖ ثُمَّ تَابَ مِنۢ بَعۡدِهِۦ وَأَصۡلَحَ فَأَنَّهُۥ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٥٤

55. እንደዚሁም (እውነቱ እንዲገለጽና) የወንጀለኞችም መንገድ ትብራራ ዘንድ አንቀጾችን እንገልጻለን፡፡

وَكَذَٰلِكَ نُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ وَلِتَسۡتَبِينَ سَبِيلُ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ٥٥

56. «እኔ እነዚያን ከአላህ ሌላ የምትጠሩዋቸውን ከመገዛት ተከልክያለሁ» በላቸው፡፡ «ዝንባሌያችሁን አልከተልም፡፡ ያን ጊዜ በእርግጥ ተሳሳትኩ፡፡ እኔም ከተመሪዎቹ አይደለሁም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنِّى نُهِيتُ أَنۡ أَعۡبُدَ ٱلَّذِينَ تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِۚ قُل لَّآ أَتَّبِعُ أَهۡوَآءَكُمۡ قَدۡ ضَلَلۡتُ إِذٗا وَمَآ أَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُهۡتَدِينَ ٥٦

57. «እኔ ከጌታዬ በኾነች ግልጽ ማስረጃ ላይ ነኝ፡፡ በእርሱም አስተባበላችሁ፡፡ በርሱ የምትቻኮሉበት ቅጣት እኔ ዘንድ አይደለም፡፡ ፍርዱ ለአላህ ብቻ ነው፡፡ እውነትን ይፈርዳል፡፡ እርሱም ከፈራጆች ሁሉ በላጭ ነው» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنِّى عَلَىٰ بَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّى وَكَذَّبۡتُم بِهِۦۚ مَا عِندِى مَا تَسۡتَعۡجِلُونَ بِهِۦٓۚ إِنِ ٱلۡحُكۡمُ إِلَّا لِلَّهِۖ يَقُصُّ ٱلۡحَقَّۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلۡفَٰصِلِينَ ٥٧

58. «በእርሱ የምትቻኮሉበት ቅጣት እኔ ዘንድ በኾነ ኖሮ በእኔና በእናንተ መካከል ነገሩ (ቅጣታችሁ) በተፈጸመ ነበር፡፡ አላህም በደለኞችን ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

قُل لَّوۡ أَنَّ عِندِى مَا تَسۡتَعۡجِلُونَ بِهِۦ لَقُضِىَ ٱلۡأَمۡرُ بَيۡنِى وَبَيۡنَكُمۡۗ وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِٱلظَّٰلِمِينَ ٥٨

59. የሩቅ ነገርም መክፈቻዎች እርሱ ዘንድ ናቸው፡፡ ከእርሱ በቀር ማንም አያውቃቸውም፡፡ በየብስና በባሕር ያለውንም ሁሉ ያውቃል፡፡ ከቅጠልም አንዲትም አትረግፍም የሚያውቃት ቢኾን እንጅ፡፡ ከቅንጣትም በመሬት ጨለማዎች ውስጥ የለም ከእርጥብም ከደረቅም አንድም የለም ግልጽ በኾነው መጽሐፍ ውስጥ (የተመዘገበ) ቢኾን እንጅ፡፡

۞وَعِندَهُۥ مَفَاتِحُ ٱلۡغَيۡبِ لَا يَعۡلَمُهَآ إِلَّا هُوَۚ وَيَعۡلَمُ مَا فِي ٱلۡبَرِّ وَٱلۡبَحۡرِۚ وَمَا تَسۡقُطُ مِن وَرَقَةٍ إِلَّا يَعۡلَمُهَا وَلَا حَبَّةٖ فِي ظُلُمَٰتِ ٱلۡأَرۡضِ وَلَا رَطۡبٖ وَلَا يَابِسٍ إِلَّا فِي كِتَٰبٖ مُّبِينٖ ٥٩

60. እርሱም ያ በሌሊት የሚያስተኛችሁ በቀንም የሠራችሁትን ሁሉ የሚያውቅ ከዚያም የተወሰነው ጊዜ ይፈፀም ዘንድ በእርሱ (በቀን) ውስጥ የሚቀሰቅሳችሁ ነው፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደ እርሱ ነው፡፡ ከዚያም ትሠሩት የነበራችሁትን ሁሉ ይነግራችኋል፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي يَتَوَفَّىٰكُم بِٱلَّيۡلِ وَيَعۡلَمُ مَا جَرَحۡتُم بِٱلنَّهَارِ ثُمَّ يَبۡعَثُكُمۡ فِيهِ لِيُقۡضَىٰٓ أَجَلٞ مُّسَمّٗىۖ ثُمَّ إِلَيۡهِ مَرۡجِعُكُمۡ ثُمَّ يُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٦٠

61. እርሱም ከባሮቹ በላይ ሲኾን ሁሉን አሸናፊ ነው፡፡ በናንተም ላይ ጠባቂዎችን (መላእክት) ይልካል፡፡ አንዳችሁንም ሞት በመጣበት ጊዜ (የሞት) መልእክተኞቻችን እነርሱ (ትእዛዛትን) የማያጓድሉ ሲኾኑ ይገድሉታል፡፡

وَهُوَ ٱلۡقَاهِرُ فَوۡقَ عِبَادِهِۦۖ وَيُرۡسِلُ عَلَيۡكُمۡ حَفَظَةً حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَ أَحَدَكُمُ ٱلۡمَوۡتُ تَوَفَّتۡهُ رُسُلُنَا وَهُمۡ لَا يُفَرِّطُونَ ٦١

62. ከዚያም እውነተኛ ወደ ኾነው ጌታቸው ወደ አላህ ይመለሳሉ፡፡ ንቁ! ፍርዱ ለእርሱ ብቻ ነው፡፡ እርሱም ከተቆጣጣሪዎች ሁሉ ይበልጥ ፈጣን ነው፡፡

ثُمَّ رُدُّوٓاْ إِلَى ٱللَّهِ مَوۡلَىٰهُمُ ٱلۡحَقِّۚ أَلَا لَهُ ٱلۡحُكۡمُ وَهُوَ أَسۡرَعُ ٱلۡحَٰسِبِينَ ٦٢

63. ከየብስና ከባሕር ጨለማዎች በግልጽና በምስጢር የምትጠሩት ስትኾኑ «ከነዚህ ቢያድነን በእርግጥ ከአመስጋኞች እንኾናለን (ስትሉ) የሚያድናችሁ ማነው» በላቸው፡፡

قُلۡ مَن يُنَجِّيكُم مِّن ظُلُمَٰتِ ٱلۡبَرِّ وَٱلۡبَحۡرِ تَدۡعُونَهُۥ تَضَرُّعٗا وَخُفۡيَةٗ لَّئِنۡ أَنجَىٰنَا مِنۡ هَٰذِهِۦ لَنَكُونَنَّ مِنَ ٱلشَّٰكِرِينَ ٦٣

64. አላህ ከሷና ከጭንቅም ሁሉ ያድናችኋል፡፡ ከዚያም እናንተ ታጋራላችሁ በላቸው፡፡

قُلِ ٱللَّهُ يُنَجِّيكُم مِّنۡهَا وَمِن كُلِّ كَرۡبٖ ثُمَّ أَنتُمۡ تُشۡرِكُونَ ٦٤

65. «እርሱ (አላህ) ከበላያችሁ ወይም ከእግሮቻችሁ በታች ቅጣትን በእናንተ ላይ ሊልክ ወይም የተለያዩ ሕዝቦች ስትኾኑ ሊያደባልቃችሁና ከፊላችሁን የከፊሉን ጭካኔ ሊያቀምስ ቻይ ነው» በላቸው፡፡ ያውቁ ዘንድ አንቀጾችን እንዴት እንደምናብራራ ተመልከት፡፡

قُلۡ هُوَ ٱلۡقَادِرُ عَلَىٰٓ أَن يَبۡعَثَ عَلَيۡكُمۡ عَذَابٗا مِّن فَوۡقِكُمۡ أَوۡ مِن تَحۡتِ أَرۡجُلِكُمۡ أَوۡ يَلۡبِسَكُمۡ شِيَعٗا وَيُذِيقَ بَعۡضَكُم بَأۡسَ بَعۡضٍۗ ٱنظُرۡ كَيۡفَ نُصَرِّفُ ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّهُمۡ يَفۡقَهُونَ ٦٥

66. በእርሱም (በቁርኣን) እሱ እውነት ሲኾን ሕዝቦችህ አስተባበሉ፡፡ በላቸው፡- «በናንተ ላይ ጠባቂ አይደለሁም፡፡»

وَكَذَّبَ بِهِۦ قَوۡمُكَ وَهُوَ ٱلۡحَقُّۚ قُل لَّسۡتُ عَلَيۡكُم بِوَكِيلٖ ٦٦

67. ለትንቢት ሁሉ (የሚደርስበት) መርጊያ አለው፡፡ ወደፊትም ታውቁታላችሁ፡፡

لِّكُلِّ نَبَإٖ مُّسۡتَقَرّٞۚ وَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ٦٧

68. እነዚያንም በአንቀጾቻችን የሚገቡትን ባየህ ጊዜ ከእርሱ ሌላ በኾነ ወሬ እስከሚገቡ ድረስ ተዋቸው:: ሰይጣንም (መከልከልህን) ቢያስረሳህ ከትውስታ በኋላ ከበደለኞች ሕዝቦች ጋር አትቀመጥ::

وَإِذَا رَأَيْتَ ٱلَّذِينَ يَخُوضُونَ فِىٓ ءَايَـٰتِنَا فَأَعْرِضْ عَنْهُمْ حَتَّىٰ يَخُوضُوا۟ فِى حَدِيثٍ غَيْرِهِۦ ۚ وَإِمَّا يُنسِيَنَّكَ ٱلشَّيْطَـٰنُ فَلَا تَقْعُدْ بَعْدَ ٱلذِّكْرَىٰ مَعَ ٱلْقَوْمِ ٱلظَّـٰلِمِينَ ٦٨

69. በእነዚያም በሚጠነቀቁት ላይ ከሒሳባቸው ምንም የለባቸውም:: ግን ይጠነቀቁ ዘንድ መገሰጽ (አለባቸው)::

وَمَا عَلَى ٱلَّذِينَ يَتَّقُونَ مِنْ حِسَابِهِم مِّن شَىْءٍ وَلَـٰكِن ذِكْرَىٰ لَعَلَّهُمْ يَتَّقُونَ ٦٩

70. እነዚያንም ሃይማኖታቸውን ጨዋታና ላግጣ አድርገው የያዙትን ቅርቢቱም ሕይወት ያታለለቻቸውን ተዋቸው:: በእርሱም (በቁርኣን) ነፍስ በሠራችው ሥራ እንዳትጠፋ አስታውስ:: ለእርሷ ከአላህ ሌላ ረዳትና አማላጅ የላትም:: በመበዢያም ሁሉ ብትበዥ ከርሷ አይወሰድም:: እነዚህ እነዚያ በሠሩት ሥራ የተጠፉት ናቸው:: ለነሱ ይክዱ በነበሩት ምክንያት ከፈላ ውሃ መጠጥና አሳማሚ ቅጣት አላቸው::

وَذَرِ ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُوا۟ دِينَهُمْ لَعِبًا وَلَهْوًا وَغَرَّتْهُمُ ٱلْحَيَوٰةُ ٱلدُّنْيَا ۚ وَذَكِّرْ بِهِۦٓ أَن تُبْسَلَ نَفْسٌۢ بِمَا كَسَبَتْ لَيْسَ لَهَا مِن دُونِ ٱللَّهِ وَلِىٌّ وَلَا شَفِيعٌ وَإِن تَعْدِلْ كُلَّ عَدْلٍ لَّا يُؤْخَذْ مِنْهَآ ۗ أُو۟لَـٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ أُبْسِلُوا۟ بِمَا كَسَبُوا۟ ۖ لَهُمْ شَرَابٌ مِّنْ حَمِيمٍ وَعَذَابٌ أَلِيمٌۢ بِمَا كَانُوا۟ يَكْفُرُونَ ٧٠

71. «ከአላህ ሌላ የማይጠቅመንን እና የማይጎዳንን እንገዛለን አላህም ከመራን ጊዜ በኋላ የኋሊት እንመለሳለን እንደዚያ በምድር ላይ የዋለለ ሲኾን ሰይጣናት እንዳሳሳቱት ለእርሱ ወደኛ ና እያሉ ወደ ቅን መንገድ የሚጠሩ ወዳጆች እንዳሉት (እንደማይከተላቸውም) ሰው እንኾናለን» በላቸው:: «የአላህ መንገድ እርሱ ቀጥተኛው መንገድ ነው:: ለዓለማት ጌታ ልንገዛም ታዘዝን» በላቸው::

قُلْ أَنَدْعُوا۟ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَنفَعُنَا وَلَا يَضُرُّنَا وَنُرَدُّ عَلَىٰٓ أَعْقَابِنَا بَعْدَ إِذْ هَدَىٰنَا ٱللَّهُ كَٱلَّذِى ٱسْتَهْوَتْهُ ٱلشَّيَـٰطِينُ فِى ٱلْأَرْضِ حَيْرَانَ لَهُۥٓ أَصْحَـٰبٌ يَدْعُونَهُۥٓ إِلَى ٱلْهُدَى ٱئْتِنَا ۗ قُلْ إِنَّ هُدَى ٱللَّهِ هُوَ ٱلْهُدَىٰ ۖ وَأُمِرْنَا لِنُسْلِمَ لِرَبِّ ٱلْعَـٰلَمِينَ ٧١

72. ሶላትንም በደንቡ ስገዱ ፍሩትም፤ (በማለት ታዘዝን):: እርሱም ያ ወደርሱ ብቻ የምትሰበሰቡበት ነው::

وَأَنْ أَقِيمُوا۟ ٱلصَّلَوٰةَ وَٱتَّقُوهُ ۚ وَهُوَ ٱلَّذِىٓ إِلَيْهِ تُحْشَرُونَ ٧٢

73. እርሱም ያ ሰማያትንና ምድርን በእውነት የፈጠረ ነው:: «ኹን» የሚልበትንና ወዲያውም የሚኾንበትን ቀን (አስታውስ):: ቃሉ እውነት ነው:: በቀንዱም በሚነፋ ቀን ንግሥናው የርሱ ብቻ ነው:: ሩቁንና ቅርቡን ዐዋቂ ነው:: እርሱም ጥበበኛው ውስጥ ዐዋቂው ነው::

وَهُوَ ٱلَّذِى خَلَقَ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ بِٱلْحَقِّ ۖ وَيَوْمَ يَقُولُ كُن فَيَكُونُ ۚ قَوْلُهُ ٱلْحَقُّ ۚ وَلَهُ ٱلْمُلْكُ يَوْمَ يُنفَخُ فِى ٱلصُّورِ ۚ عَـٰلِمُ ٱلْغَيْبِ وَٱلشَّهَـٰدَةِ ۚ وَهُوَ ٱلْحَكِيمُ ٱلْخَبِيرُ ٧٣

74. ኢብራሒምም ለአባቱ ለአዘር «ጣዖታትን አማልክት አድርገህ ትይዛለህን እኔ፤ አንተንም ሕዝቦችህንም በግልጽ መሳሳት ውስጥ ኾናችሁ አያችኋለሁ» ባለ ጊዜ (አስታውስ)

۞ وَإِذْ قَالَ إِبْرَٰهِيمُ لِأَبِيهِ ءَازَرَ أَتَتَّخِذُ أَصْنَامًا ءَالِهَةً ۖ إِنِّىٓ أَرَىٰكَ وَقَوْمَكَ فِى ضَلَـٰلٍ مُّبِينٍ ٧٤

75. እንደዚሁም ኢብራሂምን (እንዲያውቅና) ከአረጋጋጮቹም ይኾን ዘንድ የሰማያትንና የምድርን መለኮት አሳየነው::

وَكَذَٰلِكَ نُرِىٓ إِبْرَٰهِيمَ مَلَكُوتَ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ وَلِيَكُونَ مِنَ ٱلْمُوقِنِينَ ٧٥

76. ሌሊቱም በእርሱ ላይ ባጨለመ ጊዜ ኮከብን አየ፡፡ «ይህ ጌታዬ ነው» አለ፡፡ በጠለቀም ጊዜ፡- «ጠላቂዎችን አልወድም» አለ፡፡

فَلَمَّا جَنَّ عَلَيۡهِ ٱلَّيۡلُ رَءَا كَوۡكَبٗاۖ قَالَ هَٰذَا رَبِّيۖ فَلَمَّآ أَفَلَ قَالَ لَآ أُحِبُّ ٱلۡأٓفِلِينَ ٧٦

77. ጨረቃንም ወጪ ኾኖ ባየ ጊዜ፡- «ይህ ጌታዬ ነው» አለ፡፡ በገባም ጊዜ፡- «ጌታዬ (ቅኑን መንገድ) ባይመራኝ በእርግጥ ከተሳሳቱት ሕዝቦች እኾናለሁ» አለ፡፡

فَلَمَّا رَءَا ٱلۡقَمَرَ بَازِغٗا قَالَ هَٰذَا رَبِّيۖ فَلَمَّآ أَفَلَ قَالَ لَئِن لَّمۡ يَهۡدِنِي رَبِّي لَأَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلضَّآلِّينَ ٧٧

78. ፀሐይንም ጮራዋን ዘርግታ ባየ ጊዜ፡- «ይህ ጌታዬ ነው፡፡ ይህ በጣም ትልቅ ነው» አለ፡፡ በገባችም ጊዜ፡- «ወገኖቼ ሆይ! እኔ ከምታጋሩት ሁሉ ንጹሕ ነኝ» አለ፡፡

فَلَمَّا رَءَا ٱلشَّمۡسَ بَازِغَةٗ قَالَ هَٰذَا رَبِّي هَٰذَآ أَكۡبَرُۖ فَلَمَّآ أَفَلَتۡ قَالَ يَٰقَوۡمِ إِنِّي بَرِيٓءٞ مِّمَّا تُشۡرِكُونَ ٧٨

79. «እኔ ለዚያ ሰማያትንና ምድርን ለፈጠረው (አምላክ) ቀጥተኛ ስኾን ፊቴን አዞርኩ፡፡ እኔም ከአጋሪዎቹ አይደለሁም» (አለ)፡፡

إِنِّي وَجَّهۡتُ وَجۡهِيَ لِلَّذِي فَطَرَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ حَنِيفٗاۖ وَمَآ أَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٧٩

80. ወገኖቹም ተከራከሩት፡፡ «በአላህ (አንድነት) በእርግጥ የመራኝ ሲኾን ትከራከሩኛላችሁን በእርሱም የምታጋሩትን ነገር አልፈራም፡፡ ግን ጌታዬ ነገርን ቢሻ (ያገኘኛል)፡፡ ጌታዬም ነገሩን ሁሉ ዕውቀቱ ሰፋ፡፡ አትገነዘቡምን» አላቸው፡፡

وَحَآجَّهُۥ قَوۡمُهُۥۚ قَالَ أَتُحَٰٓجُّوٓنِّي فِي ٱللَّهِ وَقَدۡ هَدَىٰنِۚ وَلَآ أَخَافُ مَا تُشۡرِكُونَ بِهِۦٓ إِلَّآ أَن يَشَآءَ رَبِّي شَيۡـٔٗاۚ وَسِعَ رَبِّي كُلَّ شَيۡءٍ عِلۡمًاۚ أَفَلَا تَتَذَكَّرُونَ ٨٠

81. «በእናንተ ላይ በእርሱ ማስረጃን ያላወረደበትን እናንተ ማጋራታችሁን የማትፈሩ ስትኾኑ የምታጋሩትን (ጣዖታት) እንዴት እፈራለሁ! የምታውቁም ብትኾኑ ከሁለቱ ክፍሎች በጸጥታ ይበልጥ ተገቢው ማንኛው ነው» (አለ)፡፡

وَكَيۡفَ أَخَافُ مَآ أَشۡرَكۡتُمۡ وَلَا تَخَافُونَ أَنَّكُمۡ أَشۡرَكۡتُم بِٱللَّهِ مَا لَمۡ يُنَزِّلۡ بِهِۦ عَلَيۡكُمۡ سُلۡطَٰنٗاۚ فَأَيُّ ٱلۡفَرِيقَيۡنِ أَحَقُّ بِٱلۡأَمۡنِۖ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٨١

82. እነዚያ ያመኑና እምነታቸውን በበደል ያልቀላቀሉ እነዚያ ለእነርሱ ጸጥታ አላቸው፡፡ እነሱም የተመሩ ናቸው፤

ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَلَمۡ يَلۡبِسُوٓاْ إِيمَٰنَهُم بِظُلۡمٍ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمُ ٱلۡأَمۡنُ وَهُم مُّهۡتَدُونَ ٨٢

83. ይህችም ማስረጃችን ናት፡፡ ለኢብራሂም በሕዝቦቹ ላይ (አስረጅ እንድትኾን) ሰጠናት፡፡ የምንሻውን ሰው በደረጃዎች ከፍ እናደርጋለን፡፡ ጌታህ ጥበበኛ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَتِلۡكَ حُجَّتُنَآ ءَاتَيۡنَٰهَآ إِبۡرَٰهِيمَ عَلَىٰ قَوۡمِهِۦۚ نَرۡفَعُ دَرَجَٰتٖ مَّن نَّشَآءُۗ إِنَّ رَبَّكَ حَكِيمٌ عَلِيمٞ ٨٣

84. ለርሱም ኢስሐቅን (የልጅ ልጁን) ያዕቁብንም ሰጠነው፡፡ ሁሉንም መራን፡፡ ኑሕንም በፊት መራን፡፡ ከዘሮቹም ዳውድን፣ ሱለይማንንም፣ አዩብንም፣ ዩሱፍንም፣ ሙሳንም፣ ሃሩንንም (መራን)፡፡ እንደዚሁም በጎ ሰሪዎችን እንመነዳለን፡፡

وَوَهَبۡنَا لَهُۥٓ إِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَۚ كُلًّا هَدَيۡنَاۚ وَنُوحًا هَدَيۡنَا مِن قَبۡلُۖ وَمِن ذُرِّيَّتِهِۦ دَاوُۥدَ وَسُلَيۡمَٰنَ وَأَيُّوبَ وَيُوسُفَ وَمُوسَىٰ وَهَٰرُونَۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٨٤

85. ዘከሪያንም፣ የሕያንም፣ ዒሳንም፣ ኢልያስንም (መራን)፡፡ ሁሉም ከመልካሞቹ ናቸው፡፡

وَزَكَرِيَّا وَيَحۡيَىٰ وَعِيسَىٰ وَإِلۡيَاسَۖ كُلّٞ مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ٨٥

| | |
|---|---|
| 86. ኢስማዒልንም፣ አልየስዕንም፣ ዩኑስንም፣ ሉጥንም (መራን)፡፡ ሁሉንም በዓለማት ላይ አበለጥናቸውም፡፡ | وَإِسۡمَٰعِيلَ وَٱلۡيَسَعَ وَيُونُسَ وَلُوطٗاۚ وَكُلّٗا فَضَّلۡنَا عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ٨٦ |
| 87. ከአባቶቻቸውም፣ ከዘሮቻቸውም፣ ከወንድሞቻቸውም (መራን)፡፡ መረጥናቸውም፤ ወደ ቀጥታውም መንገድ መራናቸው፡፡ | وَمِنۡ ءَابَآئِهِمۡ وَذُرِّيَّٰتِهِمۡ وَإِخۡوَٰنِهِمۡۖ وَٱجۡتَبَيۡنَٰهُمۡ وَهَدَيۡنَٰهُمۡ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ٨٧ |
| 88. ይህ የአላህ መምሪያ ነው፡፡ በእርሱ ከባሮቹ የሚሻውን ሰው ይመራል፡፡ ባጋሩም ኖሮ ይሠሩት የነበሩት ከነሱ በታበሰ ነበር፡፡ | ذَٰلِكَ هُدَى ٱللَّهِ يَهۡدِي بِهِۦ مَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦۚ وَلَوۡ أَشۡرَكُواْ لَحَبِطَ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٨٨ |
| 89. እነዚህ እነዚያ መጻሕፍትንና ጥበብን፣ ነቢይነትንም የሰጠናቸው ናቸው፡፡ እነዚህ (የመካ ከሓዲዎች) በእርሷ ቢክዱም በእርሷ የማይክዱን ሕዝቦች ለእርሷ በእርግጥ አዘጋጅተናል፡፡ | أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحُكۡمَ وَٱلنُّبُوَّةَۚ فَإِن يَكۡفُرۡ بِهَا هَٰٓؤُلَآءِ فَقَدۡ وَكَّلۡنَا بِهَا قَوۡمٗا لَّيۡسُواْ بِهَا بِكَٰفِرِينَ ٨٩ |
| 90. እነዚህ (ነቢያት)፤ እነዚያ አላህ የመራቸው ናቸው፡፡ በመንገዳቸውም ተከተል፡፡ «በእርሱ (በቁርአን) ላይ ምንም ዋጋ አልጠይቃችሁም፡፡ እርሱ ለዓለማት ግሣጼ እንጅ ሌላ አይደለም» በላቸው፡፡ | أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ هَدَى ٱللَّهُۖ فَبِهُدَىٰهُمُ ٱقۡتَدِهۡۗ قُل لَّآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ أَجۡرًاۖ إِنۡ هُوَ إِلَّا ذِكۡرَىٰ لِلۡعَٰلَمِينَ ٩٠ |
| 91. «አላህ በሰው ላይ ምንም አላወረደም» ባሉም ጊዜ አላህን ተገቢ ክብሩን አላከበሩትም፡፡ (እንዲህ) በላቸው፡- «ያንን ብርሃንና ለሰዎች መሪ ኾኖ ሙሳ ያመጣውን መጽሐፍ ክፍልፍሎች የምታደርጉት ስትኾኑ ማን አወረደው (የወደዳችኋትን) ትገልጿታላችሁ ብዙውንም ትደብቃላችሁ፡፡ እናንተም አባቶቻችሁም ያላወቃችሁትን ተስተማራችሁ፤» | وَمَا قَدَرُواْ ٱللَّهَ حَقَّ قَدۡرِهِۦٓ إِذۡ قَالُواْ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ عَلَىٰ بَشَرٖ مِّن شَيۡءٖۗ قُلۡ مَنۡ أَنزَلَ ٱلۡكِتَٰبَ ٱلَّذِي جَآءَ بِهِۦ مُوسَىٰ نُورٗا وَهُدٗى لِّلنَّاسِۖ تَجۡعَلُونَهُۥ قَرَاطِيسَ تُبۡدُونَهَا وَتُخۡفُونَ كَثِيرٗاۖ وَعُلِّمۡتُم مَّا لَمۡ تَعۡلَمُوٓاْ أَنتُمۡ وَلَآ ءَابَآؤُكُمۡۖ قُلِ ٱللَّهُۖ ثُمَّ ذَرۡهُمۡ فِي خَوۡضِهِمۡ يَلۡعَبُونَ ٩١ |
| 92. «አላህ (አወረደው)» በላቸው፡፡ ከዚያም በውሸታቸው ውስጥ የሚጫወቱ ሲኾኑ ተዋቸው፡፡ ይህም ያወረድነው የኾነ ብሩክ ያንንም በፊቱ የነበረውን (መጽሐፍ) አረጋጋጭ መጽሐፍ ነው፡፡ የከተሞችን እናት (መካን) እና በዙሪያዋ ያሉትንም ሰዎች ልታስጠነቅቅበት (አወረድነው)፡፡ እነዚያም በመጨረሻይቱ ዓለም የሚያምኑት እነርሱ በሶላታቸው ላይ የሚጠባበቁ ሲኾኑ በርሱ ያምናሉ፡፡ | وَهَٰذَا كِتَٰبٌ أَنزَلۡنَٰهُ مُبَارَكٞ مُّصَدِّقُ ٱلَّذِي بَيۡنَ يَدَيۡهِ وَلِتُنذِرَ أُمَّ ٱلۡقُرَىٰ وَمَنۡ حَوۡلَهَاۚ وَٱلَّذِينَ يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ يُؤۡمِنُونَ بِهِۦۖ وَهُمۡ عَلَىٰ صَلَاتِهِمۡ يُحَافِظُونَ ٩٢ |

93. በአላህም ላይ እብለትን ከቀጣጠፈ ወይም ወደርሱ ምንም ያልተወረደለት ሲኾን «ወደኔ ተወረደልኝ» ካለና:-«አላህም ያወረደውን ብጤ በእርግጥ አወርዳለሁ» ካለ ሰው ይበልጥ በዳይ ማን ነው በደለኞችንም በሞት መከራዎች ውስጥ በኾኑ ጊዜ መላእክት እጆቻቸውን ዘርጊዎች ኾነው « (ለቅጥጥብ) ነፍሶቻችሁን አውጡ፤ በአላህ ላይ እውነት ያልኾነን ነገር ትናገሩ በነበራችሁትና ከአንቀጾቹም ትኮሩ በነበራችሁት ምክንያት ዛሬ የውርደትን ቅጣት ትመነዳላችሁ» (የሚሏቸው ሲኾኑ) ብታይ ኖሮ (አስደናቂን ነገር ባየህ ነበር)፡፡

وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا أَوۡ قَالَ أُوحِيَ إِلَيَّ وَلَمۡ يُوحَ إِلَيۡهِ شَيۡءٞ وَمَن قَالَ سَأُنزِلُ مِثۡلَ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُۗ وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذِ ٱلظَّٰلِمُونَ فِي غَمَرَٰتِ ٱلۡمَوۡتِ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ بَاسِطُوٓاْ أَيۡدِيهِمۡ أَخۡرِجُوٓاْ أَنفُسَكُمُۖ ٱلۡيَوۡمَ تُجۡزَوۡنَ عَذَابَ ٱلۡهُونِ بِمَا كُنتُمۡ تَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ غَيۡرَ ٱلۡحَقِّ وَكُنتُمۡ عَنۡ ءَايَٰتِهِۦ تَسۡتَكۡبِرُونَ ٩٣

94. መጀመሪያም ጊዜ እንደ ፈጠርናችሁ ኾናችሁ የሰጠናችሁን ሁሉ በጀርባዎቻችሁ ኋላ የተዋችሁ ስትኾኑ የሰጠናችሁን ሁሉ በጀርባዎቻችሁ ኋላ የተዋችሁ ስትኾኑ ለየብቻችሁ ኾናችሁ በእርግጥ መጣችሁን እነዚያንም እነሱ በእናንተ ውስጥ (ለአላህ) ተጋሪዎች ናቸው የምትሉዋቸውን አማላጆቻችሁን ከእናንተ ጋር አናይም፡፡ ግንኙነታችሁ በእርግጥ ተቋረጠ፡፡ ከእናንተም ያ (ያማልደናል) የምትሉት ጠፋ (ይባላሉ)፡፡

وَلَقَدۡ جِئۡتُمُونَا فُرَٰدَىٰ كَمَا خَلَقۡنَٰكُمۡ أَوَّلَ مَرَّةٖ وَتَرَكۡتُم مَّا خَوَّلۡنَٰكُمۡ وَرَآءَ ظُهُورِكُمۡۖ وَمَا نَرَىٰ مَعَكُمۡ شُفَعَآءَكُمُ ٱلَّذِينَ زَعَمۡتُمۡ أَنَّهُمۡ فِيكُمۡ شُرَكَٰٓؤُاْۚ لَقَد تَّقَطَّعَ بَيۡنَكُمۡ وَضَلَّ عَنكُم مَّا كُنتُمۡ تَزۡعُمُونَ ٩٤

95. አላህ ቅንጣትንና የፍሬን አጥንት ፈልቃቂ ነው፡፡ ሕያውን ከሙት ያወጣል፤ ሙትንም ከሕያው አውጪ ነው፡፡ እርሱ አላህ ነው፤ ታዲያ (ከእምነት) እንዴት ትመለሳላችሁ (ትርቃላችሁ)

۞إِنَّ ٱللَّهَ فَالِقُ ٱلۡحَبِّ وَٱلنَّوَىٰۖ يُخۡرِجُ ٱلۡحَيَّ مِنَ ٱلۡمَيِّتِ وَمُخۡرِجُ ٱلۡمَيِّتِ مِنَ ٱلۡحَيِّۚ ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُۖ فَأَنَّىٰ تُؤۡفَكُونَ ٩٥

96. እርሱም ጎህን (ከሌሊት ጨለማ) ፈልቃቂ ሌሊትንም ማረፊያ ፀሐይንና ጨረቃንም (ለጊዜ) መቁጠሪያ አድራጊ ነው፡፡ ይህ የአሸናፊው የዐዋቂው (አላህ) ችሎታ ነው፡፡

فَالِقُ ٱلۡإِصۡبَاحِ وَجَعَلَ ٱلَّيۡلَ سَكَنٗا وَٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَ حُسۡبَانٗاۚ ذَٰلِكَ تَقۡدِيرُ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡعَلِيمِ ٩٦

97. እርሱም ያ ከዋክብትን በየብስና በባሕር ጨለማዎች ውስጥ በእርሷ ትመሩ ዘንድ ለእናንተ ያደረገ ነው፡፡ ለሚያውቁ ሕዝቦች አንቀጾችን በእርግጥ ዘረዘርን፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلنُّجُومَ لِتَهۡتَدُواْ بِهَا فِي ظُلُمَٰتِ ٱلۡبَرِّ وَٱلۡبَحۡرِۗ قَدۡ فَصَّلۡنَا ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَعۡلَمُونَ ٩٧

98. እርሱም ያ ከአንዲት ነፍስ ያስገኛችሁ፤ ነው፡፡ (በማሕፀን) መርጊያና (በጀርባ) መቀመጫም (አላችሁ)፡ ፡ ለሚያወቁ ሕዝቦች አንቀጾችን በእርግጥ ዘረዘርን፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَنشَأَكُم مِّن نَّفۡسٖ وَٰحِدَةٖ فَمُسۡتَقَرّٞ وَمُسۡتَوۡدَعٞۗ قَدۡ فَصَّلۡنَا ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَفۡقَهُونَ ٩٨

99. እርሱም ያ ከሰማይ ውሃን ያወረደ ነው፡፡ በርሱም የነገሩን ሁሉ በቃይ አወጣን፡፡ የተደራረበንም ቅንጣት ከርሱ የምናወጣ የኾነን ለምለም (አዝመራ) ከርሱ አወጣን፡፡ ከዘንባባም ከእንቡጧ የተቀራረቡ የኾኑ ዘለላዎች አሉ፡፡ ከወይኖችም፣ ከወይራም፣ ከሩማንም (ቅጠላቸው) ተመሳሳይና (ፍሬያቸው) የማይመሳሰል ሲኾኑ አትክልቶችን (አወጣን)፡፡ ባፈራ ጊዜ ወደ ፍሬውና ወደ መብሰሉ ተመልከቱ፡፡ በእነዚህ ተዓምራት ለሚያምኑ ሕዝቦች ምልክቶች አሉ፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَخۡرَجۡنَا بِهِۦ نَبَاتَ كُلِّ شَيۡءٖ فَأَخۡرَجۡنَا مِنۡهُ خَضِرٗا نُّخۡرِجُ مِنۡهُ حَبّٗا مُّتَرَاكِبٗا وَمِنَ ٱلنَّخۡلِ مِن طَلۡعِهَا قِنۡوَانٞ دَانِيَةٞ وَجَنَّٰتٖ مِّنۡ أَعۡنَابٖ وَٱلزَّيۡتُونَ وَٱلرُّمَّانَ مُشۡتَبِهٗا وَغَيۡرَ مُتَشَٰبِهٍۗ ٱنظُرُوٓاْ إِلَىٰ ثَمَرِهِۦٓ إِذَآ أَثۡمَرَ وَيَنۡعِهِۦٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكُمۡ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ﴿٩٩﴾

100. ለአላህም አጋንንትን የፈጠራቸው ሲኾን (በመታዘዝ) ተጋሪዎች አደረጉ፡፡ ወንዶች ልጆችንና ሴቶች ልጆችንም ያለ ዕውቀት ለእርሱ ቀጠፉ፡፡ (አላህ) ጥራት የተገባው ከሚሉት ነገር የላቀ ነው፡፡

وَجَعَلُواْ لِلَّهِ شُرَكَآءَ ٱلۡجِنَّ وَخَلَقَهُمۡۖ وَخَرَقُواْ لَهُۥ بَنِينَ وَبَنَٰتِۭ بِغَيۡرِ عِلۡمٖۚ سُبۡحَٰنَهُۥ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿١٠٠﴾

101. (እርሱ) ሰማያትንና ምድርን ያለ ብጤ ፈጣሪ ነው፡፡ ለእርሱ ሚስት የሌለችው ሲኾን እንዴት ለእርሱ ልጅ ይኖረዋል ነገርንም ሁሉ ፈጠረ፡፡ እርሱም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

بَدِيعُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ أَنَّىٰ يَكُونُ لَهُۥ وَلَدٞ وَلَمۡ تَكُن لَّهُۥ صَٰحِبَةٞۖ وَخَلَقَ كُلَّ شَيۡءٖۖ وَهُوَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ﴿١٠١﴾

102. ይህ ጌታችሁ አላህ ነው፡፡ ከእርሱ በቀር አምላክ የለም፡፡ ነገርን ሁሉ ፈጣሪ ነው፡፡ ስለዚህ ተገዙት፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ተጠባባቂ ነው፡፡

ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبُّكُمۡۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ خَٰلِقُ كُلِّ شَيۡءٖ فَٱعۡبُدُوهُۚ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ وَكِيلٞ ﴿١٠٢﴾

103. ዓይኖች አያገኙትም፤ (አያዩትም)፡፡ እርሱም ዓይኖችን ያያል፡፡ እርሱም ርኅራኄው ረቂቁ ውስጠ ዐዋቂው ነው፡፡

لَّا تُدۡرِكُهُ ٱلۡأَبۡصَٰرُ وَهُوَ يُدۡرِكُ ٱلۡأَبۡصَٰرَۖ وَهُوَ ٱللَّطِيفُ ٱلۡخَبِيرُ ﴿١٠٣﴾

104. «ከጌታችሁ ዘንድ ብርሃኖች በእርግጥ መጡላችሁ፡፡ የተመለከተም ሰው (ጥቅሙ) ለነፍሱ ብቻ ነው፡፡ የታወረም ሰው (ጉዳቱ) በራሱ ላይ ብቻ ነው፡፡ እኔም በእናንተ ላይ ጠባቂ አይደለሁም» (በላቸው)፡፡

قَدۡ جَآءَكُم بَصَآئِرُ مِن رَّبِّكُمۡۖ فَمَنۡ أَبۡصَرَ فَلِنَفۡسِهِۦۖ وَمَنۡ عَمِيَ فَعَلَيۡهَاۚ وَمَآ أَنَا۠ عَلَيۡكُم بِحَفِيظٖ ﴿١٠٤﴾

105. እንደዚሁም « (እንዲገመግሙና ያለፉትን መጻሕፍት) አጥንተሃልም» እንዲሉ ለሚያውቁ ሕዝቦችም (ቁርኣንን) እንድናብራራው አንቀጾችን እንገልጻለን፡፡

وَكَذَٰلِكَ نُصَرِّفُ ٱلۡأٓيَٰتِ وَلِيَقُولُواْ دَرَسۡتَ وَلِنُبَيِّنَهُۥ لِقَوۡمٖ يَعۡلَمُونَ ﴿١٠٥﴾

106. ከጌታህ ወደ አንተ የተወረደውን ተከተል፡፡ ከእርሱ በቀር አምላክ የለም፡፡ አጋሪዎችንም ተዋቸው፡፡

ٱتَّبِعۡ مَآ أُوحِيَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ وَأَعۡرِضۡ عَنِ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ﴿١٠٦﴾

107. አላህም በሻ ኖሮ ባላጋሩ ነበር፡፡ በእነሱም ላይ ጠባቂ አላደረግንህም፡፡ አንተም በእነሱ ላይ ኃላፊ አይደለህም፡፡

وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَآ أَشۡرَكُواْۗ وَمَا جَعَلۡنَٰكَ عَلَيۡهِمۡ حَفِيظٗاۖ وَمَآ أَنتَ عَلَيۡهِم بِوَكِيلٖ ﴿١٠٧﴾

108. እነዚያንም ከአላህ ሌላ የሚገዙዋቸውን (ጣዖታትን) አትስደቡ፡፡ ድንበርን በማለፍ ያለዕውቀት አላህን ይሰድባሉና፡፡ እንደዚሁ ለሕዝቦች ሁሉ ሥራቸውን ደግ አስመሰልንላቸው፡፡ ከዚያም መመለሻቸው ወደ ጌታቸው ነው፡፡ ይሠሩት የነበሩትንም ሁሉ ይነግራቸዋል፡፡

وَلَا تَسُبُّواْ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ فَيَسُبُّواْ ٱللَّهَ عَدۡوَۢا بِغَيۡرِ عِلۡمٖۗ كَذَٰلِكَ زَيَّنَّا لِكُلِّ أُمَّةٍ عَمَلَهُمۡ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّهِم مَّرۡجِعُهُمۡ فَيُنَبِّئُهُم بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٠٨

109. ተዓምርም ብትመጣላቸው በእርሷ በቁርጥ ሊያምኑ ጥብቅ መሐሎቻቸውን በአላህ ማሉ፡፡ «ተዓምራት ሁሉ አላህ ዘንድ ናት» በላቸው፡፡ እርሷ በመጣች ጊዜም አለማመናቸውን (ወይም ማመናቸውን) ምን አሳወቃችሁ

وَأَقۡسَمُواْ بِٱللَّهِ جَهۡدَ أَيۡمَٰنِهِمۡ لَئِن جَآءَتۡهُمۡ ءَايَةٞ لَّيُؤۡمِنُنَّ بِهَاۚ قُلۡ إِنَّمَا ٱلۡأٓيَٰتُ عِندَ ٱللَّهِۖ وَمَا يُشۡعِرُكُمۡ أَنَّهَآ إِذَا جَآءَتۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ١٠٩

110. በመጀመሪያም ጊዜ በእርሱ እንዳላመኑ ሁሉ ልቦቻቸውንና ዓይኖቻቸውን እናገላብጣለን፡፡ በጥመታቸውም ውስጥ የሚዋልሉ ሲኾኑ እንተዋቸዋለን፡፡

وَنُقَلِّبُ أَفۡـِٔدَتَهُمۡ وَأَبۡصَٰرَهُمۡ كَمَا لَمۡ يُؤۡمِنُواْ بِهِۦٓ أَوَّلَ مَرَّةٖ وَنَذَرُهُمۡ فِي طُغۡيَٰنِهِمۡ يَعۡمَهُونَ ١١٠

111. እኛም ወደእነርሱ መላእክትን ባወረድን ሙታንም ባነጋገሩዋቸው ነገሩንም ሁሉ ጭፍራ ጭፍራ አድርገን በእነሱ ላይ በሰበሰብን ኖሮ አላህ ካልሻ በስተቀር የሚያምኑ ባልኾኑ ነበር፡፡ ግን አብዛኞቻቸው (ይህንን) ይስታሉ፡፡

۞وَلَوۡ أَنَّنَا نَزَّلۡنَآ إِلَيۡهِمُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ وَكَلَّمَهُمُ ٱلۡمَوۡتَىٰ وَحَشَرۡنَا عَلَيۡهِمۡ كُلَّ شَيۡءٖ قُبُلٗا مَّا كَانُواْ لِيُؤۡمِنُوٓاْ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ يَجۡهَلُونَ ١١١

112. እንደዚሁም ለነቢያት ሁሉ ከሰውና ከጋኔን የኾኑን ሰይጣናት ጠላት አደረግን፡፡ ከፊላቸው ወደ ከፊሉ ለማታለል ልብስብስን ቃል ይጥላሉ፡፡ ጌታህም በሻ ኖሮ ባልሠሩት ነበር፡፡ ከቅጥፈታቸውም ጋር ተዋቸው፡፡

وَكَذَٰلِكَ جَعَلۡنَا لِكُلِّ نَبِيٍّ عَدُوّٗا شَيَٰطِينَ ٱلۡإِنسِ وَٱلۡجِنِّ يُوحِي بَعۡضُهُمۡ إِلَىٰ بَعۡضٖ زُخۡرُفَ ٱلۡقَوۡلِ غُرُورٗاۚ وَلَوۡ شَآءَ رَبُّكَ مَا فَعَلُوهُۖ فَذَرۡهُمۡ وَمَا يَفۡتَرُونَ ١١٢

113. (የሚጥሉትም ሊያታልሉና) የእነዚያም በመጨረሻይቱ ሕይወት የማያምኑት ሰዎች ልቦች ወደእርሱ እንዲያዘነብሉ እንዲወዱትም እነርሱ ይቀጥፉ የነበሩትንም እንዲቀጣጥፉ ነው፡፡

وَلِتَصۡغَىٰٓ إِلَيۡهِ أَفۡـِٔدَةُ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ وَلِيَرۡضَوۡهُ وَلِيَقۡتَرِفُواْ مَا هُم مُّقۡتَرِفُونَ ١١٣

114. እርሱ ያ መጽሐፉን የተብራራ ኾኖ ወደእናንተ ያወረደ ሲኾን «ከአላህ ሌላ ዳኛን እፈልጋለሁን» (በላቸው)፡፡ እነዚያም መጽሐፍን የሰጠናቸው እርሱ ከጌታህ ዘንድ በእውነት የተወረደ መኾኑን ያውቃሉ፡፡ ከተጠራጣሪዎቹም አትኹን፡፡

أَفَغَيۡرَ ٱللَّهِ أَبۡتَغِي حَكَمٗا وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ إِلَيۡكُمُ ٱلۡكِتَٰبَ مُفَصَّلٗاۚ وَٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يَعۡلَمُونَ أَنَّهُۥ مُنَزَّلٞ مِّن رَّبِّكَ بِٱلۡحَقِّۖ فَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُمۡتَرِينَ ١١٤

115. የጌታህም ቃላት እውነተኛና ትክክለኛ ስትኾን ተፈጸመች፡፡ ለቃላቱ ለዋጭ የለም፡፡ እርሱም ሰሚው ዐዋቂው ነው፡፡

وَتَمَّتۡ كَلِمَتُ رَبِّكَ صِدۡقٗا وَعَدۡلٗاۚ لَّا مُبَدِّلَ لِكَلِمَٰتِهِۦۚ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ١١٥

116. በምድርም ካሉት ሰዎች አብዛኞቹን ብትከተል ከአላህ መንገድ ያሳስቱሃል፡፡ ጥርጣሬን እንጅ ሌላን አይከተሉም፡፡ እነርሱም የሚዋሹ እንጂ ሌላ አይደሉም፡፡

وَإِن تُطِعۡ أَكۡثَرَ مَن فِي ٱلۡأَرۡضِ يُضِلُّوكَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِۚ إِن يَتَّبِعُونَ إِلَّا ٱلظَّنَّ وَإِنۡ هُمۡ إِلَّا يَخۡرُصُونَ ١١٦

117. ጌታህ እርሱ ከመንገዱ የሚሳሳቱትን ዐዋቂ ነው፡፡ እርሱም ተመሪዎቹን ዐዋቂ ነው፡፡

إِنَّ رَبَّكَ هُوَ أَعۡلَمُ مَن يَضِلُّ عَن سَبِيلِهِۦۖ وَهُوَ أَعۡلَمُ بِٱلۡمُهۡتَدِينَ ١١٧

118. በአንቀጾቹም አማኞች እንደ ኾናችሁ (ሲታረድ) የአላህ ስም በእርሱ ላይ ከተወሳበት እንስሳ ብሉ፡፡

فَكُلُواْ مِمَّا ذُكِرَ ٱسۡمُ ٱللَّهِ عَلَيۡهِ إِن كُنتُم بِـَٔايَٰتِهِۦ مُؤۡمِنِينَ ١١٨

119. ወደርሱም (መብላት) ከተገደዳችሁበት በስተቀር በእናንተ ላይ እርም የተደረገውን ለእናንተ (አላህ) በእርግጥ የዘረዘረ ሲኾን ከዚያ በእርሱ ላይ የአላህ ስም ከተጠራበት የማትበሉት ለናንተ ምን (ምክንያት) አላችሁ ብዙዎቹም ያለ ዕውቀት በዝንባሌዎቻቸው ያሳስታሉ፡፡ ጌታህ እርሱ ወሰን አላፊዎቹን ዐዋቂ ነው፡፡

وَمَا لَكُمۡ أَلَّا تَأۡكُلُواْ مِمَّا ذُكِرَ ٱسۡمُ ٱللَّهِ عَلَيۡهِ وَقَدۡ فَصَّلَ لَكُم مَّا حَرَّمَ عَلَيۡكُمۡ إِلَّا مَا ٱضۡطُرِرۡتُمۡ إِلَيۡهِۗ وَإِنَّ كَثِيرٗا لَّيُضِلُّونَ بِأَهۡوَآئِهِم بِغَيۡرِ عِلۡمٍۚ إِنَّ رَبَّكَ هُوَ أَعۡلَمُ بِٱلۡمُعۡتَدِينَ ١١٩

120. የኃጢአትንም ግልጹንም ድብቁንም ተውዉ፡፡ እነዚያ ኃጢአትን የሚሠሩ፤ ይሠሩት በነበሩት ነገር በእርግጥ ይቀጣሉ፡፡

وَذَرُواْ ظَٰهِرَ ٱلۡإِثۡمِ وَبَاطِنَهُۥٓۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَكۡسِبُونَ ٱلۡإِثۡمَ سَيُجۡزَوۡنَ بِمَا كَانُواْ يَقۡتَرِفُونَ ١٢٠

121. በእርሱም ላይ የአላህ ስም ካልተጠራበት ነገር አትብሉ፡፡ እርሱም በእርግጥ አመጽ ነው፡፡ ሰይጣናትም ወደ ወዳጆቻቸው (በክትን በመብላት) ይከራከሯችሁ ዘንድ ያሾከሹካሉ፡፡ ብትታዘዙዋቸውም እናንተ በእርግጥ አጋሪዎች ናችሁ፡፡

وَلَا تَأۡكُلُواْ مِمَّا لَمۡ يُذۡكَرِ ٱسۡمُ ٱللَّهِ عَلَيۡهِ وَإِنَّهُۥ لَفِسۡقٞۗ وَإِنَّ ٱلشَّيَٰطِينَ لَيُوحُونَ إِلَىٰٓ أَوۡلِيَآئِهِمۡ لِيُجَٰدِلُوكُمۡۖ وَإِنۡ أَطَعۡتُمُوهُمۡ إِنَّكُمۡ لَمُشۡرِكُونَ ١٢١

122. ሙት የነበረና ሕያው ያደረግነው ለእርሱም በሰዎች መካከል በእርሱ የሚኼድበትን ብርሃን ያደረግንለት ሰው በጨለማዎች ውስጥ ከርሷ የማይወጣ ኾኖ እንዳለለ ሰው ብጤ ነውን እንደዚሁ ለከሓዲዎች ይሠሩት የነበሩት ነገር ተጌጠላቸው፡፡

أَوَمَن كَانَ مَيۡتٗا فَأَحۡيَيۡنَٰهُ وَجَعَلۡنَا لَهُۥ نُورٗا يَمۡشِي بِهِۦ فِي ٱلنَّاسِ كَمَن مَّثَلُهُۥ فِي ٱلظُّلُمَٰتِ لَيۡسَ بِخَارِجٖ مِّنۡهَاۚ كَذَٰلِكَ زُيِّنَ لِلۡكَٰفِرِينَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٢٢

123. እንደዚሁም በየከተማይቱ በውስጧ ያሴሩ ዘንድ የተንኮለኞችዋን ታላላቆች አደረግን፡፡ በነፍሶቻቸውም ላይ እንጅ በሌላ ላይ አያሴሩም፤ ግን አያውቁም፡፡

وَكَذَٰلِكَ جَعَلۡنَا فِي كُلِّ قَرۡيَةٍ أَكَٰبِرَ مُجۡرِمِيهَا لِيَمۡكُرُواْ فِيهَاۖ وَمَا يَمۡكُرُونَ إِلَّا بِأَنفُسِهِمۡ وَمَا يَشۡعُرُونَ ١٢٣

124. ተዓምርም በመጣቻቸው ጊዜ፡- «የአላህ መልክተኞች የተሰጡትን ብጤ እስከንሰጥ ድረስ በፍጹም አናምንም» አሉ፡፡ አላህ መልክቱን የሚያደርግበትን ስፍራ ዐዋቂ ነው፡፡ እነዚያን ያመጹትን ሰዎች ይዶልቱ በነበሩት ነገር አላህ ዘንድ ውርደትና ብርቱ ቅጣት ያገኛቸዋል፡፡

وَإِذَا جَآءَتۡهُمۡ ءَايَةٞ قَالُواْ لَن نُّؤۡمِنَ حَتَّىٰ نُؤۡتَىٰ مِثۡلَ مَآ أُوتِيَ رُسُلُ ٱللَّهِۘ ٱللَّهُ أَعۡلَمُ حَيۡثُ يَجۡعَلُ رِسَالَتَهُۥۗ سَيُصِيبُ ٱلَّذِينَ أَجۡرَمُواْ صَغَارٌ عِندَ ٱللَّهِ وَعَذَابٞ شَدِيدُۢ بِمَا كَانُواْ يَمۡكُرُونَ ١٢٤

125. አላህም ሊመራው የሚሻውን ሰው ደረቱን (ልቡን) ለኢስላም ይከፍትለታል፡፡ ሊያጠመውም የሚሻውን ሰው ደረቱን ጠባብ ቸጋራ ወደ ሰማይ ለመውጣት እንደሚታገል ያደርገዋል፡፡ እንደዚሁ አላህ በእነዚያ በማያምኑት ላይ ርክሰትን ያደርጋል፡፡

فَمَن يُرِدِ ٱللَّهُ أَن يَهۡدِيَهُۥ يَشۡرَحۡ صَدۡرَهُۥ لِلۡإِسۡلَٰمِۖ وَمَن يُرِدۡ أَن يُضِلَّهُۥ يَجۡعَلۡ صَدۡرَهُۥ ضَيِّقًا حَرَجٗا كَأَنَّمَا يَصَّعَّدُ فِي ٱلسَّمَآءِۚ كَذَٰلِكَ يَجۡعَلُ ٱللَّهُ ٱلرِّجۡسَ عَلَى ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ ١٢٥

126. ይህም (ያለህበት) ቀጥተኛ ሲኾን የጌታህ መንገድ ነው:: ለሚያስታውሱ ሕዝቦች አንቀጾችን በእርግጥ ዘርዝረናል::

وَهَٰذَا صِرَٰطُ رَبِّكَ مُسۡتَقِيمٗاۗ قَدۡ فَصَّلۡنَا ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَذَّكَّرُونَ ١٢٦

127. ለእነርሱ በጌታቸው ዘንድ የሰላም አገር አላቸው:: እርሱም (ጌታህ) ይሠሩት በነበሩት ምክንያት ረዳታቸው ነው::

۞لَهُمۡ دَارُ ٱلسَّلَٰمِ عِندَ رَبِّهِمۡۖ وَهُوَ وَلِيُّهُم بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٢٧

128. ሁሉንም የሚሰበስብባቸውንም ቀን (አስታውስ):: የአጋንንት ጭፍሮች ሆይ! ከሰዎች (ጭፍራን በማጥመም) በእርግጥ አበዛችሁ (ይባላሉ):: ከሰዎችም የኾኑት ወዳጆቻቸው:-«ጌታችን ሆይ! ከፊላችን በከፊሉ ተጠቀመ:: ያንንም ለእኛ የወሰንክልንን ጊዜያችንን ደረስን» ይላሉ:: እሳት አላህ የሻው ጊዜ ሲቀር በውስጧ ዘውታሪዎች ስትኾኑ መኖሪያችሁ ናት ይላቸዋል:: ጌታህ ጥበበኛ ዐዋቂ ነውና::

وَيَوۡمَ يَحۡشُرُهُمۡ جَمِيعٗا يَٰمَعۡشَرَ ٱلۡجِنِّ قَدِ ٱسۡتَكۡثَرۡتُم مِّنَ ٱلۡإِنسِۖ وَقَالَ أَوۡلِيَآؤُهُم مِّنَ ٱلۡإِنسِ رَبَّنَا ٱسۡتَمۡتَعَ بَعۡضُنَا بِبَعۡضٖ وَبَلَغۡنَآ أَجَلَنَا ٱلَّذِيٓ أَجَّلۡتَ لَنَاۚ قَالَ ٱلنَّارُ مَثۡوَىٰكُمۡ خَٰلِدِينَ فِيهَآ إِلَّا مَا شَآءَ ٱللَّهُۗ إِنَّ رَبَّكَ حَكِيمٌ عَلِيمٞ ١٢٨

129. እንደዚሁም የበደለኞችን ከፊል በከፊሉ ላይ ይሠሩት በነበሩት ጥፋት ምክንያት እንሾማለን::

وَكَذَٰلِكَ نُوَلِّي بَعۡضَ ٱلظَّٰلِمِينَ بَعۡضَۢا بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ١٢٩

130. የጋኔንና የሰዎች ጭፍሮች ሆይ!:- «አንቀጾቼን በእናንተ ላይ የሚተርኩ የዚህንም ቀናችሁን (ቅጣት) ማግኘትን የሚያስፈራሩዋችሁ ከእናንተው የኾኑ መልክተኞች አልመጧችሁምን» (ይባላሉ):: «በነፍሶቻችን ላይ መሰከርን፤ (መጥተውልናል)» ይላሉ:: የቅርቢቱም ሕይወት አታለለቻቸው:: በነፍሶቻቸውም ላይ እነርሱ ከሓዲዎች የነበሩ መኾናቸውን መሰከሩ::

يَٰمَعۡشَرَ ٱلۡجِنِّ وَٱلۡإِنسِ أَلَمۡ يَأۡتِكُمۡ رُسُلٞ مِّنكُمۡ يَقُصُّونَ عَلَيۡكُمۡ ءَايَٰتِي وَيُنذِرُونَكُمۡ لِقَآءَ يَوۡمِكُمۡ هَٰذَاۚ قَالُواْ شَهِدۡنَا عَلَىٰٓ أَنفُسِنَاۖ وَغَرَّتۡهُمُ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا وَشَهِدُواْ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡ أَنَّهُمۡ كَانُواْ كَٰفِرِينَ ١٣٠

131. ይህ ጌታህ ከተሞችን ባለቤቶችዋ ዘንጊዎች ኾነው ሳሉ በበደል ምክንያት አጥፊ ባለመኾኑ ነው::

ذَٰلِكَ أَن لَّمۡ يَكُن رَّبُّكَ مُهۡلِكَ ٱلۡقُرَىٰ بِظُلۡمٖ وَأَهۡلُهَا غَٰفِلُونَ ١٣١

132. ለሁሉም ከሠሩት ሥራ (የተበላለጡ) ደረጃዎች አልሏቸው:: ጌታህም ከሚሠሩት ሁሉ ዘንጊ አይደለም::

وَلِكُلّٖ دَرَجَٰتٞ مِّمَّا عَمِلُواْۚ وَمَا رَبُّكَ بِغَٰفِلٍ عَمَّا يَعۡمَلُونَ ١٣٢

133. ጌታህም ተብቃቂ የእዝነት ባለቤት ነው:: ቢሻ ያስወግዳችኋል፤ (ያጠፋችኋል):: ከሌሎች ሕዝቦችም ዘሮች እንዳስገኛችሁ ከበኋላችሁ የሚሻውን ይተካል::

وَرَبُّكَ ٱلۡغَنِيُّ ذُو ٱلرَّحۡمَةِۚ إِن يَشَأۡ يُذۡهِبۡكُمۡ وَيَسۡتَخۡلِفۡ مِنۢ بَعۡدِكُم مَّا يَشَآءُ كَمَآ أَنشَأَكُم مِّن ذُرِّيَّةِ قَوۡمٍ ءَاخَرِينَ ١٣٣

134. የምትቀጠሩት ሁሉ በእርግጥ መጪ ነው:: እናንተም አምላጮች አይደላችሁም::

إِنَّ مَا تُوعَدُونَ لَأٓتٖۖ وَمَآ أَنتُم بِمُعۡجِزِينَ ١٣٤

135. «ሕዝቦቼ ሆይ! በችሎታችሁ ላይ ሥሩ፤ እኔ (በችሎታዬ ላይ) ሠሪ ነኝና:: ምስጉኒቱም አገር (ገነት) ለእርሱ የምትኾንለት ሰው ማን እንደኾነ ወደ ፊት ታውቃላችሁ:: እነሆ በደለኞች አይድኑም» በላቸው::

قُلۡ يَٰقَوۡمِ ٱعۡمَلُواْ عَلَىٰ مَكَانَتِكُمۡ إِنِّي عَامِلٞۖ فَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَ مَن تَكُونُ لَهُۥ عَٰقِبَةُ ٱلدَّارِۚ إِنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلظَّٰلِمُونَ ١٣٥

136. ለአላህም ከፈጠረው ከአዝመራና ከግመል፣ ከከብት፣ ከፍየልም ድርሻን አደረጉ፡፡ በሐሳባቸውም «ይህ ለአላህ ነው፡፡ ይህም ለተጋሪዎቻችን ነው፡፡» ለተጋሪዎቻቸውም «(ለጣዖታት) የኾነው ነገር ወደ አላህ አይደርስም፡፡ ለአላህም የኾነው እርሱ ወደ ተጋሪዎቻቸው ይደርሳል» አሉ፡፡ የሚፈርዱት ፍርድ ከፋ!

وَجَعَلُواْ لِلَّهِ مِمَّا ذَرَأَ مِنَ ٱلۡحَرۡثِ وَٱلۡأَنۡعَٰمِ نَصِيبٗا فَقَالُواْ هَٰذَا لِلَّهِ بِزَعۡمِهِمۡ وَهَٰذَا لِشُرَكَآئِنَاۖ فَمَا كَانَ لِشُرَكَآئِهِمۡ فَلَا يَصِلُ إِلَى ٱللَّهِۖ وَمَا كَانَ لِلَّهِ فَهُوَ يَصِلُ إِلَىٰ شُرَكَآئِهِمۡۗ سَآءَ مَا يَحۡكُمُونَ ١٣٦

137. እንደዚሁም ከአጋሪዎቹ ለብዙዎቹ፤ ተጋሪዎቻቸው ሊያጠፉዋቸው ሃይማኖ ታቸውንም በእነሱ ላይ ሊያቀላቅሉባቸው (ሊያመሳስሉባቸው) ልጆቻቸውን መግደልን አሳመሩላቸው፡፡ አላህም በሻ ኖሮ ባልሠሩት ነበር፡፡ ከቅጥፈታቸውም ጋር ተዋቸው፡፡

وَكَذَٰلِكَ زَيَّنَ لِكَثِيرٖ مِّنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ قَتۡلَ أَوۡلَٰدِهِمۡ شُرَكَآؤُهُمۡ لِيُرۡدُوهُمۡ وَلِيَلۡبِسُواْ عَلَيۡهِمۡ دِينَهُمۡۖ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَا فَعَلُوهُۖ فَذَرۡهُمۡ وَمَا يَفۡتَرُونَ ١٣٧

138. በሐሳባቸውም ይህች እርም የኾነች ለማዳ እንስሳና አዝመራ ናት፡፡ የምንሻው ሰው እንጂ ሌላ አይበላትም፡፡ (ይህች) ጀርባዎችዋ እርም የተደረገች ለማዳ እንስሳም ናት (አትጫንም)፡፡ ይህች በርሷ ላይ የአላህን ስም (ስትታረድ) የማይጠሩባትም እንስሳ ናት አሉ፡፡ በእርሱ ላይ ለመቅጠፍ (ነገሩን ወደ አላህ አስጠጉ)፡፡ ይቀጥፉት በነበሩት ነገር በእርግጥ ይቀጣቸዋል፡፡

وَقَالُواْ هَٰذِهِۦٓ أَنۡعَٰمٞ وَحَرۡثٌ حِجۡرٞ لَّا يَطۡعَمُهَآ إِلَّا مَن نَّشَآءُ بِزَعۡمِهِمۡ وَأَنۡعَٰمٌ حُرِّمَتۡ ظُهُورُهَا وَأَنۡعَٰمٞ لَّا يَذۡكُرُونَ ٱسۡمَ ٱللَّهِ عَلَيۡهَا ٱفۡتِرَآءً عَلَيۡهِۚ سَيَجۡزِيهِم بِمَا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ١٣٨

139. «በነዚህም እንስሶች ሆዶች ውስጥ ያለው ለወንዶቻችን በተለይ የተፈቀደ ነው፡፡ በሚስቶቻችንም ላይ እርም የተደረገ ነው፡፡ ሙትም ቢኾን (ሙት ኾኖ ቢወለድ) እነርሱ (ወንዶቹም ሴቶቹም) በርሱ ተጋሪዎች ናቸው» አሉ፡፡ በመቅጠፋቸው አላህ በእርግጥ ይቀጣቸዋል፡፡ እርሱ ጥበበኛ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَقَالُواْ مَا فِي بُطُونِ هَٰذِهِ ٱلۡأَنۡعَٰمِ خَالِصَةٞ لِّذُكُورِنَا وَمُحَرَّمٌ عَلَىٰٓ أَزۡوَٰجِنَاۖ وَإِن يَكُن مَّيۡتَةٗ فَهُمۡ فِيهِ شُرَكَآءُۚ سَيَجۡزِيهِمۡ وَصۡفَهُمۡۚ إِنَّهُۥ حَكِيمٌ عَلِيمٞ ١٣٩

140. እነዚያ ያለ ዕውቀት በሞኝነት ልጆቻቸውን የገደሉና አላህም የሰጣቸውን (ሲሳይ) በአላህ ላይ በመቅጠፍ እርም ያደረጉ በእርግጥ ከሰሩ፡፡ በእርግጥ ተሳሳቱ፡፡ ተመሪዎችም አልነበሩም፡፡

قَدۡ خَسِرَ ٱلَّذِينَ قَتَلُوٓاْ أَوۡلَٰدَهُمۡ سَفَهَۢا بِغَيۡرِ عِلۡمٖ وَحَرَّمُواْ مَا رَزَقَهُمُ ٱللَّهُ ٱفۡتِرَآءً عَلَى ٱللَّهِۚ قَدۡ ضَلُّواْ وَمَا كَانُواْ مُهۡتَدِينَ ١٤٠

141. እርሱም ያ ዳስ የሚደረግላቸውንና ዳስ የማይደረግላቸውን አትክልቶች የፈጠረ ነው፡፡ ዘምባባንም (የተምርን ዛፍ) አዝመራንም ፍሬዎቹ የተለያዩ ሲኾኑ ወይራንና ሩማንንም (ቅጠላቸው) ተመሳሳይና (ጣዕማቸው) የማይመሳሰል ሲኾኑ (ፈጠረ)፡፡ ባፈራ ጊዜ ከፍሬው ብሉ፡፡ በአጨዳውም ቀን ተገቢውን (ዘካ) ስጡ፡፡ አታባክኑም፡፡ እርሱ አባካኞችን አይወድምና፡፡

۞وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَنشَأَ جَنَّٰتٖ مَّعۡرُوشَٰتٖ وَغَيۡرَ مَعۡرُوشَٰتٖ وَٱلنَّخۡلَ وَٱلزَّرۡعَ مُخۡتَلِفًا أُكُلُهُۥ وَٱلزَّيۡتُونَ وَٱلرُّمَّانَ مُتَشَٰبِهٗا وَغَيۡرَ مُتَشَٰبِهٖۚ كُلُواْ مِن ثَمَرِهِۦٓ إِذَآ أَثۡمَرَ وَءَاتُواْ حَقَّهُۥ يَوۡمَ حَصَادِهِۦۖ وَلَا تُسۡرِفُوٓاْۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ١٤١

142. ከለማዳ እንስሳዎችም የሚጫኑትንና የማይጫኑትን (ፈጠረ)፡፡ አላህ ከሰጣችሁ ሲሳይ ብሉ፡፡ የሰይጣንንም እርምጃዎች አትከተሉ፡፡ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና፡፡

وَمِنَ ٱلۡأَنۡعَٰمِ حَمُولَةٗ وَفَرۡشٗاۚ كُلُواْ مِمَّا رَزَقَكُمُ ٱللَّهُ وَلَا تَتَّبِعُواْ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيۡطَٰنِۚ إِنَّهُۥ لَكُمۡ عَدُوّٞ مُّبِينٞ ١٤٢

143. ስምንትን ዓይነቶች ከበግ ሁለትን (ወንድና ሴትን) ከፍየልም ሁለትን (ፈጠረ)፡፡«ከሁለቱም ከፍሎች አላህ ወንዶቹን እርም አደረገን ወይስ ሴቶቹን ወይስ በርሱ ላይ የሁለቱ ሴቶች ማሕፀኖች ያጠቃለሉትን እውነተኞች እንደሆናችሁ በዕውቀት (በአስረጅ) ንገሩኝ» በላቸው፡፡

144. ከግመልም ሁለትን ከከብትም ሁለትን (ፈጠረ)፡፡ «አላህ (ከሁለቱ) ወንዶቹን እርም አደረገን ወይስ ሴቶቹን ወይስ የሁለቱ ሴቶች ማሕፀኖች በእርሱ ላይ ያጠቃለሉትን በእውነቱ አላህ በዚህ ባዘዛችሁ ጊዜ የተጣዳችሁ ነበራችሁን ሰዎችንም ያለ ዕውቀት ሊያጠም በአላህ ላይ ውሸትንም ከቀጠፈ ሰው ይበልጥ በደለኛ ማን ነው አላህ በደለኞችን ሕዝቦች (ቅኑን መንገድ) አይመራም፡፡»

145. (ሙሐመድ ሆይ!) በላቸው:- «ወደእኔ በተወረደው ውስጥ በክት ወይም ፈሳሽ ደም ወይም የአሳማ ስጋ እርሱ ርኩስ ነውና ወይም በአመጽ ከአላህ ስም ሌላ በእርሱ ላይ የተወሳበት ካልኾነ በስተቀር በሚመገበው ተመጋቢ ላይ እርም የኾነን ነገር አላገኝም፡ ፡ አመጸኛና ወሰን ያለፈ ሳይኾንም የተገደደ ሰው (ከተወሱት ቢበላ ኃጢአት የለበትም)፡፡ ጌታህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡»

146. በእነዚያም አይሁዳውያን በኾኑት ላይ ባለ ጥፍርን ሁሉ እርም አደረግን፡፡ ከከብት፣ ከፍየልና ከበግም ሞራዎቻቸውን ጀርባዎቻቸው ወይም አንጀቶቻቸው የተሸከሙት ወይም በአጥንት የተቀላቀለው (ስብ) ሲቀር በነርሱ ላይ እርም አደረግን፡፡ ይህንን በአመጻቸው ምክንያት ቀጣናቸው፡፡ እኛ እውነተኞች ነን፡፡

147. ቢያስተባብሉህም:- «ጌታችሁ የሰፊ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡ ብርቱ ቅጣቱም ከአመጸኞች ሕዝቦች ላይ አይመለስም» በላቸው፡፡

148. እነዚያ ያጋሩት «አላህ በሻ ኖሮ እኛም አባቶቻችንም ባላገራን ነበር፡፡ አንዳችንም ነገር እርም ባላደረግን ነበር ይላሉ፡፡ እንደዚሁ (እነዚህን እንደዋሹ) እነዚያ ከበፊታቸው የነበሩት ብርቱ ቅጣታችንን እስከቀመሱ ድረስ አስተባባሉ፡፡ ለእኛ ታዘልቁልን ዘንድ (ማጋራታችሁን ለመውደዱ) እናንተ ዘንድ ዕውቀት አለን ጥርጣሬን እንጅ ሌላ አትከተሉም፡፡ እናንተ ዋሾዎች እንጂ ሌላ አይደላችሁም» በላቸው፡፡

149. «የተሟላው ማስረጃ የአላህ ነው፡፡ በሻም ኖሮ ሁላችሁንም ባቀናችሁ ነበር» በላቸው፡፡

ثَمَٰنِيَةَ أَزۡوَٰجٖۖ مِّنَ ٱلضَّأۡنِ ٱثۡنَيۡنِ وَمِنَ ٱلۡمَعۡزِ ٱثۡنَيۡنِۗ قُلۡ ءَآلذَّكَرَيۡنِ حَرَّمَ أَمِ ٱلۡأُنثَيَيۡنِ أَمَّا ٱشۡتَمَلَتۡ عَلَيۡهِ أَرۡحَامُ ٱلۡأُنثَيَيۡنِۖ نَبِّـُٔونِي بِعِلۡمٍ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ﴿١٤٣﴾

وَمِنَ ٱلۡإِبِلِ ٱثۡنَيۡنِ وَمِنَ ٱلۡبَقَرِ ٱثۡنَيۡنِۗ قُلۡ ءَآلذَّكَرَيۡنِ حَرَّمَ أَمِ ٱلۡأُنثَيَيۡنِ أَمَّا ٱشۡتَمَلَتۡ عَلَيۡهِ أَرۡحَامُ ٱلۡأُنثَيَيۡنِۖ أَمۡ كُنتُمۡ شُهَدَآءَ إِذۡ وَصَّىٰكُمُ ٱللَّهُ بِهَٰذَاۚ فَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبٗا لِّيُضِلَّ ٱلنَّاسَ بِغَيۡرِ عِلۡمٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٤٤﴾

قُل لَّآ أَجِدُ فِي مَآ أُوحِيَ إِلَيَّ مُحَرَّمًا عَلَىٰ طَاعِمٖ يَطۡعَمُهُۥٓ إِلَّآ أَن يَكُونَ مَيۡتَةً أَوۡ دَمٗا مَّسۡفُوحًا أَوۡ لَحۡمَ خِنزِيرٖ فَإِنَّهُۥ رِجۡسٌ أَوۡ فِسۡقًا أُهِلَّ لِغَيۡرِ ٱللَّهِ بِهِۦۚ فَمَنِ ٱضۡطُرَّ غَيۡرَ بَاغٖ وَلَا عَادٖ فَإِنَّ رَبَّكَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿١٤٥﴾

وَعَلَى ٱلَّذِينَ هَادُواْ حَرَّمۡنَا كُلَّ ذِي ظُفُرٖۖ وَمِنَ ٱلۡبَقَرِ وَٱلۡغَنَمِ حَرَّمۡنَا عَلَيۡهِمۡ شُحُومَهُمَآ إِلَّا مَا حَمَلَتۡ ظُهُورُهُمَآ أَوِ ٱلۡحَوَايَآ أَوۡ مَا ٱخۡتَلَطَ بِعَظۡمٖۚ ذَٰلِكَ جَزَيۡنَٰهُم بِبَغۡيِهِمۡۖ وَإِنَّا لَصَٰدِقُونَ ﴿١٤٦﴾

فَإِن كَذَّبُوكَ فَقُل رَّبُّكُمۡ ذُو رَحۡمَةٖ وَٰسِعَةٖ وَلَا يُرَدُّ بَأۡسُهُۥ عَنِ ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ﴿١٤٧﴾

سَيَقُولُ ٱلَّذِينَ أَشۡرَكُواْ لَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَآ أَشۡرَكۡنَا وَلَآ ءَابَآؤُنَا وَلَا حَرَّمۡنَا مِن شَيۡءٖۚ كَذَٰلِكَ كَذَّبَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ حَتَّىٰ ذَاقُواْ بَأۡسَنَاۗ قُلۡ هَلۡ عِندَكُم مِّنۡ عِلۡمٖ فَتُخۡرِجُوهُ لَنَآۖ إِن تَتَّبِعُونَ إِلَّا ٱلظَّنَّ وَإِنۡ أَنتُمۡ إِلَّا تَخۡرُصُونَ ﴿١٤٨﴾

قُلۡ فَلِلَّهِ ٱلۡحُجَّةُ ٱلۡبَٰلِغَةُۖ فَلَوۡ شَآءَ لَهَدَىٰكُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿١٤٩﴾

150. «እነዚያን አላህ ይህን እርም ማድረጉን የሚመሰክሩትን ምስክሮቻችሁን አምጡ» በላቸው፡፡ ቢመሰክሩም ከእነርሱ ጋር አትመስክር፡፡ የነዚያንም በአንቀጾቻችን ያስተባበሉትን የነዚያንም እነርሱ በጌታቸው (ሌላን) የሚያስተካክሉ ሲኾኑ በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑትን ሰዎች ዝንባሌዎች አትከተል፡፡

قُلْ هَلُمَّ شُهَدَآءَكُمُ ٱلَّذِينَ يَشْهَدُونَ أَنَّ ٱللَّهَ حَرَّمَ هَٰذَا ۖ فَإِن شَهِدُوا۟ فَلَا تَشْهَدْ مَعَهُمْ ۚ وَلَا تَتَّبِعْ أَهْوَآءَ ٱلَّذِينَ كَذَّبُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَا وَٱلَّذِينَ لَا يُؤْمِنُونَ بِٱلْءَاخِرَةِ وَهُم بِرَبِّهِمْ يَعْدِلُونَ ﴿١٥٠﴾

151. «ኑ፤ ጌታችሁ በእናንተ ላይ እርም ያደረገውን ነገር (በእርሱም ያዘዛችሁን) ላንብብላችሁ» በላቸው፡፡ «በእርሱ (በአላህ) ምንንም ነገር አታጋሩ፡፡ ለወላጆችም በጎን ሥራ (ሥሩ)፡፡ ልጆቻችሁንም ከድህነት (ፍራቻ) አትግደሉ፡፡ እኛ እናንተንም እነርሱንም እንመግባችኋለንና፡፡ መጥፎ ሥራዎችንም ከእርሷ የተገለጸውንም የተደበቀውንም ሁሉ አትቅረቡ፡፡ ያችንም አላህ እርም ያደረጋትን ነፍስ በሕግ ቢኾን እንጅ አትግደሉ፡፡ ይህን ታውቁ ዘንድ (አላህ) በእርሱ አዘዛችሁ፡፡»

۞ قُلْ تَعَالَوْا۟ أَتْلُ مَا حَرَّمَ رَبُّكُمْ عَلَيْكُمْ ۖ أَلَّا تُشْرِكُوا۟ بِهِۦ شَيْـًٔا ۖ وَبِٱلْوَٰلِدَيْنِ إِحْسَٰنًا ۖ وَلَا تَقْتُلُوٓا۟ أَوْلَٰدَكُم مِّنْ إِمْلَٰقٍ ۖ نَّحْنُ نَرْزُقُكُمْ وَإِيَّاهُمْ ۖ وَلَا تَقْرَبُوا۟ ٱلْفَوَٰحِشَ مَا ظَهَرَ مِنْهَا وَمَا بَطَنَ ۖ وَلَا تَقْتُلُوا۟ ٱلنَّفْسَ ٱلَّتِى حَرَّمَ ٱللَّهُ إِلَّا بِٱلْحَقِّ ۚ ذَٰلِكُمْ وَصَّىٰكُم بِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَعْقِلُونَ ﴿١٥١﴾

152. «የየቲምንም ገንዘብ ብርታቱን (አካለ መጠን) እስኪደርስ ድረስ በዚያች እርሷ መልካም በኾነች ኹኔታ እንጅ አትቅረቡ፡፡ ስፍርንና ሚዛንንም በትክክሉ ሙሉ፡፡ ነፍስን ችሎታዋን እንጂ አናስገድድም፡፡ በተናገራችሁም ጊዜ በዘመዶቻችሁ ላይ ቢኾንም እንኳ (እውነትን በመናገር) አስተካክሉ፡፡ በአላህም ቃል ኪዳን ሙሉ፡፡ እነሆ ትገሰጹ ዘንድ በርሱ አዘዛችሁ፡፡»

وَلَا تَقْرَبُوا۟ مَالَ ٱلْيَتِيمِ إِلَّا بِٱلَّتِى هِىَ أَحْسَنُ حَتَّىٰ يَبْلُغَ أَشُدَّهُۥ ۖ وَأَوْفُوا۟ ٱلْكَيْلَ وَٱلْمِيزَانَ بِٱلْقِسْطِ ۖ لَا نُكَلِّفُ نَفْسًا إِلَّا وُسْعَهَا ۖ وَإِذَا قُلْتُمْ فَٱعْدِلُوا۟ وَلَوْ كَانَ ذَا قُرْبَىٰ ۖ وَبِعَهْدِ ٱللَّهِ أَوْفُوا۟ ۚ ذَٰلِكُمْ وَصَّىٰكُم بِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَذَكَّرُونَ ﴿١٥٢﴾

153. «ይህም ቀጥተኛ ሲኾን መንገዴ ነው፤ ተከተሉትም፡፡ (የጥመት) መንገዶችንም አትከተሉ፡፡ ከ(ቀጥተኛው) መንገዱ እናንተን ይለያዩዋችኋልና፡፡ እነሆ ትጠነቀቁ ዘንድ በርሱ አዘዛችሁ፡፡»

وَأَنَّ هَٰذَا صِرَٰطِى مُسْتَقِيمًا فَٱتَّبِعُوهُ ۖ وَلَا تَتَّبِعُوا۟ ٱلسُّبُلَ فَتَفَرَّقَ بِكُمْ عَن سَبِيلِهِۦ ۚ ذَٰلِكُمْ وَصَّىٰكُم بِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَتَّقُونَ ﴿١٥٣﴾

154. ከዚያም ለሙሳ በዚያ መልካም በሠራው ላይ (ጸጋችንን) ለማሟላት ነገርንም ሁሉ ለመዘርዘር መጽሐፉን (ለእስራኤል ልጆች) መሪና እዝነት ይኾን ዘንድ ሰጠነው፡፡ እነርሱ በጌታቸው መገናኘት ሊያምኑ ይከጀላልና፡፡

ثُمَّ ءَاتَيْنَا مُوسَى ٱلْكِتَٰبَ تَمَامًا عَلَى ٱلَّذِىٓ أَحْسَنَ وَتَفْصِيلًا لِّكُلِّ شَىْءٍ وَهُدًى وَرَحْمَةً لَّعَلَّهُم بِلِقَآءِ رَبِّهِمْ يُؤْمِنُونَ ﴿١٥٤﴾

155. ይህም ያወረድነው የኾነ የተባረከ መጽሐፍ ነው፡፡ ተከተሉትም፡፡ ይታዘንላችሁም ዘንድ (ከክህደት) ተጠንቀቁ፡፡

وَهَٰذَا كِتَٰبٌ أَنزَلْنَٰهُ مُبَارَكٌ فَٱتَّبِعُوهُ وَٱتَّقُوا۟ لَعَلَّكُمْ تُرْحَمُونَ ﴿١٥٥﴾

156. «(ያወረድነውም) መጽሐፍ የተወረደው ከፊታችን በሁለቱ ጭፍሮች ላይ ብቻ ነው፡፡ እኛም ከንባባቸው ዘንጊዎች ነበርን» እንዳትሉ ነው፡፡

أَن تَقُولُوٓا۟ إِنَّمَآ أُنزِلَ ٱلْكِتَٰبُ عَلَىٰ طَآئِفَتَيْنِ مِن قَبْلِنَا وَإِن كُنَّا عَن دِرَاسَتِهِمْ لَغَٰفِلِينَ ﴿١٥٦﴾

157. ወይም «እኛ መጽሐፍ በእኛ ላይ በተወረደ ኖሮ ከእነሱ ይበልጥ የተመራን እንኾን ነበር» እንዳትሉ ነው፡፡ ስለዚህ ከጌታችሁ ግልጽ ማስረጃ፣ መምሪያም፣ እዝነትም በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ በአላህም አንቀጾች ካስተባበለና ከእርሷም ከዞረ ሰው ይበልጥ በዳይ ማን ነው እነዚያን አንቀጾቻችንን የሚተውትን ይተውት በነበሩት ምክንያት ብርቱን ቅጣት በእርግጥ እንቀጣቸዋለን፡፡

أَوۡ تَقُولُواْ لَوۡ أَنَّآ أُنزِلَ عَلَيۡنَا ٱلۡكِتَٰبُ لَكُنَّآ أَهۡدَىٰ مِنۡهُمۡۚ فَقَدۡ جَآءَكُم بَيِّنَةٞ مِّن رَّبِّكُمۡ وَهُدٗى وَرَحۡمَةٞۚ فَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّن كَذَّبَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَصَدَفَ عَنۡهَاۗ سَنَجۡزِي ٱلَّذِينَ يَصۡدِفُونَ عَنۡ ءَايَٰتِنَا سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِ بِمَا كَانُواْ يَصۡدِفُونَ ١٥٧

158. መላእክት ልትመጣላቸው ወይም ጌታህ (ቅጣቱ) ሊመጣ ወይም ከጌታህ ምልክቶች ከፊሉ ሊመጣ እንጂ ይጠባበቃሉን ከጌታህ ምልክቶች ከፊሉ በሚመጣ ቀን ከዚህ በፊት አማኝ ያልኾነችን ነፍስ እምነትዋ ወይም በእምነትዋ (ጊዜ) በጎ ያልሠራችን (ነፍስ ጸጸትዋ) አይጠቅማትም፡፡ ተጠባበቁ እኛ ተጠባባቂዎች ነንና በላቸው፡፡

هَلۡ يَنظُرُونَ إِلَّآ أَن تَأۡتِيَهُمُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ أَوۡ يَأۡتِيَ رَبُّكَ أَوۡ يَأۡتِيَ بَعۡضُ ءَايَٰتِ رَبِّكَۗ يَوۡمَ يَأۡتِي بَعۡضُ ءَايَٰتِ رَبِّكَ لَا يَنفَعُ نَفۡسًا إِيمَٰنُهَا لَمۡ تَكُنۡ ءَامَنَتۡ مِن قَبۡلُ أَوۡ كَسَبَتۡ فِيٓ إِيمَٰنِهَا خَيۡرٗاۗ قُلِ ٱنتَظِرُوٓاْ إِنَّا مُنتَظِرُونَ ١٥٨

159. እነዚያ ሃይማኖታቸውን የለያዩ አሕዛብም የኾኑ በምንም ከእነሱ አይደለህም፡፡ ነገራቸው ወደ አላህ ብቻ ነው፡፡ ከዚያም ይሠሩት የነበሩትን ሁሉ ይነገራቸዋል፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ فَرَّقُواْ دِينَهُمۡ وَكَانُواْ شِيَعٗا لَّسۡتَ مِنۡهُمۡ فِي شَيۡءٍۚ إِنَّمَآ أَمۡرُهُمۡ إِلَى ٱللَّهِ ثُمَّ يُنَبِّئُهُم بِمَا كَانُواْ يَفۡعَلُونَ ١٥٩

160. በመልካም ሥራ የመጣ ሰው ለእርሱ ዐሥር ብጤዎችዋ አሉት፡፡ በክፉ ሥራም የመጣ ሰው ብጤዋን እንጅ አይመነዳም፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

مَن جَآءَ بِٱلۡحَسَنَةِ فَلَهُۥ عَشۡرُ أَمۡثَالِهَاۖ وَمَن جَآءَ بِٱلسَّيِّئَةِ فَلَا يُجۡزَىٰٓ إِلَّا مِثۡلَهَا وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ١٦٠

161. «እኔ ጌታዬ ወደ ቀጥተኛው መንገድ ትክክለኛን ሃይማኖት ወደ እውነት አዘንባይ ሲኾን የአብርሃምን መንገድ መራኝ፡፡ እርሱም ከአጋሪዎቹ አልነበረም» በል፡፡

قُلۡ إِنَّنِي هَدَىٰنِي رَبِّيٓ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ دِينٗا قِيَمٗا مِّلَّةَ إِبۡرَٰهِيمَ حَنِيفٗاۚ وَمَا كَانَ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ١٦١

162. «ስግደቴ፣ መገዛቴም፣ ሕይወቴም፣ ሞቴም ለዓለማት ጌታ ለአላህ ነው» በል፡፡

قُلۡ إِنَّ صَلَاتِي وَنُسُكِي وَمَحۡيَايَ وَمَمَاتِي لِلَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٦٢

163. «ለእርሱ ተጋሪ የለውም፡፡ በዚህም (በማጥራት) ታዘዝኩ፡፡ እኔም የሙስሊሞች መጀመሪያ ነኝ» (በል)፡፡

لَا شَرِيكَ لَهُۥۖ وَبِذَٰلِكَ أُمِرۡتُ وَأَنَا۠ أَوَّلُ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ١٦٣

164. በላቸው «እርሱ (አላህ) የሁሉ ጌታ ሲኾን ከአላህ በቀር ሌላን ጌታ እፈልጋለሁን ነፍስም ሁሉ በራሷ ላይ እንጅ (ክፉን) አትሠራም፡፡ ተሸካሚም (ነፍስ) የሌላይቱን ሸክም (ኃጢአት) አትሸከምም፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደ ጌታችሁ ነው፡፡ ወዲያውም በእርሱ ትለያዩበት የነበራችሁትን ሁሉ ይነገራችኋል፡፡»

قُلۡ أَغَيۡرَ ٱللَّهِ أَبۡغِي رَبّٗا وَهُوَ رَبُّ كُلِّ شَيۡءٖۚ وَلَا تَكۡسِبُ كُلُّ نَفۡسٍ إِلَّا عَلَيۡهَاۚ وَلَا تَزِرُ وَازِرَةٞ وِزۡرَ أُخۡرَىٰۚ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّكُم مَّرۡجِعُكُمۡ فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ فِيهِ تَخۡتَلِفُونَ ١٦٤

وَهُوَ ٱلَّذِى جَعَلَكُمْ خَلَـٰٓئِفَ ٱلْأَرْضِ وَرَفَعَ بَعْضَكُمْ فَوْقَ بَعْضٍ دَرَجَـٰتٍ لِّيَبْلُوَكُمْ فِى مَآ ءَاتَىٰكُمْ ۗ إِنَّ رَبَّكَ سَرِيعُ ٱلْعِقَابِ وَإِنَّهُۥ لَغَفُورٌ رَّحِيمٌۢ ﴿١٦٥﴾

165. እርሱም ያ በምድር ምትኮች ያደረጋችሁ በሰጣችሁም ጸጋ ሊፈትናችሁ ከፊላችሁን ከከፊሉ በላይ በደረጃዎች ከፍ ያደረገ ነው፡፡ ጌታህ ቅጣቱ ፈጣን ነው፡ ፡ እርሱም እጅግ መሓሪ ሩኅሩኅ ነው፡፡

# سورة الأعراف

# ሱረቱ አል-አዕራፍ

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

الٓمٓصٓ ﴿١﴾

1. አ.ለ.መ.ሰ (አሊፍ፤ ላም ፤ሚም፤ ሷድ)፡፡

كِتَـٰبٌ أُنزِلَ إِلَيْكَ فَلَا يَكُن فِى صَدْرِكَ حَرَجٌ مِّنْهُ لِتُنذِرَ بِهِۦ وَذِكْرَىٰ لِلْمُؤْمِنِينَ ﴿٢﴾

2. (ይህ) ወደ አንተ የተወረደ መጽሐፍ ነው፡፡ በደረትህም ውስጥ ከእርሱ ጭንቀት አይኑር፡፡ (የተወረደውም) በእርሱ ልታስፈራራበትና ለምእምናን መገሠጫ እንዲኾን ነው፡፡

ٱتَّبِعُوا۟ مَآ أُنزِلَ إِلَيْكُم مِّن رَّبِّكُمْ وَلَا تَتَّبِعُوا۟ مِن دُونِهِۦٓ أَوْلِيَآءَ ۗ قَلِيلًا مَّا تَذَكَّرُونَ ﴿٣﴾

3. ከጌታችሁ ወደእናንተ የተወረደውን ተከተሉ፡፡ ከአላህም ሌላ ረዳቶችን አትከተሉ፡፡ ጥቂትን ብቻ ትገሰጻላችሁ፡፡

وَكَم مِّن قَرْيَةٍ أَهْلَكْنَـٰهَا فَجَآءَهَا بَأْسُنَا بَيَـٰتًا أَوْ هُمْ قَآئِلُونَ ﴿٤﴾

4. ከከተማም ልናጠፋት የሻነው ወዲያውም ብርቱ ቅጣታችን ሌሊት ወይም ቀን እነርሱ በቀትር አርፈው ሳሉ የመጣባቸው ብዙ ናቸው፡፡

فَمَا كَانَ دَعْوَىٰهُمْ إِذْ جَآءَهُم بَأْسُنَآ إِلَّآ أَن قَالُوٓا۟ إِنَّا كُنَّا ظَـٰلِمِينَ ﴿٥﴾

5. ቅጣታችንም በመጣባቸው ጊዜ «ጸሎታቸው እኛ በደለኞች ነበርን» ከማለት በቀር ሌላ አልነበረም፡፡

فَلَنَسْـَٔلَنَّ ٱلَّذِينَ أُرْسِلَ إِلَيْهِمْ وَلَنَسْـَٔلَنَّ ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿٦﴾

6. እነዚያንም ወደነሱ የተላከባቸውን (ሕዝቦች) በእርግጥ መልክተኞቹንም እንጠይቃለን፡፡

فَلَنَقُصَّنَّ عَلَيْهِم بِعِلْمٍ ۖ وَمَا كُنَّا غَآئِبِينَ ﴿٧﴾

7. በእነርሱም ላይ (የነበሩበትን ሁሉ) ከዕውቀት ጋር በእርግጥ እንተርክላቸዋለን፡፡ የራቅንም አልነበርንም፡፡

وَٱلْوَزْنُ يَوْمَئِذٍ ٱلْحَقُّ ۚ فَمَن ثَقُلَتْ مَوَٰزِينُهُۥ فَأُو۟لَـٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُفْلِحُونَ ﴿٨﴾

8. ትክክለኛውም ሚዛን የዚያን ቀን ነው፡፡ ሚዛኖቻቸው የከበዱላቸው ሰዎችም እነዚያ እነርሱ የፈለጉትን ያገኙ ናቸው፡፡

وَمَنْ خَفَّتْ مَوَٰزِينُهُۥ فَأُو۟لَـٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓا۟ أَنفُسَهُم بِمَا كَانُوا۟ بِـَٔايَـٰتِنَا يَظْلِمُونَ ﴿٩﴾

9. ሚዛኖቻቸው የቀለሉባቸው ሰዎችም እነዚያ እነርሱ ተአምራቶቻችንን ይክዱ በነበሩት ምክንያት ነፍሶቻቸውን ያከሰሩ ናቸው፡፡

وَلَقَدۡ مَكَّنَّٰكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَجَعَلۡنَا لَكُمۡ فِيهَا مَعَٰيِشَۗ قَلِيلٗا مَّا تَشۡكُرُونَ ١٠

10. በምድርም ላይ በእርግጥ አስመቸናችሁ፡፡ በእርሷም ላይ ለናንተ መኖሪያዎችን አደረግንላችሁ፤ ምስጋናችሁ በጣም ጥቂት ነው፡፡

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَٰكُمۡ ثُمَّ صَوَّرۡنَٰكُمۡ ثُمَّ قُلۡنَا لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ ٱسۡجُدُواْ لِأٓدَمَ فَسَجَدُوٓاْ إِلَّآ إِبۡلِيسَ لَمۡ يَكُن مِّنَ ٱلسَّٰجِدِينَ ١١

11. በእርግጥም ፈጠርናችሁ፡፡ ከዚያም ቀረጽናችሁ፡፡ ከዚያም ለመላእክቶች «ለአዳም ስገዱ» አልን፡፡ ወዲያውም ሰገዱ፡፡ ኢብሊስ (ዲያብሎስ) ሲቀር ከሰጋጆቹ አልኾነም፡፡

قَالَ مَا مَنَعَكَ أَلَّا تَسۡجُدَ إِذۡ أَمَرۡتُكَۖ قَالَ أَنَا۠ خَيۡرٞ مِّنۡهُ خَلَقۡتَنِي مِن نَّارٖ وَخَلَقۡتَهُۥ مِن طِينٖ ١٢

12. (አላህ) «ባዘዝኩህ ጊዜ ከመስገድ ምን ከለከለህ» አለው፡፡ «እኔ ከርሱ የበለጥኩ ነኝ፡፡ ከእሳት ፈጠርከኝ፡ ፡ እርሱን ግን ከጭቃ ፈጠርከው» አለ፡፡

قَالَ فَٱهۡبِطۡ مِنۡهَا فَمَا يَكُونُ لَكَ أَن تَتَكَبَّرَ فِيهَا فَٱخۡرُجۡ إِنَّكَ مِنَ ٱلصَّٰغِرِينَ ١٣

13. ከእርሷ ውረድ፤ በእርሷ ውስጥ ልትኮራ አይገባህምና፡፡ ውጣም አንተ ከወራዶቹ ነህና አለው፡፡

قَالَ أَنظِرۡنِيٓ إِلَىٰ يَوۡمِ يُبۡعَثُونَ ١٤

14. «እስከሚቀሰቀሱበት ቀን ድረስ አቆየኝ» አለ፡፡

قَالَ إِنَّكَ مِنَ ٱلۡمُنظَرِينَ ١٥

15. ፡-አንተ ከሚቆዩት ነህ አለው፡፡

قَالَ فَبِمَآ أَغۡوَيۡتَنِي لَأَقۡعُدَنَّ لَهُمۡ صِرَٰطَكَ ٱلۡمُسۡتَقِيمَ ١٦

16. «ስለአጠመምከኝም ለእነርሱ በቀጥተኛው መንገድ ላይ በእርግጥ እቀመጥባቸዋለሁ» አለ፡፡

ثُمَّ لَأٓتِيَنَّهُم مِّنۢ بَيۡنِ أَيۡدِيهِمۡ وَمِنۡ خَلۡفِهِمۡ وَعَنۡ أَيۡمَٰنِهِمۡ وَعَن شَمَآئِلِهِمۡۖ وَلَا تَجِدُ أَكۡثَرَهُمۡ شَٰكِرِينَ ١٧

17. «ከዚያም ከስተፊቶቻቸው ከኋላቸውም ከቀኞቻቸውም ከግራዎቻቸውም በእርግጥ እመጣባቸዋለሁ፡፡ አብዛኞቻቸውንም አመስጋኞች ኾነው አታገኛቸውም» (አለ)፡፡

قَالَ ٱخۡرُجۡ مِنۡهَا مَذۡءُومٗا مَّدۡحُورٗاۖ لَّمَن تَبِعَكَ مِنۡهُمۡ لَأَمۡلَأَنَّ جَهَنَّمَ مِنكُمۡ أَجۡمَعِينَ ١٨

18. «የተጠላህ ብራሪ ስትኾን ከእርሷ ውጣ፡፡ ከእነርሱ የተከተለህ ከእናንተ ከመላችሁም ገሀነምን በእርግጥ እሞላታለሁ» አለው፡፡

وَيَٰٓـَٔادَمُ ٱسۡكُنۡ أَنتَ وَزَوۡجُكَ ٱلۡجَنَّةَ فَكُلَا مِنۡ حَيۡثُ شِئۡتُمَا وَلَا تَقۡرَبَا هَٰذِهِ ٱلشَّجَرَةَ فَتَكُونَا مِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٩

19. «አዳም ሆይ! አንተም ሚስትህም በገነት ተቀመጡ፡፡ ከሻችሁትም ስፍራ ብሉ፡፡ ግን ይህችን ዛፍ አትቅረቡ፡፡ (ራሳቸውን) ከሚበድሉት ትኾናላችሁና» (አላቸው)፡፡

فَوَسۡوَسَ لَهُمَا ٱلشَّيۡطَٰنُ لِيُبۡدِيَ لَهُمَا مَا وُۥرِيَ عَنۡهُمَا مِن سَوۡءَٰتِهِمَا وَقَالَ مَا نَهَىٰكُمَا رَبُّكُمَا عَنۡ هَٰذِهِ ٱلشَّجَرَةِ إِلَّآ أَن تَكُونَا مَلَكَيۡنِ أَوۡ تَكُونَا مِنَ ٱلۡخَٰلِدِينَ ٢٠

20. ሰይጣንም ከሐፍረተ ገላቸው የተሸሸገውን ለእነርሱ ሊገልጽባቸው በድብቅ ንግግር ጎተጎታቸው፡፡ «ጌታችሁም መልአኮች እንዳትኾኑ ወይም ከዘላለም ነዋሪዎች እንዳትኾኑ እንጂ ከዚህች ዛፍ አልከለከላችሁም» አላቸው፡፡

وَقَاسَمَهُمَآ إِنِّي لَكُمَا لَمِنَ ٱلنَّٰصِحِينَ ٢١

21. «እኔ ለእናንተ በእርግጥ ከሚመክሩዋችሁ ነኝ» ሲልም አማለላቸው፡፡

22. በማታለልም አዋረዳቸው፡፡ ከዛፊቱም በቀመሱ ጊዜ ኀፍረተ ገላቸው ለሁለቱም ተገለጠችላቸው፡፡ ከገነት ቅጠልም በላያቸው ላይ ይደርቱ ጀመር፡፡ ጌታቸውም «ከዚህ ዛፍ አልከለከልኋችሁምን ሰይጣንም ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነው አላልኳችሁምን» ሲል ጠራቸው፡፡

فَدَلَّىٰهُمَا بِغُرُورٍۚ فَلَمَّا ذَاقَا ٱلشَّجَرَةَ بَدَتۡ لَهُمَا سَوۡءَٰتُهُمَا وَطَفِقَا يَخۡصِفَانِ عَلَيۡهِمَا مِن وَرَقِ ٱلۡجَنَّةِۖ وَنَادَىٰهُمَا رَبُّهُمَآ أَلَمۡ أَنۡهَكُمَا عَن تِلۡكُمَا ٱلشَّجَرَةِ وَأَقُل لَّكُمَآ إِنَّ ٱلشَّيۡطَٰنَ لَكُمَا عَدُوٌّ مُّبِينٞ ﴿٢٢﴾

23. «ጌታችን ሆይ! ነፍሶቻችንን በደልን፡፡ ለእኛ ባትምር ባታዝንልንም በእርግጥ ከከሳሪዎቹ እንኾናለን» አሉ፡፡

قَالَا رَبَّنَا ظَلَمۡنَآ أَنفُسَنَا وَإِن لَّمۡ تَغۡفِرۡ لَنَا وَتَرۡحَمۡنَا لَنَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ﴿٢٣﴾

24. (አላህ) « ከፊላችሁ ለከፊሉ ጠላት ሲኾን ውረዱ፡ ፡ ለእናንተም በምድር ላይ እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ መርጊያና መጠቀሚያ አላችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ ٱهۡبِطُواْ بَعۡضُكُمۡ لِبَعۡضٍ عَدُوّٞۖ وَلَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُسۡتَقَرّٞ وَمَتَٰعٌ إِلَىٰ حِينٖ ﴿٢٤﴾

25. «በእርሷ ላይ ትኖራላችሁ፡፡ በእርሷም ላይ ትሞታላችሁ፡፡ ከእርሷም ውስጥ ትወጣላችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ فِيهَا تَحۡيَوۡنَ وَفِيهَا تَمُوتُونَ وَمِنۡهَا تُخۡرَجُونَ ﴿٢٥﴾

26. የአዳም ልጆች ሆይ! ኀፍረተ ገላችሁን የሚሸሽግን ልብስ ጌጥንም በእርግጥ በናንተ ላይ አወረድን፡፡ አላህን የመፍራትም ልብስ ይህ የተሻለ ነው፡፡ ይህ ከአላህ ታምራቶች ነው፡፡ ይገሠጹ ዘንድ (አወረደላቸው)፡፡

يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ قَدۡ أَنزَلۡنَا عَلَيۡكُمۡ لِبَاسٗا يُوَٰرِي سَوۡءَٰتِكُمۡ وَرِيشٗاۖ وَلِبَاسُ ٱلتَّقۡوَىٰ ذَٰلِكَ خَيۡرٞۚ ذَٰلِكَ مِنۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ لَعَلَّهُمۡ يَذَّكَّرُونَ ﴿٢٦﴾

27. የአዳም ልጆች ሆይ! ሰይጣን አባትና እናታችሁን ኀፍረተ ገላቸውን ሊያሳያቸው ልብሶቻቸውን ከነሱ የገፈፋቸው ሲኾን ከገነት እንዳወጣቸው ሁሉ እናንተን አይሞክራችሁ፡፡ እነሆ እርሱ ከነሰራዊቱ ከማታዩዋቸው ስፍራ ያዩዋችኋልና፡፡ እኛ ሰይጣናትን ለእነዚያ ለማያምኑት ወዳጆች አድርገናል፡፡

يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ لَا يَفۡتِنَنَّكُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ كَمَآ أَخۡرَجَ أَبَوَيۡكُم مِّنَ ٱلۡجَنَّةِ يَنزِعُ عَنۡهُمَا لِبَاسَهُمَا لِيُرِيَهُمَا سَوۡءَٰتِهِمَآۚ إِنَّهُۥ يَرَىٰكُمۡ هُوَ وَقَبِيلُهُۥ مِنۡ حَيۡثُ لَا تَرَوۡنَهُمۡۗ إِنَّا جَعَلۡنَا ٱلشَّيَٰطِينَ أَوۡلِيَآءَ لِلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿٢٧﴾

28. መጥፎንም ሥራ በሠሩ ጊዜ በእርሷ ላይ አባቶቻችንን አገኘን አላህም በእርሷ አዞናል ይላሉ፡፡ «አላህ በመጥፎ ነገር አያዝም፡፡ በአላህ ላይ የማታውቁትን ትናገራላችሁን» በላቸው፡፡

وَإِذَا فَعَلُواْ فَٰحِشَةٗ قَالُواْ وَجَدۡنَا عَلَيۡهَآ ءَابَآءَنَا وَٱللَّهُ أَمَرَنَا بِهَاۗ قُلۡ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَأۡمُرُ بِٱلۡفَحۡشَآءِۖ أَتَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٢٨﴾

29. ጌታዬ በማስተካከል አዘዘ፡፡ በየመስጊዱም ዘንድ ፊቶቻችሁን (እርሱን ለመገዛት) አስተካክሉ፡፡ ሃይማኖትንም ለእርሱ ፍጹም አድርጋችሁ ተገዙት፡፡ እንደጀመራችሁ ትመለሳላችሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ أَمَرَ رَبِّي بِٱلۡقِسۡطِۖ وَأَقِيمُواْ وُجُوهَكُمۡ عِندَ كُلِّ مَسۡجِدٖ وَٱدۡعُوهُ مُخۡلِصِينَ لَهُ ٱلدِّينَۚ كَمَا بَدَأَكُمۡ تَعُودُونَ ﴿٢٩﴾

30. ከፊሉን ወደ ቅን መንገድ መራ:: ከፊሎቹም በእነሱ ላይ ጥመት ተረጋገጠባቸዋል:: እነርሱ ሰይጣናትን ከአላህ ሌላ ረዳቶች አድርገው ይዘዋልና:: እነርሱም (ቅኑን መንገድ) የተመራን ነን ብለው ያስባሉ::

فَرِيقًا هَدَىٰ وَفَرِيقًا حَقَّ عَلَيۡهِمُ ٱلضَّلَٰلَةُۚ إِنَّهُمُ ٱتَّخَذُواْ ٱلشَّيَٰطِينَ أَوۡلِيَآءَ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَيَحۡسَبُونَ أَنَّهُم مُّهۡتَدُونَ ﴿٣٠﴾

31. የአዳም ልጆች ሆይ! (ኀፍረተ ገላችሁን የሚሸፍኑትን) ጌጦቻችሁን በመስገጃው ሁሉ ዘንድ ያዙ:: ብሉም፤ ጠጡም፤ አታባክኑም:: እርሱ አባካኞችን አይወድምና::

۞يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ خُذُواْ زِينَتَكُمۡ عِندَ كُلِّ مَسۡجِدٖ وَكُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ وَلَا تُسۡرِفُوٓاْۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ﴿٣١﴾

32. «የአላህን ጌጥ ያችን ለባሮቹ የፈጠራትን ከሲሳይም ጥሩዎቹን እርም ያደረገ ማን ነው» በላቸው:: «እርሷ በትንሣኤ ቀን ለእነዚያ ላመኑት ብቻ ስትኾን በቅርቢቱ ሕይወት ተገቢያቸው ናት» በላቸው:: እንደዚሁ ለሚያውቁ ሕዝቦች አንቀጾችን እናብራራለን::

قُلۡ مَنۡ حَرَّمَ زِينَةَ ٱللَّهِ ٱلَّتِيٓ أَخۡرَجَ لِعِبَادِهِۦ وَٱلطَّيِّبَٰتِ مِنَ ٱلرِّزۡقِۚ قُلۡ هِيَ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا خَالِصَةٗ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۗ كَذَٰلِكَ نُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَعۡلَمُونَ ﴿٣٢﴾

33. «ጌታዬ እርም ያደረገው መጥፎ ሥራዎችን፣ ከርሷ የተገለጸውንና የተደበቀውን ኃጢኣትንም፣ ያላግባብ መበደልንም፣ በርሱም ማስረጃ ያላወረደበትን (ጣዖት) በአላህ ማጋራታችሁን፣ በአላህም ላይ የማታውቁትን መናገራችሁን ብቻ ነው» በላቸው::

قُلۡ إِنَّمَا حَرَّمَ رَبِّيَ ٱلۡفَوَٰحِشَ مَا ظَهَرَ مِنۡهَا وَمَا بَطَنَ وَٱلۡإِثۡمَ وَٱلۡبَغۡيَ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّ وَأَن تُشۡرِكُواْ بِٱللَّهِ مَا لَمۡ يُنَزِّلۡ بِهِۦ سُلۡطَٰنٗا وَأَن تَقُولُواْ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٣٣﴾

34. ለሕዝብም ሁሉ የተወሰነ ጊዜ አላቸው:: ጊዜያቸውም በመጣ ወቅት አንዲትን ሰዓት አይቆዩም:: (ከጊዜያቱ) አይቀደሙምም::

وَلِكُلِّ أُمَّةٍ أَجَلٞۖ فَإِذَا جَآءَ أَجَلُهُمۡ لَا يَسۡتَأۡخِرُونَ سَاعَةٗ وَلَا يَسۡتَقۡدِمُونَ ﴿٣٤﴾

35. የአዳም ልጆች ሆይ! ከእናንተ ውስጥ በናንተ ላይ አንቀጾቼን የሚያነቡ መልክተኞች ቢመጧችሁ ከእናንተ ክሕደትን የተጠነቀቁና መልካምንም የሠሩ በነሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም:: እነሱም አያዝኑም::

يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ إِمَّا يَأۡتِيَنَّكُمۡ رُسُلٞ مِّنكُمۡ يَقُصُّونَ عَلَيۡكُمۡ ءَايَٰتِي فَمَنِ ٱتَّقَىٰ وَأَصۡلَحَ فَلَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ﴿٣٥﴾

36. እነዚያም በአንቀጾቻችን ያስተባበሉ ከእርሷም የኮሩ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው:: እነሱ በርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው::

وَٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَٱسۡتَكۡبَرُواْ عَنۡهَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿٣٦﴾

37. በአላህ ላይ ውሸትን ከቀጠፈ ወይም በአንቀጾቹ ከአስዋሸ ሰው ይበልጥ በዳይ ማን ነው እነዚያ (ከተጻፈላቸው) ከመጽሐፉ ውስጥ ሲኾን ዕድላቸው ያገኛቸዋል:: (የሞት) መልክተኞቻችንም የሚገድሏቸው ኾነው በመጡባቸው ጊዜ «ከአላህ ሌላ ትገዟቸው የነበራችሁት የት አሉ» ይሏቸዋል:: «ከእኛ ተሰወሩን» ይላሉ:: እነርሱም ከሓዲያን እንደነበሩ በነፍሶቻቸው ላይ ይመሰክራሉ::

فَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا أَوۡ كَذَّبَ بِـَٔايَٰتِهِۦٓۚ أُوْلَٰٓئِكَ يَنَالُهُمۡ نَصِيبُهُم مِّنَ ٱلۡكِتَٰبِۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَتۡهُمۡ رُسُلُنَا يَتَوَفَّوۡنَهُمۡ قَالُوٓاْ أَيۡنَ مَا كُنتُمۡ تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِۖ قَالُواْ ضَلُّواْ عَنَّا وَشَهِدُواْ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡ أَنَّهُمۡ كَانُواْ كَٰفِرِينَ ﴿٣٧﴾

38. «ከጋኔንም ከሰውም ከእናንተ በፊት በእርግጥ ካለፉት ሕዝቦች ጋር ኾናችሁ እሳት ውስጥ ግቡ» ይላቸዋል፡፡ አንዲቱ ሕዝብ ወደ እሳት በገባች ቁጥር (ያሳሳተቻትን) ብጤዋን ትረግማለች፡፡ መላውም በውስጧ ተሰብስበው በተገናኙም ጊዜ የኋለኛይቱ ለመጀመሪያይቱ (ተከታዮች ለአስከታዮች) «ጌታችን ሆይ! እነዚህ አሳሳቱን፡፡ ከእሳትም ስቃይ እጥፍን ስጣቸው» ትላለች፡፡ (አላህም)፡- ለሁሉም እጥፍ አለው ግን አታውቁም ይላቸዋል፡፡

قَالَ ٱدۡخُلُواْ فِيٓ أُمَمٖ قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِكُم مِّنَ ٱلۡجِنِّ وَٱلۡإِنسِ فِي ٱلنَّارِۖ كُلَّمَا دَخَلَتۡ أُمَّةٞ لَّعَنَتۡ أُخۡتَهَاۖ حَتَّىٰٓ إِذَا ٱدَّارَكُواْ فِيهَا جَمِيعٗا قَالَتۡ أُخۡرَىٰهُمۡ لِأُولَىٰهُمۡ رَبَّنَا هَٰٓؤُلَآءِ أَضَلُّونَا فَـَٔاتِهِمۡ عَذَابٗا ضِعۡفٗا مِّنَ ٱلنَّارِۖ قَالَ لِكُلّٖ ضِعۡفٞ وَلَٰكِن لَّا تَعۡلَمُونَ ٣٨

39. «መጀመሪያይቱም ለኋለኛይቱ ለእናንተ በእኛ ላይ ምንም ብልጫ አልነበራችሁም» ትላለች፡፡ «ትሠሩትም በነበራችሁት ቅጣቱን ቅመሱ» (ይላቸዋል)፡፡

وَقَالَتۡ أُولَىٰهُمۡ لِأُخۡرَىٰهُمۡ فَمَا كَانَ لَكُمۡ عَلَيۡنَا مِن فَضۡلٖ فَذُوقُواْ ٱلۡعَذَابَ بِمَا كُنتُمۡ تَكۡسِبُونَ ٣٩

40. እነዚያ አንቀጾቻችንን ያስተባበሉ ከእርሷም የኮሩ ለእነርሱ የሰማይ ደጃፎች አይከፈቱላቸውም፡፡ ግመል በመርፌ ቀዳዳ እስከሚገባም ድረስ ገነትን አይገቡም፡፡ እንደዚሁም አጋሪዎችን እንቀጣለን፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَٱسۡتَكۡبَرُواْ عَنۡهَا لَا تُفَتَّحُ لَهُمۡ أَبۡوَٰبُ ٱلسَّمَآءِ وَلَا يَدۡخُلُونَ ٱلۡجَنَّةَ حَتَّىٰ يَلِجَ ٱلۡجَمَلُ فِي سَمِّ ٱلۡخِيَاطِۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُجۡرِمِينَ ٤٠

41. ለእነርሱ ከገሀነም እሳት (በሥራቸው) ምንጣፍ ከበላያቸውም (የእሳት) መሸፈኛዎች አሏቸው፡፡ እንደዚሁም በደለኞችን እንቀጣለን፡፡

لَهُم مِّن جَهَنَّمَ مِهَادٞ وَمِن فَوۡقِهِمۡ غَوَاشٖۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلظَّٰلِمِينَ ٤١

42. እነዚያም ያመኑና መልካሞችን የሠሩ ነፍስን ችሎታዋን እንጂ አናስገድድምና፤ እነዚያ የገነት ሰዎች ናቸው፡፡ እነርሱ በርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَا نُكَلِّفُ نَفۡسًا إِلَّا وُسۡعَهَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٤٢

43. በደረቶቻቸው ውስጥ ያለውንም ጥላቻ እናስወግዳለን፡፡ ወንዞች በሥሮቻቸው ይፈሳሉ፡፡ «ለዚያም ወደዚህ (ላደረሰን ሥራ) ለመራን አላህ ምስጋና ይገባው፡፡ አላህ ባልመራንም ኖሮ አንመራም ነበር፡፡ የጌታችን መልክተኞች በእውነት ላይ ሲኾኑ በእርግጥ መጥተውልናል» ይላሉ፡፡ ይህች ገነት ትሠሩት በነበራችሁት ተሰጣችኋት በማለት ይጠራሉ፡፡

وَنَزَعۡنَا مَا فِي صُدُورِهِم مِّنۡ غِلّٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهِمُ ٱلۡأَنۡهَٰرُۖ وَقَالُواْ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ ٱلَّذِي هَدَىٰنَا لِهَٰذَا وَمَا كُنَّا لِنَهۡتَدِيَ لَوۡلَآ أَنۡ هَدَىٰنَا ٱللَّهُۖ لَقَدۡ جَآءَتۡ رُسُلُ رَبِّنَا بِٱلۡحَقِّۖ وَنُودُوٓاْ أَن تِلۡكُمُ ٱلۡجَنَّةُ أُورِثۡتُمُوهَا بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٤٣

44. የገነትም ሰዎች የእሳትን ሰዎች «ጌታችን ቃል የገባልንን እውነት ኾኖ አገኘን፡፡ ጌታችሁ የዛተባችሁንስ እውነት ኾኖ አገኛችሁትን» ሲሉ ይጣራሉ፡፡ «አዎን አገኘን» ይላሉ፡፡ በመካከላቸውም «የአላህ ርግማን በበደለኞች ላይ ይኹን» ሲል ለፋፊ ይለፍፋል፡፡

وَنَادَىٰٓ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِ أَصۡحَٰبَ ٱلنَّارِ أَن قَدۡ وَجَدۡنَا مَا وَعَدَنَا رَبُّنَا حَقّٗا فَهَلۡ وَجَدتُّم مَّا وَعَدَ رَبُّكُمۡ حَقّٗاۖ قَالُواْ نَعَمۡۚ فَأَذَّنَ مُؤَذِّنُۢ بَيۡنَهُمۡ أَن لَّعۡنَةُ ٱللَّهِ عَلَى ٱلظَّٰلِمِينَ ٤٤

45. (በደለኞች) እነዚያ ከአላህ መንገድ የሚከለክሉ፣ (የአላህም መንገድ) እንድትጣመምም የሚፈልጉዋት፣ እነርሱም በመጨረሻዋ ዓለም ከሓዲዎች የኾኑ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ يَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَيَبۡغُونَهَا عِوَجٗا وَهُم بِٱلۡأٓخِرَةِ كَٰفِرُونَ ٤٥

46. በመካከላቸውም ግርዶሽ አልለ፡፡ በአዕራፍም ላይ ሁሉንም በምልክታቸው የሚያውቁ ሰዎች አልሉ፡፡ የገነትንም ሰዎች ሰላም ለናንተ ይኹን በማለት ይጣራሉ፡፡ እነርሱም (የአዕራፍ ሰዎች) የሚከጅሉ ሲኾኑ ገና አልገቧትም፡፡

وَبَيۡنَهُمَا حِجَابٞۚ وَعَلَى ٱلۡأَعۡرَافِ رِجَالٞ يَعۡرِفُونَ كُلَّۢا بِسِيمَىٰهُمۡۚ وَنَادَوۡاْ أَصۡحَٰبَ ٱلۡجَنَّةِ أَن سَلَٰمٌ عَلَيۡكُمۡۚ لَمۡ يَدۡخُلُوهَا وَهُمۡ يَطۡمَعُونَ ٤٦

47. ዓይኖቻቸውም ወደ እሳት ሰዎች አቅጣጫ በተዞሩ ጊዜ፡- «ጌታችን ሆይ! ከበደለኞች ጋር አታድርገን» ይላሉ፡፡

۞وَإِذَا صُرِفَتۡ أَبۡصَٰرُهُمۡ تِلۡقَآءَ أَصۡحَٰبِ ٱلنَّارِ قَالُواْ رَبَّنَا لَا تَجۡعَلۡنَا مَعَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ٤٧

48. የአዕራፍም ሰዎች በምልክታቸው የሚያውቁዋቸውን (ታላላቅ) ሰዎች ይጣራሉ፡፡ «ስብስባችሁና በብዛታችሁ የምትኮሩ መኾናችሁም ከእናንተ ምንም አልጠቀማችሁ» ይሏቸዋል፡፡

وَنَادَىٰٓ أَصۡحَٰبُ ٱلۡأَعۡرَافِ رِجَالٗا يَعۡرِفُونَهُم بِسِيمَىٰهُمۡ قَالُواْ مَآ أَغۡنَىٰ عَنكُمۡ جَمۡعُكُمۡ وَمَا كُنتُمۡ تَسۡتَكۡبِرُونَ ٤٨

49. እነዚያ አላህ በችሮታው አያገኛቸውም ብላችሁ የማላችሁት (ደካሞች) እነዚህ ናቸውን «ገነትን ግቡ ፍርሃት የለባችሁም እናንተም አታዝኑም» (ተባሉ ይሏቸዋል)፡፡

أَهَٰٓؤُلَآءِ ٱلَّذِينَ أَقۡسَمۡتُمۡ لَا يَنَالُهُمُ ٱللَّهُ بِرَحۡمَةٍۚ ٱدۡخُلُواْ ٱلۡجَنَّةَ لَا خَوۡفٌ عَلَيۡكُمۡ وَلَآ أَنتُمۡ تَحۡزَنُونَ ٤٩

50. የእሳትም ሰዎች የገነትን ሰዎች «በእኛ ላይ ከውሃ አፍስሱብን ወይም አላህ ከሰጣችሁ ሲሳይ (ጣሉልን)» ብለው ጠሩዋቸዋል፡፡ እነርሱም «አላህ በከሓዲዎች ላይ እርም አድርጓቸዋል» ይሏቸዋል፡፡

وَنَادَىٰٓ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِ أَصۡحَٰبَ ٱلۡجَنَّةِ أَنۡ أَفِيضُواْ عَلَيۡنَا مِنَ ٱلۡمَآءِ أَوۡ مِمَّا رَزَقَكُمُ ٱللَّهُۚ قَالُوٓاْ إِنَّ ٱللَّهَ حَرَّمَهُمَا عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ ٥٠

51. እነዚያ ሃይማኖታቸውን መሳለቂያና መጫወቻ አድርገው የያዙ የቅርቢቱም ሕይወት ያታለለቻቸው ይህንን ቀናቸውን መገናኘትን እንደረሱ በተአምራታችንም ይክዱ እንደነበሩ ዛሬ እንረሳቸዋልን፡፡

ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُواْ دِينَهُمۡ لَهۡوٗا وَلَعِبٗا وَغَرَّتۡهُمُ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَاۚ فَٱلۡيَوۡمَ نَنسَىٰهُمۡ كَمَا نَسُواْ لِقَآءَ يَوۡمِهِمۡ هَٰذَا وَمَا كَانُواْ بِـَٔايَٰتِنَا يَجۡحَدُونَ ٥١

52. ከዕውቀት ጋርም የዘረዘርነው የኾነን መጽሐፍ ለሚያምኑ ሕዝቦች መምሪያና እዝነት ሲኾን በእርግጥ አመጣንላቸው፡፡

وَلَقَدۡ جِئۡنَٰهُم بِكِتَٰبٖ فَصَّلۡنَٰهُ عَلَىٰ عِلۡمٍ هُدٗى وَرَحۡمَةٗ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ٥٢

53. (የዛቻውን) ፍጻሜውን እንጂ ሌላ አይጠባበቁም፡፡ ፍጻሜው በሚመጣበት ቀን እነዚያ ከመምጣቱ በፊት የረሱት ሰዎች «የጌታችን መልክተኞች በእርግጥ በውነት መጥተዋል፡፡ ለእኛ ያማልዱም ዘንድ አማላጆች አልሉን ወይስ ከዚያ እንሠራው ከነበርነው ሌላን ሥራ እንሠራ ዘንድ (ወደ ምድረ ዓለም) እንመለሳለን» ይላሉ፡፡ ነፍሶቻቸውን በእርግጥ አከሰሩ፡፡ ይቀጥፉት የነበሩትም ከእነርሱ ጠፉቸው፡፡

هَلۡ يَنظُرُونَ إِلَّا تَأۡوِيلَهُۥۚ يَوۡمَ يَأۡتِي تَأۡوِيلُهُۥ يَقُولُ ٱلَّذِينَ نَسُوهُ مِن قَبۡلُ قَدۡ جَآءَتۡ رُسُلُ رَبِّنَا بِٱلۡحَقِّ فَهَل لَّنَا مِن شُفَعَآءَ فَيَشۡفَعُواْ لَنَآ أَوۡ نُرَدُّ فَنَعۡمَلَ غَيۡرَ ٱلَّذِي كُنَّا نَعۡمَلُۚ قَدۡ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ٥٣

54. ጌታችሁ ያ ሰማያትንና ምድርን በስድስት ቀኖች ውስጥ የፈጠረ አላህ ነው፡፡ ከዚያም (ስልጣኑ) በዐርሹ ላይ ተደላደለ፡፡ (አላህ) ሌሊትን በቀን ፈጥኖ የሚፈልገው ሲኾን ይሸፍናል፡፡ ፀሐይንና ጨረቃንም ከዋክብትንም በትእዛዙ የተገሩ ሲኾኑ (ፈጠራቸው)፡፡ ንቁ! መፍጠርና ማዘዝ የእርሱ ብቻ ነው፡፡ የዓለማት ጌታ አላህ (ክብሩ) ላቀ፡፡

إِنَّ رَبَّكُمُ ٱللَّهُ ٱلَّذِى خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ فِى سِتَّةِ أَيَّامٍ ثُمَّ ٱسْتَوَىٰ عَلَى ٱلْعَرْشِ يُغْشِى ٱلَّيْلَ ٱلنَّهَارَ يَطْلُبُهُۥ حَثِيثًا وَٱلشَّمْسَ وَٱلْقَمَرَ وَٱلنُّجُومَ مُسَخَّرَٰتٍۭ بِأَمْرِهِۦٓ أَلَا لَهُ ٱلْخَلْقُ وَٱلْأَمْرُ تَبَارَكَ ٱللَّهُ رَبُّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٥٤﴾

55. ጌታችሁን ተዋርዳችሁ በድብቅም ለምኑት፡፡ እርሱ ወሰን አላፊዎችን አይወድምና፡፡

ٱدْعُوا۟ رَبَّكُمْ تَضَرُّعًا وَخُفْيَةً إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلْمُعْتَدِينَ ﴿٥٥﴾

56. በምድርም ውስጥ ከተበጀች በኋላ አታበላሹ፡፡ ፈርታችሁና ከጅላችሁም ተገዙት፡፡ የአላህ ችሮታ ከበጎ አድራጊዎች ቅርብ ነውና፡፡

وَلَا تُفْسِدُوا۟ فِى ٱلْأَرْضِ بَعْدَ إِصْلَٰحِهَا وَٱدْعُوهُ خَوْفًا وَطَمَعًا إِنَّ رَحْمَتَ ٱللَّهِ قَرِيبٌ مِّنَ ٱلْمُحْسِنِينَ ﴿٥٦﴾

57. እርሱም ያ ነፋሶችን ከችሮታው (ከዝናም) በፊት አብሳሪዎች አድርጎ የሚልክ ነው፡፡ ከባዳዎችንም ደመናዎች በተሸከሙ ጊዜ ሙት ወደ ኾነ አገር እንነዳዋለን፡፡ በእርሱም ውሃን እናወርዳለን፡፡ ከፍሬዎችም ሁሉ በእርሱ እናወጣለን፡፡ እንደዚሁ ትገነዘቡ ዘንድ ሙታንን (ከመቃብር) እናወጣለን፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِى يُرْسِلُ ٱلرِّيَٰحَ بُشْرًۢا بَيْنَ يَدَىْ رَحْمَتِهِۦ حَتَّىٰٓ إِذَآ أَقَلَّتْ سَحَابًا ثِقَالًا سُقْنَٰهُ لِبَلَدٍ مَّيِّتٍ فَأَنزَلْنَا بِهِ ٱلْمَآءَ فَأَخْرَجْنَا بِهِۦ مِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِ كَذَٰلِكَ نُخْرِجُ ٱلْمَوْتَىٰ لَعَلَّكُمْ تَذَكَّرُونَ ﴿٥٧﴾

58. መልካሙም አገር በጌታው ፈቃድ በቃዩ (ያማረ ኾኖ) ይወጣል፡፡ ያም መጥፎ የኾነው (በቃዩ) ደካማ ኾኖ እንጂ አይወጣም፡፡ እንደዚሁ ለሚያመሰግኑ ሕዝቦች ታምራትን እናብራራለን፡፡

وَٱلْبَلَدُ ٱلطَّيِّبُ يَخْرُجُ نَبَاتُهُۥ بِإِذْنِ رَبِّهِۦ وَٱلَّذِى خَبُثَ لَا يَخْرُجُ إِلَّا نَكِدًا كَذَٰلِكَ نُصَرِّفُ ٱلْءَايَٰتِ لِقَوْمٍ يَشْكُرُونَ ﴿٥٨﴾

59. ኑሕን ወደ ወገኖቹ በእርግጥ ላክነው፡፡ አላቸውም፡- «ወገኖቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ለእናንተ ከርሱ ሌላ ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ እኔ በእናንተ ላይ የከባድ ቀንን ቅጣት እፈራላችኋለሁ፡፡»

لَقَدْ أَرْسَلْنَا نُوحًا إِلَىٰ قَوْمِهِۦ فَقَالَ يَٰقَوْمِ ٱعْبُدُوا۟ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنْ إِلَٰهٍ غَيْرُهُۥٓ إِنِّىٓ أَخَافُ عَلَيْكُمْ عَذَابَ يَوْمٍ عَظِيمٍ ﴿٥٩﴾

60. ከሕዝቦቹ (የካዱት) መሪዎቹ፡- «እኛ በግልጽ መሳሳት ውስጥ ኾነህ በእርግጥ እናይሃለን» አሉት፡፡

قَالَ ٱلْمَلَأُ مِن قَوْمِهِۦٓ إِنَّا لَنَرَىٰكَ فِى ضَلَٰلٍ مُّبِينٍ ﴿٦٠﴾

61. አላቸው «ወገኖቼ ሆይ! ምንም መሳሳት የለብኝም፡፡ ግን እኔ ከዓለማት ጌታ መልእክተኛ ነኝ፡፡»

قَالَ يَٰقَوْمِ لَيْسَ بِى ضَلَٰلَةٌ وَلَٰكِنِّى رَسُولٌ مِّن رَّبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٦١﴾

62. «የጌታዬን መልክቶች አደርስላችኋለሁ፡፡ ለእናንተም እመክራችኋለሁ፡፡ ከአላህም በኩል የማታውቁትን ዐውቃለሁ፡፡»

أُبَلِّغُكُمْ رِسَٰلَٰتِ رَبِّى وَأَنصَحُ لَكُمْ وَأَعْلَمُ مِنَ ٱللَّهِ مَا لَا تَعْلَمُونَ ﴿٦٢﴾

أَوَعَجِبْتُمْ أَن جَآءَكُمْ ذِكْرٌ مِّن رَّبِّكُمْ عَلَىٰ رَجُلٍ مِّنكُمْ لِيُنذِرَكُمْ وَلِتَتَّقُواْ وَلَعَلَّكُمْ تُرْحَمُونَ ﴿٦٣﴾

63. «አላህን ልትፈሩና ይታዘንላችሁም ዘንድ ከእናንተው (ጎሳ) በኾነ ሰው ላይ እንዲያስጠነቅቃችሁ ከጌታችሁ ግሳጼ ቢመጣላችሁ ትደነቃላችሁን» (አላቸው)፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَأَنجَيْنَٰهُ وَٱلَّذِينَ مَعَهُۥ فِى ٱلْفُلْكِ وَأَغْرَقْنَا ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ ۚ إِنَّهُمْ كَانُواْ قَوْمًا عَمِينَ ﴿٦٤﴾

64. ወዲያውም አስተባበሉት፡፡ እርሱንና እነዚያንም ከእርሱ ጋር ያሉትን (አማኞች) በታንኳዋ ውስጥ አዳንናቸው፡፡ እነዚያንም በአንቀጾቻችን ያስተባበሉትን አሰጠምን፡፡ እነርሱ (ልበ) ዕውራን ሕዝቦች ነበሩና፡፡

۞ وَإِلَىٰ عَادٍ أَخَاهُمْ هُودًا ۗ قَالَ يَٰقَوْمِ ٱعْبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنْ إِلَٰهٍ غَيْرُهُۥٓ ۚ أَفَلَا تَتَّقُونَ ﴿٦٥﴾

65. ወደ ዓድም ወንድማቸውን ሁድን ላክን፡፡ «ወገኖቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ (የአላህን ቅጣት) አትፈሩምን» አላቸው፡፡

قَالَ ٱلْمَلَأُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن قَوْمِهِۦٓ إِنَّا لَنَرَىٰكَ فِى سَفَاهَةٍ وَإِنَّا لَنَظُنُّكَ مِنَ ٱلْكَٰذِبِينَ ﴿٦٦﴾

66. ከሕዝቦቹ እነዚያ የካዱት መሪዎች «እኛ በሞኝነት ላይ ኾነህ በእርግጥ እናይሃለን፡፡ እኛም ከውሸተኞቹ ነህ ብለን እንጠረጥርሃለን» አሉት፡፡

قَالَ يَٰقَوْمِ لَيْسَ بِى سَفَاهَةٌ وَلَٰكِنِّى رَسُولٌ مِّن رَّبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٦٧﴾

67. (እርሱም) አላቸው «ወገኖቼ ሆይ! እኔ ሞኝነት የለብኝም፡፡ ግን እኔ ከዓለማት ጌታ የተላክሁ ነኝ፡፡»

أُبَلِّغُكُمْ رِسَٰلَٰتِ رَبِّى وَأَنَا۠ لَكُمْ نَاصِحٌ أَمِينٌ ﴿٦٨﴾

68. «የጌታዬን መልክቶች አደርስላችኋለሁ፡፡ እኔም ለእናንተ ታማኝ መካሪ ነኝ፡፡»

أَوَعَجِبْتُمْ أَن جَآءَكُمْ ذِكْرٌ مِّن رَّبِّكُمْ عَلَىٰ رَجُلٍ مِّنكُمْ لِيُنذِرَكُمْ ۚ وَٱذْكُرُوٓاْ إِذْ جَعَلَكُمْ خُلَفَآءَ مِنۢ بَعْدِ قَوْمِ نُوحٍ وَزَادَكُمْ فِى ٱلْخَلْقِ بَصْۜطَةً ۖ فَٱذْكُرُوٓاْ ءَالَآءَ ٱللَّهِ لَعَلَّكُمْ تُفْلِحُونَ ﴿٦٩﴾

69. «ከጌታችሁ የኾነ ግሣጼ ከእናንተው ውስጥ ባንድ ሰው ላይ ያስጠነቅቃችሁ ዘንድ ቢመጣባችሁ ትደነቃላችሁን ከኑሕም ሕዝቦች በኋላ ምትኮች ባደረጋችሁና በፍጠረትም ግዙፍነትን በጨመረላችሁ ጊዜ አስታውሱ፡፡ የሻችሁትንም ታገኙ ዘንድ የአላህን ጸጋዎች አስታውሱ፡፡»

قَالُوٓاْ أَجِئْتَنَا لِنَعْبُدَ ٱللَّهَ وَحْدَهُۥ وَنَذَرَ مَا كَانَ يَعْبُدُ ءَابَآؤُنَا ۖ فَأْتِنَا بِمَا تَعِدُنَآ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿٧٠﴾

70. «አላህን ብቻውን እንድንገዛ አባቶቻችንም ይገዙት የነበረውን (አማልክት) እንድንተው መጣህብን ከውነተኞች ከኾንክ የምታስፈራብንን (ቅጣት) አምጣብን» አሉ፡፡

قَالَ قَدْ وَقَعَ عَلَيْكُم مِّن رَّبِّكُمْ رِجْسٌ وَغَضَبٌ ۖ أَتُجَٰدِلُونَنِى فِىٓ أَسْمَآءٍ سَمَّيْتُمُوهَآ أَنتُمْ وَءَابَآؤُكُم مَّا نَزَّلَ ٱللَّهُ بِهَا مِن سُلْطَٰنٍ ۚ فَٱنتَظِرُوٓاْ إِنِّى مَعَكُم مِّنَ ٱلْمُنتَظِرِينَ ﴿٧١﴾

71. «ከጌታችሁ የኾነ ቅጣትና ቁጣ በእናንተ ላይ በእውነት ተረጋገጠ፡፡ እናንተና አባቶቻችሁም (አማልክት ብላችሁ) በጠራችኋቸው ስሞች አላህ በእርሷ ምንም ማስረጃ ያላወረደባት ስትኾን ትከራከሩኛላችሁን ተጠባባቂም እኔ ከእናንተ ጋር ከተጠባባቂዎቹ ነኝና» አለ፡፡

فَأَنجَيۡنَٰهُ وَٱلَّذِينَ مَعَهُۥ بِرَحۡمَةٖ مِّنَّا وَقَطَعۡنَا دَابِرَ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَاۖ وَمَا كَانُواْ مُؤۡمِنِينَ ٧٢

72. እርሱንና እነዚያንም አብረውት የነበሩትን ከእኛ በኾነው ችሮታ (ከቅጣት) አዳንናቸው፡፡ የእነዚያንም በተአምራታችን ያስተባበሉትንና አማኞች ያልነበሩትን መሠረት ቆረጥን፡፡

وَإِلَىٰ ثَمُودَ أَخَاهُمۡ صَٰلِحٗاۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرُهُۥۖ قَدۡ جَآءَتۡكُم بَيِّنَةٞ مِّن رَّبِّكُمۡۖ هَٰذِهِۦ نَاقَةُ ٱللَّهِ لَكُمۡ ءَايَةٗۖ فَذَرُوهَا تَأۡكُلۡ فِيٓ أَرۡضِ ٱللَّهِۖ وَلَا تَمَسُّوهَا بِسُوٓءٖ فَيَأۡخُذَكُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٧٣

73. ወደ ሰሙድም ወንድማቸውን ሷሊህን ላክን፡፡ አላቸው «ወገኖቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ለእናንተ ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ (እውነተኛ ለመኾኔ) ከጌታችሁ የኾነች ምልክት በእርግጥ መጥታላችኋለች፡፡ ይህች ለእናንተ ተዓምር ስትኾን የአላህ ግመል ናትና ተዋት፡፡ በአላህ ምድር ውስጥ ትብላ፤ (ትጠጣም)፡፡ በክፉ አትንኳትም፡፡ አሳማሚ ቅጣት ይይዛችኋልና፡፡»

وَٱذۡكُرُوٓاْ إِذۡ جَعَلَكُمۡ خُلَفَآءَ مِنۢ بَعۡدِ عَادٖ وَبَوَّأَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ تَتَّخِذُونَ مِن سُهُولِهَا قُصُورٗا وَتَنۡحِتُونَ ٱلۡجِبَالَ بُيُوتٗاۖ فَٱذۡكُرُوٓاْ ءَالَآءَ ٱللَّهِ وَلَا تَعۡثَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُفۡسِدِينَ ٧٤

74. «ከዓድም በኋላ ምትኮች ባደረጋችሁና በምድሪቱም ላይ ባስቀመጣችሁ ጊዜ አስታውሱ፡፡ ከሜዳዎቿ (ሸክላ) ሕንጻዎችን ትገነባላችሁ፡፡ ከተራራዎችም ቤቶችን ትጠርባላችሁ፡፡ ስለዚህ የአላህን ጸጋዎች አስታውሱ፡፡ በምድርም ውስጥ አጥፊዎች ኾናችሁ አታበላሹ፡፡»

قَالَ ٱلۡمَلَأُ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُواْ مِن قَوۡمِهِۦ لِلَّذِينَ ٱسۡتُضۡعِفُواْ لِمَنۡ ءَامَنَ مِنۡهُمۡ أَتَعۡلَمُونَ أَنَّ صَٰلِحٗا مُّرۡسَلٞ مِّن رَّبِّهِۦۚ قَالُوٓاْ إِنَّا بِمَآ أُرۡسِلَ بِهِۦ مُؤۡمِنُونَ ٧٥

75. ከወገኖቹ እነዚያ የኮሩት መሪዎች ለእነዚያ ለተሸነፉት ከነሱ ላመኑት፡- «ሷሊህ ከጌታው መላኩን ታውቃላችሁን» አሏቸው፡፡ « (አዎን)፡- እኛ እርሱ በተላከበት ነገር አማኞች ነን» አሉ፡፡

قَالَ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُوٓاْ إِنَّا بِٱلَّذِيٓ ءَامَنتُم بِهِۦ كَٰفِرُونَ ٧٦

76. እነዚያ የኮሩት፡- «እኛ በዚያ እናንተ በርሱ ባመናችሁበት ከሓዲዎች ነን» አሉ፡፡

فَعَقَرُواْ ٱلنَّاقَةَ وَعَتَوۡاْ عَنۡ أَمۡرِ رَبِّهِمۡ وَقَالُواْ يَٰصَٰلِحُ ٱئۡتِنَا بِمَا تَعِدُنَآ إِن كُنتَ مِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ٧٧

77. ወዲያውም ግመሊቱን ወጓት፡፡ ከጌታቸውም ትዕዛዝ ወጡ፡፡ አሉም፡- «ሷሊህ ሆይ! ከመልክተኞቹ እንደኾንክ የምታስፈራራብንን (ቅጣት) አምጣብን፡፡»

فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلرَّجۡفَةُ فَأَصۡبَحُواْ فِي دَارِهِمۡ جَٰثِمِينَ ٧٨

78. ወዲያውም የምድር መንቀጥቀጥ (ጩኸትም) ያዘቻቸው፡፡ በቤቶቻቸውም ውስጥ ተንከፍርረው አነጉ፡፡

فَتَوَلَّىٰ عَنۡهُمۡ وَقَالَ يَٰقَوۡمِ لَقَدۡ أَبۡلَغۡتُكُمۡ رِسَالَةَ رَبِّي وَنَصَحۡتُ لَكُمۡ وَلَٰكِن لَّا تُحِبُّونَ ٱلنَّٰصِحِينَ ٧٩

79. (ሷሊህ) ከእነርሱም ዞረ፡፡ (እንዲህም) አለ «ወገኖቼ ሆይ! የጌታዬን መልክት በእርግጥ አደረስኩላችሁ፡፡ ለእናንተም መከርኳችሁ፡፡ ግን መካሪዎችን አትወዱም፡፡»

وَلُوطًا إِذۡ قَالَ لِقَوۡمِهِۦٓ أَتَأۡتُونَ ٱلۡفَٰحِشَةَ مَا سَبَقَكُم بِهَا مِنۡ أَحَدٖ مِّنَ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٨٠

80. ሉጥንም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «አስቀያሚን ሥራ ትሠራላችሁን በእርሷ ከዓለማት አንድም አልቀደማችሁም፡፡»

81. «እናንተ ከሴቶች ሌላ ወንዶችን በመከጀል በእርግጥ ትመጡባቸዋላችሁ፡፡ በእውነቱ እናንተ ወሰንን አላፊዎች ሕዝቦች ናችሁ፡፡»

إِنَّكُمۡ لَتَأۡتُونَ ٱلرِّجَالَ شَهۡوَةٗ مِّن دُونِ ٱلنِّسَآءِۚ بَلۡ أَنتُمۡ قَوۡمٞ مُّسۡرِفُونَ ﴿٨١﴾

82. የሕዝቦቹም መልስ « (ሎጥንና ተከታዮቹን) ከከተማችሁ አውጧቸው፡፡ እነሱ የሚጥራሩ ሰዎች ናቸውና» ማለት እንጂ ሌላ አልነበረም፡፡

وَمَا كَانَ جَوَابَ قَوۡمِهِۦٓ إِلَّآ أَن قَالُوٓاْ أَخۡرِجُوهُم مِّن قَرۡيَتِكُمۡۖ إِنَّهُمۡ أُنَاسٞ يَتَطَهَّرُونَ ﴿٨٢﴾

83. እርሱንና ቤተሰቦቹንም አዳንናቸው ሚስቱ ብቻ ስትቀር፡፡ እርሷ (ለጥፋት) ከቀሩት ኾነች፡፡

فَأَنجَيۡنَٰهُ وَأَهۡلَهُۥٓ إِلَّا ٱمۡرَأَتَهُۥ كَانَتۡ مِنَ ٱلۡغَٰبِرِينَ ﴿٨٣﴾

84. በእነሱም ላይ (የእሳት) ዝናብን አዘነብንባቸው፡፡ የኃጢአተኞችም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከት፡፡

وَأَمۡطَرۡنَا عَلَيۡهِم مَّطَرٗاۖ فَٱنظُرۡ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ﴿٨٤﴾

85. ወደ መድየንም (ምድያን) ወንድማቸውን ሹዓይብን (ላክን)፤ አላቸው፡- «ወገኖቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ በቀር ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ ከጌታችሁ ዘንድ ግልጽ ማስረጃ በእርግጥ መጥታላችኋለች፡፡ ስፍርንና ሚዛንን ሙሉ፡፡ ሰዎችንም እንዳቾቻቸውን (ገንዘቦቻቸውን) አታጉድሉባቸው፡፡ በምድርም ውስጥ ከተበጀች በኋላ አታበላሹ፡፡ ይህ ምእምናን እንደኾናችሁ ለእናንተ የተሻለ ነው፡፡»

وَإِلَىٰ مَدۡيَنَ أَخَاهُمۡ شُعَيۡبٗاۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرُهُۥۖ قَدۡ جَآءَتۡكُم بَيِّنَةٞ مِّن رَّبِّكُمۡۖ فَأَوۡفُواْ ٱلۡكَيۡلَ وَٱلۡمِيزَانَ وَلَا تَبۡخَسُواْ ٱلنَّاسَ أَشۡيَآءَهُمۡ وَلَا تُفۡسِدُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ بَعۡدَ إِصۡلَٰحِهَاۚ ذَٰلِكُمۡ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ﴿٨٥﴾

86. « (ሰዎችን) የምታስፈራሩና ከአላህም መንገድ በእርሱ ያመኑትን የምታግዱ መጥመሟንም የምትፈልጉዋት ኾናችሁ በየመንገዱ አትቀመጡ፡፡ ጥቂቶችም በነበራችሁና ባበዛችሁ ጊዜ አስታውሱ፡፡ የአጥፊዎችም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከቱ፡፡ »

وَلَا تَقۡعُدُواْ بِكُلِّ صِرَٰطٖ تُوعِدُونَ وَتَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ مَنۡ ءَامَنَ بِهِۦ وَتَبۡغُونَهَا عِوَجٗاۚ وَٱذۡكُرُوٓاْ إِذۡ كُنتُمۡ قَلِيلٗا فَكَثَّرَكُمۡۖ وَٱنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ﴿٨٦﴾

87. «ከእናንተም በዚያ እኔ በእርሱ በተላክሁበት ያመኑ ጭፍሮችና ያላመኑ ጭፍሮችም ቢኖሩ በመካከላችን አላህ እስከሚፈርድ ታገሱ፡፡ እርሱም ከፈራጆች ሁሉ በላጭ ነው፡፡»

وَإِن كَانَ طَآئِفَةٞ مِّنكُمۡ ءَامَنُواْ بِٱلَّذِيٓ أُرۡسِلۡتُ بِهِۦ وَطَآئِفَةٞ لَّمۡ يُؤۡمِنُواْ فَٱصۡبِرُواْ حَتَّىٰ يَحۡكُمَ ٱللَّهُ بَيۡنَنَاۚ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلۡحَٰكِمِينَ ﴿٨٧﴾

88. ከሕዝቦቹ እነዚያ የኮሩት መሪዎች፡- «ሹዓይብ ሆይ! አንተንና እነዚያን ከአንተጋር ያመኑትን ከከተማችን በእርግጥ እናስወጣችኋለን፡፡ ወይም ወደ ሃይማኖታችን መመለስ አለባችሁ አሉ፡፡ የጠላንም ብንኾን» አላቸው፡፡

۞قَالَ ٱلۡمَلَأُ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُواْ مِن قَوۡمِهِۦ لَنُخۡرِجَنَّكَ يَٰشُعَيۡبُ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَكَ مِن قَرۡيَتِنَآ أَوۡ لَتَعُودُنَّ فِي مِلَّتِنَاۚ قَالَ أَوَلَوۡ كُنَّا كَٰرِهِينَ ﴿٨٨﴾

89. «አላህ ከእርሷ ከአዳነን በኋላ ወደ ሃይማኖታችሁ ብንመለስ በአላህ ላይ በእርግጥ ውሸትን ቀጠፍን፡፡ አላህ ጌታችን ካልሻም በስተቀር ለእኛ ወደእርሷ ልንመለስ አይገባንም፡፡ ጌታችን ዕውቀቱ ሁሉን ነገር ሰፋ፡፡ በአላህ ላይ ተጠጋን፡፡ ጌታችን ሆይ! በኛና በወገኖቻችን መካከል በውነት ፍረድ፡፡ አንተም ከፈራጆቹ ሁሉ በላጭ ነህ» (አለ)

قَدِ ٱفۡتَرَيۡنَا عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا إِنۡ عُدۡنَا فِي مِلَّتِكُم بَعۡدَ إِذۡ نَجَّىٰنَا ٱللَّهُ مِنۡهَاۚ وَمَا يَكُونُ لَنَآ أَن نَّعُودَ فِيهَآ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُ رَبُّنَاۚ وَسِعَ رَبُّنَا كُلَّ شَيۡءٍ عِلۡمًاۚ عَلَى ٱللَّهِ تَوَكَّلۡنَاۚ رَبَّنَا ٱفۡتَحۡ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَ قَوۡمِنَا بِٱلۡحَقِّ وَأَنتَ خَيۡرُ ٱلۡفَٰتِحِينَ ٨٩

90. ከወገኖቹም እነዚያ የካዱት መሪዎች «ሹዓይብን ብትከተሉ እናንተ ያን ጊዜ ከሳሪዎች ናችሁ» አሉ፡፡

وَقَالَ ٱلۡمَلَأُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن قَوۡمِهِۦ لَئِنِ ٱتَّبَعۡتُمۡ شُعَيۡبًا إِنَّكُمۡ إِذٗا لَّخَٰسِرُونَ ٩٠

91. ወዲያውም የምድር መንቀጥቀጥ (ጩኸትም) ያዘቻቸው፡፡ በከተማቸውም ውስጥ ተንከፍርረው አነጉ፡፡

فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلرَّجۡفَةُ فَأَصۡبَحُواْ فِي دَارِهِمۡ جَٰثِمِينَ ٩١

92. እነዚያ ሹዓይብን ያስተባበሉት በእርሷ እንዳልነበሩባት ኾኑ፡፡ እነዚ ሹዓይብን ያስተባበሉት እነርሱ ከሳሪዎች ኾኑ፡፡

ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ شُعَيۡبٗا كَأَن لَّمۡ يَغۡنَوۡاْ فِيهَاۚ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ شُعَيۡبٗا كَانُواْ هُمُ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٩٢

93. ከእነርሱም (ትቷቸው) ዞረ፡- «ወገኖቼ ሆይ! የጌታዬን መልክቶች በእርግጥ አደረስኩላችሁ፡፡ ለእናንተም መከርኩ፡፡ ታዲያ በከሓዲዎች ሰዎች ላይ እንዴት አዝናለሁ» አለም፡፡

فَتَوَلَّىٰ عَنۡهُمۡ وَقَالَ يَٰقَوۡمِ لَقَدۡ أَبۡلَغۡتُكُمۡ رِسَٰلَٰتِ رَبِّي وَنَصَحۡتُ لَكُمۡۖ فَكَيۡفَ ءَاسَىٰ عَلَىٰ قَوۡمٖ كَٰفِرِينَ ٩٣

94. በከተማ አንድንም ነቢይ አልላክንም ሰዎችዋን ይዋደቁ ዘንድ በድህነትና በጉዳት የያዝናቸው ብንኾን እንጂ፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا فِي قَرۡيَةٖ مِّن نَّبِيٍّ إِلَّآ أَخَذۡنَآ أَهۡلَهَا بِٱلۡبَأۡسَآءِ وَٱلضَّرَّآءِ لَعَلَّهُمۡ يَضَّرَّعُونَ ٩٤

95. ከዚያም እስከበዙና «አባቶቻችንን ድህነትና በሺታ በእርግጥ ነክቷቸዋል፡፡ (ይኸም የጊዜ ልማድ ነው)» እስካሉ ድረስ በመጥፎው ስፍራ በጎውን ለወጥን፡፡ ወዲያውም እነርሱ የማያውቁ ኾነው በድንገት ያዝናቸው፡፡

ثُمَّ بَدَّلۡنَا مَكَانَ ٱلسَّيِّئَةِ ٱلۡحَسَنَةَ حَتَّىٰ عَفَواْ وَّقَالُواْ قَدۡ مَسَّ ءَابَآءَنَا ٱلضَّرَّآءُ وَٱلسَّرَّآءُ فَأَخَذۡنَٰهُم بَغۡتَةٗ وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ٩٥

96. የከተማዋም ሰዎች ባመኑና በተጠነቀቁ ኖሮ በእነሱ ላይ ከሰማይም ከምድርም በረከቶችን በከፈትንላቸው ነበር፡፡ ግን አስተባበሉ፡፡ ይሠሩት በነበሩትም ኃጢአት ያዝናቸው፡፡

وَلَوۡ أَنَّ أَهۡلَ ٱلۡقُرَىٰٓ ءَامَنُواْ وَٱتَّقَوۡاْ لَفَتَحۡنَا عَلَيۡهِم بَرَكَٰتٖ مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِ وَلَٰكِن كَذَّبُواْ فَأَخَذۡنَٰهُم بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ٩٦

97. የከተማዋ ሰዎችም እነሱ የተኙ ኾነው ቅጣታችን ሌሊት ሊመጣባቸው አይፈሩምን

أَفَأَمِنَ أَهۡلُ ٱلۡقُرَىٰٓ أَن يَأۡتِيَهُم بَأۡسُنَا بَيَٰتٗا وَهُمۡ نَآئِمُونَ ٩٧

98. የከተማዋ ሰዎችም እነሱ የሚጫወቱ ኾነው ሳሉ ቅጣታችን ቀን በረፋድ ሊመጣባቸው አይፈሩምን

أَوَ أَمِنَ أَهۡلُ ٱلۡقُرَىٰٓ أَن يَأۡتِيَهُم بَأۡسُنَا ضُحٗى وَهُمۡ يَلۡعَبُونَ ٩٨

99. የአላህንም ማዘናጋት አይፈሩምን የአላህንም ማዘናጋት ከከሳሪዎች ሕዝቦች በስተቀር የሚተማመን የለም፡፡

أَفَأَمِنُواْ مَكۡرَ ٱللَّهِۚ فَلَا يَأۡمَنُ مَكۡرَ ٱللَّهِ إِلَّا ٱلۡقَوۡمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ٩٩

100. ለእነዚያ ምድርን ከባለቤቶችዋ (ጥፋት) በኋላ ለሚወርሱት ብንሻ ኖሮ በኃጢኣቶቻቸው የምንቀጣቸው መኾናችን አልተገለጸላቸውምን በልቦቻቸውም ላይ እናትማለን፡፡ ስለዚህ እነርሱ አይሰሙም፡፡

أَوَ لَمۡ يَهۡدِ لِلَّذِينَ يَرِثُونَ ٱلۡأَرۡضَ مِنۢ بَعۡدِ أَهۡلِهَآ أَن لَّوۡ نَشَآءُ أَصَبۡنَٰهُم بِذُنُوبِهِمۡۚ وَنَطۡبَعُ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ فَهُمۡ لَا يَسۡمَعُونَ ١٠٠

101. እነዚህ ከተሞች (ከኑሕ እስከ ሹዓይብ ሰዎች የተነገሩት) ከወሬዎቻቸው ባንተ ላይ እንተርካለን፡፡ መልክተኞቻቸውም በግልጽ ተዓምራት በእርግጥ መጥተዋቸዋል፡፡ ከመምጣታቸው በፊት ባስተባበሉትም ነገር የሚያምኑ አልኾኑም፡፡ እንደዚሁ አላህ በከሓዲያን ልቦች ላይ ያትማል፡፡

تِلۡكَ ٱلۡقُرَىٰ نَقُصُّ عَلَيۡكَ مِنۡ أَنۢبَآئِهَاۚ وَلَقَدۡ جَآءَتۡهُمۡ رُسُلُهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَمَا كَانُواْ لِيُؤۡمِنُواْ بِمَا كَذَّبُواْ مِن قَبۡلُۚ كَذَٰلِكَ يَطۡبَعُ ٱللَّهُ عَلَىٰ قُلُوبِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ١٠١

102. ለብዙዎቻቸውም በቃል ኪዳናቸው መሙላትን አላገኘንም፡፡ አብዛኞቻቸውንም በእርግጥ አመጸኞች ኾነው አገኘናቸው፡፡

وَمَا وَجَدۡنَا لِأَكۡثَرِهِم مِّنۡ عَهۡدٖۖ وَإِن وَجَدۡنَآ أَكۡثَرَهُمۡ لَفَٰسِقِينَ ١٠٢

103. ከዚያም ከበኋላቸው ሙሳን ወደ ፈርዖንና ወደ መማክርቶቹ በተዓምራታችን ላክነው፡፡ በእርሷም ካዱ፡ ፡ ያጥፊዎችም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከት፡፡

ثُمَّ بَعَثۡنَا مِنۢ بَعۡدِهِم مُّوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَآ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِۦ فَظَلَمُواْ بِهَاۖ فَٱنظُرۡ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ١٠٣

104. ሙሳም አለ፡- «ፈርዖን ሆይ! እኔ ከዓለማት ጌታ የተላከሁ መልክተኛ ነኝ፡፡»

وَقَالَ مُوسَىٰ يَٰفِرۡعَوۡنُ إِنِّي رَسُولٞ مِّن رَّبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٠٤

105. «»በአላህ ላይ ከእውነት በቀር አለመናገር ተገቢዬ ነው፡፡ ከጌታችሁ በተዓምር በእርግጥ መጣኋችሁ፡፡ የእስራኤልንም ልጆች ከእኔ ጋር ልቀቅ፡፡

حَقِيقٌ عَلَىٰٓ أَن لَّآ أَقُولَ عَلَى ٱللَّهِ إِلَّا ٱلۡحَقَّۚ قَدۡ جِئۡتُكُم بِبَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّكُمۡ فَأَرۡسِلۡ مَعِيَ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ١٠٥

106. (ፈርዖንም «በተዓምር የመጣህ እንደኾንክ ከውነተኞቹ ከኾንክ እርሷን አምጣት» አለው፡፡

قَالَ إِن كُنتَ جِئۡتَ بِـَٔايَةٖ فَأۡتِ بِهَآ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ١٠٦

107. በትሩንም ጣለ፡፡ እርስዋም ወዲያውኑ ግልጽ እባብ ኾነች፡፡

فَأَلۡقَىٰ عَصَاهُ فَإِذَا هِيَ ثُعۡبَانٞ مُّبِينٞ ١٠٧

108. እጁንም አወጣ፡፡ እርሷም ወዲያውኑ ለተመልካቾች ነጭ ኾነች፡፡

وَنَزَعَ يَدَهُۥ فَإِذَا هِيَ بَيۡضَآءُ لِلنَّٰظِرِينَ ١٠٨

109. ከፈርዖን ሰዎች መማክርቶቹ፡- «ይህ በእርግጥ ዐዋቂ ድግምተኛ ነው» አሉ፡፡

قَالَ ٱلۡمَلَأُ مِن قَوۡمِ فِرۡعَوۡنَ إِنَّ هَٰذَا لَسَٰحِرٌ عَلِيمٞ ١٠٩

110. «ከምድራችሁ ሊያወጣችሁ ይሻል» (አሉ)፡፡ «ታዲያ ምን ታዛላችሁ» (አለ)

يُرِيدُ أَن يُخۡرِجَكُم مِّنۡ أَرۡضِكُمۡۖ فَمَاذَا تَأۡمُرُونَ ١١٠

111. (እነርሱም) አሉ «እርሱንና ወንድሙን አቆይ፡፡ ወደ ከተሞቹም ሁሉ ሰብሳቢዎችን (ዘበኞች) ላክ፡፡»

قَالُوٓاْ أَرۡجِهۡ وَأَخَاهُ وَأَرۡسِلۡ فِي ٱلۡمَدَآئِنِ حَٰشِرِينَ ١١١

112. «ዐዋቂ ድግምተኛ የኾነን ሁሉ ያመጡልሃልና፡፡»

يَأۡتُوكَ بِكُلِّ سَٰحِرٍ عَلِيمٖ ١١٢

113. ድግምተኞቹም ወደ ፈርዖን መጡ፡፡ «እኛ አሸናፊዎች ብንኾን ለእኛ በእርግጥ ዋጋ አለን» አሉ፡፡

وَجَآءَ ٱلسَّحَرَةُ فِرۡعَوۡنَ قَالُوٓاْ إِنَّ لَنَا لَأَجۡرًا إِن كُنَّا نَحۡنُ ٱلۡغَٰلِبِينَ ١١٣

114. «አዎን እናንተም በእርግጥ ከባለሟሎቹ ትኾናላችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ نَعَمۡ وَإِنَّكُمۡ لَمِنَ ٱلۡمُقَرَّبِينَ ١١٤

115. «ሙሳ ሆይ (በትርህን) ወይም (በፊት) ትጥላለህ ወይም እኛ ጣዮች እንኾናለን» አሉት፡፡

قَالُواْ يَٰمُوسَىٰٓ إِمَّآ أَن تُلۡقِيَ وَإِمَّآ أَن نَّكُونَ نَحۡنُ ٱلۡمُلۡقِينَ ١١٥

116. «ጣሉ» አላቸው፡፡ (ገመዶቻቸውን) በጣሉም ጊዜ የሰዎቹን ዓይኖች ደገሙባቸው፡፡ አስፈራሩዋቸውም፡፡ ትልቅ ድግምትንም አመጡ፡፡

قَالَ أَلۡقُواْۖ فَلَمَّآ أَلۡقَوۡاْ سَحَرُوٓاْ أَعۡيُنَ ٱلنَّاسِ وَٱسۡتَرۡهَبُوهُمۡ وَجَآءُو بِسِحۡرٍ عَظِيمٖ ١١٦

117. ወደ ሙሳም፡- «በትርህን ጣል» ስንል ላክን፡፡ (ጣላትም) ወዲያውኑም የሚቀጣጥፉትን (ማታለያ) ትውጣለች፡፡

۞وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰٓ أَنۡ أَلۡقِ عَصَاكَۖ فَإِذَا هِيَ تَلۡقَفُ مَا يَأۡفِكُونَ ١١٧

118. እውነቱም ተገለጸ፡፡ ይሠሩት የነበሩትም (ድግምት) ተበላሸ፡፡

فَوَقَعَ ٱلۡحَقُّ وَبَطَلَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١١٨

119. እዚያ ዘንድ ተሸነፉም፡፡ ወራዶችም ኾነው ተመለሱ፡፡

فَغُلِبُواْ هُنَالِكَ وَٱنقَلَبُواْ صَٰغِرِينَ ١١٩

120. ድግምተኞቹም ሰጋጆች ኾነው ወደቁ፡፡

وَأُلۡقِيَ ٱلسَّحَرَةُ سَٰجِدِينَ ١٢٠

121. አሉ፡- «በዓለማት ጌታ አመንን፡፡»

قَالُوٓاْ ءَامَنَّا بِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٢١

122. «በሙሳና በሃሩን ጌታ፡፡»

رَبِّ مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ١٢٢

123. ፈርዖን አለ፡- «እኔ ለእናንተ ሳልፈቅድላችሁ በፊት በእርሱ አመናችሁን ይህ በከተማይቱ ውስጥ ሰዎቿን ከእርሷ ለማውጣት በእርግጥ የተስማማችሁበት ተንኮል ነው፡፡ ወደፊትም (የሚደርስባችሁን) ታውቃላችሁ፡፡»

قَالَ فِرۡعَوۡنُ ءَامَنتُم بِهِۦ قَبۡلَ أَنۡ ءَاذَنَ لَكُمۡۖ إِنَّ هَٰذَا لَمَكۡرٞ مَّكَرۡتُمُوهُ فِي ٱلۡمَدِينَةِ لِتُخۡرِجُواْ مِنۡهَآ أَهۡلَهَاۖ فَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ١٢٣

124. «እጆቻችሁንና እግሮቻችሁን በማፈራረቅ በእርግጥ እቆራርጣለሁ፡፡ ከዚያም ሁላችሁንም በእርግጥ እሰቅላችኋለሁ፡፡»

لَأُقَطِّعَنَّ أَيۡدِيَكُمۡ وَأَرۡجُلَكُم مِّنۡ خِلَٰفٖ ثُمَّ لَأُصَلِّبَنَّكُمۡ أَجۡمَعِينَ ١٢٤

125. አሉ፡- «እኛ ወደ ጌታችን ተመላሾች ነን፡፡»

قَالُوٓاْ إِنَّآ إِلَىٰ رَبِّنَا مُنقَلِبُونَ ١٢٥

126. «የጌታችንም ተዓምራቶች በመጡልን ጊዜ ከማመናችን በቀር ከእኛ አትጠላም፡፡ ጌታችን ሆይ! በእኛ ላይ ትዕግስትን አፍስስ፡፡ ሙስሊሞች ኾነን ግደለን፡፡»

وَمَا تَنقِمُ مِنَّآ إِلَّآ أَنْ ءَامَنَّا بِـَٔايَٰتِ رَبِّنَا لَمَّا جَآءَتْنَا ۚ رَبَّنَآ أَفْرِغْ عَلَيْنَا صَبْرًا وَتَوَفَّنَا مُسْلِمِينَ ﴿١٢٦﴾

127. ከፈርዖንም ሰዎች ታላላቆቹ (ለፈርዖን) «ሙሳንና ሰዎቹን በምድር ላይ እንዲያበላሹና (ሙሳም) አንተንና አማልክቶችህን እንዲተው ትተዋቸዋለህን» አሉ፡፡ «ወንዶች ልጆቻቸውን እንገድላለን፡፡ ሴቶቻቸውንም እናስቀራለን፡፡ እኛም ከበላያቸው ነን፡፡ አሸናፊዎች (ነን)» አለ፡፡

وَقَالَ ٱلْمَلَأُ مِن قَوْمِ فِرْعَوْنَ أَتَذَرُ مُوسَىٰ وَقَوْمَهُۥ لِيُفْسِدُوا۟ فِى ٱلْأَرْضِ وَيَذَرَكَ وَءَالِهَتَكَ ۚ قَالَ سَنُقَتِّلُ أَبْنَآءَهُمْ وَنَسْتَحْىِۦ نِسَآءَهُمْ وَإِنَّا فَوْقَهُمْ قَٰهِرُونَ ﴿١٢٧﴾

128. ሙሳ ለሰዎቹ፡- «ለአላህ ተገዙ ታገሱም፡፡ ምድር ለአላህ ናትና፡፡ ከባሮቹ ለሚሻው ያወርሳታል፡፡ ምስጉንዋም ፍጻሜ ለጥንቁቆቹ ናት» አላቸው፡፡

قَالَ مُوسَىٰ لِقَوْمِهِ ٱسْتَعِينُوا۟ بِٱللَّهِ وَٱصْبِرُوٓا۟ ۖ إِنَّ ٱلْأَرْضَ لِلَّهِ يُورِثُهَا مَن يَشَآءُ مِنْ عِبَادِهِۦ ۖ وَٱلْعَٰقِبَةُ لِلْمُتَّقِينَ ﴿١٢٨﴾

129. «ከመምጣትህም በፊት ከመጣኽልንም በኋላ ተሰቃየን» አሉት፡፡ «ጌታችሁ ጠላቶቻችሁን ሊያጠፋ እንዴት እንደምትሠሩም ይመለከት ዘንድ በምድር ላይ ሊተካችሁ ይሻል» አላቸው፡፡

قَالُوٓا۟ أُوذِينَا مِن قَبْلِ أَن تَأْتِيَنَا وَمِنۢ بَعْدِ مَا جِئْتَنَا ۚ قَالَ عَسَىٰ رَبُّكُمْ أَن يُهْلِكَ عَدُوَّكُمْ وَيَسْتَخْلِفَكُمْ فِى ٱلْأَرْضِ فَيَنظُرَ كَيْفَ تَعْمَلُونَ ﴿١٢٩﴾

130. የፈርዖንንም ቤተሰቦች እንዲገሰጹ በድርቅ ዓመታትና ከፍሬዎችም በመቀነስ በእርግጥ ያዝናቸው፡፡

وَلَقَدْ أَخَذْنَآ ءَالَ فِرْعَوْنَ بِٱلسِّنِينَ وَنَقْصٍ مِّنَ ٱلثَّمَرَٰتِ لَعَلَّهُمْ يَذَّكَّرُونَ ﴿١٣٠﴾

131. ደጊቱም ነገር (ምቾት) በመጣችላቸው ጊዜ «ይህች ለእኛ (ተገቢ) ናት» ይላሉ፡፡ ክፉትም ብታገኛቸው በሙሳና አብረውት ባሉት ገደቢስነት ያመካኛሉ፡፡ ንቁ! ገደቢስነታቸው አላህ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ ግን አብዛኛዎቻቸው አያውቁም፡፡

فَإِذَا جَآءَتْهُمُ ٱلْحَسَنَةُ قَالُوا۟ لَنَا هَٰذِهِۦ ۖ وَإِن تُصِبْهُمْ سَيِّئَةٌ يَطَّيَّرُوا۟ بِمُوسَىٰ وَمَن مَّعَهُۥٓ ۗ أَلَآ إِنَّمَا طَٰٓئِرُهُمْ عِندَ ٱللَّهِ وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَهُمْ لَا يَعْلَمُونَ ﴿١٣١﴾

132. (ለሙሳም) «በማንኛይቱም ተዓምር በእርሷ ልትደግምብን ብትመጣብን እኛ ለአንተ የምናምንልህ አይደለንም» አሉ፡፡

وَقَالُوا۟ مَهْمَا تَأْتِنَا بِهِۦ مِنْ ءَايَةٍ لِّتَسْحَرَنَا بِهَا فَمَا نَحْنُ لَكَ بِمُؤْمِنِينَ ﴿١٣٢﴾

133. ወዲያም የወሃን ማጥለቅለቅ አንበጣንም ነቀዝንም እንቁራሪቶችንም ደምንም የተለያዩ ተዓምራት ሲኾኑ በነሱ ላይ ላክን ኮሩም ተንኮለኞችም ሕዝቦች ነበሩ፡፡

فَأَرْسَلْنَا عَلَيْهِمُ ٱلطُّوفَانَ وَٱلْجَرَادَ وَٱلْقُمَّلَ وَٱلضَّفَادِعَ وَٱلدَّمَ ءَايَٰتٍ مُّفَصَّلَٰتٍ فَٱسْتَكْبَرُوا۟ وَكَانُوا۟ قَوْمًا مُّجْرِمِينَ ﴿١٣٣﴾

134. በእነርሱም ላይ ቅጣቱ በወደቀባቸው ጊዜ «ሙሳ ሆይ! ጌታህን ላንተ ቃል ኪዳን በገባልህ ነገር ለእኛ ለምንልን፡፡ ከእኛ ቅጣቱን ብታነሳልን ለአንተ በእርግጥ እናምንልሃለን፡፡ የእስራኤልንም ልጆች ከአንተ ጋር በእርግጥ እንለቃለን፤» አሉ፡፡

وَلَمَّا وَقَعَ عَلَيْهِمُ ٱلرِّجْزُ قَالُوا۟ يَٰمُوسَى ٱدْعُ لَنَا رَبَّكَ بِمَا عَهِدَ عِندَكَ ۖ لَئِن كَشَفْتَ عَنَّا ٱلرِّجْزَ لَنُؤْمِنَنَّ لَكَ وَلَنُرْسِلَنَّ مَعَكَ بَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ ﴿١٣٤﴾

135. እነርሱም ደራሾቹ እኾኑበት ጊዜ ድረስ ቅጣትን ከእነሱ ላይ ባነሳን ጊዜ ወዲያውኑ እነርሱ ቃላቸውን ያፈርሳሉ፡፡

فَلَمَّا كَشَفۡنَا عَنۡهُمُ ٱلرِّجۡزَ إِلَىٰٓ أَجَلٍ هُم بَٰلِغُوهُ إِذَا هُمۡ يَنكُثُونَ ١٣٥

136. እነርሱ በተዓምራታችን ስለአስተባበሉም ከእርሷ ዘንጊዎች ስለኾኑም፤ ከእነሱ ተበቀልን፡፡ በባሕርም ውስጥ አሰጠምናቸው፡፡

فَٱنتَقَمۡنَا مِنۡهُمۡ فَأَغۡرَقۡنَٰهُمۡ فِي ٱلۡيَمِّ بِأَنَّهُمۡ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَكَانُواْ عَنۡهَا غَٰفِلِينَ ١٣٦

137. እነዚያንም ደካሞች የነበሩትን ሕዝቦች ያችን በውስጧ በረከት ያደረግንባትን ምድር ምሥራቆችዋንም ምዕራቦቿንም አወረስናቸው፡፡ የጌታህም መልካሚቱ ቃል በእስራኤል ልጆች ላይ በመታገሳቸው ተፈጸመች፡፡ ፈርዖንና ሰዎቹም ይሠሩት የነበረውን (ሕንጻ) ዳስ ያደርጉትም የነበረውን አፈረስን፡፡

وَأَوۡرَثۡنَا ٱلۡقَوۡمَ ٱلَّذِينَ كَانُواْ يُسۡتَضۡعَفُونَ مَشَٰرِقَ ٱلۡأَرۡضِ وَمَغَٰرِبَهَا ٱلَّتِي بَٰرَكۡنَا فِيهَاۖ وَتَمَّتۡ كَلِمَتُ رَبِّكَ ٱلۡحُسۡنَىٰ عَلَىٰ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ بِمَا صَبَرُواْۖ وَدَمَّرۡنَا مَا كَانَ يَصۡنَعُ فِرۡعَوۡنُ وَقَوۡمُهُۥ وَمَا كَانُواْ يَعۡرِشُونَ ١٣٧

138. የእስራኤልንም ልጆች ባሕሩን አሻገርናቸው፡፡ ለእነርሱ በኾኑ ጣዖታት (መገዛት) ላይ በሚዘወትሩ ሕዝቦች ላይ አለፉም፡፡ «ሙሳ ሆይ፡- ለእነርሱ (ለሰዎቹ) አማልክት እንዷላቸው ለእኛም አምላክን አድርግልን» አሉት፡፡ «እናንተ የምትሳሳቱ ሕዝቦች ናችሁ፤» አላቸው፡፡

وَجَٰوَزۡنَا بِبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱلۡبَحۡرَ فَأَتَوۡاْ عَلَىٰ قَوۡمٖ يَعۡكُفُونَ عَلَىٰٓ أَصۡنَامٖ لَّهُمۡۚ قَالُواْ يَٰمُوسَى ٱجۡعَل لَّنَآ إِلَٰهٗا كَمَا لَهُمۡ ءَالِهَةٞۚ قَالَ إِنَّكُمۡ قَوۡمٞ تَجۡهَلُونَ ١٣٨

139. «እነዚህ እነርሱ በውስጡ ያሉበት ነገር ጠፊ ነው፡፡ ይሰሩት የነበሩትም ብልሹ ነው» (አላቸው)፤

إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ مُتَبَّرٞ مَّا هُمۡ فِيهِ وَبَٰطِلٞ مَّا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٣٩

140. «ከአላህ ሌላ እርሱ ከዓለማት ያበለጣችሁ ሲኾን (የምትገዙት) አምላክን እፈልግላችኋለሁን» አለ፡፡

قَالَ أَغَيۡرَ ٱللَّهِ أَبۡغِيكُمۡ إِلَٰهٗا وَهُوَ فَضَّلَكُمۡ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٤٠

141. ከፈርዖንም ቤተሰቦች ብርቱን ቅጣት የሚያቀምሱዋችሁ ወንዶች ልጆቻችሁን የሚገድሉ ሴቶቻችሁንም የሚተዉ ሲኾኑ ባዳናችሁ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ በዚህም ውስጥ ከጌታችሁ ዘንድ የኾነ ከባድ ፈተና አለበት፡፡

وَإِذۡ أَنجَيۡنَٰكُم مِّنۡ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ يَسُومُونَكُمۡ سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِ يُقَتِّلُونَ أَبۡنَآءَكُمۡ وَيَسۡتَحۡيُونَ نِسَآءَكُمۡۚ وَفِي ذَٰلِكُم بَلَآءٞ مِّن رَّبِّكُمۡ عَظِيمٞ ١٤١

142. ሙሳንም ሰላሳን ሌሊት (ሊጾምና ልናነጋግረው) ቀጠርነው፡፡ በዐስርም (ሌሊት) ሞላናት፡፡ የጌታውም ቀጠሮ አርባ ሌሊት ሲኾን ተፈጸመ፡፡ ሙሳም ለወንድሙ ሃሩን «በሕዝቦቼ ላይ ተተካኝ፡፡ አሳምርም የአጥፊዎችንም መንገድ አትከተል» አለው፡፡

۞وَوَٰعَدۡنَا مُوسَىٰ ثَلَٰثِينَ لَيۡلَةٗ وَأَتۡمَمۡنَٰهَا بِعَشۡرٖ فَتَمَّ مِيقَٰتُ رَبِّهِۦٓ أَرۡبَعِينَ لَيۡلَةٗۚ وَقَالَ مُوسَىٰ لِأَخِيهِ هَٰرُونَ ٱخۡلُفۡنِي فِي قَوۡمِي وَأَصۡلِحۡ وَلَا تَتَّبِعۡ سَبِيلَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ١٤٢

143. ሙሳም ለቀጠሯችን በመጣና ጌታውም ባነጋገረው ጊዜ፡- «ጌታዬ ሆይ! (ነፍስህን) አሳየኝ ወደ አንተ እመለከታለሁና» አለ፡፡ (አላህም)፡- «በፍጹም አታየኝም ግን ወደ ተራራው ተመልከት፡፡ በስፍራውም ቢረጋ በእርግጥ ታየኛለህ» አለው፡፡ ጌታው ለተራራው በተገለጸ ጊዜ እንኩትኩት አደረገው፡፡ ሙሳም ጮሆ ወደቀ፡፡ በአንሰራራም ጊዜ «ጥራት ይገባህ፡፡ ወዳንተ ተመለስኩ፡፡ እኔም (በወቅቱ) የምእምናን መጀመሪያ ነኝ» አለ፡፡

وَلَمَّا جَآءَ مُوسَىٰ لِمِيقَٰتِنَا وَكَلَّمَهُۥ رَبُّهُۥ قَالَ رَبِّ أَرِنِيٓ أَنظُرۡ إِلَيۡكَۚ قَالَ لَن تَرَىٰنِي وَلَٰكِنِ ٱنظُرۡ إِلَى ٱلۡجَبَلِ فَإِنِ ٱسۡتَقَرَّ مَكَانَهُۥ فَسَوۡفَ تَرَىٰنِيۚ فَلَمَّا تَجَلَّىٰ رَبُّهُۥ لِلۡجَبَلِ جَعَلَهُۥ دَكّٗا وَخَرَّ مُوسَىٰ صَعِقٗاۚ فَلَمَّآ أَفَاقَ قَالَ سُبۡحَٰنَكَ تُبۡتُ إِلَيۡكَ وَأَنَا۠ أَوَّلُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٤٣

144. (አላህም) አለው፡- «ሙሳ ሆይ! እኔ በመልክቶቼና በማናገሬ በሰዎች ላይ መረጥኩህ፡፡ የሰጡህንም ያዝ፡፡ ከአመስጋኞቹም ኹን፡፡»

قَالَ يَٰمُوسَىٰٓ إِنِّي ٱصۡطَفَيۡتُكَ عَلَى ٱلنَّاسِ بِرِسَٰلَٰتِي وَبِكَلَٰمِي فَخُذۡ مَآ ءَاتَيۡتُكَ وَكُن مِّنَ ٱلشَّٰكِرِينَ ١٤٤

145. ለእርሱም በሰሌዳዎቹ ላይ ከነገሩ ሁሉ ግሳጼንና ለነገሩም ሁሉ ማብራራትን ጻፍንለት፡፡ (አልንም) በብርታትም ያዛት፡፡ ሕዝቦችህንም በመልካሟ እንዲይዙ እዘዛቸው፡፡ የአመጸኞቹን አገር በእርግጥ አሳያችኋለሁ፡፡

وَكَتَبۡنَا لَهُۥ فِي ٱلۡأَلۡوَاحِ مِن كُلِّ شَيۡءٖ مَّوۡعِظَةٗ وَتَفۡصِيلٗا لِّكُلِّ شَيۡءٖ فَخُذۡهَا بِقُوَّةٖ وَأۡمُرۡ قَوۡمَكَ يَأۡخُذُواْ بِأَحۡسَنِهَاۚ سَأُوْرِيكُمۡ دَارَ ٱلۡفَٰسِقِينَ ١٤٥

146. እነዚያን ያለአግባብ በምድር ላይ የሚኮሩትን ከአንቀጾቼ በእርግጥ አዞራቸዋለሁ፡፡ ተዓምርንም ሁሉ ቢያዩ በርሷ አያምኑም፡፡ ቅንንም መንገድ ቢያዩ መንገድ አድርገው አይዙትም፡፡ ግን የጥመትን መንገድ ቢያዩ መንገድ አድርገው ይይዙታል፡፡ ይህ እነርሱ በአንቀጾቻችን ስለአስተባበሉና ከእርሷም ዘንጊዎች ስለኾኑ ነው፡፡

سَأَصۡرِفُ عَنۡ ءَايَٰتِيَ ٱلَّذِينَ يَتَكَبَّرُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّ وَإِن يَرَوۡاْ كُلَّ ءَايَةٖ لَّا يُؤۡمِنُواْ بِهَا وَإِن يَرَوۡاْ سَبِيلَ ٱلرُّشۡدِ لَا يَتَّخِذُوهُ سَبِيلٗا وَإِن يَرَوۡاْ سَبِيلَ ٱلۡغَيِّ يَتَّخِذُوهُ سَبِيلٗاۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَكَانُواْ عَنۡهَا غَٰفِلِينَ ١٤٦

147. እነዚያም በአንቀጾቻችንና መጨረሻይቱን ዓለም በመገናኘት ያስተባበሉት ሥራዎቻቸው ተበላሹ፡፡ ይሠሩት የነበረውን እንጂ ይመነዳሉን

وَٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَلِقَآءِ ٱلۡأٓخِرَةِ حَبِطَتۡ أَعۡمَٰلُهُمۡۚ هَلۡ يُجۡزَوۡنَ إِلَّا مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٤٧

148. የሙሳም ሕዝቦች ከእርሱ (መኼድ) በኋላ ከጌጦቻቸው ወይፈንን አካልን ለርሱ ማግሳት ያለውን (አምላክ አድርገው) ያዙ፡፡ እርሱ የማያናግራቸው መንገድንም የማይመራቸው መኾኑን አይመለከቱምን (አምላክ አድርገው) ያዙት፡፡ በዳዮችም ኾኑ፡፡

وَٱتَّخَذَ قَوۡمُ مُوسَىٰ مِنۢ بَعۡدِهِۦ مِنۡ حُلِيِّهِمۡ عِجۡلٗا جَسَدٗا لَّهُۥ خُوَارٌۚ أَلَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّهُۥ لَا يُكَلِّمُهُمۡ وَلَا يَهۡدِيهِمۡ سَبِيلًاۘ ٱتَّخَذُوهُ وَكَانُواْ ظَٰلِمِينَ ١٤٨

149. በተጸጸቱና እነሱም በእርግጥ የተሳሳቱ መኾናቸውን ባዩ ጊዜ፡- «ጌታችን ባያዝንልንና ባይምረን በእርግጥ ከከሳሪዎቹ እንኾናለን» አሉ፡፡

وَلَمَّا سُقِطَ فِيٓ أَيۡدِيهِمۡ وَرَأَوۡاْ أَنَّهُمۡ قَدۡ ضَلُّواْ قَالُواْ لَئِن لَّمۡ يَرۡحَمۡنَا رَبُّنَا وَيَغۡفِرۡ لَنَا لَنَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ١٤٩

وَلَمَّا رَجَعَ مُوسَىٰٓ إِلَىٰ قَوۡمِهِۦ غَضۡبَٰنَ أَسِفٗا قَالَ بِئۡسَمَا خَلَفۡتُمُونِي مِنۢ بَعۡدِيٓۖ أَعَجِلۡتُمۡ أَمۡرَ رَبِّكُمۡۖ وَأَلۡقَى ٱلۡأَلۡوَاحَ وَأَخَذَ بِرَأۡسِ أَخِيهِ يَجُرُّهُۥٓ إِلَيۡهِۚ قَالَ ٱبۡنَ أُمَّ إِنَّ ٱلۡقَوۡمَ ٱسۡتَضۡعَفُونِي وَكَادُواْ يَقۡتُلُونَنِي فَلَا تُشۡمِتۡ بِيَ ٱلۡأَعۡدَآءَ وَلَا تَجۡعَلۡنِي مَعَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٥٠

150. ሙሳም እየተቆጣና እያዘነ ወደ ሕዝቦቹ በተመለሰ ጊዜ «ከእኔ በኋላ በእኔ ላይ የተካችሁት ነገር ከፋ! የጌታችሁን ትእዛዝ ተቻኮላችሁን» አላቸው፡፡ ሰሌዳዎቹንም ጣላቸው፡፡ የወንድሙንም ራስ (ጸጉር) ወደርሱ የሚጎትተው ሲኾን ያዘ፡፡ (ወንድሙም)፡- «የናቴ ልጅ ሆይ! ሕዝቦቹ ናቁኝ፡፡ ሊገድሉኝም ተቃረቡ፡፡ ስለዚህ በእኔ ጠላቶችን አታስደስትብኝ፡፡ ከአመጸኞች ሕዝቦችም ጋር አታድርገኝ» አለው፡፡

قَالَ رَبِّ ٱغۡفِرۡ لِي وَلِأَخِي وَأَدۡخِلۡنَا فِي رَحۡمَتِكَۖ وَأَنتَ أَرۡحَمُ ٱلرَّٰحِمِينَ ١٥١

151. (ሙሳም)፡- «ጌታዬ ሆይ! ለእኔም ለወንድሜም ማር፡፡ በእዝነትህም ውስጥ አግባን፡፡ አንተም ከአዛኞች ሁሉ ይበልጥ አዛኝ ነህ» አለ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُواْ ٱلۡعِجۡلَ سَيَنَالُهُمۡ غَضَبٞ مِّن رَّبِّهِمۡ وَذِلَّةٞ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُفۡتَرِينَ ١٥٢

152. እነዚያ ወይፈኑን (አምላክ አድርገው) የያዙ ከጌታቸው ዘንድ ቁጣ፤ በቅርቢቱም ሕይወት ውርደት በእርግጥ ያገኛቸዋል፡፡ እንዲሁም ቀጣፊዎችን እንቀጣለን፡፡

وَٱلَّذِينَ عَمِلُواْ ٱلسَّيِّـَٔاتِ ثُمَّ تَابُواْ مِنۢ بَعۡدِهَا وَءَامَنُوٓاْ إِنَّ رَبَّكَ مِنۢ بَعۡدِهَا لَغَفُورٞ رَّحِيمٞ ١٥٣

153. እነዚያም ኃጢአቶችን የሠሩ ከዚያም ከእርሷ በኋላ የተጸጸቱ ያመኑም ጌታህ ከእርሷ በኋላ በእርግጥ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلَمَّا سَكَتَ عَن مُّوسَى ٱلۡغَضَبُ أَخَذَ ٱلۡأَلۡوَاحَۖ وَفِي نُسۡخَتِهَا هُدٗى وَرَحۡمَةٞ لِّلَّذِينَ هُمۡ لِرَبِّهِمۡ يَرۡهَبُونَ ١٥٤

154. ከሙሳም ቁጣው በበረደ ጊዜ ሰሌዳዎቹን በግልባጫቸው ውስጥ ለእነዚያ እነርሱ ጌታቸውን የሚፈሩ ለኾኑት መምሪያና እዝነት ያለባቸው ሲኾኑ ያዘ፡፡

وَٱخۡتَارَ مُوسَىٰ قَوۡمَهُۥ سَبۡعِينَ رَجُلٗا لِّمِيقَٰتِنَاۖ فَلَمَّآ أَخَذَتۡهُمُ ٱلرَّجۡفَةُ قَالَ رَبِّ لَوۡ شِئۡتَ أَهۡلَكۡتَهُم مِّن قَبۡلُ وَإِيَّٰيَۖ أَتُهۡلِكُنَا بِمَا فَعَلَ ٱلسُّفَهَآءُ مِنَّآۖ إِنۡ هِيَ إِلَّا فِتۡنَتُكَ تُضِلُّ بِهَا مَن تَشَآءُ وَتَهۡدِي مَن تَشَآءُۖ أَنتَ وَلِيُّنَا فَٱغۡفِرۡ لَنَا وَٱرۡحَمۡنَاۖ وَأَنتَ خَيۡرُ ٱلۡغَٰفِرِينَ ١٥٥

155. ሙሳም ከሕዝቦቹ ውስጥ ለቀጠሮዋችን ሰባን ሰዎች መረጠ፡፡ ብርቱ የምድር እንቅጥቃጤ በያዘቻቸውም ጊዜ ሙሳ አለ «ጌታዬ ሆይ! በሻህ ኖሮ ከአሁን በፊት በአጠፋሃቸው ነበር፡፡ እኔንም (ባጠፋኸኝ ነበር)፡፡ ከእኛ ቂሎቹ በሠሩት ነገር ታጠፋናለህን እርሷ (ፈተናይቱ) ያንተ ፈተና እንጂ ሌላ አይደለችም፡፡ በእርሷ የምትሻውን ታሳስታለህ፡፡ የምትሻውንም ታቀናለህ፡፡ አንተ ረዳታችን ነህና ለእኛ ምሕረት አድርግልን፡፡ እዘንልንም፡፡ አንተም ከመሓሪዎች ሁሉ በላጭ ነህ፡፡»

۞وَٱكۡتُبۡ لَنَا فِي هَٰذِهِ ٱلدُّنۡيَا حَسَنَةٗ وَفِي ٱلۡأٓخِرَةِ إِنَّا هُدۡنَآ إِلَيۡكَۚ قَالَ عَذَابِيٓ أُصِيبُ بِهِۦ مَنۡ أَشَآءُۖ وَرَحۡمَتِي وَسِعَتۡ كُلَّ شَيۡءٖۚ فَسَأَكۡتُبُهَا لِلَّذِينَ يَتَّقُونَ وَيُؤۡتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَٱلَّذِينَ هُم بِـَٔايَٰتِنَا يُؤۡمِنُونَ ١٥٦

156. «ለእኛም በዚች በቅርቢቱ ዓለም መልካሚን በመጨረሻይቱም (መልካሚን) ጻፍልን፡፡ እኛ ወደ አንተ ተመለስን፡፡» (ሲል ሙሳ ጸለየ፤ አላህም) አለ፡- «ቅጣቴ በእርሱ የምሻውን ሰው እቀጣበታለሁ፡፡ ችሮታየም ነገሩን ሁሉ ሰፋች፡፡ ለእነዚያም ለሚጠነቀቁ፣ ዘካንም ለሚሰጡ፣ ለእነዚያም እነሱ በአንቀጾቻችን ለሚያምኑ በእርግጥ» እጽፋታለሁ፡፡

157. ለእነዚያ ያንን እነሱ ዘንድ በተውራትና በኢንጂል ተጽፎ የሚያገኙትን የማይጽፍና የማያነብ ነቢይ የኾነውን መልክተኛ የሚከተሉ ለኾኑት (በእርግጥ እጽፍለታለሁ)፡፡ በበጎ ሥራ ያዛቸዋል፡፡ ከክፉም ነገር ይከለክላቸዋል፡፡ መልካም ነገሮችንም ለነርሱ ይፈቅድላቸዋል፡፡ መጥፎ ነገሮችንም በእነርሱ ላይ እርም ያደርግባቸዋል፡፡ ከእነሱም ላይ ሸክማቸውንና እነዚያንም በእነርሱ ላይ የነበሩትን እንዛዝላዎች (ከባድ ሕግጋቶች) ያነሳላቸዋል፡፡ እነዚያም በእርሱ ያመኑ ያከበሩትም የረዱትም ያንንም ከእርሱ ጋር የተወረደውን ብርሃን የተከተሉ እነዚያ እነሱ የሚያድኑ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ يَتَّبِعُونَ ٱلرَّسُولَ ٱلنَّبِيَّ ٱلۡأُمِّيَّ ٱلَّذِي يَجِدُونَهُۥ مَكۡتُوبًا
عِندَهُمۡ فِي ٱلتَّوۡرَىٰةِ وَٱلۡإِنجِيلِ يَأۡمُرُهُم بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَيَنۡهَىٰهُمۡ
عَنِ ٱلۡمُنكَرِ وَيُحِلُّ لَهُمُ ٱلطَّيِّبَٰتِ وَيُحَرِّمُ عَلَيۡهِمُ ٱلۡخَبَٰٓئِثَ
وَيَضَعُ عَنۡهُمۡ إِصۡرَهُمۡ وَٱلۡأَغۡلَٰلَ ٱلَّتِي كَانَتۡ عَلَيۡهِمۡۚ فَٱلَّذِينَ
ءَامَنُواْ بِهِۦ وَعَزَّرُوهُ وَنَصَرُوهُ وَٱتَّبَعُواْ ٱلنُّورَ ٱلَّذِيٓ أُنزِلَ مَعَهُۥٓ
أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ١٥٧

158. (ሙሐመድ ሆይ!) በላቸው፡- «እናንተ ሰዎች ሆይ! እኔ ወደናንተ ወደሁላችሁም የአላህ መልክተኛ ነኝ፡፡ (እርሱም) ያ የሰማያትና የምድር ንግሥና ለእርሱ ብቻ የኾነ ነው፡፡ እርሱ እንጂ ሌላ አምላክ የለም፡፡ ሕያው ያደርጋል፡፡ ይገድላልም፡፡ በአላህ በዚያም በአላህና በቃላቶቹ በሚያምነው የማይጽፍ የማያነብ ነቢይ በኾነው መልክተኛው እመኑ፡፡ ቅንንም መንገድ ትመሩ ዘንድ ተከተሉት፡፡»

قُلۡ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِنِّي رَسُولُ ٱللَّهِ إِلَيۡكُمۡ جَمِيعًا ٱلَّذِي لَهُۥ
مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ يُحۡيِۦ وَيُمِيتُۖ
فَـَٔامِنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِ ٱلنَّبِيِّ ٱلۡأُمِّيِّ ٱلَّذِي يُؤۡمِنُ بِٱللَّهِ وَكَلِمَٰتِهِۦ
وَٱتَّبِعُوهُ لَعَلَّكُمۡ تَهۡتَدُونَ ١٥٨

159. ከሙሳም ሕዝቦች በእውነት የሚመሩት በእርሱም (ፍርድን) የሚያስተካክሉ ጭፍሮች አሉ፡፡

وَمِن قَوۡمِ مُوسَىٰٓ أُمَّةٞ يَهۡدُونَ بِٱلۡحَقِّ وَبِهِۦ يَعۡدِلُونَ ١٥٩

160. ዐሥራ ሁለት ነገዶች ሕዝቦች አድርገንም ከፋፈልናቸው፡፡ ወደ ሙሳም ወገኖቹ መጠጣትን በፈለጉበት ጊዜ «ድንጋዩን በበትርህ ምታው» ስንል ላክን፡፡ (መታውም) ከእርሱ ዐሥራ ሁለት ምንጮችም ፈለቁ፡፡ ሰዎቹ ሁሉ መጠጫቸውን በእርግጥ ዐወቁ፡፡ በእነሱም ላይ ደመናን አጠለልን፡፡ በእነሱም ላይ መናንና ድርጭትን አወረድን፡፡ «ከሰጠናችሁም መልካም ሲሳይ ብሉ» (አልን፤ ጸጋችንን በመካዳቸው) አልበደሉንምም፡፡ ግን ነፍሶቻቸውን የሚበድሉ ነበሩ፡፡

وَقَطَّعۡنَٰهُمُ ٱثۡنَتَيۡ عَشۡرَةَ أَسۡبَاطًا أُمَمٗاۚ وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰٓ إِذِ
ٱسۡتَسۡقَىٰهُ قَوۡمُهُۥٓ أَنِ ٱضۡرِب بِّعَصَاكَ ٱلۡحَجَرَۖ فَٱنۢبَجَسَتۡ مِنۡهُ
ٱثۡنَتَا عَشۡرَةَ عَيۡنٗاۖ قَدۡ عَلِمَ كُلُّ أُنَاسٖ مَّشۡرَبَهُمۡۚ وَظَلَّلۡنَا عَلَيۡهِمُ
ٱلۡغَمَٰمَ وَأَنزَلۡنَا عَلَيۡهِمُ ٱلۡمَنَّ وَٱلسَّلۡوَىٰۖ كُلُواْ مِن طَيِّبَٰتِ مَا
رَزَقۡنَٰكُمۡۚ وَمَا ظَلَمُونَا وَلَٰكِن كَانُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ يَظۡلِمُونَ ١٦٠

161. ለእነርሱም በተባሉ ጊዜ (አስታውስ) «በዚህች ከተማ ተቀመጡ፡፡ ከእርሷም በሻችሁት ስፍራ ብሉ፡፡ (የምንፈልገው) የኃጢኣታችንን መርገፍ ነው በሉም፡፡ የከተማይቱንም በር አጎንብሳችሁ ግቡ፡፡ ኃጢአቶቻችሁን ለእናንተ እንምራለንና፡፡ በጎ ለሠሩት በእርግጥ እንጨምራለን፡፡»

وَإِذۡ قِيلَ لَهُمُ ٱسۡكُنُواْ هَٰذِهِ ٱلۡقَرۡيَةَ وَكُلُواْ مِنۡهَا حَيۡثُ شِئۡتُمۡ
وَقُولُواْ حِطَّةٞ وَٱدۡخُلُواْ ٱلۡبَابَ سُجَّدٗا نَّغۡفِرۡ لَكُمۡ
خَطِيٓـَٰٔتِكُمۡۚ سَنَزِيدُ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٦١

162. ከእነሱም ውስጥ እነዚያ (ራሳቸውን) የበደሉት ሰዎች ከዚያ ለእነርሱ ከተባለው ሌላ የኾነን ቃል ለወጡ፡፡ በእነርሱም ላይ ይበድሉ በነበሩት በደል መዐትን ከሰማይ ላክንባቸው፡፡

فَبَدَّلَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنۡهُمۡ قَوۡلًا غَيۡرَ ٱلَّذِي قِيلَ لَهُمۡ فَأَرۡسَلۡنَا
عَلَيۡهِمۡ رِجۡزٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ بِمَا كَانُواْ يَظۡلِمُونَ ١٦٢

163. ከዚያችም በባህሩ ዳርቻ ከነበረችው ከተማ በቅዳሜ (ቀን) ወሰን ባለፉ ጊዜ በሰንበታቸው ቀን ዐሳዎቻቸው የተከማቹ ኾነው በሚመጡላቸው ጊዜ (የኾነውን) ጠይቃቸው፡፡ ሰንበትንም በማያከብሩበት (በሌላው) ቀን አይመጡላቸውም፡፡ እንደዚሁ ያምጹበት በነበሩት ምክንያት እንሞክራቸዋለን፡፡

وَسۡـَٔلۡهُمۡ عَنِ ٱلۡقَرۡيَةِ ٱلَّتِي كَانَتۡ حَاضِرَةَ ٱلۡبَحۡرِ إِذۡ يَعۡدُونَ فِي ٱلسَّبۡتِ إِذۡ تَأۡتِيهِمۡ حِيتَانُهُمۡ يَوۡمَ سَبۡتِهِمۡ شُرَّعٗا وَيَوۡمَ لَا يَسۡبِتُونَ لَا تَأۡتِيهِمۡۚ كَذَٰلِكَ نَبۡلُوهُم بِمَا كَانُواْ يَفۡسُقُونَ ﴿١٦٣﴾

164. ከእነሱም (ከፊሎቹ) ሕዝቦች «አላህ አጥፊያቸው ወይም በብርቱ ቅጣት ቀጪአቸው የኾኑትን ሕዝቦች ለምን ትገስፃላችሁ» ባሉ ጊዜ (ገሳጮቹ) «ወደ ጌታችሁ በቂ ምክንያት እንዲኾንና እነርሱም ቢከለከሉ ብለን ነው» አሉ፡፡

وَإِذۡ قَالَتۡ أُمَّةٞ مِّنۡهُمۡ لِمَ تَعِظُونَ قَوۡمًا ٱللَّهُ مُهۡلِكُهُمۡ أَوۡ مُعَذِّبُهُمۡ عَذَابٗا شَدِيدٗاۖ قَالُواْ مَعۡذِرَةً إِلَىٰ رَبِّكُمۡ وَلَعَلَّهُمۡ يَتَّقُونَ ﴿١٦٤﴾

165. በእርሱም የተገሰጹበትን ነገር በተዉ ጊዜ እነዚያን ከክፉ የሚከለከሉትን አዳንን፤ እነዚያንም የበደሉትን ያምጹ በነበሩት ምክንያት በብርቱ ቅጣት ያዝናቸው፡፡

فَلَمَّا نَسُواْ مَا ذُكِّرُواْ بِهِۦٓ أَنجَيۡنَا ٱلَّذِينَ يَنۡهَوۡنَ عَنِ ٱلسُّوٓءِ وَأَخَذۡنَا ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ بِعَذَابِۭ بَـِٔيسِۭ بِمَا كَانُواْ يَفۡسُقُونَ ﴿١٦٥﴾

166. ከእርሱም ከተከለከሉት ነገር በኮሩ ጊዜ ለእነሱ «ወረዶች ዝንጀሮች ኹኑ አልን፤» (ኾኑም)፡፡

فَلَمَّا عَتَوۡاْ عَن مَّا نُهُواْ عَنۡهُ قُلۡنَا لَهُمۡ كُونُواْ قِرَدَةً خَٰسِـِٔينَ ﴿١٦٦﴾

167. ጌታህም እስከ ትንሣኤ ቀን ክፉ ቅጣትን የሚያቀምሳቸውን ሰው በነሱ ላይ በእርግጥ የሚልክ መኾኑን ባስታወቀ ጊዜ (አስታውሳቸው)፡፡ ጌታህ በእርግጥ ቅጣተ ፈጣን ነው፡፡ እርሱም በእርግጥ እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَإِذۡ تَأَذَّنَ رَبُّكَ لَيَبۡعَثَنَّ عَلَيۡهِمۡ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ مَن يَسُومُهُمۡ سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِۗ إِنَّ رَبَّكَ لَسَرِيعُ ٱلۡعِقَابِ وَإِنَّهُۥ لَغَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿١٦٧﴾

168. (የእስራኤልን ልጆች) በምድር ላይ የተለያዩ ሕዝቦች አድርገንም ከፋፈልናቸው፡፡ ከእነሱ መልካሞች አሉ፡፡ ከእነሱም ከዚያ ሌላ አልሉ፡፡ ይመለሱ ዘንድም በተድላዎችም በመከራዎችም ሞከርናቸው፡፡

وَقَطَّعۡنَٰهُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ أُمَمٗاۖ مِّنۡهُمُ ٱلصَّٰلِحُونَ وَمِنۡهُمۡ دُونَ ذَٰلِكَۖ وَبَلَوۡنَٰهُم بِٱلۡحَسَنَٰتِ وَٱلسَّيِّـَٔاتِ لَعَلَّهُمۡ يَرۡجِعُونَ ﴿١٦٨﴾

169. ከኋላቸውም:- መጽሐፉን የወረሱ መጥፎ ምትኮች ተተኩ፡፡ የዚህን የቅርቡን ጠፊ ጥቅም ይይዛሉ፡፡ ብጤውም ጥቅም ቢመጣላቸው የሚይዙት ሲኾኑ « (በሠራነው):- ለኛ ምሕረት ይደረግልናል» ይላሉ፡፡ በአላህ ላይ ከእውነት በቀር እንዳይናገሩ በእነርሱ ላይ የመጽሐፉ ቃል ኪዳን አልተያዘባቸውምን በእርሱ ውስጥ ያለውንም አላነበቡምን የመጨረሻይቱም አገር ለእነዚያ ጌታቸውን ለሚፈሩት በላጭ ናት፡፡ አታውቁምን

فَخَلَفَ مِنۢ بَعۡدِهِمۡ خَلۡفٞ وَرِثُواْ ٱلۡكِتَٰبَ يَأۡخُذُونَ عَرَضَ هَٰذَا ٱلۡأَدۡنَىٰ وَيَقُولُونَ سَيُغۡفَرُ لَنَا وَإِن يَأۡتِهِمۡ عَرَضٞ مِّثۡلُهُۥ يَأۡخُذُوهُۚ أَلَمۡ يُؤۡخَذۡ عَلَيۡهِم مِّيثَٰقُ ٱلۡكِتَٰبِ أَن لَّا يَقُولُواْ عَلَى ٱللَّهِ إِلَّا ٱلۡحَقَّ وَدَرَسُواْ مَا فِيهِۗ وَٱلدَّارُ ٱلۡأٓخِرَةُ خَيۡرٞ لِّلَّذِينَ يَتَّقُونَۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ﴿١٦٩﴾

170. እነዚያም መጽሐፉን ጠብቀው የሚይዙ ሶላትንም በደንቡ የሰገዱ እኛ የመልካም ሠሪዎችን ዋጋ አናጠፉም፡፡

وَٱلَّذِينَ يُمَسِّكُونَ بِٱلۡكِتَٰبِ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ إِنَّا لَا نُضِيعُ أَجۡرَ ٱلۡمُصۡلِحِينَ ﴿١٧٠﴾

171. የጡርን ተራራ ነቅለን ከበላያቸው እንደ ጥላ ኾኖ በአነሳነውና እርሱም በነሱ ላይ ወዳቂ መኾኑን ባረጋገጡ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «የሰጠናችሁን በብርታት ያዙ፡፡ ትጠነቀቁም ዘንድ በውስጡ ያለውን ተገንዘቡ» (አልን)፡፡

۞وَإِذۡ نَتَقۡنَا ٱلۡجَبَلَ فَوۡقَهُمۡ كَأَنَّهُۥ ظُلَّةٞ وَظَنُّوٓاْ أَنَّهُۥ وَاقِعُۢ بِهِمۡ خُذُواْ مَآ ءَاتَيۡنَٰكُم بِقُوَّةٖ وَٱذۡكُرُواْ مَا فِيهِ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ١٧١

172. ጌታህም ከአደም ልጆች ከጀርባቸቻቸው ዘሮቻቸውን ባወጣና «ጌታችሁ አይደለሁምን» ሲል በነፍሶቻቸው ላይ ባስመሰከራቸው ጊዜ (የኾነውን አስታውስ)፡፡ «ጌታችን ነህ መሰከርን» አሉ፡፡ «በትንሣኤ ቀን ከዚህ (ኪዳን) ዘንጊዎች ነበርን እንዳትሉ፡፡»

وَإِذۡ أَخَذَ رَبُّكَ مِنۢ بَنِيٓ ءَادَمَ مِن ظُهُورِهِمۡ ذُرِّيَّتَهُمۡ وَأَشۡهَدَهُمۡ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡ أَلَسۡتُ بِرَبِّكُمۡۖ قَالُواْ بَلَىٰ شَهِدۡنَآۚ أَن تَقُولُواْ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ إِنَّا كُنَّا عَنۡ هَٰذَا غَٰفِلِينَ ١٧٢

173. ወይም «(ጣዖታትን) ያጋሩት ከእኛ በፊት የነበሩት አባቶቻችን ብቻ ናቸው፡፡ እኛም ከእነሱ በኋላ የኾን ዘሮች ነበርን፡፡ አጥፊዎቹ በሠሩት ታጠፋናለህን» እንዳትሉ (አስመሰከርናችሁ)፡፡

أَوۡ تَقُولُوٓاْ إِنَّمَآ أَشۡرَكَ ءَابَآؤُنَا مِن قَبۡلُ وَكُنَّا ذُرِّيَّةٗ مِّنۢ بَعۡدِهِمۡۖ أَفَتُهۡلِكُنَا بِمَا فَعَلَ ٱلۡمُبۡطِلُونَ ١٧٣

174. እንደዚሁም (እንዲያስቡ) እንዲመለሱም አንቀጾችን እናብራራለን፡፡

وَكَذَٰلِكَ نُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ وَلَعَلَّهُمۡ يَرۡجِعُونَ ١٧٤

175. የዚያንም ተዓምራታችንን የሰጠነውንና ከእርሷ የወጣውን ሰይጣንም ያስከተለውን ከጠማሞቹም የኾነውን ሰው ወሬ በእነርሱ ላይ አንብብላቸው፡፡

وَٱتۡلُ عَلَيۡهِمۡ نَبَأَ ٱلَّذِيٓ ءَاتَيۡنَٰهُ ءَايَٰتِنَا فَٱنسَلَخَ مِنۡهَا فَأَتۡبَعَهُ ٱلشَّيۡطَٰنُ فَكَانَ مِنَ ٱلۡغَاوِينَ ١٧٥

176. በሻንም ኖሮ በእርሷ ከፍ ባደረግነው ነበር፡፡ እርሱ ግን ወደ ምድር ተዘነበለ፡፡ ፍላጎቱንም ተከተለ፡፡ ብጤውም ብታባርረው ምላሱን አውጥቶ የሚያለከልክ ወይም ብትተወው ምላሱን አውጥቶ የሚያለከልክ እንደ ኾነ ውሻ ነው፡፡ ይህ የእነዚያ በአንቀጾቻችን ያስተባበሉት ሕዝቦች ምሳሌ ነው፡፡ ያስተነትኑም ዘንድ ታሪኮችን ተርክላቸው፡፡

وَلَوۡ شِئۡنَا لَرَفَعۡنَٰهُ بِهَا وَلَٰكِنَّهُۥٓ أَخۡلَدَ إِلَى ٱلۡأَرۡضِ وَٱتَّبَعَ هَوَىٰهُۚ فَمَثَلُهُۥ كَمَثَلِ ٱلۡكَلۡبِ إِن تَحۡمِلۡ عَلَيۡهِ يَلۡهَثۡ أَوۡ تَتۡرُكۡهُ يَلۡهَثۚ ذَّٰلِكَ مَثَلُ ٱلۡقَوۡمِ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَاۚ فَٱقۡصُصِ ٱلۡقَصَصَ لَعَلَّهُمۡ يَتَفَكَّرُونَ ١٧٦

177. የእነዚያ በአንቀጾቻችን ያስተባበሉትና ነፍሶቻቸውን ይበድሉ የነበሩት ሰዎች ምሳሌ ከፋ!

سَآءَ مَثَلًا ٱلۡقَوۡمُ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَأَنفُسَهُمۡ كَانُواْ يَظۡلِمُونَ ١٧٧

178. አላህ የሚያቀናው ሰው ቅን እርሱ ነው፡፡ የሚያጠመውም ሰው እነዚያ ከሳሪዎቹ እነሱ ናቸው፡፡

مَن يَهۡدِ ٱللَّهُ فَهُوَ ٱلۡمُهۡتَدِيۖ وَمَن يُضۡلِلۡ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ١٧٨

179. ከጋኔንም ከሰዎችም ብዙዎችን ለገሀነም በእርግጥ ፈጠርን፡፡ ለእነርሱ በርሳቸው የማያውቁባቸው ልቦች አሏቸው፡፡ ለእነሱም በሳቸው የማያዩባቸው ዓይኖች አሉዋቸው፡፡ ለእነሱም በሳቸው የማይሰሙባቸው ጆሮዎች አሉዋቸው፡፡ እነዚያ እንደ እንስሳዎች ናቸው፡፡ ይልቁንም እነርሱ በጣም የተሳሳቱ ናቸው፡፡ እነዚያ ዘንጊዎቹ እነርሱ ናቸው፤

وَلَقَدۡ ذَرَأۡنَا لِجَهَنَّمَ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلۡجِنِّ وَٱلۡإِنسِۖ لَهُمۡ قُلُوبٞ لَّا يَفۡقَهُونَ بِهَا وَلَهُمۡ أَعۡيُنٞ لَّا يُبۡصِرُونَ بِهَا وَلَهُمۡ ءَاذَانٞ لَّا يَسۡمَعُونَ بِهَآۚ أُوْلَٰٓئِكَ كَٱلۡأَنۡعَٰمِ بَلۡ هُمۡ أَضَلُّۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡغَٰفِلُونَ ١٧٩

180. ለአላህም መልካም ስሞች አሉት፡፡ (ስትጸልዩ) በእርሷም ጥሩት፡፡ እነዚያንም ስሞቹን የሚያጣምሙትን ተውዋቸው፡፡ ይሠሩት የነበሩትን ነገር በእርግጥ ይምመነዳሉ፡፡

وَلِلَّهِ ٱلۡأَسۡمَآءُ ٱلۡحُسۡنَىٰ فَٱدۡعُوهُ بِهَاۖ وَذَرُواْ ٱلَّذِينَ يُلۡحِدُونَ فِيٓ أَسۡمَٰٓئِهِۦۚ سَيُجۡزَوۡنَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٨٠

181. ከፈጠርናቸውም ሰዎች በእውነት የሚመሩ በእርሱም (ፍርድን) የሚያስተካክሉ ሕዝቦች አልሉ፡፡

وَمِمَّنۡ خَلَقۡنَآ أُمَّةٞ يَهۡدُونَ بِٱلۡحَقِّ وَبِهِۦ يَعۡدِلُونَ ١٨١

182. እነዚያንም በአንቀጾቻችን ያስተባበሉትን ከማያውቁት ስፍራ ቀስ በቀስ (ምቾትን በመጨመር) እናዘነጋቸዋለን፡፡

وَٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا سَنَسۡتَدۡرِجُهُم مِّنۡ حَيۡثُ لَا يَعۡلَمُونَ ١٨٢

183. ለእነርሱም ጊዜ እሰጣቸዋለሁ ጥበቤ ብርቱ ነውና፡፡

وَأُمۡلِي لَهُمۡۚ إِنَّ كَيۡدِي مَتِينٌ ١٨٣

184. በነቢያቸው (በሙሐመድ) ምንም ዕብደት የሌለበት መኾኑን አያስተውሉምን እርሱ ግልጽ አስጠንቃቂ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

أَوَلَمۡ يَتَفَكَّرُواْۗ مَا بِصَاحِبِهِم مِّن جِنَّةٍۚ إِنۡ هُوَ إِلَّا نَذِيرٞ مُّبِينٌ ١٨٤

185. በሰማያትና በምድር ግዛት ውስጥ ከማንኛው ነገር አላህ በፈጠረውም ሁሉ የሞት ጊዜያቸውም በእርግጥ መቅረቡ የሚፈራ መኾኑን አያስተውሉምን ከእርሱም (ከቁርኣን) ወዲያ በየትኛው ንግግር ያምናሉ፡፡

أَوَلَمۡ يَنظُرُواْ فِي مَلَكُوتِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا خَلَقَ ٱللَّهُ مِن شَيۡءٖ وَأَنۡ عَسَىٰٓ أَن يَكُونَ قَدِ ٱقۡتَرَبَ أَجَلُهُمۡۖ فَبِأَيِّ حَدِيثِۭ بَعۡدَهُۥ يُؤۡمِنُونَ ١٨٥

186. አላህ የሚያጠመው ሰው ለእርሱ ምንም አቅኚ የለውም፡፡ በጥምመታቸውም ውስጥ እየዋለሉ ይተዋቸዋል፡፡

مَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَلَا هَادِيَ لَهُۥۚ وَيَذَرُهُمۡ فِي طُغۡيَٰنِهِمۡ يَعۡمَهُونَ ١٨٦

187. ከሰዓቲቱ መቼ እንደምትረጋ (እንደምትመጣ) ይጠይቁሃል፡፡ «ዕውቀቷ በጌታዬ ዘንድ ነው፡፡ በጊዜዋ እርሱ እንጂ ሌላ አይገልጣትም፡፡ በሰማያትና በምድርም ከበደች፡፡ በድንገት ቢኾን እንጂ አትመጣችሁም» በላቸው፡፡ ከእርሷ አጥብቀህ እንደ ተረዳህ አድርገው ይጠይቁሃል፡፡ «ዕውቀቷ አላህ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያውቁም» በላቸው፡፡

يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلسَّاعَةِ أَيَّانَ مُرۡسَىٰهَاۖ قُلۡ إِنَّمَا عِلۡمُهَا عِندَ رَبِّيۖ لَا يُجَلِّيهَا لِوَقۡتِهَآ إِلَّا هُوَۚ ثَقُلَتۡ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ لَا تَأۡتِيكُمۡ إِلَّا بَغۡتَةٗۗ يَسۡـَٔلُونَكَ كَأَنَّكَ حَفِيٌّ عَنۡهَاۖ قُلۡ إِنَّمَا عِلۡمُهَا عِندَ ٱللَّهِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ١٨٧

قُل لَّآ أَمۡلِكُ لِنَفۡسِي نَفۡعٗا وَلَا ضَرًّا إِلَّا مَا شَآءَ ٱللَّهُۚ وَلَوۡ كُنتُ أَعۡلَمُ ٱلۡغَيۡبَ لَٱسۡتَكۡثَرۡتُ مِنَ ٱلۡخَيۡرِ وَمَا مَسَّنِيَ ٱلسُّوٓءُۚ إِنۡ أَنَا۠ إِلَّا نَذِيرٞ وَبَشِيرٞ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ١٨٨

188. «አላህ የሻውን በስተቀር ለእራሴ ጥቅምንም ጉዳትንም ማምጣት አልችልም፡፡ ሩቅንም (ምስጢር) የማውቅ በነበርኩ ኖሮ ከመልካም ነገር ባበዛሁና ከፉም ነገር ባልነካኝ ነበር፡፡ እኔ ለሚያምኑ ሕዝቦች አስፈራሪና አብሳሪ እንጂ ሌላ አይደለሁም» በላቸው፡፡

۞هُوَ ٱلَّذِي خَلَقَكُم مِّن نَّفۡسٖ وَٰحِدَةٖ وَجَعَلَ مِنۡهَا زَوۡجَهَا لِيَسۡكُنَ إِلَيۡهَاۖ فَلَمَّا تَغَشَّىٰهَا حَمَلَتۡ حَمۡلًا خَفِيفٗا فَمَرَّتۡ بِهِۦۖ فَلَمَّآ أَثۡقَلَت دَّعَوَا ٱللَّهَ رَبَّهُمَا لَئِنۡ ءَاتَيۡتَنَا صَٰلِحٗا لَّنَكُونَنَّ مِنَ ٱلشَّٰكِرِينَ ١٨٩

189. እርሱ ያ ከአንዲት ነፍስ (ከአደም) የፈጠራችሁ ከእርሷም መቀናጆዋን ወደርሷ ይረካ ዘንድ ያደረገ ነው፡ ፡ በተገናኛትም ጊዜ ቀላልን እርግዝና አረገዘች፡፡ እርሱንም (ፅንሱን) ይዛው ኼደች፡፡ በከበደችም ጊዜ «ደግን ልጅ ብትሰጠን በእርግጥ ከአመስጋኞቹ እንኾናለን፤» ሲሉ ጌታቸውን አላህን ለመኑ፡፡

فَلَمَّآ ءَاتَىٰهُمَا صَٰلِحٗا جَعَلَا لَهُۥ شُرَكَآءَ فِيمَآ ءَاتَىٰهُمَاۚ فَتَعَٰلَى ٱللَّهُ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ١٩٠

190. መልካም ልጅ በሰጣቸውም ጊዜ በሰጣቸው ልጅ (ስም) ለእርሱ ተጋሪዎችን አደረጉለት፡፡ አላህም ከሚያጋሩት ሁሉ ላቀ፡፡

أَيُشۡرِكُونَ مَا لَا يَخۡلُقُ شَيۡـٔٗا وَهُمۡ يُخۡلَقُونَ ١٩١

191. ምንንም የማይፈጥሩትንና እነርሱም የሚፈጠሩትን (በአላህ) ያጋራሉን

وَلَا يَسۡتَطِيعُونَ لَهُمۡ نَصۡرٗا وَلَآ أَنفُسَهُمۡ يَنصُرُونَ ١٩٢

192. ለእነርሱም መርዳትን የማይችሉትን ነፍሶቻቸውንም የማይረዱትን (ያጋራሉን)

وَإِن تَدۡعُوهُمۡ إِلَى ٱلۡهُدَىٰ لَا يَتَّبِعُوكُمۡۚ سَوَآءٌ عَلَيۡكُمۡ أَدَعَوۡتُمُوهُمۡ أَمۡ أَنتُمۡ صَٰمِتُونَ ١٩٣

193. (ጣዖቶቹን) ወደ ቅን መንገድ ብትጠሩዋቸውም አይከተሉዋችሁም፡፡ ብትጠሩዋቸው ወይም እናንተ ዝምተኞችም ብትኾኑ በእናንተ ላይ እኩል ነው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ عِبَادٌ أَمۡثَالُكُمۡۖ فَٱدۡعُوهُمۡ فَلۡيَسۡتَجِيبُواْ لَكُمۡ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ١٩٤

194. እነዚያ ከአላህ ሌላ የምትገ[3]ቸው ብጤዎቻችሁ ተገዢዎች ናቸው፡፡ እውነተኞችም እንደኾናችሁ ጥሩዋቸውና ለእናንተ ይመልሱላችሁ፤ (መመለስ ግን አይችሉም)፡፡

أَلَهُمۡ أَرۡجُلٞ يَمۡشُونَ بِهَآۖ أَمۡ لَهُمۡ أَيۡدٖ يَبۡطِشُونَ بِهَآۖ أَمۡ لَهُمۡ أَعۡيُنٞ يُبۡصِرُونَ بِهَآۖ أَمۡ لَهُمۡ ءَاذَانٞ يَسۡمَعُونَ بِهَاۗ قُلِ ٱدۡعُواْ شُرَكَآءَكُمۡ ثُمَّ كِيدُونِ فَلَا تُنظِرُونِ ١٩٥

195. ለእነርሱ በእርሳቸው የሚኼዱባቸው እግሮች አሉዋቸውን ወይስ ለእነሱ በርሳቸው የሚጨብጡባቸው እጆች አሉዋቸውን ወይስ ለእነሱ በእርሳቸው የሚያዩባቸው ዓይኖች አሉዋቸውን ወይስ ለእነሱ በእርሳቸው የሚሰሙባቸው ጆሮዎች አሉዋቸውን «ያጋራችኋቸውን ጥሩ ከዚያም ተተናኮሉኝ፡፡ ጊዜም አትስጡኝ፤ (አልፈራችሁም)» በላቸው፡፡

إِنَّ وَلِـِّۧيَ ٱللَّهُ ٱلَّذِي نَزَّلَ ٱلۡكِتَٰبَۖ وَهُوَ يَتَوَلَّى ٱلصَّٰلِحِينَ ١٩٦

196. «የእኔ ረዳቴ ያ መጽሐፉን (ቁርኣንን) ያወረደልኝ አላህ ነውና፤ እርሱም መልካም ሠሪዎችን ይረዳል» (በላቸው)፡፡

وَٱلَّذِينَ تَدۡعُونَ مِن دُونِهِۦ لَا يَسۡتَطِيعُونَ نَصۡرَكُمۡ وَلَآ أَنفُسَهُمۡ يَنصُرُونَ ١٩٧

197. እነዚያም ከእርሱ በቀር የምትገ[3]ቸው ሊረርችሁ አይችሉም፡፡ ነፍሶቻቸውንም አይረዱም፡፡

وَإِن تَدۡعُوهُمۡ إِلَى ٱلۡهُدَىٰ لَا يَسۡمَعُواْۖ وَتَرَىٰهُمۡ يَنظُرُونَ إِلَيۡكَ وَهُمۡ لَا يُبۡصِرُونَ ١٩٨

198. «ወደ ቅንም መንገድ (እንዲመሩዋችሁ) ብትጠሩዋቸው አይሰሙም፤» (በላቸው)፡፡ እነርሱንም የማያዩ ሲኾኑ ወደ አንተ ሲመለከቱ ታያቸዋለህ፡፡

خُذِ ٱلۡعَفۡوَ وَأۡمُرۡ بِٱلۡعُرۡفِ وَأَعۡرِضۡ عَنِ ٱلۡجَٰهِلِينَ ١٩٩

199. ገርን ጠባይ ያዝ፡፡ በመልካምም እዘዝ፡፡ ባለጌዎቹንም ተዋቸው፡፡

وَإِمَّا يَنزَغَنَّكَ مِنَ ٱلشَّيۡطَٰنِ نَزۡغٞ فَٱسۡتَعِذۡ بِٱللَّهِۚ إِنَّهُۥ سَمِيعٌ عَلِيمٌ ٢٠٠

200. ከሰይጣንም (በኩል) ጉትጎታ ቢያገኝህ በአላህ ተጠበቅ፡፡ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْ إِذَا مَسَّهُمۡ طَٰٓئِفٞ مِّنَ ٱلشَّيۡطَٰنِ تَذَكَّرُواْ فَإِذَا هُم مُّبۡصِرُونَ ٢٠١

201. እነዚያ የተጠነቀቁት ከሰይጣን የኾነ ዘዋሪ በነካቸው ጊዜ (ጌታቸውን) ይገነዘባሉ፡፡ ወዲያውም እነሱ ተመልካቾች ይኾናሉ፡፡

وَإِخۡوَٰنُهُمۡ يَمُدُّونَهُمۡ فِي ٱلۡغَيِّ ثُمَّ لَا يُقۡصِرُونَ ٢٠٢

202. ወንድሞቻቸውም ጥመትን ይጨምሩላቸዋል፤ ከዚያም (እነርሱ) አይገቱም፡፡

وَإِذَا لَمۡ تَأۡتِهِم بِـَٔايَةٖ قَالُواْ لَوۡلَا ٱجۡتَبَيۡتَهَاۚ قُلۡ إِنَّمَآ أَتَّبِعُ مَا يُوحَىٰٓ إِلَيَّ مِن رَّبِّيۚ هَٰذَا بَصَآئِرُ مِن رَّبِّكُمۡ وَهُدٗى وَرَحۡمَةٞ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ٢٠٣

203. በተዓምርም ባልመጣሃቸው ጊዜ (በራስህ) «ለምን አትፈጥራትም» ይላሉ፡፡ ከጌታዬ ወደኔ የተወረደውን ብቻ እከተላለሁ፡፡ ይህ (ቁርኣን) ከጌታችሁ ሲኾን ለሚያምኑ ሕዝቦች መረጃዎችና መምሪያ እዝነትም ነው በላቸው፡፡

وَإِذَا قُرِئَ ٱلۡقُرۡءَانُ فَٱسۡتَمِعُواْ لَهُۥ وَأَنصِتُواْ لَعَلَّكُمۡ تُرۡحَمُونَ ٢٠٤

204. ቁርኣንም በተነበበ ጊዜ እርሱን አዳምጡ፡፡ ጸጥም በሉ፡፡ ይታዘንላችኋልና፡፡

وَٱذۡكُر رَّبَّكَ فِي نَفۡسِكَ تَضَرُّعٗا وَخِيفَةٗ وَدُونَ ٱلۡجَهۡرِ مِنَ ٱلۡقَوۡلِ بِٱلۡغُدُوِّ وَٱلۡأٓصَالِ وَلَا تَكُن مِّنَ ٱلۡغَٰفِلِينَ ٢٠٥

205. ጌታህንም በምስጢር ተዋድቀህና ፈርተህ ከጮኽት በታችም በኾነ ቃል በጧትም በማታም አውሳው፡፡ ከዘንጊዎቹም አትኹን፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ عِندَ رَبِّكَ لَا يَسۡتَكۡبِرُونَ عَنۡ عِبَادَتِهِۦ وَيُسَبِّحُونَهُۥ وَلَهُۥ يَسۡجُدُونَ۩ ٢٠٦

206. እነዚያ እጌታህ ዘንድ ያሉት (መላእክት) እርሱን ከመገዛት አይኮሩም፡፡ ያወድሱታልም፡፡ ለእርሱም ብቻ ይሰግዳሉ፡፡

# ሱረቱ አል-አንፋል

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

1. ከጦር ዘረፋ ገንዘቦች ይጠይቁሃል:: «የዘረፋ ገንዘቦች የአላህና የመልክተኛው ናቸው::» ስለዚህ አላህን ፍሩ:: በመካከላችሁ ያለችውንም ኹኔታ አሳምሩ:: አማኞችም እንደኾናችሁ አላህንና መልክተኛውን ታዘዙ በላቸው::

2. ፍጹም ምእምናን እነዚያ አላህ በተወሳ ጊዜ ልቦቻቸው የሚፈሩት፣ በነሱም ላይ አንቀጾቻችን በተነበቡ ጊዜ እምነትን የሚጨምሩላቸው፣ በጌታቸውም ላይ ብቻ የሚመኩት ናቸው::

3. እነዚያ ሶላትን ደንቡን አሟልተው የሚሰግዱ ከሰጠናቸውም ሲሳይ የሚለግሱ ናቸው::

4. እነዚያ በእውነት አማኞች እነሱ ብቻ ናቸው:: ለእነሱ በጌታቸው ዘንድ ደረጃዎች ምህረትና የከበረ ሲሳይም አላቸው::

5. (ይህ በዘረፋ ክፍያ የከፊሉ ሰው መጥላት) ከምእምናን ከፊሉ የጠሉ ሲኾኑ ጌታህ ከቤትህ በእውነት ላይ ኾነህ እንዳወጣህ ነው::

6. እነርሱ እያዩ ወደሞት እንደሚነዱ ኾነው በእውነቱ ነገር (በመጋደል ግዴታነት) ከተገለጸላቸው በኋላ ይከራከሩሃል::

7. አላህም ከሁለቱ ጭፍሮች አንደኛዋን እርሷ ለናንተ ናት ሲል ተስፋ በሰጣችሁ ጊዜ፣ የሀይል ባለቤት ያልኾነችውም (ነጋዴይቱ) ለናንተ ልትኾን በወደዳችሁ ጊዜ፣ አላህም በተስፋ ቃላቱ እውነትን ማረጋገጡን ሊገልጽና የከሓዲዎችንም መጨረሻ ሊቆርጥ በሻ ጊዜ (የኾነውን አስታውስ)::

8. (ይህንንም ያደረገው) አጋሪዎቹ ቢጠሉም እውነቱን ሊያረጋግጥ ከህደትንም ሊያጠፋ ነው::

# سورة الأنفال

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

يَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلۡأَنفَالِۖ قُلِ ٱلۡأَنفَالُ لِلَّهِ وَٱلرَّسُولِۖ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَصۡلِحُواْ ذَاتَ بَيۡنِكُمۡۖ وَأَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥٓ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ١

إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِرَ ٱللَّهُ وَجِلَتۡ قُلُوبُهُمۡ وَإِذَا تُلِيَتۡ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُهُۥ زَادَتۡهُمۡ إِيمَٰنٗا وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٢

ٱلَّذِينَ يُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ٣

أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ حَقّٗاۚ لَّهُمۡ دَرَجَٰتٌ عِندَ رَبِّهِمۡ وَمَغۡفِرَةٞ وَرِزۡقٞ كَرِيمٞ ٤

كَمَآ أَخۡرَجَكَ رَبُّكَ مِنۢ بَيۡتِكَ بِٱلۡحَقِّ وَإِنَّ فَرِيقٗا مِّنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ لَكَٰرِهُونَ ٥

يُجَٰدِلُونَكَ فِي ٱلۡحَقِّ بَعۡدَ مَا تَبَيَّنَ كَأَنَّمَا يُسَاقُونَ إِلَى ٱلۡمَوۡتِ وَهُمۡ يَنظُرُونَ ٦

وَإِذۡ يَعِدُكُمُ ٱللَّهُ إِحۡدَى ٱلطَّآئِفَتَيۡنِ أَنَّهَا لَكُمۡ وَتَوَدُّونَ أَنَّ غَيۡرَ ذَاتِ ٱلشَّوۡكَةِ تَكُونُ لَكُمۡ وَيُرِيدُ ٱللَّهُ أَن يُحِقَّ ٱلۡحَقَّ بِكَلِمَٰتِهِۦ وَيَقۡطَعَ دَابِرَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٧

لِيُحِقَّ ٱلۡحَقَّ وَيُبۡطِلَ ٱلۡبَٰطِلَ وَلَوۡ كَرِهَ ٱلۡمُجۡرِمُونَ ٨

9. ከጌታችሁ ርዳታን በፈለጋችሁ ጊዜ «እኔ በሺህ መላእክት ተከታታዮች ሲኾኑ እረዳችኋለሁ» ሲል ለናንተ የተቀበላችሁን (አስታውሱ)፡፡

إِذۡ تَسۡتَغِيثُونَ رَبَّكُمۡ فَٱسۡتَجَابَ لَكُمۡ أَنِّي مُمِدُّكُم بِأَلۡفٖ مِّنَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ مُرۡدِفِينَ ٩

10. አላህም (ይኸንን ርዳታ) ለብስራትና ልቦቻችሁ በርሱ ሊረኩበት እንጂ ለሌላ አላደረገውም፡፡ ድልም መንሳት ከአላህ ዘንድ እንጂ ከሌላ አይደለም፡፡ አላህ አሸናፊ ጥበበኛ ነውና፡፡

وَمَا جَعَلَهُ ٱللَّهُ إِلَّا بُشۡرَىٰ وَلِتَطۡمَئِنَّ بِهِۦ قُلُوبُكُمۡۚ وَمَا ٱلنَّصۡرُ إِلَّا مِنۡ عِندِ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٌ ١٠

11. ከእርሱ በኾነው ጸጥታ (በጦር ግንባር) በእንቅልፍ በሸፈናችሁና ውሃውንም በእርሱ ሊያጠራችሁ፣ የሰይጣንንም ጉትጎታ ከእናንተ ሊያስወግድላችሁ፣ ልቦቻችሁንም (በትዕግስት) ሊያጠነክርላችሁ፣ በእርሱም ጫማዎችን (በአሸዋው ላይ) ሊያደላድልላችሁ በእናንተ ላይ ከሰማይ ባወረደላችሁ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡

إِذۡ يُغَشِّيكُمُ ٱلنُّعَاسَ أَمَنَةٗ مِّنۡهُ وَيُنَزِّلُ عَلَيۡكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ لِّيُطَهِّرَكُم بِهِۦ وَيُذۡهِبَ عَنكُمۡ رِجۡزَ ٱلشَّيۡطَٰنِ وَلِيَرۡبِطَ عَلَىٰ قُلُوبِكُمۡ وَيُثَبِّتَ بِهِ ٱلۡأَقۡدَامَ ١١

12. ጌታህ ወደ መላእክቱ «»እኔ (በእርዳታዬ) ከእናንተ ጋር ነኝና እነዚያን ያመኑትን አጽናኑ፡፡ በእነዚያ በካዱት ልቦች ውስጥ ፍርሃትን በእርግጥ እጥላለሁ፡፡ ከአንገቶችም በላይ (ራሶችን) ምቱ፡፡ ከእነሱም የቅርንጫፎችን መለያልይ ሁሉ ምቱ፡፡ ሲል ያወረደውን (አስታውስ)፡፡

إِذۡ يُوحِي رَبُّكَ إِلَى ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ أَنِّي مَعَكُمۡ فَثَبِّتُواْ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۚ سَأُلۡقِي فِي قُلُوبِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱلرُّعۡبَ فَٱضۡرِبُواْ فَوۡقَ ٱلۡأَعۡنَاقِ وَٱضۡرِبُواْ مِنۡهُمۡ كُلَّ بَنَانٖ ١٢

13. ይህ እነርሱ አላህንና መልክተኛውን ስለተቃወሙ ነው፡፡ አላህንና መልክተኛውንም የሚቃወም ሁሉ አላህ ቅጣቱ ብርቱ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ شَآقُّواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥۚ وَمَن يُشَاقِقِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ فَإِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ١٣

14. ይህ (ቅጣታችሁ ነው) ቅመሱትም፡፡ ለከሓዲዎችም የእሳት ቅጣት በእርግጥ አለባቸው፡፡

ذَٰلِكُمۡ فَذُوقُوهُ وَأَنَّ لِلۡكَٰفِرِينَ عَذَابَ ٱلنَّارِ ١٤

15. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እነዚያን የካዱትን ሰዎች (ለጦር) ሲጓዙ ባገኛችኋቸው ጊዜ ጀርባዎችን አታዙሩላቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا لَقِيتُمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ زَحۡفٗا فَلَا تُوَلُّوهُمُ ٱلۡأَدۡبَارَ ١٥

16. ያን ጊዜም ለግድያ ለመዘዋወር ወይም ወደ ሠራዊት ለመቀላቀል ሳይኾን ጀርባውን የሚያዞርላቸው ሰው ከአላህ በኾነ ቁጣ በእርግጥ ተመለሰ፡፡ መኖሪያውም ገሀነም ናት፡፡ መመለሻይቱም ከፋች፡፡

وَمَن يُوَلِّهِمۡ يَوۡمَئِذٖ دُبُرَهُۥٓ إِلَّا مُتَحَرِّفٗا لِّقِتَالٍ أَوۡ مُتَحَيِّزًا إِلَىٰ فِئَةٖ فَقَدۡ بَآءَ بِغَضَبٖ مِّنَ ٱللَّهِ وَمَأۡوَىٰهُ جَهَنَّمُۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ١٦

17. አልገደላችኋቸውም ግን አላህ ገደላቸው፡፡ (ጭብጥን ዐፈር) በወረወርክም ጊዜ አንተ አልወረወርክም፡፡ ግን አላህ ወረወረ (ወደ ዓይኖቻቸው አደረሰው)፡፡ ለአማኞችም ከርሱ የኾነን መልካም ጸጋ ለመስጠት (ይህን አደረገ)፡፡ አላህ ሰሚ ዐዋቂ ነውና፡፡

فَلَمۡ تَقۡتُلُوهُمۡ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ قَتَلَهُمۡۚ وَمَا رَمَيۡتَ إِذۡ رَمَيۡتَ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ رَمَىٰ وَلِيُبۡلِيَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ مِنۡهُ بَلَآءً حَسَنًاۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ١٧

18. ይህ (ዕውነት ነው)፡፡ አላህም የከሓዲዎችን ተንኮል አድካሚ ነው፡፡

ذَٰلِكُمۡ وَأَنَّ ٱللَّهَ مُوهِنُ كَيۡدِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ١٨

19. ፍትሕን (ፍርድን) ብትጠይቁ ፍትሑ በእርግጥ መጥቶላችኋል፡፡ (ከህደትንና መዋጋትን) ብትከለከሉም እርሱ ለእናንተ የተሻለ ነው፡፡ (ወደ መጋደል) ብትመለሱም እንመለሳለን፡፡ ሰራዊታችሁም ብትበዛም እንኳ ከናንተ ምንም አትጠቅማችሁም፡፡ አላህም ከምእምናን ጋር ነው፡፡

إِن تَسۡتَفۡتِحُواْ فَقَدۡ جَآءَكُمُ ٱلۡفَتۡحُۖ وَإِن تَنتَهُواْ فَهُوَ خَيۡرٞ لَّكُمۡۖ وَإِن تَعُودُواْ نَعُدۡ وَلَن تُغۡنِيَ عَنكُمۡ فِئَتُكُمۡ شَيۡـٔٗا وَلَوۡ كَثُرَتۡ وَأَنَّ ٱللَّهَ مَعَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٩

20. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህንና መልክተኛውን ታዘዙ፡፡ እናንተም የምትሰሙ ስትኾኑ ከርሱ አትሽሹ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَلَا تَوَلَّوۡاْ عَنۡهُ وَأَنتُمۡ تَسۡمَعُونَ ٢٠

21. እንደነዚያም እነሱ የማይሰሙ ሲኾኑ ሰማን እንዳሉት አትሁኑ፡፡

وَلَا تَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ قَالُواْ سَمِعۡنَا وَهُمۡ لَا يَسۡمَعُونَ ٢١

22. ከተንቀሳቃሾች ሁሉ አላህ ዘንድ መጥፎ ተንኮለኞች እነዚያ የማያውቁት፣ ደንቆሮዎቹ፣ ዲዳዎቹ ናቸው፡፡

۞إِنَّ شَرَّ ٱلدَّوَآبِّ عِندَ ٱللَّهِ ٱلصُّمُّ ٱلۡبُكۡمُ ٱلَّذِينَ لَا يَعۡقِلُونَ ٢٢

23. በውስጣቸውም ደግ መኖሩን አላህ ባወቀ ኖሮ (የመረዳትን መስማት) ባሰማቸው ነበር፡፡ (ደግ የሌለባቸው መኾኑን ሲያውቅ) ባሰማቸውም ኖሮ እነሱ እውነትን የተው ኾነው በሸሹ ነበር፡፡

وَلَوۡ عَلِمَ ٱللَّهُ فِيهِمۡ خَيۡرٗا لَّأَسۡمَعَهُمۡۖ وَلَوۡ أَسۡمَعَهُمۡ لَتَوَلَّواْ وَّهُم مُّعۡرِضُونَ ٢٣

24. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! (መልክተኛው) ሕያው ወደሚያደርጋችሁ እምነት በጠራችሁ ጊዜ ለአላህና ለመልክተኛው ታዘዙ፡፡ አላህም በሰውየውና በልቡ መካከል የሚጋርድ መኾኑን ወደርሱም የምትሰበሰቡ መኾናችሁን እወቁ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱسۡتَجِيبُواْ لِلَّهِ وَلِلرَّسُولِ إِذَا دَعَاكُمۡ لِمَا يُحۡيِيكُمۡۖ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ يَحُولُ بَيۡنَ ٱلۡمَرۡءِ وَقَلۡبِهِۦ وَأَنَّهُۥٓ إِلَيۡهِ تُحۡشَرُونَ ٢٤

25. ከናንተም ውስጥ እነዚያን የበደሉትን ብቻ ለይታ የማትነካን ፈተና ተጠንቀቁ፡፡ አላህም ቅጣቱ ብርቱ መኾኑን እወቁ፡፡

وَٱتَّقُواْ فِتۡنَةٗ لَّا تُصِيبَنَّ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنكُمۡ خَآصَّةٗۖ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٢٥

26. እናንተም በምድር ላይ የተናቃችሁ ጥቂቶች ኾናችሁ ሳላችሁ ሰዎች ሊነጥቁዋችሁ የምትፈሩ ስትኾኑ ያስጠጋችሁን በእርዳታውም ያበረታችሁን ከመልካሞች ሲሳዮችም ታመሰግኑ ዘንድ የሰጣችሁን አስታውሱ፡፡

وَٱذۡكُرُوٓاْ إِذۡ أَنتُمۡ قَلِيلٞ مُّسۡتَضۡعَفُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ تَخَافُونَ أَن يَتَخَطَّفَكُمُ ٱلنَّاسُ فَـَٔاوَىٰكُمۡ وَأَيَّدَكُم بِنَصۡرِهِۦ وَرَزَقَكُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ لَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ٢٦

27. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህንና መልክተኛውን አትክዱ፡፡ አደራዎቻችሁንም እናንተ እያወቃችሁ አትክዱ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَخُونُواْ ٱللَّهَ وَٱلرَّسُولَ وَتَخُونُوٓاْ أَمَٰنَٰتِكُمۡ وَأَنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٢٧

28. ገንዘቦቻችሁና ልጆቻችሁም ፈተና ብቻ መኾናቸውንና አላህም እሱ ዘንድ ታላቅ ምንዳ ያለው መኾኑን እወቁ፡፡

وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّمَآ أَمۡوَٰلُكُمۡ وَأَوۡلَٰدُكُمۡ فِتۡنَةٞ وَأَنَّ ٱللَّهَ عِندَهُۥٓ أَجۡرٌ عَظِيمٞ ٢٨

29. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ብትፈሩ የእውነት መለያን ብርሃን ያደርግላችኋል፡፡ ክፉ ሥራዎቻችሁንም ከእናንተ ላይ ያብስላችኋል፡፡ ለእናንተም ይምራችኋል፡፡ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِن تَتَّقُواْ ٱللَّهَ يَجۡعَل لَّكُمۡ فُرۡقَانٗا وَيُكَفِّرۡ عَنكُمۡ سَيِّـَٔاتِكُمۡ وَيَغۡفِرۡ لَكُمۡۗ وَٱللَّهُ ذُو ٱلۡفَضۡلِ ٱلۡعَظِيمِ ٢٩

30. እነዚያም የካዱት ሊያስሩህ ወይም ሊገድሉህ ወይም (ከመካ) ሊያወጡህ ባንተ ላይ በመከሩብህ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ይመክራሉም አላህም ተንኮላቸውን ይመልስባቸዋል፡፡ አላህም ከመካሪዎቹ ሁሉ በላይ ነው፡፡

وَإِذۡ يَمۡكُرُ بِكَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لِيُثۡبِتُوكَ أَوۡ يَقۡتُلُوكَ أَوۡ يُخۡرِجُوكَۚ وَيَمۡكُرُونَ وَيَمۡكُرُ ٱللَّهُۖ وَٱللَّهُ خَيۡرُ ٱلۡمَٰكِرِينَ ٣٠

31. አንቀጾቻችንም በነሱ ላይ በተነበቡ ጊዜ «በእርግጥ ሰምተናል፤ በሻን ኖሮ የዚህን ብጤ ባልን ነበር፤ ይህ የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ጽሑፍ ተረቶች እንጂ ሌላ አይደለም» ይላሉ፡፡

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُنَا قَالُواْ قَدۡ سَمِعۡنَا لَوۡ نَشَآءُ لَقُلۡنَا مِثۡلَ هَٰذَآ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّآ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٣١

32. «ጌታችን ሆይ! ይህ እርሱ ካንተ ዘንድ (የተወረደ) እውነት እንደ ኾነ በኛ ላይ ከሰማይ ድንጋዮችን አዝንብብን ወይም አሳማሚ ቅጣትን አምጣብን» ባሉም ጊዜ (አስታውስ)

وَإِذۡ قَالُواْ ٱللَّهُمَّ إِن كَانَ هَٰذَا هُوَ ٱلۡحَقَّ مِنۡ عِندِكَ فَأَمۡطِرۡ عَلَيۡنَا حِجَارَةٗ مِّنَ ٱلسَّمَآءِ أَوِ ٱئۡتِنَا بِعَذَابٍ أَلِيمٖ ٣٢

33. አላህም አንተ በውስጣቸው እያለህ (ድንጋይ በማዝነብና ባሳማሚ ቅጣት) የሚቀጣቸው አይደለም፡፡ አላህም እነሱ ምህረትን የሚለምኑ ሲኾኑ የሚቀጣቸው አይደለም፡፡

وَمَا كَانَ ٱللَّهُ لِيُعَذِّبَهُمۡ وَأَنتَ فِيهِمۡۚ وَمَا كَانَ ٱللَّهُ مُعَذِّبَهُمۡ وَهُمۡ يَسۡتَغۡفِرُونَ ٣٣

34. እነሱ ከተከበረው መስጊድ የሚከለክሉ ሲኾኑም አላህ (በሰይፍ) የማይቀጣቸው ለነሱ ምን አልላቸው (የቤቱ) ጠባቂዎችም አልነበሩም፡፡ ጠባቂዎቹ (ከሕደትን) ተጠንቃቂዎቹ እንጂ ሌሎቹ አይደሉም፡፡ ግን አብዛኞዎቻቸው አያውቁም፡፡

وَمَا لَهُمۡ أَلَّا يُعَذِّبَهُمُ ٱللَّهُ وَهُمۡ يَصُدُّونَ عَنِ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِ وَمَا كَانُوٓاْ أَوۡلِيَآءَهُۥٓۚ إِنۡ أَوۡلِيَآؤُهُۥٓ إِلَّا ٱلۡمُتَّقُونَ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٣٤

35. በቤቱ ዘንድም (በካዕባ) ስግደታቸው ማፏጨትና ማጨብጨብ እንጂ ሌላ አልነበረም፡፡ ትክዱት በነበራችሁትም ነገር ቅጣትን ቅመሱ (ይባላሉ)፡፡

وَمَا كَانَ صَلَاتُهُمۡ عِندَ ٱلۡبَيۡتِ إِلَّا مُكَآءٗ وَتَصۡدِيَةٗۚ فَذُوقُواْ ٱلۡعَذَابَ بِمَا كُنتُمۡ تَكۡفُرُونَ ٣٥

36. እነዚያ የካዱት ከአላህ መንገድ ሊከለክሉ ገንዘቦቻቸውን ያወጣሉ፡፡ በእርግጥም ያወጡዋታል፡፡ ከዚያም በእነሱ ላይ ጸጸት ትኾንባቸዋለች፡፡ ከዚያም ይሸነፋሉ፡፡ እነዚያም የካዱት ወደ ገሀነም ይሰበሰባሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يُنفِقُونَ أَمۡوَٰلَهُمۡ لِيَصُدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِۚ فَسَيُنفِقُونَهَا ثُمَّ تَكُونُ عَلَيۡهِمۡ حَسۡرَةٗ ثُمَّ يُغۡلَبُونَۗ وَٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِلَىٰ جَهَنَّمَ يُحۡشَرُونَ ٣٦

37. አላህ መጥፎውን ከመልካሙ ሊለይ መጥፎውንም ከፊሉን በከፊሉ ላይ ሊያደርግና ባንድ ላይ ሊያነባብረው በገሀነም ውስጥም ሊያደርገው (ይሰበስባሉ)፡፡ እነዚያ እነሱ ከሳሪዎቹ ናቸው፡፡

لِيَمِيزَ ٱللَّهُ ٱلۡخَبِيثَ مِنَ ٱلطَّيِّبِ وَيَجۡعَلَ ٱلۡخَبِيثَ بَعۡضَهُۥ عَلَىٰ بَعۡضٖ فَيَرۡكُمَهُۥ جَمِيعٗا فَيَجۡعَلَهُۥ فِي جَهَنَّمَۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ٣٧

38. ለነዚያ ለካዱት በላቸው:- ቢከለከሉ ለእነሱ በእርግጥ ያለፈውን (ሥራ) ምሕረት ይደረግላቸዋል፡፡ (ወደ መጋደል) ቢመለሱም (እናጠፋቸዋለን)፡፡ የቀድሞዎቹ ሕዝቦች ልማድ በእርግጥ አልፋለችና፡፡

قُل لِّلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِن يَنتَهُواْ يُغْفَرْ لَهُم مَّا قَدْ سَلَفَ وَإِن يَعُودُواْ فَقَدْ مَضَتْ سُنَّتُ ٱلْأَوَّلِينَ ﴿٣٨﴾

39. ሁከትም እስከማትገኝ ሃይማኖትም ሁሉ ለአላህ ብቻ እስከሚኾን ድረስ ተጋደሏቸው፡፡ ቢከለከሉም አላህ የሚሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

وَقَٰتِلُوهُمْ حَتَّىٰ لَا تَكُونَ فِتْنَةٌ وَيَكُونَ ٱلدِّينُ كُلُّهُۥ لِلَّهِ ۚ فَإِنِ ٱنتَهَوْاْ فَإِنَّ ٱللَّهَ بِمَا يَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ﴿٣٩﴾

40. (ከእምነት) ቢዞሩም አላህ ረዳታችሁ መኾኑን ዕወቁ፡፡ (እርሱ) ምን ያምር ጠባቂ! ምን ያምርም ረዳት!

وَإِن تَوَلَّوْاْ فَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ مَوْلَىٰكُمْ ۚ نِعْمَ ٱلْمَوْلَىٰ وَنِعْمَ ٱلنَّصِيرُ ﴿٤٠﴾

41. ከማንኛውም ነገር በጦር (ከከሓዲዎች) የዘረፋችሁትም አንድ አምስተኛው ለአላህና ለመልክተኛው፣ (ለነቢዩ) የዝምድና ባለቤቶችም፣ ለየቲሞችም፣ ለምስኪኖችም፣ ለመንገደኛም የተገባ መኾኑን ዕውቁ፣ በአላህና በዚያም እውነትና ውሸት በተለየበት ቀን ሁለቱ ጭፍሮች በተገናኙበት (በበድር) ቀን በባሪያችን ላይ ባወረድነው የምታምኑ እንደኾናችሁ (ይህንን ዕወቁ)፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

۞ وَٱعْلَمُوٓاْ أَنَّمَا غَنِمْتُم مِّن شَىْءٍ فَأَنَّ لِلَّهِ خُمُسَهُۥ وَلِلرَّسُولِ وَلِذِى ٱلْقُرْبَىٰ وَٱلْيَتَٰمَىٰ وَٱلْمَسَٰكِينِ وَٱبْنِ ٱلسَّبِيلِ إِن كُنتُمْ ءَامَنتُم بِٱللَّهِ وَمَآ أَنزَلْنَا عَلَىٰ عَبْدِنَا يَوْمَ ٱلْفُرْقَانِ يَوْمَ ٱلْتَقَى ٱلْجَمْعَانِ ۗ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٤١﴾

42. እናንተ በቅርቢቱ ዳርቻ ኾናችሁ እነርሱም በሩቂቱ ዳርቻ ኾነው የነጋዴዎቹም ጭፍራ ከናንተ በታች ሲኾኑ በሰፈራችሁ ጊዜ (ያደረግንላችሁን አስታውሱ)፡፡ በተቃጠራችሁም ኖሮ በቀጠሮው በተለያያችሁ ነበር፡፡ ግን አላህ ሊሠራው የሚገባውን ነገር ሊፈጽም የሚጠፋ ሰው ከአስረጅ በኋላ እንዲጠፋ ሕያው የሚኾንም ሰው ከአስረጅ በኋላ ሕያው እንዲኾን (ያለቀጠሮ አጋጠማችሁ)፡፡ አላህም በእርግጥ ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

إِذْ أَنتُم بِٱلْعُدْوَةِ ٱلدُّنْيَا وَهُم بِٱلْعُدْوَةِ ٱلْقُصْوَىٰ وَٱلرَّكْبُ أَسْفَلَ مِنكُمْ ۚ وَلَوْ تَوَاعَدتُّمْ لَٱخْتَلَفْتُمْ فِى ٱلْمِيعَٰدِ ۙ وَلَٰكِن لِّيَقْضِىَ ٱللَّهُ أَمْرًا كَانَ مَفْعُولًا لِّيَهْلِكَ مَنْ هَلَكَ عَنۢ بَيِّنَةٍ وَيَحْيَىٰ مَنْ حَىَّ عَنۢ بَيِّنَةٍ ۗ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَسَمِيعٌ عَلِيمٌ ﴿٤٢﴾

43. አላህ በሕልምህ እነሱን ጥቂት አድርጎ ባሳየህ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ እነሱን ብዙ አድርጎ ባሳየህም ኖሮ በፈራችሁና በነገሩ በተጨቃጨቃችሁ ነበር፡፡ ግን አላህ አዳናችሁ፡፡ እርሱ በደረቶች ውስጥ ያለን ሁሉ ዐዋቂ ነውና፡፡

إِذْ يُرِيكَهُمُ ٱللَّهُ فِى مَنَامِكَ قَلِيلًا ۖ وَلَوْ أَرَىٰكَهُمْ كَثِيرًا لَّفَشِلْتُمْ وَلَتَنَٰزَعْتُمْ فِى ٱلْأَمْرِ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ سَلَّمَ ۗ إِنَّهُۥ عَلِيمٌۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ﴿٤٣﴾

44. አላህም ሊሠራው የሚገባን ነገር ይፈጽም ዘንድ በተጋጠማችሁ ጊዜ እነርሱን በዓይኖቻችሁ ጥቂት አድርጎ ያሳያችሁንና በዓይኖቻቸውም ላይ ያሳነሳችሁን (አስታውሱ)፡፡ ነገሮቹም ሁሉ ወደ አላህ ብቻ ይመለሳሉ፡፡

وَإِذْ يُرِيكُمُوهُمْ إِذِ ٱلْتَقَيْتُمْ فِىٓ أَعْيُنِكُمْ قَلِيلًا وَيُقَلِّلُكُمْ فِىٓ أَعْيُنِهِمْ لِيَقْضِىَ ٱللَّهُ أَمْرًا كَانَ مَفْعُولًا ۗ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرْجَعُ ٱلْأُمُورُ ﴿٤٤﴾

45. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ሰራዊትን በገጠማችሁ ጊዜ እርጉ፤ (መክቱ)፡፡ አላህንም በብዙ አውሱ፤ በእርግጥ ትድናላችሁና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا لَقِيتُمْ فِئَةً فَٱثْبُتُواْ وَٱذْكُرُواْ ٱللَّهَ كَثِيرًا لَّعَلَّكُمْ تُفْلِحُونَ ﴿٤٥﴾

46. አላህንና መልክተኛውንም ታዘዙ:: አትጨቃጨቁም:: ትፈራላችሁና ኃይላችሁም ትኼዳለችና:: ታገሱም፤ አላህ ከትዕግስተኞች ጋር ነውና::

وَأَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَلَا تَنَٰزَعُواْ فَتَفۡشَلُواْ وَتَذۡهَبَ رِيحُكُمۡۖ وَٱصۡبِرُوٓاْۚ إِنَّ ٱللَّهَ مَعَ ٱلصَّٰبِرِينَ ﴿٤٦﴾

47. እንደነዚያ ለትዕቢትና ለሰዎች ይዩልኝ ሲሉ ከአላህም መንገድ ለማገድ ከአገራቸው እንደወጡት አትኹኑ:: አላህም በሚሠሩት ሁሉ (በዕውቀቱ) ከባቢ ነው::

وَلَا تَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ خَرَجُواْ مِن دِيَٰرِهِم بَطَرٗا وَرِئَآءَ ٱلنَّاسِ وَيَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِۚ وَٱللَّهُ بِمَا يَعۡمَلُونَ مُحِيطٞ ﴿٤٧﴾

48. ሰይጣንም ሥራዎቻቸውን ለእነርሱ ባሳመረላቸውና «ዛሬ ለእናንተ ከሰዎች አሸናፊ የላችሁም እኔም ለእናንተ ረዳት ነኝ» ባለ ጊዜም (አስታውስ):: ሁለቱ ጭፍሮችም በተያዩ ጊዜ፤ ወደኋላው አፈገፈገ:: «እኔ ከናንተ ንጹህ ነኝ:: እኔ እናንተ የማታዩትን አያለሁ:: እኔ አላህን እፈራለሁ:: አላህም ቅጣተ ብርቱ ነው» አላቸውም::

وَإِذۡ زَيَّنَ لَهُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ أَعۡمَٰلَهُمۡ وَقَالَ لَا غَالِبَ لَكُمُ ٱلۡيَوۡمَ مِنَ ٱلنَّاسِ وَإِنِّي جَارٞ لَّكُمۡۖ فَلَمَّا تَرَآءَتِ ٱلۡفِئَتَانِ نَكَصَ عَلَىٰ عَقِبَيۡهِ وَقَالَ إِنِّي بَرِيٓءٞ مِّنكُمۡ إِنِّيٓ أَرَىٰ مَا لَا تَرَوۡنَ إِنِّيٓ أَخَافُ ٱللَّهَۚ وَٱللَّهُ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ﴿٤٨﴾

49. መናፍቃንና እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ በሽታ ያለባቸው «እነዚህን (ሙስሊሞች) ሃይማኖታቸው አታለላቸው» ባሉ ጊዜ (አስታውስ):: በአላህም ላይ የሚጠጋ (ያሸንፋል)፤ አላህ አሸናፊ ጥበበኛ ነውና::

إِذۡ يَقُولُ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ وَٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٌ غَرَّ هَٰٓؤُلَآءِ دِينُهُمۡۗ وَمَن يَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِ فَإِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ﴿٤٩﴾

50. እነዚያንም የካዱትን መላእክት ፊቶቻቸውንና ጀርባዎቻቸውን እየመቱ «የቃጠሎንም ስቃይ ቅመሱ» (እያሉ) በሚገድሏቸው ጊዜ ብታይ ኖሮ (አስደንጋጭን ነገር ታይ ነበር)::

وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذۡ يَتَوَفَّى ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَضۡرِبُونَ وُجُوهَهُمۡ وَأَدۡبَٰرَهُمۡ وَذُوقُواْ عَذَابَ ٱلۡحَرِيقِ ﴿٥٠﴾

51. ይህ እጆቻችሁ ባስቀደሙት ምክንያት አላህም ለባሮቹ በዳይ ባለመኾኑ ነው (ይባላሉ)::

ذَٰلِكَ بِمَا قَدَّمَتۡ أَيۡدِيكُمۡ وَأَنَّ ٱللَّهَ لَيۡسَ بِظَلَّٰمٖ لِّلۡعَبِيدِ ﴿٥١﴾

52. (የነዚያ ልማድ) እንደ ፈርዖን ቤተሰብና እንደነዚያም ከእነሱ በፊት እንደ ነበሩት ልማድ ነው:: በአላህ አንቀጾች ካዱ፤ አላህም በኃጢአቶቻቸው ያዛቸው፤ አላህ ኀይለኛ ቅጣተ ብርቱ ነውና::

كَدَأۡبِ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ وَٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ فَأَخَذَهُمُ ٱللَّهُ بِذُنُوبِهِمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ قَوِيّٞ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ﴿٥٢﴾

53. ይህ (ቅጣት) አላህ በሕዝቦች ላይ የለገሰውን ጸጋ በነፍሶቻቸው ያለውን ነገር እስከሚለውጡ ድረስ የማይለውጥ በመኾኑ ምክንያት ነው:: አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው::

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ لَمۡ يَكُ مُغَيِّرٗا نِّعۡمَةً أَنۡعَمَهَا عَلَىٰ قَوۡمٍ حَتَّىٰ يُغَيِّرُواْ مَا بِأَنفُسِهِمۡ وَأَنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ﴿٥٣﴾

54. እንደ ፈርዖን ቤተሰቦችና እንደእነዚያም ከእነሱ በፊት እንደ ነበሩት ልማድ (እስከሚለውጡ ድረስ አይለውጥባቸውም):: በጌታቸው ተአምራት አስተባበሉና በኃጢአቶቻቸው አጠፋናቸው:: የፈርዖንንም ቤተሰቦች አሰጠምናቸው:: ሁሉም በዳዮች ነበሩም::

كَدَأۡبِ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ وَٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمۡ فَأَهۡلَكۡنَٰهُم بِذُنُوبِهِمۡ وَأَغۡرَقۡنَآ ءَالَ فِرۡعَوۡنَۚ وَكُلّٞ كَانُواْ ظَٰلِمِينَ ﴿٥٤﴾

55. ከሚንቀሳቀሱ እንስሳዎች ሁሉ አላህ ዘንድ ይበልጥ ክፉዎቹ እነዚያ ዘወትር የካዱት ናቸው፡፡ ስለዚህ እነሱ አያምኑም፡፡

إِنَّ شَرَّ ٱلدَّوَآبِّ عِندَ ٱللَّهِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ٥٥

56. እነዚያ ከነሱ ቃል ኪዳን የያዝክባቸው ከዚያም በየጊዜው ቃል ኪዳናቸውን የሚያፈርሱ ናቸው፡፡ እነሱም አይጠነቀቁም፡፡

ٱلَّذِينَ عَٰهَدتَّ مِنۡهُمۡ ثُمَّ يَنقُضُونَ عَهۡدَهُمۡ فِي كُلِّ مَرَّةٖ وَهُمۡ لَا يَتَّقُونَ ٥٦

57. በጦርም ላይ ብታገኛቸው በእነርሱ ቅጣት ምክንያት (ሌሎቹ ከሓዲዎች) ይገሰጹ ዘንድ ከኋላቸው ያሉትን በትንባቸው፡፡

فَإِمَّا تَثۡقَفَنَّهُمۡ فِي ٱلۡحَرۡبِ فَشَرِّدۡ بِهِم مَّنۡ خَلۡفَهُمۡ لَعَلَّهُمۡ يَذَّكَّرُونَ ٥٧

58. ከሕዝቦችም ከዳትን ብትፈራ (የኪዳኑን መፍረስ በማወቅ) በመተካከል ላይ ኾናችሁ ኪዳናቸውን ወደነሱ ጣልላቸው፡፡ አላህ ከዳተኞችን አይወድምና፡፡

وَإِمَّا تَخَافَنَّ مِن قَوۡمٍ خِيَانَةٗ فَٱنۢبِذۡ إِلَيۡهِمۡ عَلَىٰ سَوَآءٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلۡخَآئِنِينَ ٥٨

59. እነዚያም የካዱት ከአላህ ቅጣት ያመለጡ መኾናቸውን አያስቡ፡፡ እነሱ አያቅቱምና፡፡

وَلَا يَحۡسَبَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ سَبَقُوٓاْۚ إِنَّهُمۡ لَا يُعۡجِزُونَ ٥٩

60. ለእነሱም ከማንኛውም ኃይልና ከታጀቡ ፈረሶችም የቻላችሁትን ሁሉ በእርሱ የአላህን ጠላትና ጠላታችሁን ሌሎችንም ከእነርሱ በቀር ያሉትን የማታውቋቸውን አላህ የሚያውቃቸውን (መናፍቃን) የምታሸብሩበት ስትኾኑ አዘጋጁላቸው፡፡ ከማንኛውም ነገር በአላህ መንገድ የምትለግሱትም ምንዳው ወደናንተ በሙሉ ይሰጣል፡፡ እናንተም አትበደሉም፡፡

وَأَعِدُّواْ لَهُم مَّا ٱسۡتَطَعۡتُم مِّن قُوَّةٖ وَمِن رِّبَاطِ ٱلۡخَيۡلِ تُرۡهِبُونَ بِهِۦ عَدُوَّ ٱللَّهِ وَعَدُوَّكُمۡ وَءَاخَرِينَ مِن دُونِهِمۡ لَا تَعۡلَمُونَهُمُ ٱللَّهُ يَعۡلَمُهُمۡۚ وَمَا تُنفِقُواْ مِن شَيۡءٖ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ يُوَفَّ إِلَيۡكُمۡ وَأَنتُمۡ لَا تُظۡلَمُونَ ٦٠

61. ወደ ዕርቅም ቢያዘነብሉ ወደ እርሷ አዘንብል፡፡ በአላህም ላይ ተጠጋ፡፡ እነሆ እርሱ ሰሚ ዐዋቂ ነውና፡፡

۞وَإِن جَنَحُواْ لِلسَّلۡمِ فَٱجۡنَحۡ لَهَا وَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٦١

62. ሊያታልሉህም ቢፈልጉ አላህ በቂህ ነው፡፡ እርሱ ያ በእርዳታውና በምእምናን ያበረታህ ነው፡፡

وَإِن يُرِيدُوٓاْ أَن يَخۡدَعُوكَ فَإِنَّ حَسۡبَكَ ٱللَّهُۚ هُوَ ٱلَّذِيٓ أَيَّدَكَ بِنَصۡرِهِۦ وَبِٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٦٢

63. በልቦቻቸውም መካከል ያስማማ ነው፡፡ በምድር ያለውን ሁሉ (ሀብት) በለገስክ ኖሮ በልቦቻቸው መካከል ባላስማማህ ነበር፡፡ ግን አላህ በመካከላቸው አስማማ፡፡ እርሱ አሸናፊ ጥበበኛ ነውና፡፡

وَأَلَّفَ بَيۡنَ قُلُوبِهِمۡۚ لَوۡ أَنفَقۡتَ مَا فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا مَّآ أَلَّفۡتَ بَيۡنَ قُلُوبِهِمۡ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ أَلَّفَ بَيۡنَهُمۡۚ إِنَّهُۥ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٦٣

64. አንተ ነቢዩ ሆይ! አላህ በቂህ ነው፡፡ ለተከተሉህም ምእምናን (አላህ በቂያቸው ነው)፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ حَسۡبُكَ ٱللَّهُ وَمَنِ ٱتَّبَعَكَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٦٤

65. አንተ ነቢዩ ሆይ! ምእምናንን በመዋጋት ላይ አደፋፍራቸው፡፡ ከእናንተ ውስጥ ሃያ ታጋሾች ኖሩ ሁለት መቶን ያሸንፋሉ፡፡ ከእናንተም መቶ ቢኖሩ ከእነዚያ ከካዱት እነሱ የማያውቁ ሕዝቦች ስለኾኑ ሺህን ያሸንፋሉ፤

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ حَرِّضِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ عَلَى ٱلۡقِتَالِۚ إِن يَكُن مِّنكُمۡ عِشۡرُونَ صَٰبِرُونَ يَغۡلِبُواْ مِاْئَتَيۡنِۚ وَإِن يَكُن مِّنكُم مِّاْئَةٞ يَغۡلِبُوٓاْ أَلۡفٗا مِّنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِأَنَّهُمۡ قَوۡمٞ لَّا يَفۡقَهُونَ ٦٥

66. አሁን አላህ ከእናንተ ላይ አቀለለላችሁ፡፡ በእናንተ ውስጥም ድክመት መኖሩን ዐወቀ፡፡ ስለዚህ ከእናንተ መቶ ታጋሾች ቢኖሩ ሁለት መቶን ያሸንፋሉ፡፡ ከእናንተም ሺህ ቢኖሩ በአላህ ፈቃድ ሁለት ሺህን ያሸንፋሉ፡፡ አላህም ከታጋሾቹ ጋር ነው፡፡

ٱلۡـَٰٔنَ خَفَّفَ ٱللَّهُ عَنكُمۡ وَعَلِمَ أَنَّ فِيكُمۡ ضَعۡفٗاۚ فَإِن يَكُن مِّنكُم مِّاْئَةٞ صَابِرَةٞ يَغۡلِبُواْ مِاْئَتَيۡنِۚ وَإِن يَكُن مِّنكُمۡ أَلۡفٞ يَغۡلِبُوٓاْ أَلۡفَيۡنِ بِإِذۡنِ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ مَعَ ٱلصَّٰبِرِينَ ٦٦

67. ለነቢይ በምድር ላይ እስቲያደክም ድረስ ለእርሱ ምርኮኞች ሊኖሩት አይገባም፡፡ የቅርቢቱን ዓለም ጠፊ ጥቅም ትፈልጋላችሁ፡፡ አላህም መጨረሻይቱን ይሻል፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

مَا كَانَ لِنَبِيٍّ أَن يَكُونَ لَهُۥٓ أَسۡرَىٰ حَتَّىٰ يُثۡخِنَ فِي ٱلۡأَرۡضِۚ تُرِيدُونَ عَرَضَ ٱلدُّنۡيَا وَٱللَّهُ يُرِيدُ ٱلۡأٓخِرَةَۗ وَٱللَّهُ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ٦٧

68. ከአላህ ያለፈ ፍርድ ባልነበረ ኖሮ በወሰዳችሁት (ቤዛ) ከባድ ቅጣት በነካችሁ ነበር፡፡

لَّوۡلَا كِتَٰبٞ مِّنَ ٱللَّهِ سَبَقَ لَمَسَّكُمۡ فِيمَآ أَخَذۡتُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٞ ٦٨

69. (ከጠላት) ከዘረፋችሁትም (ሀብት) የተፈቀደ መልካም ሲኾን ብሉ፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

فَكُلُواْ مِمَّا غَنِمۡتُمۡ حَلَٰلٗا طَيِّبٗاۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٦٩

70. አንተ ነቢዩ ሆይ! ከምርኮኞች በእጆቻችሁ ላሉት በላቸው፡- «አላህ በልቦቻችሁ ውስጥ በጎን ነገር (እምነትን) ቢያውቅ ከእናንተ ከተወሰደባችሁ የተሻለን ይሰጣችኋል፡፡ ለእናንተም ይምራችኋል፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡»

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ قُل لِّمَن فِيٓ أَيۡدِيكُم مِّنَ ٱلۡأَسۡرَىٰٓ إِن يَعۡلَمِ ٱللَّهُ فِي قُلُوبِكُمۡ خَيۡرٗا يُؤۡتِكُمۡ خَيۡرٗا مِّمَّآ أُخِذَ مِنكُمۡ وَيَغۡفِرۡ لَكُمۡۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٧٠

71. ሊከዱህም ቢፈልጉ ከዚህ በፊት አላህን በእርግጥ ከድተዋል፡፡ ከነሱም አስመችቶሃል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَإِن يُرِيدُواْ خِيَانَتَكَ فَقَدۡ خَانُواْ ٱللَّهَ مِن قَبۡلُ فَأَمۡكَنَ مِنۡهُمۡۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ٧١

72. እነዚያ ያመኑና የተሰደዱ። በአላህም መንገድ ላይ በገንዘቦቻቸውና በነፍሶቻቸው የታገሉ። እነዚያም (ስደተኞቹን) ያስጠጉና የረዱ። እነዚያ ከፊሎቻቸው ለከፊሉ ረዳቶች ናቸው። እነዚያም ያመኑና ያልተሰደዱ እስከሚሰደዱ ድረስ ከነሱ ምንም ዝምድና የላችሁም። በሃይማኖትም እርዳታን ቢፈልጉባችሁ በእናንተና በነሱ መካከል ቃል ኪዳን ባላችሁ ሕዝቦች ላይ ካልኾነ በስተቀር በናንተ ላይ መርዳት አለባችሁ። አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው።

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَهَاجَرُواْ وَجَٰهَدُواْ بِأَمۡوَٰلِهِمۡ وَأَنفُسِهِمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَٱلَّذِينَ ءَاوَواْ وَّنَصَرُوٓاْ أُوْلَٰٓئِكَ بَعۡضُهُمۡ أَوۡلِيَآءُ بَعۡضٖۚ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَلَمۡ يُهَاجِرُواْ مَا لَكُم مِّن وَلَٰيَتِهِم مِّن شَيۡءٍ حَتَّىٰ يُهَاجِرُواْۚ وَإِنِ ٱسۡتَنصَرُوكُمۡ فِي ٱلدِّينِ فَعَلَيۡكُمُ ٱلنَّصۡرُ إِلَّا عَلَىٰ قَوۡمِۭ بَيۡنَكُمۡ وَبَيۡنَهُم مِّيثَٰقٞۗ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ٧٢

73. እነዚያም የካዱት ከፊሎቻቸው ለከፊሉ ረዳቶች ናቸው። (ከምእምናን መረዳዳትን ከከሓዲያን መቆራረጥን) ባትሠሩት በምድር ላይ ሁከትና ታላቅ ጥፋት ይኾናል።

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بَعۡضُهُمۡ أَوۡلِيَآءُ بَعۡضٍۚ إِلَّا تَفۡعَلُوهُ تَكُن فِتۡنَةٞ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَفَسَادٞ كَبِيرٞ ٧٣

74. እነዚያም ያመኑና የተሰደዱ በአላህም መንገድ ላይ የታገሉ፣ እነዚያም ያስጠጉና የረዱ እነዚያ እነሱ በእውነት አማኞች ናቸው። ለእነሱም ምሕረትና የከበረ ሲሳይ አላቸው።

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَهَاجَرُواْ وَجَٰهَدُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَٱلَّذِينَ ءَاوَواْ وَّنَصَرُوٓاْ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ حَقّٗاۚ لَّهُم مَّغۡفِرَةٞ وَرِزۡقٞ كَرِيمٞ ٧٤

75. እነዚያም በኋላ ያመኑና የተሰደዱ፣ ከእናንተም ጋር ኾነው የታገሉ እነዚያ ከናንተው ናቸው። የዝምድናዎች ባለቤቶችም በአላህ መጽሐፍ ከፊሎቻቸው በከፊሉ (መውረስ) የተገቡ ናቸው። አላህ በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው።

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مِنۢ بَعۡدُ وَهَاجَرُواْ وَجَٰهَدُواْ مَعَكُمۡ فَأُوْلَٰٓئِكَ مِنكُمۡۚ وَأُوْلُواْ ٱلۡأَرۡحَامِ بَعۡضُهُمۡ أَوۡلَىٰ بِبَعۡضٖ فِي كِتَٰبِ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمُۢ ٧٥

# ሱረቱ አል-ተውባህ

# سورة التوبة

1. (ይህች) ከአላህና ከመልክተኛው ወደእነዚያ ቃል ኪዳን ወደ ተጋባቻችኋቸው አጋሪዎች የምትደርስ ንጽሕና ናት፡፡

بَرَآءَةٌ مِّنَ ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦٓ إِلَى ٱلَّذِينَ عَٰهَدتُّم مِّنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ﴿١﴾

2. በምድር ላይም አራት ወሮችን (ጸጥተኞች ስትኾኑ) ኺዱ፡፡ እናንተም ከአላህ (ቅጣት) የማታመልጡ መኾናችሁንና አላህም ከሓዲዎችን አዋራጅ መኾኑን ዕወቁ፤ (በሏቸው)፡፡

فَسِيحُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ أَرۡبَعَةَ أَشۡهُرٖ وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّكُمۡ غَيۡرُ مُعۡجِزِي ٱللَّهِ وَأَنَّ ٱللَّهَ مُخۡزِي ٱلۡكَٰفِرِينَ ﴿٢﴾

3. (ይህ) ከአላህና ከመልክተኛው በታላቁ ሐጅ ቀን የወጣ አላህ ከአጋሪዎቹ ንጹሕ ነው መልክተኛውም (እንደዚሁ)፡፡ (ከክህደት) ብትጸጸቱም እርሱ ለእናንተ በላጭ ነው፡፡ (ከእምነት) ብትሸሹም እናንተ አላህን የማታቅቱት መኾናችሁን ዕወቁ በማለት ወደ ሰዎች የሚደርስ ማስታወቂያ ነው፡፡ እነዚያን የካዱትንም በአሳማሚ ቅጣት አብስራቸው፡፡

وَأَذَٰنٞ مِّنَ ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦٓ إِلَى ٱلنَّاسِ يَوۡمَ ٱلۡحَجِّ ٱلۡأَكۡبَرِ أَنَّ ٱللَّهَ بَرِيٓءٞ مِّنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ وَرَسُولُهُۥۚ فَإِن تُبۡتُمۡ فَهُوَ خَيۡرٞ لَّكُمۡۖ وَإِن تَوَلَّيۡتُمۡ فَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّكُمۡ غَيۡرُ مُعۡجِزِي ٱللَّهِۗ وَبَشِّرِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِعَذَابٍ أَلِيمٍ ﴿٣﴾

4. ከአጋሪዎቹ እነዚያ ቃል ኪዳን የተጋባቻችኋቸውና ከዚያም ምንንም ያላጎደሉባችሁ በናንተ ላይም አንድንም ያልረዱባችሁ ሲቀሩ፤ (እነዚህን) ቃል ኪዳናቸውን እስከጊዜያታቸው (መጨረሻ) ሙሉላቸው፡፡ አላህ ጥንቁቆችን ይወዳልና፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ عَٰهَدتُّم مِّنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ثُمَّ لَمۡ يَنقُصُوكُمۡ شَيۡـٔٗا وَلَمۡ يُظَٰهِرُواْ عَلَيۡكُمۡ أَحَدٗا فَأَتِمُّوٓاْ إِلَيۡهِمۡ عَهۡدَهُمۡ إِلَىٰ مُدَّتِهِمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُتَّقِينَ ﴿٤﴾

5. የተከበሩትም ወሮች ባለቁ ጊዜ አጋሪዎቹን በአገኛችሁባቸው ስፍራ ግደሉዋቸው፡፡ ያዙዋቸውም፣ ከበቡዋቸውም፣ ለእነሱም (መጠባበቅ) በየመንገዱ ተቀመጡ፡፡ ቢጸጸቱም፣ ሶላትንም በደንቡ ቢሰግዱ፣ ግዴታ ምጽዋትንም ቢሰጡ መንገዳቸውን ልቀቁላቸው፡፡ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

فَإِذَا ٱنسَلَخَ ٱلۡأَشۡهُرُ ٱلۡحُرُمُ فَٱقۡتُلُواْ ٱلۡمُشۡرِكِينَ حَيۡثُ وَجَدتُّمُوهُمۡ وَخُذُوهُمۡ وَٱحۡصُرُوهُمۡ وَٱقۡعُدُواْ لَهُمۡ كُلَّ مَرۡصَدٖۚ فَإِن تَابُواْ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَوُاْ ٱلزَّكَوٰةَ فَخَلُّواْ سَبِيلَهُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿٥﴾

6. ከአጋሪዎችም አንዱ ጥገኝነትን ቢጠይቅ የአላህን ቃል ይሰማ ዘንድ አስጠጋው፡፡ ከዚያም ወደ መጠበቂያው ስፍራ አድርሰው፡፡ ይህ እነሱ የማያውቁ ሕዝቦች በመኾናቸው ነው፡፡

وَإِنۡ أَحَدٞ مِّنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٱسۡتَجَارَكَ فَأَجِرۡهُ حَتَّىٰ يَسۡمَعَ كَلَٰمَ ٱللَّهِ ثُمَّ أَبۡلِغۡهُ مَأۡمَنَهُۥۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَوۡمٞ لَّا يَعۡلَمُونَ ﴿٦﴾

7. ለአጋሪዎቹ አላህ ዘንድና እመልክተኛው ዘንድ ቃል ኪዳን እንዴት ይኖራቸዋል እነዚያ በተከበረው መስጊድ ዘንድ ቃል ኪዳን የተጋባቻችኋቸው ብቻ ሲቀሩ፡፡ (እነዚህ) በቃል ኪዳናቸው ለእናንተ ቀጥ እስካሉላችሁ ድረስ ለነርሱም ቀጥ በሉላቸው፡፡ አላህ ጥንቁቆችን ይወዳልና፡፡

كَيۡفَ يَكُونُ لِلۡمُشۡرِكِينَ عَهۡدٌ عِندَ ٱللَّهِ وَعِندَ رَسُولِهِۦٓ إِلَّا ٱلَّذِينَ عَٰهَدتُّمۡ عِندَ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِۖ فَمَا ٱسۡتَقَٰمُواْ لَكُمۡ فَٱسۡتَقِيمُواْ لَهُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُتَّقِينَ ﴿٧﴾

8. በእናንተ ላይ ቢያይሉም በእናንተ ውስጥ ዝምድናንና ቃል ኪዳንን የማይጠብቁ ሲኾኑ እንዴት (ቃል ኪዳን ይኖራቸዋል)፡፡ በአፎቻቸው ያስወድዷችኋል፡፡ ልቦቻቸውም እንቢ ይላሉ፡፡ አብዛኞቻቸውም አመጸኞች ናቸው፡፡

كَيۡفَ وَإِن يَظۡهَرُواْ عَلَيۡكُمۡ لَا يَرۡقُبُواْ فِيكُمۡ إِلّٗا وَلَا ذِمَّةٗۚ يُرۡضُونَكُم بِأَفۡوَٰهِهِمۡ وَتَأۡبَىٰ قُلُوبُهُمۡ وَأَكۡثَرُهُمۡ فَٰسِقُونَ ٨

9. በአላህ አንቀጾች ጥቂትን ዋጋ ገዙ፡፡ ከመንገዱም አገዱ፡፡ እነርሱ ይሠሩት የነበሩት ሥራ ከፋ!

ٱشۡتَرَوۡاْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ ثَمَنٗا قَلِيلٗا فَصَدُّواْ عَن سَبِيلِهِۦٓۚ إِنَّهُمۡ سَآءَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٩

10. በምእምን ነገር ዝምድናንም ኪዳንንም አይጠብቁም፤ እነዚያም እነሱ ወሰን አላፊዎች ናቸው፡፡

لَا يَرۡقُبُونَ فِي مُؤۡمِنٍ إِلّٗا وَلَا ذِمَّةٗۚ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُعۡتَدُونَ ١٠

11. ቢጸጸቱም፣ ሶላትንም ቢሰግዱ፣ ዘካንም ቢሰጡ የሃይማኖት ወንድሞቻችሁ ናቸው፡፡ ለሚያውቁ ሕዝቦችም አንቀጾችን እናብራራለን፡፡

فَإِن تَابُواْ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَوُاْ ٱلزَّكَوٰةَ فَإِخۡوَٰنُكُمۡ فِي ٱلدِّينِۗ وَنُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَعۡلَمُونَ ١١

12. ከቃል ኪዳናቸው በኋላ መሓላዎቻቸውን ቢያፈርሱ፣ ሃይማኖታችሁንም ቢያነውሩ፣ የክህደት መሪዎችን (ከክህደት) ይከለከሉ ዘንድ ተዋጉዋቸው፡፡ እነርሱ ቃል ኪዳን የላቸውምና፡፡

وَإِن نَّكَثُوٓاْ أَيۡمَٰنَهُم مِّنۢ بَعۡدِ عَهۡدِهِمۡ وَطَعَنُواْ فِي دِينِكُمۡ فَقَٰتِلُوٓاْ أَئِمَّةَ ٱلۡكُفۡرِ إِنَّهُمۡ لَآ أَيۡمَٰنَ لَهُمۡ لَعَلَّهُمۡ يَنتَهُونَ ١٢

13. መሓላዎቻቸውን ያፈረሱትን መልክተኛውንም ለማውጣት ያሰቡትን ሕዝቦች እነሱ ለመጀመሪያ ጊዜ የጀመሩዋችሁ ሲኾኑ ለምን አትዋጉዋቸውም ትፈሩዋቸዋላችሁን ምእምናን እንደ ኾናችሁም አላህ ይበልጥ ልትፈሩት የተገባው ነው፡፡

أَلَا تُقَٰتِلُونَ قَوۡمٗا نَّكَثُوٓاْ أَيۡمَٰنَهُمۡ وَهَمُّواْ بِإِخۡرَاجِ ٱلرَّسُولِ وَهُم بَدَءُوكُمۡ أَوَّلَ مَرَّةٍۚ أَتَخۡشَوۡنَهُمۡۚ فَٱللَّهُ أَحَقُّ أَن تَخۡشَوۡهُ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ١٣

14. ተጋደሉዋቸው፡፡ አላህ በእጆቻችሁ ያሰቃያቸዋል፡፡ ያዋርዳቸዋልም፡፡ በእነሱም ላይ ይረዳችኋል፡፡ የምእምናን ሕዝቦችንም ልቦች ያሽራል፡፡

قَٰتِلُوهُمۡ يُعَذِّبۡهُمُ ٱللَّهُ بِأَيۡدِيكُمۡ وَيُخۡزِهِمۡ وَيَنصُرۡكُمۡ عَلَيۡهِمۡ وَيَشۡفِ صُدُورَ قَوۡمٖ مُّؤۡمِنِينَ ١٤

15. የልቦቻችሁንም ቁጭት ያስወግዳል፡፡ አላህም ከሚሻው ሰው ላይ ጸጸትን ይቀበላል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَيُذۡهِبۡ غَيۡظَ قُلُوبِهِمۡۗ وَيَتُوبُ ٱللَّهُ عَلَىٰ مَن يَشَآءُۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ١٥

16. እነዚያን ከእናንተ ውስጥ የታገሉትንና ከአላህም ከመልክተኛውም ከምእመናንም ሌላ ምስጢረኛ ወዳጅ ያልያዙትን አላህ ሳይገልጽ ልትተው ታስባላችሁን አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

أَمۡ حَسِبۡتُمۡ أَن تُتۡرَكُواْ وَلَمَّا يَعۡلَمِ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ جَٰهَدُواْ مِنكُمۡ وَلَمۡ يَتَّخِذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَلَا رَسُولِهِۦ وَلَا ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَلِيجَةٗۚ وَٱللَّهُ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١٦

مَا كَانَ لِلْمُشْرِكِينَ أَن يَعْمُرُوا مَسَاجِدَ اللَّهِ شَاهِدِينَ عَلَىٰ أَنفُسِهِم بِالْكُفْرِ ۚ أُولَٰئِكَ حَبِطَتْ أَعْمَالُهُمْ وَفِي النَّارِ هُمْ خَالِدُونَ

17. ለከሓዲዎች በነፍሶቻቸው ላይ በክህደት የሚመሰክሩ ሲኾኑ የአላህን መስጊዶች ሊሠሩ አይገባቸውም፡፡ እነዚያ ሥራዎቻቸው ተበላሹ፡፡ እነሱም በእሳት ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

إِنَّمَا يَعْمُرُ مَسَاجِدَ اللَّهِ مَنْ آمَنَ بِاللَّهِ وَالْيَوْمِ الْآخِرِ وَأَقَامَ الصَّلَاةَ وَآتَى الزَّكَاةَ وَلَمْ يَخْشَ إِلَّا اللَّهَ ۖ فَعَسَىٰ أُولَٰئِكَ أَن يَكُونُوا مِنَ الْمُهْتَدِينَ

18. የአላህን መስጊዶች የሚሠራው በአላህና በመጨረሻው ቀን ያመነ፣ ሶላትንም በደንቡ የሰገደ፣ ግዴታ ምጽዋትንም የሰጠ ከአላህም ሌላ (ማንንም) ያልፈራ ሰው ብቻ ነው፡፡ እነዚያም ከተመሩት ጭምር መኾናቸው ተረጋገጠ፡፡

۞ أَجَعَلْتُمْ سِقَايَةَ الْحَاجِّ وَعِمَارَةَ الْمَسْجِدِ الْحَرَامِ كَمَنْ آمَنَ بِاللَّهِ وَالْيَوْمِ الْآخِرِ وَجَاهَدَ فِي سَبِيلِ اللَّهِ ۚ لَا يَسْتَوُونَ عِندَ اللَّهِ ۗ وَاللَّهُ لَا يَهْدِي الْقَوْمَ الظَّالِمِينَ

19. ካዕባን ጎብኚዎችን ማጠጣትንና የተከበረውን መስጊድ መሥራትን በአላህና በመጨረሻው ቀን እንዳመነና በአላህ መንገድ እንደታገለ ሰው (እምነትና ትግል) አደረጋችሁን አላህ ዘንድ አይተካከሉም፡፡ አላህም በዳዮች ሕዝቦችን አይመራም፡፡

الَّذِينَ آمَنُوا وَهَاجَرُوا وَجَاهَدُوا فِي سَبِيلِ اللَّهِ بِأَمْوَالِهِمْ وَأَنفُسِهِمْ أَعْظَمُ دَرَجَةً عِندَ اللَّهِ ۚ وَأُولَٰئِكَ هُمُ الْفَائِزُونَ

20. እነዚያ ያመኑት፣ ከአገራቸውም የተሰደዱት፣ በገንዘቦቻቸውና በነፍሶቻቸውም በአላህ መንገድ ላይ የታገሉት አላህ ዘንድ በደረጃ በጣም የላቁ ናቸው፡፡ እነዚያም እነሱ ፍላጎታቸውን ያገኙ ናቸው፡፡

يُبَشِّرُهُمْ رَبُّهُم بِرَحْمَةٍ مِّنْهُ وَرِضْوَانٍ وَجَنَّاتٍ لَّهُمْ فِيهَا نَعِيمٌ مُّقِيمٌ

21. ጌታቸው ከርሱ በኾነው እዝነትና ውዴታ በገነቶችም ለነሱ በውስጥዋ የማያቋርጥ መጠቀሚያ ያለባት ስትኾን ያበስራቸዋል፡፡

خَالِدِينَ فِيهَا أَبَدًا ۚ إِنَّ اللَّهَ عِندَهُ أَجْرٌ عَظِيمٌ

22. በውስጧ ዘላለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ (ያበስራቸዋል)፡፡ አላህ እርሱ ዘንድ ታላቅ ምንዳ አለና፡፡

يَا أَيُّهَا الَّذِينَ آمَنُوا لَا تَتَّخِذُوا آبَاءَكُمْ وَإِخْوَانَكُمْ أَوْلِيَاءَ إِنِ اسْتَحَبُّوا الْكُفْرَ عَلَى الْإِيمَانِ ۚ وَمَن يَتَوَلَّهُم مِّنكُمْ فَأُولَٰئِكَ هُمُ الظَّالِمُونَ

23. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አባቶቻችሁና ወንድሞቻችሁ ክህደትን ከእምነት አብልጠው ቢወዱ ወዳጆች አድርጋችሁ አትያዙዋቸው፡፡ ከእናንተም ውስጥ ወዳጅ የሚያደርጋቸው እነዚያ እነሱ በዳዮች ናቸው፤

قُلْ إِن كَانَ آبَاؤُكُمْ وَأَبْنَاؤُكُمْ وَإِخْوَانُكُمْ وَأَزْوَاجُكُمْ وَعَشِيرَتُكُمْ وَأَمْوَالٌ اقْتَرَفْتُمُوهَا وَتِجَارَةٌ تَخْشَوْنَ كَسَادَهَا وَمَسَاكِنُ تَرْضَوْنَهَا أَحَبَّ إِلَيْكُم مِّنَ اللَّهِ وَرَسُولِهِ وَجِهَادٍ فِي سَبِيلِهِ فَتَرَبَّصُوا حَتَّىٰ يَأْتِيَ اللَّهُ بِأَمْرِهِ ۗ وَاللَّهُ لَا يَهْدِي الْقَوْمَ الْفَاسِقِينَ

24. «አባቶቻችሁና ወንዶች ልጆቻችሁ፣ ወንድሞቻችሁም፣ ሚስቶቻችሁም፣ ዘመዶቻችሁም፣ የሰበሰባችኋቸው ሀብቶችም፣ መክሰሩዋን የምትፈሩዋት ንግድም፣ የምትወዷቸው መኖሪያዎችም እናንተ ዘንድ ከአላህና ከመልክተኛው በርሱ መንገድም ከመታገል ይበልጥ የተወደዱ እንደኾኑ አላህ ትእዛዙን እስከሚያመጣ ድረስ ተጠባበቁ» በላቸው፡፡ አላህም አመጸኞች ሕዝቦችን አይመራም፡፡

25. አላህም በብዙ ስፍራዎች በእርግጥ ረዳችሁ፤ የሑነይንም ቀን ብዛታችሁ በአስደነቀቻችሁና ከእናንተም ምንም ባልጠቀመቻችሁ ጊዜ ምድርም ከስፋቷ ጋር በጠበበቻችሁና ከዚያም ተሸናፊዎች ኾናችሁ በዞራችሁ ጊዜ (ረዳችሁ)፡፡

لَقَدْ نَصَرَكُمُ ٱللَّهُ فِى مَوَاطِنَ كَثِيرَةٍ وَيَوْمَ حُنَيْنٍ إِذْ أَعْجَبَتْكُمْ كَثْرَتُكُمْ فَلَمْ تُغْنِ عَنكُمْ شَيْـًٔا وَضَاقَتْ عَلَيْكُمُ ٱلْأَرْضُ بِمَا رَحُبَتْ ثُمَّ وَلَّيْتُم مُّدْبِرِينَ ﴿٢٥﴾

26. ከዚያም አላህ እርጋታውን በመልክተኛውና በምእምናኖቹ ላይ አወረደ፡፡ ያላያችኋቸውንም ሰራዊት አወረደ፡፡ እነዚያን የካዱትንም በመገደልና በመማረክ አሰቃየ፡፡ ይህም የከሓዲያን ፍዳ ነው፡፡

ثُمَّ أَنزَلَ ٱللَّهُ سَكِينَتَهُۥ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ وَعَلَى ٱلْمُؤْمِنِينَ وَأَنزَلَ جُنُودًا لَّمْ تَرَوْهَا وَعَذَّبَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ ۚ وَذَٰلِكَ جَزَآءُ ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿٢٦﴾

27. ከዚያም ከዚህ በኋላ አላህ በሚሻው ሰው ላይ ጸጸትን ይቀበላል፡፡ አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

ثُمَّ يَتُوبُ ٱللَّهُ مِنۢ بَعْدِ ذَٰلِكَ عَلَىٰ مَن يَشَآءُ ۗ وَٱللَّهُ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿٢٧﴾

28. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አጋሪዎች እርኩሶች ብቻ ናቸው፡፡ ከዚህም ዓመታቸው በኋላ የተከበረውን መስጊድ አይቅረቡ፡፡ ድኽነትንም ብትፈሩ አላህ ቢሻ ከችሮታው በእርግጥ ያከብራችኋል፡፡ አላህ ዐዋቂ ጥበበኛ ነውና፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ إِنَّمَا ٱلْمُشْرِكُونَ نَجَسٌ فَلَا يَقْرَبُوا۟ ٱلْمَسْجِدَ ٱلْحَرَامَ بَعْدَ عَامِهِمْ هَـٰذَا ۚ وَإِنْ خِفْتُمْ عَيْلَةً فَسَوْفَ يُغْنِيكُمُ ٱللَّهُ مِن فَضْلِهِۦٓ إِن شَآءَ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ﴿٢٨﴾

29. ከእነዚያ መጽሐፍን ከተሰጡት ሰዎች እነዚያን በአላህና በመጨረሻው ቀን የማያምኑትን፣ አላህና መልክተኛው እርም ያደረጉትንም እርም የማያደርጉትንና እውነተኛውንም ሃይማኖት የማይቀበሉትን እነርሱ የተዋረዱ ኾነው ግብርን በእጃቸው እስከሚሰጡ ድረስ ተዋጉዋቸው፡፡

قَـٰتِلُوا۟ ٱلَّذِينَ لَا يُؤْمِنُونَ بِٱللَّهِ وَلَا بِٱلْيَوْمِ ٱلْـَٔاخِرِ وَلَا يُحَرِّمُونَ مَا حَرَّمَ ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥ وَلَا يَدِينُونَ دِينَ ٱلْحَقِّ مِنَ ٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ ٱلْكِتَـٰبَ حَتَّىٰ يُعْطُوا۟ ٱلْجِزْيَةَ عَن يَدٍ وَهُمْ صَـٰغِرُونَ ﴿٢٩﴾

30. አይሁድ ዑዘይር የአላህ ልጅ ነው አለች፡፡ ክርስቲያኖችም አልመሲሕ የአላህ ልጅ ነው አሉ፡፡ ይህ በአፎቻቸው (የሚናገሩት) ቃላቸው ነው፡፡ የእነዚያን ከነሱ በፊት የካዱትን ሰዎች ቃል ያመሳስላሉ፡፡ አላህ ያጥፋቸው፡፡ (ከእውነት) እንዴት ይመለሳሉ!

وَقَالَتِ ٱلْيَهُودُ عُزَيْرٌ ٱبْنُ ٱللَّهِ وَقَالَتِ ٱلنَّصَـٰرَى ٱلْمَسِيحُ ٱبْنُ ٱللَّهِ ۖ ذَٰلِكَ قَوْلُهُم بِأَفْوَٰهِهِمْ ۖ يُضَـٰهِـُٔونَ قَوْلَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ مِن قَبْلُ ۚ قَـٰتَلَهُمُ ٱللَّهُ ۚ أَنَّىٰ يُؤْفَكُونَ ﴿٣٠﴾

31. ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ የሌለውን አንድን አምላክ ሊገዙ እንጂ ያልታዘዙ ሲኾኑ ሊቃውንቶቻቸውንና መነኮሳታቸውን፣ የመርየምን ልጅ አልመሲሕንም ከአላህ ሌላ አማልክት አድርገው ያዙ፡፡ ከሚያጋሩት ሁሉ የጠራ ነው፡፡

ٱتَّخَذُوٓا۟ أَحْبَارَهُمْ وَرُهْبَـٰنَهُمْ أَرْبَابًا مِّن دُونِ ٱللَّهِ وَٱلْمَسِيحَ ٱبْنَ مَرْيَمَ وَمَآ أُمِرُوٓا۟ إِلَّا لِيَعْبُدُوٓا۟ إِلَـٰهًا وَٰحِدًا ۖ لَّآ إِلَـٰهَ إِلَّا هُوَ ۚ سُبْحَـٰنَهُۥ عَمَّا يُشْرِكُونَ ﴿٣١﴾

32. የአላህን ብርሃን በአፎቻቸው ለማጥፋት ይፈልጋሉ፡፡ አላህም ከሓዲዎች ቢጠሉም እንኳ ብርሃኑን መሙላትን እንጅ ሌላን አይሻም፡፡

يُرِيدُونَ أَن يُطْفِـُٔوا۟ نُورَ ٱللَّهِ بِأَفْوَٰهِهِمْ وَيَأْبَى ٱللَّهُ إِلَّآ أَن يُتِمَّ نُورَهُۥ وَلَوْ كَرِهَ ٱلْكَـٰفِرُونَ ﴿٣٢﴾

61. (ሙሐመድ ሆይ!) በማንኛውም ነገር ላይ አትሆንም፣ ከርሱም ከቁርኣን አታነብም፣ ማንኛውንም ሥራ (አንተም ሰዎቹም) አትሠሩም በገባችሁበት ጊዜ በናንተ ላይ ተጠባባቂዎች ብንሆን እንጂ፡፡ በምድርም ሆነ በሰማይ የብናኝ ክብደት ያክል ከጌታህ (ዕውቀት) አይርቅም፡፡ ከዚያም ያነሰ የተለቀም የለም፤ በግልጹ መጽሐፍ ውስጥ የተጻፈ ቢሆን እንጂ፡፡

وَمَا تَكُونُ فِي شَأۡنٖ وَمَا تَتۡلُواْ مِنۡهُ مِن قُرۡءَانٖ وَلَا تَعۡمَلُونَ مِنۡ عَمَلٍ إِلَّا كُنَّا عَلَيۡكُمۡ شُهُودًا إِذۡ تُفِيضُونَ فِيهِۚ وَمَا يَعۡزُبُ عَن رَّبِّكَ مِن مِّثۡقَالِ ذَرَّةٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فِي ٱلسَّمَآءِ وَلَآ أَصۡغَرَ مِن ذَٰلِكَ وَلَآ أَكۡبَرَ إِلَّا فِي كِتَٰبٖ مُّبِينٍ ﴿٦١﴾

62. ንቁ! የአላህ ወዳጆች በእነሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም፤ እነሱም አያዝኑም፡፡

أَلَآ إِنَّ أَوۡلِيَآءَ ٱللَّهِ لَا خَوۡفٌ عَلَيۡهِمۡ وَلَا هُمۡ يَحۡزَنُونَ ﴿٦٢﴾

63. (እነሱም) እነዚያ ያመኑትና ይፈሩት የነበሩ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَكَانُواْ يَتَّقُونَ ﴿٦٣﴾

64. ለእነሱ በቅርቢቱ ሕይወትም በመጨረሻይቱም ብስራት አላቸው፤ የአላህ ቃላት መለወጥ የላትም፤ ይህ እርሱ ታላቅ ዕድል ነው፡፡

لَهُمُ ٱلۡبُشۡرَىٰ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَفِي ٱلۡأٓخِرَةِۚ لَا تَبۡدِيلَ لِكَلِمَٰتِ ٱللَّهِۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ﴿٦٤﴾

65. ንግግራቸውም አያሳዝንህ፡፡ ኀይል ሁሉ በሙሉ የአላህ ብቻ ነውና፡፡ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነው፡፡

وَلَا يَحۡزُنكَ قَوۡلُهُمۡۘ إِنَّ ٱلۡعِزَّةَ لِلَّهِ جَمِيعًاۚ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿٦٥﴾

66. ንቁ! በሰማያት ያሉትና በምድርም ያሉት ሁሉ በእርግጥ የአላህ ናቸው፤ እነዚያ ከአላህ ሌላ ተጋሪዎችን የሚጠሩ ምንን ይከተላሉ ጥርጣሬን እንጂ ሌላ አይከተሉም፡፡ እነርሱም የሚዋሹ እንጂ አይደሉም፡፡

أَلَآ إِنَّ لِلَّهِ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِۗ وَمَا يَتَّبِعُ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ شُرَكَآءَۚ إِن يَتَّبِعُونَ إِلَّا ٱلظَّنَّ وَإِنۡ هُمۡ إِلَّا يَخۡرُصُونَ ﴿٦٦﴾

67. እርሱ ያ ሌሊትን በውስጡ ልታርፉበት (ጨለማ)፤ ቀንንም (ልትሠሩበት) ብርሃን ያደረገላችሁ ነው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚሰሙ ሕዝቦች በእርግጥ ታምራቶች አሉ፡፡

هُوَ ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ لِتَسۡكُنُواْ فِيهِ وَٱلنَّهَارَ مُبۡصِرًاۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَسۡمَعُونَ ﴿٦٧﴾

68. «አላህ ልጅን ያዘ (ወለደ)» አሉ፡፡ (ከሚሉት) ጥራት ተገባው፡፡ እርሱ ተብቃቂ ነው፡፡ በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የርሱ ነው፡፡ እናንተ ዘንድ በዚህ (በምትሉት) ምንም አስረጅ የላችሁም፡፡ በአላህ ላይ የማታውቁትን ትናገራላችሁን

قَالُواْ ٱتَّخَذَ ٱللَّهُ وَلَدٗاۗ سُبۡحَٰنَهُۥۖ هُوَ ٱلۡغَنِيُّۖ لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۚ إِنۡ عِندَكُم مِّن سُلۡطَٰنِۭ بِهَٰذَآۚ أَتَقُولُونَ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٦٨﴾

69. «እነዚያ በአላህ ላይ ውሸትን የሚቀጣጥፉ ፈጽሞ አይድኑም፤» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَفۡتَرُونَ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَ لَا يُفۡلِحُونَ ﴿٦٩﴾

70. (እነሱ) በቅርቢቱ ዓለም መጠቀም አላቸው፡፡ ከዚያም መመለሻቸው ወደእኛ ነው፡፡ ከዚያም ይክዱ በነበሩት ምክንያት ብርቱን ቅጣት እናቀምሳቸዋለን፡፡

مَتَٰعٞ فِي ٱلدُّنۡيَا ثُمَّ إِلَيۡنَا مَرۡجِعُهُمۡ ثُمَّ نُذِيقُهُمُ ٱلۡعَذَابَ ٱلشَّدِيدَ بِمَا كَانُواْ يَكۡفُرُونَ ﴿٧٠﴾

71. የኑሕንም ወሬ በእነሱ ላይ አንብብላቸው፡፡ ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «ሕዝቦቼ ሆይ! በእናንተ ውስጥ ብዙ ጊዜ መቆየቴ በአላህም ተዓምራት ማስታወሴ በእናንተ ላይ የከበደ ቢሆን፤ በአላህ ላይ ተጠግቻለሁ፡፡ ነገራችሁንም ከምታጋሩዋቸው (ጣዖታት) ጋር ሆናችሁ ቁረጡ፡፡ ከዚያም ነገራችሁ በእናንተ ላይ ድብቅ አይሁን (ግለጹት)፡፡ ከዚያም (የሻችሁትን) ወደእኔ አድርሱ፡፡ ጊዜም አትስጡኝ (ከምንም አልቆጥራችሁም)፡፡»

۞وَٱتۡلُ عَلَيۡهِمۡ نَبَأَ نُوحٍ إِذۡ قَالَ لِقَوۡمِهِۦ يَٰقَوۡمِ إِن كَانَ كَبُرَ عَلَيۡكُم مَّقَامِي وَتَذۡكِيرِي بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ فَعَلَى ٱللَّهِ تَوَكَّلۡتُ فَأَجۡمِعُوٓاْ أَمۡرَكُمۡ وَشُرَكَآءَكُمۡ ثُمَّ لَا يَكُنۡ أَمۡرُكُمۡ عَلَيۡكُمۡ غُمَّةٗ ثُمَّ ٱقۡضُوٓاْ إِلَيَّ وَلَا تُنظِرُونِ ﴿٧١﴾

72. «ብትሸሹም (አትጎዱኝም)፡፡ ከምንዳ ምንንም አልለምናችሁምና፡፡ ምንዳዬ በአላህ ላይ እንጂ በሌላ ላይ አይደለም፡፡ ከሙስሊሞች እንድሆንም ታዝዣለሁ፡፡»

فَإِن تَوَلَّيۡتُمۡ فَمَا سَأَلۡتُكُم مِّنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَى ٱللَّهِۖ وَأُمِرۡتُ أَنۡ أَكُونَ مِنَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ﴿٧٢﴾

73. አስተባበሉትም፡፡ እርሱንና ከእርሱ ጋር የነበሩትንም በታንኳይቱ ውስጥ አዳንናቸው፡፡ (ለጠፉት) ምትኮችም አደረግናቸው፡፡ እነዚያንም በአንቀጾቻችን ያስተባበሉትን አሰጠምን፡፡ የተስፈራሩትም ሕዝቦች መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከት፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَنَجَّيۡنَٰهُ وَمَن مَّعَهُۥ فِي ٱلۡفُلۡكِ وَجَعَلۡنَٰهُمۡ خَلَٰٓئِفَ وَأَغۡرَقۡنَا ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَاۖ فَٱنظُرۡ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُنذَرِينَ ﴿٧٣﴾

74. ከዚያም ከእርሱ በኋላ መልክተኞችን ወደየሕዝቦቻቸው ላክን፡፡ በግልጽ ማስረጃዎችም መጧቸው፡፡ (ከመላካቸው) በፊት በእርሱ ባስተባበሉበትም ነገር፤ የሚያምኑ አልሆኑም፡፡ እንደዚሁ በወሰን አላፊዎች ልቦች ላይ እናትማለን፡፡

ثُمَّ بَعَثۡنَا مِنۢ بَعۡدِهِۦ رُسُلًا إِلَىٰ قَوۡمِهِمۡ فَجَآءُوهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَمَا كَانُواْ لِيُؤۡمِنُواْ بِمَا كَذَّبُواْ بِهِۦ مِن قَبۡلُۚ كَذَٰلِكَ نَطۡبَعُ عَلَىٰ قُلُوبِ ٱلۡمُعۡتَدِينَ ﴿٧٤﴾

75. ከዚያም ከእነሱ ኋላ ሙሳንና ሃሩንን ወደ ፈርዖንና ወደ መማክርቱ በተዓምራታችን ላክን፡፡ ኮሩም ትዕቢተኞች ሕዝቦችም ነበሩ፡፡

ثُمَّ بَعَثۡنَا مِنۢ بَعۡدِهِم مُّوسَىٰ وَهَٰرُونَ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِۦ بِـَٔايَٰتِنَا فَٱسۡتَكۡبَرُواْ وَكَانُواْ قَوۡمٗا مُّجۡرِمِينَ ﴿٧٥﴾

76. ከእኛም ዘንድ እውነቱ በመጣላቸው ጊዜ «ይህ በእርግጥ ግልጽ ድግምት ነው» አሉ፡፡

فَلَمَّا جَآءَهُمُ ٱلۡحَقُّ مِنۡ عِندِنَا قَالُوٓاْ إِنَّ هَٰذَا لَسِحۡرٞ مُّبِينٞ ﴿٧٦﴾

77. ሙሳ አለ፡- «እውነቱን በመጣላችሁ ጊዜ ድግምተኞች የማይድኑ ሲኾኑ (እርሱ ድግምት ነው) ትላላችሁን ይህ ድግምት ነውን»

قَالَ مُوسَىٰٓ أَتَقُولُونَ لِلۡحَقِّ لَمَّا جَآءَكُمۡۖ أَسِحۡرٌ هَٰذَا وَلَا يُفۡلِحُ ٱلسَّٰحِرُونَ ﴿٧٧﴾

78. (እነርሱም) አሉ፡- «አባቶቻችንን በእርሱ ላይ ካገኘንበት ሃይማኖት ልታዞረን ለእናንተም በምድር ውስጥ ኩራት (ሹመት) ልትኖራችሁ መጣህብን እኛም ለእናንተ አማኞች አይደለንም፡፡»

قَالُوٓاْ أَجِئۡتَنَا لِتَلۡفِتَنَا عَمَّا وَجَدۡنَا عَلَيۡهِ ءَابَآءَنَا وَتَكُونَ لَكُمَا ٱلۡكِبۡرِيَآءُ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا نَحۡنُ لَكُمَا بِمُؤۡمِنِينَ ﴿٧٨﴾

79. ፈርዖንም፡- «ዐዋቂ ድግምተኛን ሁሉ አምጡልኝ» አለ፡፡

وَقَالَ فِرۡعَوۡنُ ٱئۡتُونِي بِكُلِّ سَٰحِرٍ عَلِيمٖ ﴿٧٩﴾

80. ድግምተኞቹም በመጡ ጊዜ ሙሳ ለእነርሱ፡- «እናንተ የምትጥሉትን ነገር ጣሉ» አላቸው፡፡

فَلَمَّا جَآءَ ٱلسَّحَرَةُ قَالَ لَهُم مُّوسَىٰٓ أَلۡقُواْ مَآ أَنتُم مُّلۡقُونَ ﴿٨٠﴾

81. (ገመዶቻቸውን) በጣሉም ጊዜ ሙሳ አለ፡- «ያ በርሱ የመጣችሁበት ነገር ድግምት ነው፡፡ አላህ በእርግጥ ያፈርሰዋል፡፡ አላህ የአጥፊዎችን ሥራ ፈጽሞ አያበጅምና፡፡»

فَلَمَّآ أَلۡقَوۡاْ قَالَ مُوسَىٰ مَا جِئۡتُم بِهِ ٱلسِّحۡرُۖ إِنَّ ٱللَّهَ سَيُبۡطِلُهُۥٓ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُصۡلِحُ عَمَلَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ٨١

82. አላህም ከሓዲዎች ቢጠሉም እውነትን በቃላቱ ያረጋግጣል፡፡

وَيُحِقُّ ٱللَّهُ ٱلۡحَقَّ بِكَلِمَٰتِهِۦ وَلَوۡ كَرِهَ ٱلۡمُجۡرِمُونَ ٨٢

83. ለሙሳም ከፈርዖንና ከሹማምንቶቻቸው ማሰቃየትን ከመፍራት ጋር ከወገኖቹ የኾኑ ጥቂቶች ትውልዶች እንጂ አላመኑለትም፡፡ ፈርዖንም በምድር ላይ በእርግጥ የኮራ ነበር፡፡ እርሱም በእርግጥ ወሰን ካለፉት ነበር፡፡

فَمَآ ءَامَنَ لِمُوسَىٰٓ إِلَّا ذُرِّيَّةٞ مِّن قَوۡمِهِۦ عَلَىٰ خَوۡفٖ مِّن فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِمۡ أَن يَفۡتِنَهُمۡۚ وَإِنَّ فِرۡعَوۡنَ لَعَالٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَإِنَّهُۥ لَمِنَ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ٨٣

84. ሙሳም አለ፡- «ሕዝቦቼ ሆይ! በአላህ አምናችሁ እንደ ሆነ በርሱ ላይ ተጠጉ፡፡ ታዛዦች እንደ ሆናችሁ (በአላህ ላይ ትመካላችሁ)፡፡»

وَقَالَ مُوسَىٰ يَٰقَوۡمِ إِن كُنتُمۡ ءَامَنتُم بِٱللَّهِ فَعَلَيۡهِ تَوَكَّلُوٓاْ إِن كُنتُم مُّسۡلِمِينَ ٨٤

85. አሉም፡- «በአላህ ላይ ተጠጋን፡፡ ጌታችን ሆይ! ለበደለኞች ሕዝቦች መፈተኛ አታድርገን፡፡»

فَقَالُواْ عَلَى ٱللَّهِ تَوَكَّلۡنَا رَبَّنَا لَا تَجۡعَلۡنَا فِتۡنَةٗ لِّلۡقَوۡمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ٨٥

86. በእዝነትህም ከከሓዲዎች ሕዝቦች አድነን፡፡

وَنَجِّنَا بِرَحۡمَتِكَ مِنَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡكَٰفِرِينَ ٨٦

87. ወደ ሙሳና ወደ ወንድሙ፡- «ለሕዝቦቻችሁ በምስር ቤቶችን ሥሩ፡፡ ቤቶቻችሁንም መስገጃ አድርጉ፡፡ ሶላትንም በደንቡስገዱ፡፡ (ለሙሳ) ምእምናኖቹንም አብስር» ስንል ላክን፡፡

وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰ وَأَخِيهِ أَن تَبَوَّءَا لِقَوۡمِكُمَا بِمِصۡرَ بُيُوتٗا وَٱجۡعَلُواْ بُيُوتَكُمۡ قِبۡلَةٗ وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَۗ وَبَشِّرِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٨٧

88. ሙሳም አለ፡- «ጌታችን ሆይ! አንተ ለፈርዖንና ለሹሞቹ በቅርቢቱ ሕይወት ጌጥን ብዙ ገንዘቦችንም በእርግጥ ሰጠህ፡፡ ጌታችን ሆይ! ከመንገድህ ያሳስቱ ዘንድ (ሰጠሃቸው)፡፡ ጌታችን ሆይ! ገንዘቦቻቸውን አጥፋ፡፡ በልቦቻቸውም ላይ አትም፡፡ አሳማሚን ቅጣት እስከሚያዩ አያምኑምና፡፡»

وَقَالَ مُوسَىٰ رَبَّنَآ إِنَّكَ ءَاتَيۡتَ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَأَهُۥ زِينَةٗ وَأَمۡوَٰلٗا فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا رَبَّنَا لِيُضِلُّواْ عَن سَبِيلِكَۖ رَبَّنَا ٱطۡمِسۡ عَلَىٰٓ أَمۡوَٰلِهِمۡ وَٱشۡدُدۡ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ فَلَا يُؤۡمِنُواْ حَتَّىٰ يَرَوُاْ ٱلۡعَذَابَ ٱلۡأَلِيمَ ٨٨

89. (አላህም) «ጸሎታችሁ በእርግጥ ተሰምታለች፡፡ ቀጥም በሉ፡፡ የእነዚያንም የማያውቁትን ሰዎች መንገድ አትከተሉ» አላቸው፡፡

قَالَ قَدۡ أُجِيبَت دَّعۡوَتُكُمَا فَٱسۡتَقِيمَا وَلَا تَتَّبِعَآنِّ سَبِيلَ ٱلَّذِينَ لَا يَعۡلَمُونَ ٨٩

90. የእስራኤልንም ልጆች ባሕሩን አሳለፍናቸው፡፡ ፈርዖንና ሰራዊቱም ወሰን ለማለፍና ለመበደል ተከተሏቸው፡፡ መስጠምም ባገኘው ጊዜ፡- «አመንኩ፡፡ እነሆ ከዚያ የእስራኤል ልጆች በርሱ ከአመኑበት በስተቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ እኔም ከታዛዦቹ ነኝ» አለ፡፡

۞وَجَٰوَزۡنَا بِبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱلۡبَحۡرَ فَأَتۡبَعَهُمۡ فِرۡعَوۡنُ وَجُنُودُهُۥ بَغۡيٗا وَعَدۡوًاۖ حَتَّىٰٓ إِذَآ أَدۡرَكَهُ ٱلۡغَرَقُ قَالَ ءَامَنتُ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا ٱلَّذِيٓ ءَامَنَتۡ بِهِۦ بَنُوٓاْ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَأَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ٩٠

91. ከአሁን በፊት በእርግጥ ያመጽክ ከአጥፊዎችም የነበርክ ስትሆን አሁን (አመንኩ ትላለህ)

ءَآلۡـَٰٔنَ وَقَدۡ عَصَيۡتَ قَبۡلُ وَكُنتَ مِنَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ﴿٩١﴾

92. ዛሬማ ከኋላህ ላሉት ተዓምር ትሆን ዘንድ በድን ሆነህ (ከባሕሩ) እናወጣሃለን (ተባለ)፡፡ ከሰዎችም ብዙዎቹ ከተዓምራታችን በእርግጥ ዘንጊዎች ናቸው፡፡

فَٱلۡيَوۡمَ نُنَجِّيكَ بِبَدَنِكَ لِتَكُونَ لِمَنۡ خَلۡفَكَ ءَايَةٗۚ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِ عَنۡ ءَايَٰتِنَا لَغَٰفِلُونَ ﴿٩٢﴾

93. የእስራኤልንም ልጆች ምስጉንን ስፍራ በእርግጥ አሰፈርናቸው፡፡ ከመልካም ሲሳዮችም ሰጠናቸው፡፡ ዕውቀትም (ቁርኣን) እስከመጣቸው ድረስ አልተለያዩም፡፡ ጌታህ በርሱ ይለያዩበት በነበሩት ነገር በትንሣኤ ቀን በመካከላቸው ይፈርዳል፡፡

وَلَقَدۡ بَوَّأۡنَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ مُبَوَّأَ صِدۡقٖ وَرَزَقۡنَٰهُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ فَمَا ٱخۡتَلَفُواْ حَتَّىٰ جَآءَهُمُ ٱلۡعِلۡمُۚ إِنَّ رَبَّكَ يَقۡضِي بَيۡنَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فِيمَا كَانُواْ فِيهِ يَخۡتَلِفُونَ ﴿٩٣﴾

94. ወደ አንተም ካወረድነው በመጠራጠር ውስጥ ብትሆን እነዚያን ከአንተ በፊት መጽሐፉን የሚያነቡትን ጠይቅ፡፡ እውነቱ ከጌታህ ዘንድ በእርግጥ መጥቶልሃል፡፡ ከተጠራጣሪዎቹም አትሁን፡፡

فَإِن كُنتَ فِي شَكّٖ مِّمَّآ أَنزَلۡنَآ إِلَيۡكَ فَسۡـَٔلِ ٱلَّذِينَ يَقۡرَءُونَ ٱلۡكِتَٰبَ مِن قَبۡلِكَۚ لَقَدۡ جَآءَكَ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ فَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُمۡتَرِينَ ﴿٩٤﴾

95. ከእነዚያም የአላህን አንቀጾች ከአስተባበሉት አትሁን፡፡ ከከሳሪዎቹ ትሆናለህና፡፡

وَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ فَتَكُونَ مِنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ﴿٩٥﴾

96. እነዚያ በእነርሱ ላይ የጌታህ ቃል የተረጋገጠባቸው አያምኑም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ حَقَّتۡ عَلَيۡهِمۡ كَلِمَتُ رَبِّكَ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿٩٦﴾

97. ተዓምር ሁሉ ብትመጣላቸውም አሳማሚን ቅጣት እስከሚያዩ ድረስ (አያምኑም)፡፡

وَلَوۡ جَآءَتۡهُمۡ كُلُّ ءَايَةٍ حَتَّىٰ يَرَوُاْ ٱلۡعَذَابَ ٱلۡأَلِيمَ ﴿٩٧﴾

98. (ከዩኑስ በፊት ካለፉት ከተሞች) ያመነችና እምነትዋ የጠቀማት ከተማ ለምን አልኖረችም ግን የዩኑስ ሕዝቦች ባመኑ ጊዜ በቅርቢቱ ሕይወት የውርደትን ቅጣት ከእነሱ ላይ አነሳንላቸው፡፡ እስከ ጊዜም ድረስ አጣቀምናቸው፡፡

فَلَوۡلَا كَانَتۡ قَرۡيَةٌ ءَامَنَتۡ فَنَفَعَهَآ إِيمَٰنُهَآ إِلَّا قَوۡمَ يُونُسَ لَمَّآ ءَامَنُواْ كَشَفۡنَا عَنۡهُمۡ عَذَابَ ٱلۡخِزۡيِ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَمَتَّعۡنَٰهُمۡ إِلَىٰ حِينٖ ﴿٩٨﴾

99. ጌታህም በሻ ኖሮ በምድር ያሉት ሰዎች ሁሉም የተሰበሰቡ ሆነው ባመኑ ነበር፡፡ ታዲያ አንተ ሰዎችን አማኞች እንዲኾኑ ታስገድዳለህን

وَلَوۡ شَآءَ رَبُّكَ لَأٓمَنَ مَن فِي ٱلۡأَرۡضِ كُلُّهُمۡ جَمِيعًاۚ أَفَأَنتَ تُكۡرِهُ ٱلنَّاسَ حَتَّىٰ يَكُونُواْ مُؤۡمِنِينَ ﴿٩٩﴾

100. ለማንኛዋም ነፍስ በአላህ ፈቃድ ቢሆን እንጂ ልታምን (ችሎታ) የላትም፡፡ (አላህ ለከፊሎቹ እምነትን ይሻል)፡፡ በእነዚያም በማያውቁት ላይ ርክሰትን ያደርጋል፡፡

وَمَا كَانَ لِنَفۡسٍ أَن تُؤۡمِنَ إِلَّا بِإِذۡنِ ٱللَّهِۚ وَيَجۡعَلُ ٱلرِّجۡسَ عَلَى ٱلَّذِينَ لَا يَعۡقِلُونَ ﴿١٠٠﴾

101. «በሰማያትና በምድር ያለውን (ተዓምር) ተመልከቱ» በላቸው፡፡ ተዓምራቶችና አስፈራሪዎችም ለማያምኑ ሕዝቦች አይጠቅሙም፡፡

قُلِ ٱنظُرُواْ مَاذَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَمَا تُغۡنِي ٱلۡأٓيَٰتُ وَٱلنُّذُرُ عَن قَوۡمٖ لَّا يُؤۡمِنُونَ ﴿١٠١﴾

102. የእነዚያን ከእነሱ በፊት ያለፉትን ሕዝቦች ቀኖች ብጤ እንጂ ሌላን ይጠባበቃሉን «ተጠባበቁ፤ እኔ ከናንተ ጋር ከሚጠባበቁት ነኝ» በላቸው፡፡

فَهَلۡ يَنتَظِرُونَ إِلَّا مِثۡلَ أَيَّامِ ٱلَّذِينَ خَلَوۡاْ مِن قَبۡلِهِمۡۚ قُلۡ فَٱنتَظِرُوٓاْ إِنِّي مَعَكُم مِّنَ ٱلۡمُنتَظِرِينَ ١٠٢

103. ከዚያም መልክተኞቻችንን እነዚያንም ያመኑትን እናድናለን፡፡ እንደዚሁም ምእምናንን (ከጭንቅ ሁሉ) እናድናለን፡፡ (ይህ) በእኛ ላይ ተረጋገጠ፡፡

ثُمَّ نُنَجِّي رُسُلَنَا وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۚ كَذَٰلِكَ حَقًّا عَلَيۡنَا نُنجِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٠٣

104. «እናንተ ሰዎች ሆይ! ከእኔ ሃይማኖት በመጠራጠር ውስጥ ብትሆኑ እነዚያን ከአላህ ሌላ የምትገዟቸውን አልገዛም፡፡ ግን ያንን የሚገድላችሁን አላህን እገዛለሁ፡፡ ከምእምናን እንድሆንም ታዘዝሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِن كُنتُمۡ فِي شَكّٖ مِّن دِينِي فَلَآ أَعۡبُدُ ٱلَّذِينَ تَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَلَٰكِنۡ أَعۡبُدُ ٱللَّهَ ٱلَّذِي يَتَوَفَّىٰكُمۡۖ وَأُمِرۡتُ أَنۡ أَكُونَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٠٤

105. ፊትህንም (ወደ ቀጥታ) ያዘነበልክ ስትሆን ለሃይማኖት ቀጥ አድርግ፡፡ ከአጋሪዎቹም አትሁን፡፡

وَأَنۡ أَقِمۡ وَجۡهَكَ لِلدِّينِ حَنِيفٗا وَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ١٠٥

106. «ከአላህም በቀር የማይጠቅምንና የማይጎዳን አትገዛ፡፡ ብትሠራም አንተ ያንጊዜ ከበደለኞቹ ትሆናለህ» (ተብያለሁ በላቸው)፡፡

وَلَا تَدۡعُ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَنفَعُكَ وَلَا يَضُرُّكَۖ فَإِن فَعَلۡتَ فَإِنَّكَ إِذٗا مِّنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٠٦

107. አላህም ጉዳትን ቢያደርስብህ ከእርሱ ሌላ ለእርሱ ገላጭ የለውም፡፡ በጎንም ነገር ቢሻልህ ለችሮታው መላሽ የለም፡፡ ከባሮቹ የሚሻውን በእርሱ ይለይበታል፡፡ እርሱም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَإِن يَمۡسَسۡكَ ٱللَّهُ بِضُرّٖ فَلَا كَاشِفَ لَهُۥٓ إِلَّا هُوَۖ وَإِن يُرِدۡكَ بِخَيۡرٖ فَلَا رَآدَّ لِفَضۡلِهِۦۚ يُصِيبُ بِهِۦ مَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦۚ وَهُوَ ٱلۡغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ١٠٧

108. «እናንተ ሰዎች ሆይ! እውነቱ ከጌታችሁ በእርግጥ መጣላችሁ፡፡ (በእርሱ) የተመራም ሰው የሚመራው ለራሱ ነው፡፡ የተሳሳተም ሰው የሚሳሳተው (ጉዳቱ) በራሱ ላይ ነው፡፡ እኔም በእናንተ ላይ ተጠባባቂ አይደለሁም» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ قَدۡ جَآءَكُمُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكُمۡۖ فَمَنِ ٱهۡتَدَىٰ فَإِنَّمَا يَهۡتَدِي لِنَفۡسِهِۦۖ وَمَن ضَلَّ فَإِنَّمَا يَضِلُّ عَلَيۡهَاۖ وَمَآ أَنَا۠ عَلَيۡكُم بِوَكِيلٖ ١٠٨

109. ወዳንተም የሚወረደውን ነገር ተከተል፡፡ አላህም (በነሱ ላይ) እስከሚፈርድ ድረስ ታገስ፡፡ እርሱም ከፈራጆቹ ሁሉ በላጭ ነው፡፡

وَٱتَّبِعۡ مَا يُوحَىٰٓ إِلَيۡكَ وَٱصۡبِرۡ حَتَّىٰ يَحۡكُمَ ٱللَّهُۚ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلۡحَٰكِمِينَ ١٠٩

# ሱረቱ ሁድ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

1. አ.ሊ.ረ (አሊፍ ላም ራ፤ ይህ ቁርኣን) አንቀጾቹ በጥንካሬ የተሰካኩ ከዚያም የተዘረዘሩ የሆነ መጽሐፍ ነው:: ጥበበኛ ውስጠ ዐዋቂ ከሆነው ዘንድ (የተወረደ) ነው::

2. (እንዲህ በላቸው):- «አላህን እንጂ ሌላን አትገዙ:: እኔ ለእናንተ ከርሱ (የተላከሁ) አስፈራሪና አብሳሪ ነኝ:: »

3. ጌታችሁንም ምሕረትን ለምኑት:: ከዚያም ወደእርሱ ተመለሱ:: እስከተወሰነ ጊዜ ድረስ መልካምን መጥቀም ይጠቅማችኋልና:: የትሩፋትንም ባለቤት ሁሉ ችሮታውን (ምንዳውን) ይሰጠዋል:: ብትሸሹም እኔ በእናንተ ላይ የታላቁን ቀን ቅጣት እፈራላችኋለሁ::

4. መመለሻችሁ ወደ አላህ ብቻ ነው:: እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው::

5. ንቁ! እነሱ ከእርሱ (ከአላህ) ይደበቁ ዘንድ ደረቶቻቸውን ያጥፉሉ:: ንቁ! ልብሶቻቸውን በሚከናነቡ ጊዜ የሚደብቁትን የሚገልጹትንም ሁሉ ያውቃል:: እርሱ በደረቶች ውስጥ ያለውን ሁሉ ዐዋቂ ነውና::

6. በምድርም ላይ ምንም ተንቀሳቃሽ የለችም ምግቧ በአላህ ላይ ያለ ቢኾን እንጂ:: ማረፊያዋንም መርጊያዋንም ያውቃል:: ሁሉም ግልጽ በሆነው መጽሐፍ ውስጥ ነው::

7. እርሱም ያ ሰማያትንና ምድርን በስድስት ቀኖች ውስጥ የፈጠረ ነው:: ዐርሹም በውሃ ላይ ነበር:: የትኛችሁ ሥራው ያማረ መሆኑን ይፈትናችሁ ዘንድ (ፈጠራቸው):: «እናንተ ከሞት በኋላ በእርግጥ ተቀስቃሾች ናችሁ» ብትልም እነዚያ የካዱት ይህ ግልጽ ድግምት እንጂ ሌላ አይደለም ይላሉ::

# سورة هود

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

الٓرۚ كِتَٰبٌ أُحۡكِمَتۡ ءَايَٰتُهُۥ ثُمَّ فُصِّلَتۡ مِن لَّدُنۡ حَكِيمٍ خَبِيرٍ ١

أَلَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّا ٱللَّهَۚ إِنَّنِي لَكُم مِّنۡهُ نَذِيرٞ وَبَشِيرٞ ٢

وَأَنِ ٱسۡتَغۡفِرُواْ رَبَّكُمۡ ثُمَّ تُوبُوٓاْ إِلَيۡهِ يُمَتِّعۡكُم مَّتَٰعًا حَسَنًا إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗى وَيُؤۡتِ كُلَّ ذِي فَضۡلٖ فَضۡلَهُۥۖ وَإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ عَذَابَ يَوۡمٖ كَبِيرٍ ٣

إِلَى ٱللَّهِ مَرۡجِعُكُمۡۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ٤

أَلَآ إِنَّهُمۡ يَثۡنُونَ صُدُورَهُمۡ لِيَسۡتَخۡفُواْ مِنۡهُۚ أَلَا حِينَ يَسۡتَغۡشُونَ ثِيَابَهُمۡ يَعۡلَمُ مَا يُسِرُّونَ وَمَا يُعۡلِنُونَۚ إِنَّهُۥ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٥

۞وَمَا مِن دَآبَّةٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ إِلَّا عَلَى ٱللَّهِ رِزۡقُهَا وَيَعۡلَمُ مُسۡتَقَرَّهَا وَمُسۡتَوۡدَعَهَاۚ كُلّٞ فِي كِتَٰبٖ مُّبِينٖ ٦

وَهُوَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ فِي سِتَّةِ أَيَّامٖ وَكَانَ عَرۡشُهُۥ عَلَى ٱلۡمَآءِ لِيَبۡلُوَكُمۡ أَيُّكُمۡ أَحۡسَنُ عَمَلٗاۗ وَلَئِن قُلۡتَ إِنَّكُم مَّبۡعُوثُونَ مِنۢ بَعۡدِ ٱلۡمَوۡتِ لَيَقُولَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا سِحۡرٞ مُّبِينٞ ٧

8. ቅጣቱንም ወደ ተቆጠሩ (ጥቂት) ጊዜያቶች ከእነርሱ ብናቆይላቸው «(ከመውረድ) የሚከለክለው ምንድን ነው» ይላሉ፡፡ ንቁ! በሚመጣባቸው ቀን ከእነሱ ላይ ተመላሽ አይደለም፡፡ በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩትም (ቅጣት) በእነርሱ ላይ ይወርድባቸዋል፡፡

وَلَئِنۡ أَخَّرۡنَا عَنۡهُمُ ٱلۡعَذَابَ إِلَىٰٓ أُمَّةٖ مَّعۡدُودَةٖ لَّيَقُولُنَّ مَا يَحۡبِسُهُۥٓۗ أَلَا يَوۡمَ يَأۡتِيهِمۡ لَيۡسَ مَصۡرُوفًا عَنۡهُمۡ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ٨

9. ሰውንም ከእኛ ችሮታን ብናቀምሰው ከዚያም ከርሱ ብንወስዳት እርሱ በእርግጥ ተስፋ ቆራጭ ከህደተ ብርቱ ነው፡፡

وَلَئِنۡ أَذَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ مِنَّا رَحۡمَةٗ ثُمَّ نَزَعۡنَٰهَا مِنۡهُ إِنَّهُۥ لَيَـُٔوسٞ كَفُورٞ ٩

10. ካገኘችውም ችግር በኋላ ጸጋዎችን ብናቀምሰው «ችግሮች ከኔ ላይ በእርግጥ ተወገዱ» ይላል (አያመሰግንም)፡፡ እርሱ ተደሳች ጉረኛ ነውና፡፡

وَلَئِنۡ أَذَقۡنَٰهُ نَعۡمَآءَ بَعۡدَ ضَرَّآءَ مَسَّتۡهُ لَيَقُولَنَّ ذَهَبَ ٱلسَّيِّـَٔاتُ عَنِّيٓۚ إِنَّهُۥ لَفَرِحٞ فَخُورٌ ١٠

11. ግን እነዚያ የታገሱ መልካም ሥራዎችንም የሠሩ እነዚያ ለእነሱ ምሕረትና ታላቅ ምንዳ አልላቸው፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ صَبَرُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَأَجۡرٞ كَبِيرٞ ١١

12. በእርሱ ላይ የገንዘብ ድልብ ለምን አልተወረደም ወይም ከርሱ ጋር መልአክ ለምን አልመጣም ማለታቸውንም በመፍራት ወደ አንተ ከሚወርደው ከፊሉን ልትተው በእርሱም ልብህ ጠባብ ሊኾን ይፈራልሃል፡፡ አንተ አስፈራሪ ብቻ ነህ፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ተጠባባቂ ነው፡፡

فَلَعَلَّكَ تَارِكُۢ بَعۡضَ مَا يُوحَىٰٓ إِلَيۡكَ وَضَآئِقُۢ بِهِۦ صَدۡرُكَ أَن يَقُولُواْ لَوۡلَآ أُنزِلَ عَلَيۡهِ كَنزٌ أَوۡ جَآءَ مَعَهُۥ مَلَكٌۚ إِنَّمَآ أَنتَ نَذِيرٞۚ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ وَكِيلٌ ١٢

13. ይልቁንም «(ቁርኣንን) ቀጣጠፈው» ይላሉን፡- «እውነተኞች እንደሆናችሁ ብጤው የሆኑን ዐስር የተቀጣጠፉ ሱራዎች አምጡ፡፡ ከአላህም ሌላ የቻላችሁትን (ረዳት) ጥሩ» በላቸው፡፡

أَمۡ يَقُولُونَ ٱفۡتَرَىٰهُۖ قُلۡ فَأۡتُواْ بِعَشۡرِ سُوَرٖ مِّثۡلِهِۦ مُفۡتَرَيَٰتٖ وَٱدۡعُواْ مَنِ ٱسۡتَطَعۡتُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ١٣

14. ለእናንተም (ጥሪውን) ባይቀበሏችሁ የተወረደው በአላህ እውቀት ብቻ መሆኑንና ከእርሱ ሌላ አምላክ አለመኖሩን ዕወቁ፡፡ ታዲያ እናንተ የምትሰልሙ ናችሁን (ስለሙ በላቸው)፡፡

فَإِلَّمۡ يَسۡتَجِيبُواْ لَكُمۡ فَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّمَآ أُنزِلَ بِعِلۡمِ ٱللَّهِ وَأَن لَّآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ فَهَلۡ أَنتُم مُّسۡلِمُونَ ١٤

15. ቅርቢቱን ሕይወትና ጌጧን የሚሹ የሆኑትን ሰዎች ሥራዎቻቸውን (ምንዳዋን) በእርሷ ውስጥ ወደነሱ እንሞላላቸዋለን፡፡ እነሱም በርሷ ውስጥ ምንም አይጎድልባቸውም፤

مَن كَانَ يُرِيدُ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا وَزِينَتَهَا نُوَفِّ إِلَيۡهِمۡ أَعۡمَٰلَهُمۡ فِيهَا وَهُمۡ فِيهَا لَا يُبۡخَسُونَ ١٥

16. እነዚያ እነርሱ በመጨረሻይቱ ዓለም ለእነርሱ ከእሳት በቀር የሌላቸው ናቸው፡፡ የሠሩትም ሥራ በርሷ ውስጥ ተበላሸ፡፡ (በቅርቢቱ ዓለም) ይሠሩት የነበሩትም በከንቱ ሥራ ብልሹ ነው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ لَيۡسَ لَهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ إِلَّا ٱلنَّارُۖ وَحَبِطَ مَا صَنَعُواْ فِيهَا وَبَٰطِلٞ مَّا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٦

17. ከጌታው ከአስረጅ ጋር የኾነ ሰው፣ ከእርሱም (ከአላህ) የኾነ መስካሪ የሚከተለው፣ ከእርሱ በፊትም የሙሳ መጽሐፍ መሪና እዝነት ሲኾን (የመሰከረለት) የቅርቢቱን ሕይወት እንደሚሻው ሰው ነውን እነዚያ በእርሱ (በቁርኣን) ያምናሉ፡፡ ከአሕዛቦቹም በእርሱ የሚክድ ሰው እሳት መመለሻው ናት፡፡ ከእርሱም በመጠራጠር ውስጥ አትሁን፡፡ እርሱ ከጌታህ የሆነ እውነት ነው፡፡ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያምኑም፡፡

أَفَمَن كَانَ عَلَىٰ بَيِّنَةٍ مِّن رَّبِّهِۦ وَيَتۡلُوهُ شَاهِدٞ مِّنۡهُ وَمِن قَبۡلِهِۦ كِتَٰبُ مُوسَىٰٓ إِمَامٗا وَرَحۡمَةًۚ أُوْلَٰٓئِكَ يُؤۡمِنُونَ بِهِۦۚ وَمَن يَكۡفُرۡ بِهِۦ مِنَ ٱلۡأَحۡزَابِ فَٱلنَّارُ مَوۡعِدُهُۥۚ فَلَا تَكُ فِي مِرۡيَةٖ مِّنۡهُۚ إِنَّهُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿١٧﴾

18. በአላህ ላይ እብለትን ከሚቀጣጥፍም ይበልጥ በዳይ ማነው እነዚያ በጌታቸው ላይ ይቀርባሉ፡፡ መስካሪዎቹም «እነዚህ በጌታቸው ላይ የዋሹት ናቸው» ይላሉ፡፡ ንቁ! የአላህ ርግማን በበዳዮች ላይ ይሁን፡፡

وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًاۚ أُوْلَٰٓئِكَ يُعۡرَضُونَ عَلَىٰ رَبِّهِمۡ وَيَقُولُ ٱلۡأَشۡهَٰدُ هَٰٓؤُلَآءِ ٱلَّذِينَ كَذَبُواْ عَلَىٰ رَبِّهِمۡۚ أَلَا لَعۡنَةُ ٱللَّهِ عَلَى ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٨﴾

19. (እነሱም) እነዚያ ከአላህ መንገድ የሚከለክሉ መጥመሟንም የሚፈልጓት ናቸው፡፡ እነሱም መጨረሻይቱን ዓለም እነሱ ከሓዲዎች ናቸው፡፤

ٱلَّذِينَ يَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَيَبۡغُونَهَا عِوَجٗا وَهُم بِٱلۡأٓخِرَةِ هُمۡ كَٰفِرُونَ ﴿١٩﴾

20. እነዚያ በምድር ውስጥ (ከአላህ) የሚያመልጡ አልነበሩም፡፡ ከአላህም ሌላ ለእነርሱ ረዳቶች አልነበሯቸውም፡፡ ለእነሱ ቅጣቱ ይደራረብላቸዋል፡፡ (እውነትን) መስማትን የሚችሉ አልነበሩም የሚያዩም አልነበሩም፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ لَمۡ يَكُونُواْ مُعۡجِزِينَ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا كَانَ لَهُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ مِنۡ أَوۡلِيَآءَۘ يُضَٰعَفُ لَهُمُ ٱلۡعَذَابُۚ مَا كَانُواْ يَسۡتَطِيعُونَ ٱلسَّمۡعَ وَمَا كَانُواْ يُبۡصِرُونَ ﴿٢٠﴾

21. እነዚያ እነርሱ ነፍሶቻቸውን ያከሰሩ ከእነሱም ይቀጣጥፉት የነበሩት ነገር የጠፋቸው ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ﴿٢١﴾

22. እነርሱ በመጨረሻይቱ ዓለም በጣም ከሳሪዎቹ እነሱ መሆናቸው ጥርጥር የለውም፡፡

لَا جَرَمَ أَنَّهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ هُمُ ٱلۡأَخۡسَرُونَ ﴿٢٢﴾

23. እነዚያ ያመኑትና በጎ ሥራዎችን የሠሩት ወደ ጌታቸውም የተዋረዱት እነዚያ የገነት ሰዎች ናቸው፡፡ እነሱ በውስጧ ዘላለም ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَأَخۡبَتُوٓاْ إِلَىٰ رَبِّهِمۡ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿٢٣﴾

24. የሁለቱ ክፍሎች ምሳሌ እንደ ዕውርና እንደ ደንቆሮ እንደሚያይና እንደሚሰማም ብጤ ነው፡፡ በምሳሌ ይተካከላሉን አትገሰጹምን

۞مَثَلُ ٱلۡفَرِيقَيۡنِ كَٱلۡأَعۡمَىٰ وَٱلۡأَصَمِّ وَٱلۡبَصِيرِ وَٱلسَّمِيعِۚ هَلۡ يَسۡتَوِيَانِ مَثَلًاۚ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ﴿٢٤﴾

25. ኑሕንም ወደ ሕዝቦቹ በእርግጥ ላክን፡፡ (አላቸውም)፡- «እኔ ለእናንተ ግልጽ አስፈራሪ (አስጠንቃቂ) ነኝ፡፡»

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا نُوحًا إِلَىٰ قَوۡمِهِۦٓ إِنِّي لَكُمۡ نَذِيرٞ مُّبِينٌ ﴿٢٥﴾

26. «አላህን እንጂ ሌላን አትገዙ፡፡ እኔ በእናንተ ላይ የአሳማሚን ቀን ቅጣት እፈራላችኋለሁና፡፡»

أَن لَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّا ٱللَّهَۖ إِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ عَذَابَ يَوۡمٍ أَلِيمٖ ﴿٢٦﴾

27. ከሕዝቦቹም እነዚያ የካዱት መሪዎቹ ብጤያችን ሰው ሆነህ እንጂ አናይህም፡፡ እነዚያም እነሱ ሐሳበ ጥሬዎች የሆኑት ወራዶቻችን እንጂ ሌላ ተከትሎህ አናይህም፡፡ ለእናንተም በእኛ ላይ ምንም ብልጫን አናይም፡፡ ከቶውንም ውሽታሞች መሆናችሁን እንጠረጥራችኋለን አሉ፡፡

فَقَالَ ٱلۡمَلَأُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن قَوۡمِهِۦ مَا نَرَىٰكَ إِلَّا بَشَرٗا مِّثۡلَنَا وَمَا نَرَىٰكَ ٱتَّبَعَكَ إِلَّا ٱلَّذِينَ هُمۡ أَرَاذِلُنَا بَادِيَ ٱلرَّأۡيِ وَمَا نَرَىٰ لَكُمۡ عَلَيۡنَا مِن فَضۡلِۭ بَلۡ نَظُنُّكُمۡ كَٰذِبِينَ ٢٧

28. «ሕዝቦቼ ሆይ! ንገሩኝ ከጌታዬ በግልጽ ማስረጃ ላይ ብሆን ከእርሱም ዘንድ የሆነን ችሮታ (ነብይነት) ቢሰጠኝና በእናንተ ላይ ብትደበቅባችሁ እናንተ ለርሷ ጠይዎች ስትሆኑ እርሷን (በመቀበል) እናስገድዳችኋለን» አላቸው፡፡

قَالَ يَٰقَوۡمِ أَرَءَيۡتُمۡ إِن كُنتُ عَلَىٰ بَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّي وَءَاتَىٰنِي رَحۡمَةٗ مِّنۡ عِندِهِۦ فَعُمِّيَتۡ عَلَيۡكُمۡ أَنُلۡزِمُكُمُوهَا وَأَنتُمۡ لَهَا كَٰرِهُونَ ٢٨

29. «ሕዝቦቼም ሆይ! በርሱ (በተላከሁበት ማድረስ) ላይ ገንዘብን አልጠይቃችሁም፡፡ ምንዳዬ በአላህ ላይ እንጂ በሌላ ላይ አይደለም፡፡ እኔም እነዚያን ያመኑትን አባራሪ አይደለሁም፡፡ እነርሱ ጌታቸውን የሚገናኙ ናቸውና፡፡ ግን እኔም የምትሳሳቱ ሕዝቦች ሆናችሁ አያችኋለሁ፡፡»

وَيَٰقَوۡمِ لَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مَالًاۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَى ٱللَّهِۚ وَمَآ أَنَا۠ بِطَارِدِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْۚ إِنَّهُم مُّلَٰقُواْ رَبِّهِمۡ وَلَٰكِنِّيٓ أَرَىٰكُمۡ قَوۡمٗا تَجۡهَلُونَ ٢٩

30. «ሕዝቦቼም ሆይ ባባርራቸው ከአላህ (ቅጣት) የሚያድነኝ ማን ነው አትገሰጹምን»

وَيَٰقَوۡمِ مَن يَنصُرُنِي مِنَ ٱللَّهِ إِن طَرَدتُّهُمۡۚ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ٣٠

31. «ለእናንተም እኔ ዘንድ የአላህ ግምጃ ቤቶች አሉሉ ሩቅንም ዐውቃለሁ አልላችሁም፡፡ እኔም መልአክ ነኝ አልላችሁም፡፡ ለእነዚያም ዓይኖቻችሁ ለሚያዋርዷቸው አላህ ደግ ነገርን (እምነትን) አይሰጣቸውም አልልም፡፡ አላህ በነፍሶቻቸው ውስጥ ያለውን ነገር አዋቂ ነው፡፡ እኔ ያን ጊዜ ከበደለኞች እሆናለሁና» (አላቸው)፡፡

وَلَآ أَقُولُ لَكُمۡ عِندِي خَزَآئِنُ ٱللَّهِ وَلَآ أَعۡلَمُ ٱلۡغَيۡبَ وَلَآ أَقُولُ إِنِّي مَلَكٞ وَلَآ أَقُولُ لِلَّذِينَ تَزۡدَرِيٓ أَعۡيُنُكُمۡ لَن يُؤۡتِيَهُمُ ٱللَّهُ خَيۡرًاۖ ٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا فِيٓ أَنفُسِهِمۡ إِنِّيٓ إِذٗا لَّمِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٣١

32. «ኑህ ሆይ! በእርግጥ ተከራከርከን፡፡ እኛን መከራከርህንም አበዛኸው፡፡ ከእውነተኞቹም እንደሆንክ የምታስፈራራብንን ቅጣት አምጣው» አሉ፡

قَالُواْ يَٰنُوحُ قَدۡ جَٰدَلۡتَنَا فَأَكۡثَرۡتَ جِدَٰلَنَا فَأۡتِنَا بِمَا تَعِدُنَآ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ٣٢

33. «እርሱን የሚያመጣባችሁ የሻ እንደ ሆነ አላህ ብቻ ነው፡፡ እናንተም የምታቅቱ አይደላችሁም» አላቸው፡፡

قَالَ إِنَّمَا يَأۡتِيكُم بِهِ ٱللَّهُ إِن شَآءَ وَمَآ أَنتُم بِمُعۡجِزِينَ ٣٣

34. «ለእናንተም ልመክራችሁ ብሻ አላህ ሊያጠማችሁ ሽቶ እንደ ኾነ ምክሬ አይጠቅማችሁም፡፡ እርሱ ጌታችሁ ነው፡፡ ወደ እርሱም ትመለሳላችሁ» (አላቸው)፡፡

وَلَا يَنفَعُكُمۡ نُصۡحِيٓ إِنۡ أَرَدتُّ أَنۡ أَنصَحَ لَكُمۡ إِن كَانَ ٱللَّهُ يُرِيدُ أَن يُغۡوِيَكُمۡۚ هُوَ رَبُّكُمۡ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٣٤

35. «ይልቁንም ቀጠፈው ይላሉን ብቀጥፈው ኃጢአቴ (ቅጣቱ) በኔ ላይ ነው፡፡ እኔም ከምታጠፉት (ጥፋት) ንጹሕ ነኝ» በላቸው፡፡

أَمۡ يَقُولُونَ ٱفۡتَرَىٰهُۖ قُلۡ إِنِ ٱفۡتَرَيۡتُهُۥ فَعَلَيَّ إِجۡرَامِي وَأَنَا۠ بَرِيٓءٞ مِّمَّا تُجۡرِمُونَ ٣٥

36. ወደ ኑሕም እነሆ «ከሕዝቦችህ በእርግጥ ካመኑት በስተቀር (ወደፊት) አያምኑም፡፡ ይሠሩትም በነበሩት (ክህደት) አትዘን ማለት ተወረደ፡፡»

وَأُوحِيَ إِلَىٰ نُوحٍ أَنَّهُۥ لَن يُؤْمِنَ مِن قَوْمِكَ إِلَّا مَن قَدْ ءَامَنَ فَلَا تَبْتَئِسْ بِمَا كَانُوا۟ يَفْعَلُونَ ٣٦

37. (አላህም) «በጥበቃችንና በትእዛዛችንም ሆነህ መርከቢቱን ሥራ፡፡ በእነዚያም በበደሉት ሰዎች ነገር አታናግረኝ እነሱ በእርግጥ ሰማጮች ናቸውና» (አለው)፡፡

وَٱصْنَعِ ٱلْفُلْكَ بِأَعْيُنِنَا وَوَحْيِنَا وَلَا تُخَـٰطِبْنِى فِى ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓا۟ إِنَّهُم مُّغْرَقُونَ ٣٧

38. ከወገኖቹም መሪዎቹ በእርሱ አጠገብ ባለፉ ቁጥር ከእርሱ እየተሳለቁ መርከቢቱን ይሠራል፡፡ «ከእኛ ብትሳለቁ እኛም እንደተሳለቃችሁብን ከናንተ እንሳለቅባችኋለን» አላቸው፡፡

وَيَصْنَعُ ٱلْفُلْكَ وَكُلَّمَا مَرَّ عَلَيْهِ مَلَأٌ مِّن قَوْمِهِۦ سَخِرُوا۟ مِنْهُ ۚ قَالَ إِن تَسْخَرُوا۟ مِنَّا فَإِنَّا نَسْخَرُ مِنكُمْ كَمَا تَسْخَرُونَ ٣٨

39. «የሚያዋርደው ቅጣት የሚመጣበትን በእርሱም ላይ ዘውታሪ ቅጣት የሚሰፍርበት ሰው (ማን እንደ ሆነ) ወደፊት ታውቃላችሁ» (አላቸው)፡፡

فَسَوْفَ تَعْلَمُونَ مَن يَأْتِيهِ عَذَابٌ يُخْزِيهِ وَيَحِلُّ عَلَيْهِ عَذَابٌ مُّقِيمٌ ٣٩

40. ትእዛዛችንም በመጣና እቶኑም በገነፈለ ጊዜ «በእርሷ ውስጥ ከየዓይነቱ ሁሉ ሁለት ሁለት (ወንድና ሴት) ፤ ቤተሰቦችህንም ቃል ያለፈበት ብቻ ሲቀር ያመነንም ሰው ሁሉ ጫን» አልነው፡፡ ከእርሱም ጋር ጥቂቶች እንጂ አላመኑም፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَ أَمْرُنَا وَفَارَ ٱلتَّنُّورُ قُلْنَا ٱحْمِلْ فِيهَا مِن كُلٍّ زَوْجَيْنِ ٱثْنَيْنِ وَأَهْلَكَ إِلَّا مَن سَبَقَ عَلَيْهِ ٱلْقَوْلُ وَمَنْ ءَامَنَ ۚ وَمَآ ءَامَنَ مَعَهُۥٓ إِلَّا قَلِيلٌ ٤٠

41. «መሄዷም መቆሟም በአላህ ስም ነው እያላችሁም በውስጧ ተሳፈሩ፡፡ ጌታ መሓሪ አዛኝ ነውና» አላቸው፡፡

۞ وَقَالَ ٱرْكَبُوا۟ فِيهَا بِسْمِ ٱللَّهِ مَجْر۪ىٰهَا وَمُرْسَىٰهَآ ۚ إِنَّ رَبِّى لَغَفُورٌ رَّحِيمٌ ٤١

42. እርሷም እንደ ተራራዎች በሆነ ማዕበል ውስጥ በእነርሱ (ይዛቸው) የምትንሻለል ስትሆን (በአላህ ስም ተቀመጡባት)፡፡ ኑሕም ልጁን ከመርከቢቱ የራቀ ሆኖ ሳለ «ልጄ ሆይ! ከኛ ጋር ተሳፈር ከከሓዲዎቹም አትሁን» ሲል ጠራው፡፡

وَهِىَ تَجْرِى بِهِمْ فِى مَوْجٍ كَٱلْجِبَالِ وَنَادَىٰ نُوحٌ ٱبْنَهُۥ وَكَانَ فِى مَعْزِلٍ يَـٰبُنَىَّ ٱرْكَب مَّعَنَا وَلَا تَكُن مَّعَ ٱلْكَـٰفِرِينَ ٤٢

43. (ልጁም) «ከውሃው ወደሚጠብቀኝ ተራራ እጠጋለሁ» አለ፡፡ (አባቱም)፡- «ዛሬ ከአላህ ትዕዛዝ ምንም ጠባቂ የለም (እርሱ) ያዘነለት ካልሆነ በቀር» አለው፡፡ ማዕበሉም በመካከላቸው ጋረደ፡፡ ከሰጣሚዎቹም ሆነ፡፡

قَالَ سَـَٔاوِىٓ إِلَىٰ جَبَلٍ يَعْصِمُنِى مِنَ ٱلْمَآءِ ۚ قَالَ لَا عَاصِمَ ٱلْيَوْمَ مِنْ أَمْرِ ٱللَّهِ إِلَّا مَن رَّحِمَ ۚ وَحَالَ بَيْنَهُمَا ٱلْمَوْجُ فَكَانَ مِنَ ٱلْمُغْرَقِينَ ٤٣

44. ተባለም፡- «ምድር ሆይ! ውሃሽን ዋጪ፡፡ ሰማይም ሆይ (ዝናብሽን) ያዢ፡፡ ውሃውም ሰረገ፡፡ ቅጣቱም ተፈጸም፡፡ ጁዲይ በሚባልም ተራራ ላይ (መርከቢቱ) ተደላደለች፡፡ ለከሓዲዎችም ሰዎች ጥፋት ተገባቸው (ጠፉ)» ተባለ፡፡

وَقِيلَ يَـٰٓأَرْضُ ٱبْلَعِى مَآءَكِ وَيَـٰسَمَآءُ أَقْلِعِى وَغِيضَ ٱلْمَآءُ وَقُضِىَ ٱلْأَمْرُ وَٱسْتَوَتْ عَلَى ٱلْجُودِىِّ ۖ وَقِيلَ بُعْدًا لِّلْقَوْمِ ٱلظَّـٰلِمِينَ ٤٤

45. ኑሕም ጌታውን ጠራ፡፡ አለም «ጌታዬ ሆይ! ልጄ ከቤተሰቤ ነው፡፡ ኪዳንህም እውነት ነው፡፡ አንተም ከፈራጆች ሁሉ ይበልጥ ዐዋቂ ነህ፡፡»

وَنَادَىٰ نُوحٞ رَّبَّهُۥ فَقَالَ رَبِّ إِنَّ ٱبۡنِي مِنۡ أَهۡلِي وَإِنَّ وَعۡدَكَ ٱلۡحَقُّ وَأَنتَ أَحۡكَمُ ٱلۡحَٰكِمِينَ ﴿٤٥﴾

46. (አላህም) «ኑሕ ሆይ! እርሱ ከቤተሰብህ አይደለም፤ እርሱ መልካም ያልሆነ ሥራ ነው፤ በርሱ ዕውቀት የሌለህንም ነገር አትጠይቀኝ፤ እኔ ከሚሳሳቱት ሰዎች እንዳትሆን እገስጽሀለሁ» አለ፡፡

قَالَ يَٰنُوحُ إِنَّهُۥ لَيۡسَ مِنۡ أَهۡلِكَۖ إِنَّهُۥ عَمَلٌ غَيۡرُ صَٰلِحٖۖ فَلَا تَسۡـَٔلۡنِ مَا لَيۡسَ لَكَ بِهِۦ عِلۡمٌۖ إِنِّيٓ أَعِظُكَ أَن تَكُونَ مِنَ ٱلۡجَٰهِلِينَ ﴿٤٦﴾

47. «ጌታዬ ሆይ! በእርሱ ለእኔ ዕውቀት የሌለኝን ነገር የምጠይቅህ ከመሆን እኔ ባንተ እጠበቃለሁ፡፡ ለእኔም ባትምረኝና ባታዝንልኝ ከከሳሪዎቹ እሆናለሁ» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّيٓ أَعُوذُ بِكَ أَنۡ أَسۡـَٔلَكَ مَا لَيۡسَ لِي بِهِۦ عِلۡمٞۖ وَإِلَّا تَغۡفِرۡ لِي وَتَرۡحَمۡنِيٓ أَكُن مِّنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ﴿٤٧﴾

48. «ኑሕ ሆይ! ከእኛ በሆነ ሰላም ባንተ ላይና አንተም ጋር ባሉት ሕዝቦች (ትውልድ) ላይ በሆኑ በረከቶችም የተጎናጸፍክ ሆነህ ውረድ፡፡ (ከእነሱው ዘሮች የሆኑ) ሕዝቦችም በቅርቢቱ ዓለም በእርግጥ እናስመቻቻቸዋለን፡ ፡ ከዚያም ከኛ የሆነ አሳማሚ ቅጣት ይነካቸዋል» ተባለ፡፡

قِيلَ يَٰنُوحُ ٱهۡبِطۡ بِسَلَٰمٖ مِّنَّا وَبَرَكَٰتٍ عَلَيۡكَ وَعَلَىٰٓ أُمَمٖ مِّمَّن مَّعَكَۚ وَأُمَمٞ سَنُمَتِّعُهُمۡ ثُمَّ يَمَسُّهُم مِّنَّا عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿٤٨﴾

49. ይህቺ ከሩቁ ወሬዎች ናት፡፡ ወደ አንተ እናወርዳታለን፡፡ አንተም ሕዝቦችህም ከዚህ በፊት የምታውቋት አልነበራችሁም፡፡ ታገስም፤ ምስጉን የሆነችው ፍጻሜ ለሚጠነቀቁት ናትና፡፡

تِلۡكَ مِنۡ أَنۢبَآءِ ٱلۡغَيۡبِ نُوحِيهَآ إِلَيۡكَۖ مَا كُنتَ تَعۡلَمُهَآ أَنتَ وَلَا قَوۡمُكَ مِن قَبۡلِ هَٰذَاۖ فَٱصۡبِرۡۖ إِنَّ ٱلۡعَٰقِبَةَ لِلۡمُتَّقِينَ ﴿٤٩﴾

50. ወደ ዓድም ወንድማቸውን ሁድን (ላክን)፡፡ አላቸው፡- «ወገኖቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ እናንተም ቀጣፊዎች እንጂ ሌላ አይደላችሁም፡፡

وَإِلَىٰ عَادٍ أَخَاهُمۡ هُودٗاۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرُهُۥٓۖ إِنۡ أَنتُمۡ إِلَّا مُفۡتَرُونَ ﴿٥٠﴾

51. «ሕዝቦቼ ሆይ! በእርሱ (በማድረሴ) ላይ ምንዳን አልጠይቃችሁም፡፡ ምንዳዬ በዚህ በፈጠረኝ ላይ እንጂ በሌላ ላይ አይደለም፡፡ አታውቁምን

يَٰقَوۡمِ لَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ أَجۡرًاۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَى ٱلَّذِي فَطَرَنِيٓۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ﴿٥١﴾

52. «ሕዝቦቼም ሆይ! ጌታችሁን ምሕረትን ለምኑት፡፡ ከዚያም ወደርሱ ተጸጸቱ፡፡ ዝናብን በእናንተ ላይ ተከታታይ አድርጎ ይልክላችኋልና፡፡ ወደ ኃይላችሁም ኃይልን ይጨምርላችኋል፡፡ አመጸኞችም ሆናችሁ አትሸሹ፡፡»

وَيَٰقَوۡمِ ٱسۡتَغۡفِرُواْ رَبَّكُمۡ ثُمَّ تُوبُوٓاْ إِلَيۡهِ يُرۡسِلِ ٱلسَّمَآءَ عَلَيۡكُم مِّدۡرَارٗا وَيَزِدۡكُمۡ قُوَّةً إِلَىٰ قُوَّتِكُمۡ وَلَا تَتَوَلَّوۡاْ مُجۡرِمِينَ ﴿٥٢﴾

53. አሉ፡- «ሁድ ሆይ! በአስረጅ አልመጣህልንም፡፡ እኛም ላንተ ንግግር ብለን አማልክቶቻችንን የምንተው አይደለንም፡፡ እኛም ለአንተ አማኞች አይደለንም፡፡

قَالُواْ يَٰهُودُ مَا جِئۡتَنَا بِبَيِّنَةٖ وَمَا نَحۡنُ بِتَارِكِيٓ ءَالِهَتِنَا عَن قَوۡلِكَ وَمَا نَحۡنُ لَكَ بِمُؤۡمِنِينَ ﴿٥٣﴾

54. «ከፊሎቹ አማልክቶቻችን በክፉ ነገር (በዕብደት) ለክፈውሃል እንጂ ሌላን አንልም» (አሉ)፡፡ «እኔ አላህን አስመሰክራለሁ፡፡ ከምታጋሩትም እኔ ንጹሕ መሆኔን መስክሩ» አላቸው፡፡

إِن نَّقُولُ إِلَّا ٱعْتَرَىٰكَ بَعْضُ ءَالِهَتِنَا بِسُوٓءٍ ۗ قَالَ إِنِّىٓ أُشْهِدُ ٱللَّهَ وَٱشْهَدُوٓا۟ أَنِّى بَرِىٓءٌ مِّمَّا تُشْرِكُونَ ٥٤

55. ከእርሱ ሌላ (አማልክትን ከምታጋሩት ንጹህ ነኝ)፡፡ ሁላችሁም ሆናችሁ ተንኮልን ሥሩብኝ፤ ከዚያም አታቆዩኝ፡፡

مِن دُونِهِۦ ۖ فَكِيدُونِى جَمِيعًا ثُمَّ لَا تُنظِرُونِ ٥٥

56. «እኔ በጌታዬና በጌታችሁ በአላህ ላይ ተጠጋሁ፡፡ በምድር ላይ ምንም ተንቀሳቃሽ የለችም እርሱ አናትዋን የያዛት ብትሆን እንጂ፡፡ ጌታዬ (ቃሉም ሥራውም) በቀጥተኛው መንገድ ላይ ነው» (አላቸው)፡፡

إِنِّى تَوَكَّلْتُ عَلَى ٱللَّهِ رَبِّى وَرَبِّكُم ۚ مَّا مِن دَآبَّةٍ إِلَّا هُوَ ءَاخِذٌۢ بِنَاصِيَتِهَآ ۚ إِنَّ رَبِّى عَلَىٰ صِرَٰطٍ مُّسْتَقِيمٍ ٥٦

57. «ብትዞሩም በእርሱ ወደእናንተ የተላኩሁበትን ነገር በእርግጥ አድርሼላችኋለሁ፡፡ ጌታዬ ከእናንተ ሌላ ሕዝብም ይተካል ምንም አትጎዱትምም፡፡ ጌታዬ በነገሩ ሁሉ ላይ ተጠባባቂ ነውና» (አላቸው)፡፡

فَإِن تَوَلَّوْا۟ فَقَدْ أَبْلَغْتُكُم مَّآ أُرْسِلْتُ بِهِۦٓ إِلَيْكُمْ ۚ وَيَسْتَخْلِفُ رَبِّى قَوْمًا غَيْرَكُمْ وَلَا تَضُرُّونَهُۥ شَيْـًٔا ۚ إِنَّ رَبِّى عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ حَفِيظٌ ٥٧

58. ትዕዛዛችንም በመጣ ጊዜ ሁድንና እነዚያን ከእሱ ጋር ያመኑትን ከእኛ በሆነው ችሮታ አዳን፡፡ ከብርቱ ቅጣትም አዳናቸው፡፡

وَلَمَّا جَآءَ أَمْرُنَا نَجَّيْنَا هُودًا وَٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ مَعَهُۥ بِرَحْمَةٍ مِّنَّا وَنَجَّيْنَٰهُم مِّنْ عَذَابٍ غَلِيظٍ ٥٨

59. ይህች (ነገድ) ዓድ ናት፡፡ በጌታቸው ታምራት ካዱ፡፡ መልክተኞቹንም አመጹ፤ የኃያል ሞገደኛን ሁሉ ትዕዛዝም ተከተሉ፡፡

وَتِلْكَ عَادٌ ۖ جَحَدُوا۟ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمْ وَعَصَوْا۟ رُسُلَهُۥ وَٱتَّبَعُوٓا۟ أَمْرَ كُلِّ جَبَّارٍ عَنِيدٍ ٥٩

60. በዚህች በቅርቢቱ ዓለምም እርግማን እንዲከተላቸው ተደረጉ፡፡ በትንሣኤም ቀን (እንደዚሁ)፡፡ ንቁ! ዓዶች ጌታቸውን ካዱ፡፡ ንቁ! የሁድ ሕዝቦች ለሆኑት ዓዶች (ከእዝነት) መራቅ ይገባቸው፡፡

وَأُتْبِعُوا۟ فِى هَٰذِهِ ٱلدُّنْيَا لَعْنَةً وَيَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ ۗ أَلَآ إِنَّ عَادًا كَفَرُوا۟ رَبَّهُمْ ۗ أَلَا بُعْدًا لِّعَادٍ قَوْمِ هُودٍ ٦٠

61. ወደ ሰሙዶችም ወንድማቸውን ሷሊህን (ላክን)፡፡ «ሕዝቦቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ለእናንተ አምላክ የላችሁም፡፡ እርሱ ከምድር ፈጠራችሁ፡፡ በውስጧ እንድታለሟትም አደረጋችሁ፡፡ ምሕረቱንም ለምኑት፡፡ ከዚህም ወደእርሱ ተመለሱ፡፡ ጌታዬ ቅርብ (ለለመነው) ተቀባይ ነውና» አላቸው፡፡

۞ وَإِلَىٰ ثَمُودَ أَخَاهُمْ صَٰلِحًا ۚ قَالَ يَٰقَوْمِ ٱعْبُدُوا۟ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنْ إِلَٰهٍ غَيْرُهُۥ ۖ هُوَ أَنشَأَكُم مِّنَ ٱلْأَرْضِ وَٱسْتَعْمَرَكُمْ فِيهَا فَٱسْتَغْفِرُوهُ ثُمَّ تُوبُوٓا۟ إِلَيْهِ ۚ إِنَّ رَبِّى قَرِيبٌ مُّجِيبٌ ٦١

62. «ሷሊህ ሆይ! ከዚህ በፊት በእኛ ውስጥ (መሪ ልትሆን) በእርግጥ የምትከጅል ነበርክ፡፡ አባቶቻችን የሚገዙትን ከመገዛት ትከለክለናለህን እኛም ወደርሱ ከምትጠራን ነገር በእርግጥ አወላዋይ በሆነ መጠራጠር ውስጥ ነን» አሉ፡፡

قَالُوا۟ يَٰصَٰلِحُ قَدْ كُنتَ فِينَا مَرْجُوًّا قَبْلَ هَٰذَآ ۖ أَتَنْهَىٰنَآ أَن نَّعْبُدَ مَا يَعْبُدُ ءَابَآؤُنَا وَإِنَّنَا لَفِى شَكٍّ مِّمَّا تَدْعُونَآ إِلَيْهِ مُرِيبٍ ٦٢

63. «ሕዝቦቼ ሆይ! ንገሩኝ ከጌታዬ በሆነ ማስረጃ ላይ ብሆን ከእርሱም የሆነን ችሮታ (ነቢይነት) ቢሰጠኝና ባልታዘዘው ከአላህ (ቅጣት) የሚያድነኝ ማነው ከማሳሳትም በስተቀር ምንም አትጨምሩልኝም» አላቸው::

قَالَ يَٰقَوۡمِ أَرَءَيۡتُمۡ إِن كُنتُ عَلَىٰ بَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّي وَءَاتَىٰنِي مِنۡهُ رَحۡمَةٗ فَمَن يَنصُرُنِي مِنَ ٱللَّهِ إِنۡ عَصَيۡتُهُۥۖ فَمَا تَزِيدُونَنِي غَيۡرَ تَخۡسِيرٖ ﴿٦٣﴾

64. ሕዝቦቼም ሆይ! ይህቺ ለእናንተ ተዓምር ስትሆን የአላህ ግመል ናት:: ተውዋትም:: በአላህ ምድር ውስጥ ትብላ:: በክፉም አትንኳት:: ቅርብ የሆነ ቅጣት ይይዛችኋልና» (አላቸው)::

وَيَٰقَوۡمِ هَٰذِهِۦ نَاقَةُ ٱللَّهِ لَكُمۡ ءَايَةٗۖ فَذَرُوهَا تَأۡكُلۡ فِيٓ أَرۡضِ ٱللَّهِۖ وَلَا تَمَسُّوهَا بِسُوٓءٖ فَيَأۡخُذَكُمۡ عَذَابٞ قَرِيبٞ ﴿٦٤﴾

65. ወግተው ገደሏትም:: (ሷሊህ) «በአገራችሁም ሶስትን ቀናት (ብቻ) ተጠቀሙ:: ይህ የማይዋሽ ቀጠሮ ነው» አላቸው::

فَعَقَرُوهَا فَقَالَ تَمَتَّعُواْ فِي دَارِكُمۡ ثَلَٰثَةَ أَيَّامٖۖ ذَٰلِكَ وَعۡدٌ غَيۡرُ مَكۡذُوبٖ ﴿٦٥﴾

66. ትዕዛዛችንም በመጣ ጊዜ ሷሊህንና እነዚያን ከሱ ጋር ያመኑትን ከእኛ በሆነው እዝነት አዳን:: ከዚያም ቀን ውርደት (አዳንናቸው):: ጌታህ እርሱ ብርቱው አሸናፊው ነውና::

فَلَمَّا جَآءَ أَمۡرُنَا نَجَّيۡنَا صَٰلِحٗا وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَهُۥ بِرَحۡمَةٖ مِّنَّا وَمِنۡ خِزۡيِ يَوۡمِئِذٍۚ إِنَّ رَبَّكَ هُوَ ٱلۡقَوِيُّ ٱلۡعَزِيزُ ﴿٦٦﴾

67. እነዚያንም የበደሉትን ጩኸት ያዛቸው:: በቤቶቻቸውም ውስጥ የተንበረከኩ ሆነው ሞተው አነጉ::

وَأَخَذَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ ٱلصَّيۡحَةُ فَأَصۡبَحُواْ فِي دِيَٰرِهِمۡ جَٰثِمِينَ ﴿٦٧﴾

68. በእሷ ውስጥ እንዳልኖሩባት ሆኑ:: ንቁ! ሰሙዶች ጌታቸውን በእርግጥ ካዱ:: ንቁ! ለሰሙዶች (ከአላህ እዝነት) መራቅ ተገባቸው::

كَأَن لَّمۡ يَغۡنَوۡاْ فِيهَآۗ أَلَآ إِنَّ ثَمُودَاْ كَفَرُواْ رَبَّهُمۡۗ أَلَا بُعۡدٗا لِّثَمُودَ ﴿٦٨﴾

69. መልክተኞቻችንም ኢብራሂምን በ(ልጅ) ብስራት በእርግጥ መጡት:: ሰላም አሉት:: ሰላም አላቸው:: ጥቂትም ሳይቆይ ወዲያውኑ የተጠበሰን የወይፈን ስጋ አመጣ::

وَلَقَدۡ جَآءَتۡ رُسُلُنَآ إِبۡرَٰهِيمَ بِٱلۡبُشۡرَىٰ قَالُواْ سَلَٰمٗاۖ قَالَ سَلَٰمٞۖ فَمَا لَبِثَ أَن جَآءَ بِعِجۡلٍ حَنِيذٖ ﴿٦٩﴾

70. እጆቻቸውም ወደ እርሱ የማይደርሱ መኾናቸውን ባየ ጊዜ ሸሻቸው:: ከነሱም ፍርሃት ተሰማው:: «አትፍራ እኛ ወደ ሉጥ ሕዝቦች ተልከናልና» አሉት::

فَلَمَّا رَءَآ أَيۡدِيَهُمۡ لَا تَصِلُ إِلَيۡهِ نَكِرَهُمۡ وَأَوۡجَسَ مِنۡهُمۡ خِيفَةٗۚ قَالُواْ لَا تَخَفۡ إِنَّآ أُرۡسِلۡنَآ إِلَىٰ قَوۡمِ لُوطٖ ﴿٧٠﴾

71. ሚስቱም የቆመች ስትኾን (አትፍራ አሉት) ሳቀችም:: በኢስሐቅም አበሰርናት:: ከኢስሐቅም በኋላ (በልጁ) በያዕቁብ (አበሰርናት)::

وَٱمۡرَأَتُهُۥ قَآئِمَةٞ فَضَحِكَتۡ فَبَشَّرۡنَٰهَا بِإِسۡحَٰقَ وَمِن وَرَآءِ إِسۡحَٰقَ يَعۡقُوبَ ﴿٧١﴾

72. (እርሷም) ዋልኝ! እኔ አሮጊት ይህም ባሌ ሽማግሌ ሆኖ ሳለ እወልዳለሁን ይህ በእርግጥ አስደናቂ ነገር ነው አለች::

قَالَتۡ يَٰوَيۡلَتَىٰٓ ءَأَلِدُ وَأَنَا۠ عَجُوزٞ وَهَٰذَا بَعۡلِي شَيۡخًاۖ إِنَّ هَٰذَا لَشَيۡءٌ عَجِيبٞ ﴿٧٢﴾

73. «ከአላህ ትዕዛዝ ትደነቂያለሽን የአላህ ችሮታና በረከቶቹ በእናንተ በኢብራሂም ቤተሰቦች ላይ ይሁን እርሱ ምስጉን ሊጋስ ነውና» አሉ፡፡

قَالُوٓاْ أَتَعۡجَبِينَ مِنۡ أَمۡرِ ٱللَّهِۖ رَحۡمَتُ ٱللَّهِ وَبَرَكَٰتُهُۥ عَلَيۡكُمۡ أَهۡلَ ٱلۡبَيۡتِۚ إِنَّهُۥ حَمِيدٞ مَّجِيدٞ ٧٣

74. ከኢብራሂም ፍራቻው በሌደለትና ብስራት በመጣችለትም ጊዜ በሉጥ ሕዝቦች (ነገር) ይከራከረን ጀመር፡፡

فَلَمَّا ذَهَبَ عَنۡ إِبۡرَٰهِيمَ ٱلرَّوۡعُ وَجَآءَتۡهُ ٱلۡبُشۡرَىٰ يُجَٰدِلُنَا فِي قَوۡمِ لُوطٍ ٧٤

75. ኢብራሂም በእርግጥ ታጋሽ አልቃሻ መላሳ ነውና፡፡

إِنَّ إِبۡرَٰهِيمَ لَحَلِيمٌ أَوَّٰهٞ مُّنِيبٞ ٧٥

76. «ኢብራሂም ሆይ! ከዚህ (ክርክር) ተው፡፡ እነሆ የጌታህ ትዕዛዝ በእርግጥ መጥቷል፡፡ እነሱም የማይመለስ ቅጣት የሚመጣባቸው ናቸው» (አሉት)፡፡

يَٰٓإِبۡرَٰهِيمُ أَعۡرِضۡ عَنۡ هَٰذَآۖ إِنَّهُۥ قَدۡ جَآءَ أَمۡرُ رَبِّكَۖ وَإِنَّهُمۡ ءَاتِيهِمۡ عَذَابٌ غَيۡرُ مَرۡدُودٖ ٧٦

77. መልክተኞቻችንም ሉጥን በመጡት ጊዜ በነሱ (ምክንያት) አዘነ፡፡ ልቡም በነሱ ተጨነቀ፡፡ «ይህ ብርቱ ቀን ነውም» አለ፡፡

وَلَمَّا جَآءَتۡ رُسُلُنَا لُوطٗا سِيٓءَ بِهِمۡ وَضَاقَ بِهِمۡ ذَرۡعٗا وَقَالَ هَٰذَا يَوۡمٌ عَصِيبٞ ٧٧

78. ሕዝቦቹም ወደርሱ እየተጣደፉ መጡት፡፡ ከዚህም በፊት መጥፎ ሥራዎችን ይሠሩ ነበር፡፡ «ሕዝቦቼ ሆይ! እኚህ ሴቶች ልጆቼ ናቸው፡፡ እነሱ ለእናንተ ይልቅ በጣም የጸዱ ናቸው፤ (አግቧቸው)፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ በእንግዶቼም አታሳፍሩኝ፡፡ ከእናንተ ውስጥ ቅን ሰው የለምን» አላቸው፡፡

وَجَآءَهُۥ قَوۡمُهُۥ يُهۡرَعُونَ إِلَيۡهِ وَمِن قَبۡلُ كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٱلسَّيِّـَٔاتِۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ هَٰٓؤُلَآءِ بَنَاتِي هُنَّ أَطۡهَرُ لَكُمۡۖ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَلَا تُخۡزُونِ فِي ضَيۡفِيٓۖ أَلَيۡسَ مِنكُمۡ رَجُلٞ رَّشِيدٞ ٧٨

79. «ከሴቶች ልጆችህ ለእኛ ምንም ጉዳይ የለንም፡፡ አንተም የምንሻውን በእርግጥ ታውቃለህ» አሉት፡፡

قَالُواْ لَقَدۡ عَلِمۡتَ مَا لَنَا فِي بَنَاتِكَ مِنۡ حَقّٖ وَإِنَّكَ لَتَعۡلَمُ مَا نُرِيدُ ٧٩

80. «በእናንተ ላይ ለኔ ኀይል በኖረኝ ወይም ወደ ብርቱ ወገን ብጠጋ ኖሮ (የምሠራውን በሠራሁ ነበር)» አላቸው፡፡

قَالَ لَوۡ أَنَّ لِي بِكُمۡ قُوَّةً أَوۡ ءَاوِيٓ إِلَىٰ رُكۡنٖ شَدِيدٖ ٨٠

81. «ሉጥ ሆይ! እኛ የጌታህ መልክተኞች ነን፡፡ (ሕዝቦችህ) ወደ አንተ (በክፉ) አይደርሱብህም፡፡ ቤተሰብህንም ይዘህ ከሌሊቱ በከፊሉ ውስጥ ሊድ፡፡ ከእናንተም አንድም (ወደኋላው) አይገላመጥ፡፡ ሚስትህ ብቻ ስትቀር፡፡ እነሆ እርሷን (እነሱን) የሚያገኛቸው ስቃይ ያገኛታልና፡፡ ቀጠሯቸው እንጋቱ ላይ ነው፡፡ ንጋቱ ቅርብ አይደለምን» አሉት፡፡

قَالُواْ يَٰلُوطُ إِنَّا رُسُلُ رَبِّكَ لَن يَصِلُوٓاْ إِلَيۡكَۖ فَأَسۡرِ بِأَهۡلِكَ بِقِطۡعٖ مِّنَ ٱلَّيۡلِ وَلَا يَلۡتَفِتۡ مِنكُمۡ أَحَدٌ إِلَّا ٱمۡرَأَتَكَۖ إِنَّهُۥ مُصِيبُهَا مَآ أَصَابَهُمۡۚ إِنَّ مَوۡعِدَهُمُ ٱلصُّبۡحُۚ أَلَيۡسَ ٱلصُّبۡحُ بِقَرِيبٖ ٨١

82. 82. ትዕዛዛችንም በመጣ ጊዜ (ከተማይቱን) ላይዋን ከታችዋ አደረግን (ገለበጥናት)፡፡ ተከታታይም የሆነን የሸክላ ድንጋይ በርሷ ላይ አዘነብን፡፡

فَلَمَّا جَآءَ أَمۡرُنَا جَعَلۡنَا عَٰلِيَهَا سَافِلَهَا وَأَمۡطَرۡنَا عَلَيۡهَا حِجَارَةٗ مِّن سِجِّيلٖ مَّنضُودٖ ٨٢

83. ከጌታህ ዘንድ ምልክት የተደረገባት ስትሆን (አዘነብናት)፡፡ እርሷም ከበደለኞቹ ሩቅ አይደለችም፡፡

مُّسَوَّمَةً عِندَ رَبِّكَۖ وَمَا هِيَ مِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ بِبَعِيدٖ ٨٣

84. ወደ መድየንም ወንድማቸውን ሹዐይብን (ላክን)፡፡ አላቸው «ሕዝቦቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ለናንተ አምላክ የላችሁም፡፡ ስፍርንና ሚዛንንም አታጉድሉ፤ እኔ በጸጋ ላይ ሆናችሁ አያችኋለሁ፡፡ እኔም በእናንተ ላይ የከባቢን ቀን ቅጣት እፈራለሁ፡፡

۞وَإِلَىٰ مَدۡيَنَ أَخَاهُمۡ شُعَيۡبٗاۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرُهُۥۖ وَلَا تَنقُصُواْ ٱلۡمِكۡيَالَ وَٱلۡمِيزَانَۖ إِنِّيٓ أَرَىٰكُم بِخَيۡرٖ وَإِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ عَذَابَ يَوۡمٖ مُّحِيطٖ ﴿٨٤﴾

85. «ሕዝቦቼም ሆይ! ስፍርንና ሚዛንን በትክክል ሙሉ፡፡ ሰዎችንም ምንም ነገራቸውን አታጉድሉባቸው፡ ፡ በምድርም ውስጥ አጥፊዎች ሆናችሁ አታበላሹ፡፡

وَيَٰقَوۡمِ أَوۡفُواْ ٱلۡمِكۡيَالَ وَٱلۡمِيزَانَ بِٱلۡقِسۡطِۖ وَلَا تَبۡخَسُواْ ٱلنَّاسَ أَشۡيَآءَهُمۡ وَلَا تَعۡثَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُفۡسِدِينَ ﴿٨٥﴾

86. አላህ ያስቀረላችሁ ለእናንተ የተሻለ ነው፡፡ ምእመናን እንደሆናችሁ (አላህ በሰጣችሁ ውደዱ)፡፡ እኔም (መካሪ እንጅ) በናንተ ላይ ተጠባባቂ አይደለሁም፡፡»

بَقِيَّتُ ٱللَّهِ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَۚ وَمَآ أَنَا۠ عَلَيۡكُم بِحَفِيظٖ ﴿٨٦﴾

87. «ሹዐይብ ሆይ! ስግደትህ አባቶቻችን የሚገዙትን ጣዖታት እንድንተው ወይም በገንዘቦቻችን የምንሻውን መሥራትን (እንድንተው) ታዝሃለችን አንተ በእርግጥ ታጋሹ ቅኑ አንተ ነህና» አሉት፡፡

قَالُواْ يَٰشُعَيۡبُ أَصَلَوٰتُكَ تَأۡمُرُكَ أَن نَّتۡرُكَ مَا يَعۡبُدُ ءَابَآؤُنَآ أَوۡ أَن نَّفۡعَلَ فِيٓ أَمۡوَٰلِنَا مَا نَشَٰٓؤُاْۖ إِنَّكَ لَأَنتَ ٱلۡحَلِيمُ ٱلرَّشِيدُ ﴿٨٧﴾

88. «ሕዝቦቼ ሆይ! ንገሩኝ፤ ከጌታዬ በሆነ አስረጅ ላይ ብሆንና ከእርሱም የሆነን መልካም ሲሳይ ቢሰጠኝ (በቅጥፈት ልቀላቅለው ይገባልን) ከእርሱ ወደ ከለከልኳችሁም ነገር ልለያችሁ አልሻም፡፡ በተቻለኝ ያክል ማበጀትን እንጂ አልሻም (ለደግ ሥራ) መገጠሜም በአላህ እንጂ በሌላ አይደለም፡፡ በእርሱ ላይ ተመካሁ፡፡ ወደእርሱም እመለሳለሁ፤» አላቸው፡፡

قَالَ يَٰقَوۡمِ أَرَءَيۡتُمۡ إِن كُنتُ عَلَىٰ بَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّي وَرَزَقَنِي مِنۡهُ رِزۡقًا حَسَنٗاۚ وَمَآ أُرِيدُ أَنۡ أُخَالِفَكُمۡ إِلَىٰ مَآ أَنۡهَىٰكُمۡ عَنۡهُۚ إِنۡ أُرِيدُ إِلَّا ٱلۡإِصۡلَٰحَ مَا ٱسۡتَطَعۡتُۚ وَمَا تَوۡفِيقِيٓ إِلَّا بِٱللَّهِۚ عَلَيۡهِ تَوَكَّلۡتُ وَإِلَيۡهِ أُنِيبُ ﴿٨٨﴾

89. «ወገኖቼም ሆይ! እኔን መከራከራችሁ የኑሕን ሕዝቦች ወይም የሁድን ሕዝቦች ወይም የሷሊሕን ሕዝቦች ያገኛቸው (ቅጣት) ብጤ እንዲያገኛችሁ አይገፋፋችሁ፡፡ የሉጥም ሕዝቦች ከእናንተ ሩቅ አይደሉም፡፡

وَيَٰقَوۡمِ لَا يَجۡرِمَنَّكُمۡ شِقَاقِيٓ أَن يُصِيبَكُم مِّثۡلُ مَآ أَصَابَ قَوۡمَ نُوحٍ أَوۡ قَوۡمَ هُودٍ أَوۡ قَوۡمَ صَٰلِحٖۚ وَمَا قَوۡمُ لُوطٖ مِّنكُم بِبَعِيدٖ ﴿٨٩﴾

90. «ጌታችሁንም ምሕረትን ለምኑት፡፡ ከዚያም ወደርሱ ተመለሱ፡፡ ጌታዬ አዛኝ ወዳድ ነውና (አላቸው)፡፡

وَٱسۡتَغۡفِرُواْ رَبَّكُمۡ ثُمَّ تُوبُوٓاْ إِلَيۡهِۚ إِنَّ رَبِّي رَحِيمٞ وَدُودٞ ﴿٩٠﴾

91. «ሹዐይብ ሆይ! ከምትለው ነገር ብዙውን አናውቀውም፡፡ እኛም አንተን በእኛ ውስጥ ደካማ ሆነህ እናይሃለን፡፡ ጎሳዎችህም ባልኖሩ ኖሮ በወገርንህ ነበር፤ አንተም በእኛ ላይ የተከበርክ አይደለህም» አሉት፡፡

قَالُواْ يَٰشُعَيۡبُ مَا نَفۡقَهُ كَثِيرٗا مِّمَّا تَقُولُ وَإِنَّا لَنَرَىٰكَ فِينَا ضَعِيفٗاۖ وَلَوۡلَا رَهۡطُكَ لَرَجَمۡنَٰكَۖ وَمَآ أَنتَ عَلَيۡنَا بِعَزِيزٖ ﴿٩١﴾

92. «ሕዝቦቼ ሆይ! ጎሳዎቼ በእናንተ ላይ ከአላህ ይልቅ የከበሩ ናቸውን (አላህን) ከኋላችሁ ወደ ጀርባ አድርጋችሁም ያዛችሁት፡፡ ጌታዬ በምትሠሩት ሁሉ ከባቢ ነው» አላቸው፡፡

قَالَ يَٰقَوۡمِ أَرَهۡطِيٓ أَعَزُّ عَلَيۡكُم مِّنَ ٱللَّهِ وَٱتَّخَذۡتُمُوهُ وَرَآءَكُمۡ ظِهۡرِيًّاۖ إِنَّ رَبِّي بِمَا تَعۡمَلُونَ مُحِيطٞ ﴿٩٢﴾

93. «ሕዝቦቼም ሆይ! በችሎታችሁ ልክ ሥሩ፡፡ እኔ ሠሪ ነኝና፡፡ የሚያዋርደው ቅጣት የሚመጣበትና እርሱ ውሸታም የሆነው ማን እንደኾነ ወደ ፊት ታውቃላችሁ፡፡ ጠብቁም እኔ ከናንተ ጋር ተጠባባቂ ነኝና»(አላቸው)፡፡

وَيَٰقَوۡمِ ٱعۡمَلُواْ عَلَىٰ مَكَانَتِكُمۡ إِنِّي عَٰمِلٞۖ سَوۡفَ تَعۡلَمُونَ مَن يَأۡتِيهِ عَذَابٞ يُخۡزِيهِ وَمَنۡ هُوَ كَٰذِبٞۖ وَٱرۡتَقِبُوٓاْ إِنِّي مَعَكُمۡ رَقِيبٞ ٩٣

94. ትዕዛዛችንም በመጣ ጊዜ ሹዐይብንና እነዚያን ከርሱ ጋር ያመኑትን ከእኛ በሆነው ችሮታ አዳን፡፡ እነዚያን የበደሉትንም (የጂብሪል) ጩኸት ያዘቻቸው፡፡ በቤቶቻቸውም ውስጥ ተንከፍርረው አደሩ፡፡

وَلَمَّا جَآءَ أَمۡرُنَا نَجَّيۡنَا شُعَيۡبٗا وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَهُۥ بِرَحۡمَةٖ مِّنَّا وَأَخَذَتِ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ ٱلصَّيۡحَةُ فَأَصۡبَحُواْ فِي دِيَٰرِهِمۡ جَٰثِمِينَ ٩٤

95. በእርሷ ውስጥ እንዳልነበሩ ሆኑ፡፡ ንቁ! ሰሙድ (ከአላህ እዝነት) እንደ ራቀች መድየንም ትራቅ፡፡

كَأَن لَّمۡ يَغۡنَوۡاْ فِيهَآۗ أَلَا بُعۡدٗا لِّمَدۡيَنَ كَمَا بَعِدَتۡ ثَمُودُ ٩٥

96. ሙሳንም በተዓምራታችንና በግልጽ ብርሃን በእርግጥ ላክነው፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا مُوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَا وَسُلۡطَٰنٖ مُّبِينٍ ٩٦

97. ወደ ፈርዖንና ወደ ሰዎቹ (ላክነው)፡፡ የፈርዖንንም ነገር (ሕዝቦቹ) ተከተሉ፡፡ የፈርዖን ነገርም ቀጥተኛ አልነበረም፡፡

إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِۦ فَٱتَّبَعُوٓاْ أَمۡرَ فِرۡعَوۡنَۖ وَمَآ أَمۡرُ فِرۡعَوۡنَ بِرَشِيدٖ ٩٧

98. በትንሣኤ ቀን ሕዝቦቹን ይቀድማል፡፡ ወደ እሳትም ያወርዳቸዋል፡፡ የሚገቡትም አገባብ ምንኛ ከፋ!

يَقۡدُمُ قَوۡمَهُۥ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فَأَوۡرَدَهُمُ ٱلنَّارَۖ وَبِئۡسَ ٱلۡوِرۡدُ ٱلۡمَوۡرُودُ ٩٨

99. በዚችም (በቅርቢቱ ዓለም) እርግማንን አስከተልናቸው፡፡ በትንሣኤም ቀን (እንደዚሁ)፡፡ የተሰጡት ስጦታ ምንኛ ከፋ!

وَأُتۡبِعُواْ فِي هَٰذِهِۦ لَعۡنَةٗ وَيَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ بِئۡسَ ٱلرِّفۡدُ ٱلۡمَرۡفُودُ ٩٩

100. ይህ (የተነገረው) ከከተሞቹ ወሬዎች ነው፡፡ ባንተ ላይ እንተርከዋለን፡፡ ከእርሷ ፋናው የቀረና ሙሉ በሙሉ የተደመሰሰ አለ፡፡

ذَٰلِكَ مِنۡ أَنۢبَآءِ ٱلۡقُرَىٰ نَقُصُّهُۥ عَلَيۡكَۖ مِنۡهَا قَآئِمٞ وَحَصِيدٞ ١٠٠

101. እኛም አልበደልናቸውም፡፡ ግን ነፍሶቻቸውን በደሉ፡፡ የአላህም ትእዛዝ በመጣ ጊዜ እነዚያ ከአላህ ሌላ የሚገዙዋቸው አማልክቶቻቸው በምንም አላዳኗቸውም፡፡ ከማክሰርም በቀር ምንም አልጨመሩላቸውም፡፡

وَمَا ظَلَمۡنَٰهُمۡ وَلَٰكِن ظَلَمُوٓاْ أَنفُسَهُمۡۖ فَمَآ أَغۡنَتۡ عَنۡهُمۡ ءَالِهَتُهُمُ ٱلَّتِي يَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مِن شَيۡءٖ لَّمَّا جَآءَ أَمۡرُ رَبِّكَۖ وَمَا زَادُوهُمۡ غَيۡرَ تَتۡبِيبٖ ١٠١

102. የጌታህም ቅጣት የከተሞችን ሰዎች እነሱ በዳዮች ሲሆኑ በቀጣቸው ጊዜ እንደዚህ ነው፡፡ ቅጣቱ በእርግጥ አሳማሚ ብርቱ ነው፡፡

وَكَذَٰلِكَ أَخۡذُ رَبِّكَ إِذَآ أَخَذَ ٱلۡقُرَىٰ وَهِيَ ظَٰلِمَةٌۚ إِنَّ أَخۡذَهُۥٓ أَلِيمٞ شَدِيدٌ ١٠٢

103. በዚህ ውስጥ የመጨረሻውን ቀን ቅጣት ለሚፈሩ ሁሉ መገሰጫ አለ፡፡ ይህ (የትንሣኤ ቀን) ሰዎች በርሱ የሚሰበሰቡበት ቀን ነው፡፡ ይህም የሚጣዱት ቀን ነው፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّمَنۡ خَافَ عَذَابَ ٱلۡأٓخِرَةِۚ ذَٰلِكَ يَوۡمٞ مَّجۡمُوعٞ لَّهُ ٱلنَّاسُ وَذَٰلِكَ يَوۡمٞ مَّشۡهُودٞ ١٠٣

104. (ይህንን ቀን) ለተቆጠረም ጊዜ እንጂ አናቆየውም፡፡

وَمَا نُؤَخِّرُهُۥٓ إِلَّا لِأَجَلٖ مَّعۡدُودٖ ١٠٤

105. በሚመጣ ቀን ማንኛዋም ነፍስ በእርሱ ፈቃድ ቢሆን እንጂ አትናገርም፡፡ ከነሱም መናጢና ዕድለኛም አልለ፡፡

يَوۡمَ يَأۡتِ لَا تَكَلَّمُ نَفۡسٌ إِلَّا بِإِذۡنِهِۦۚ فَمِنۡهُمۡ شَقِيّٞ وَسَعِيدٞ ١٠٥

106. እነዚያ መናጢ የሆኑትማ፡ በእሳት ውስጥ ናቸው፡ ፡ ለእነርሱ በእርሷ ውስጥ ማናፋትና መንሰቅሰቅ አላቸው፡፡

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ شَقُواْ فَفِي ٱلنَّارِ لَهُمۡ فِيهَا زَفِيرٞ وَشَهِيقٌ ١٠٦

107. ጌታህ ከሻው (ጭማሪ) ሌላ ሰማያትና ምድር እስከ ዘወተሩ ድረስ በውስጧ ዘውተሪዎች ሲኾኑ (በእሳት ይኖራሉ)፡፡ ጌታህ የሚሻውን ሠሪ ነውና፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَا مَا دَامَتِ ٱلسَّمَٰوَٰتُ وَٱلۡأَرۡضُ إِلَّا مَا شَآءَ رَبُّكَۚ إِنَّ رَبَّكَ فَعَّالٞ لِّمَا يُرِيدُ ١٠٧

108. እነዚያም ዕድለኞቹማ ጌታህ ከሻው (ጭማሪ) ሌላ ሰማያትና ምድር እስከ ዘወተሩ ድረስ በውስጧ ዘውታሪዎች ኾነው በገነት ውስጥ ይኖራሉ፡፡ የማይቋረጥ ስጦታን ተሰጡ፡፡

۞وَأَمَّا ٱلَّذِينَ سُعِدُواْ فَفِي ٱلۡجَنَّةِ خَٰلِدِينَ فِيهَا مَا دَامَتِ ٱلسَّمَٰوَٰتُ وَٱلۡأَرۡضُ إِلَّا مَا شَآءَ رَبُّكَۖ عَطَآءً غَيۡرَ مَجۡذُوذٖ ١٠٨

109. እነዚህ (ከሓዲዎች) ከሚገዙት ጣዖት በመጠራጠር ውስጥ አትሁን፤ አባቶቻቸው ከዚህ በፊት እንደሚገዙት እንጂ አይግገዙም፡፡ እኛም (እነዚህን) ፈንታቸውን የማይጓደል ሲሆን የምንሞላላቸው ነን፡፡

فَلَا تَكُ فِي مِرۡيَةٖ مِّمَّا يَعۡبُدُ هَٰٓؤُلَآءِۚ مَا يَعۡبُدُونَ إِلَّا كَمَا يَعۡبُدُ ءَابَآؤُهُم مِّن قَبۡلُۚ وَإِنَّا لَمُوَفُّوهُمۡ نَصِيبَهُمۡ غَيۡرَ مَنقُوصٖ ١٠٩

110. ለሙሳም መጽሐፍን በእርግጥ ሰጠነው፡፡ በእርሱም ተለያዩበት፡፡ ከጌታህም ያለፈች ቃል ባልነበረች ኖሮ በመካከላቸው (አሁን) ይፈረድ ነበር፡፡ እነሱም ከእርሱ (ከቁርኣን) አወላዋይ በሆነ መጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡكِتَٰبَ فَٱخۡتُلِفَ فِيهِۚ وَلَوۡلَا كَلِمَةٞ سَبَقَتۡ مِن رَّبِّكَ لَقُضِيَ بَيۡنَهُمۡۚ وَإِنَّهُمۡ لَفِي شَكّٖ مِّنۡهُ مُرِيبٖ ١١٠

111. ሁሉንም ጌታህ ሥራዎቻቸውን (ምንዳቸውን) በእርግጥ ይሞላላቸዋል፡፡ እርሱ በሚሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَإِنَّ كُلّٗا لَّمَّا لَيُوَفِّيَنَّهُمۡ رَبُّكَ أَعۡمَٰلَهُمۡۚ إِنَّهُۥ بِمَا يَعۡمَلُونَ خَبِيرٞ ١١١

112. እንደ ታዘዝከውም ቀጥ በል፡፡ ከአንተ ጋር ያመኑትም (ቀጥ ይበሉ)፡፡ ወሰንንም አትለፉ፤ እርሱ የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነውና፡፡

فَٱسۡتَقِمۡ كَمَآ أُمِرۡتَ وَمَن تَابَ مَعَكَ وَلَا تَطۡغَوۡاْۚ إِنَّهُۥ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ١١٢

113. ወደእነዚያም ወደ በደሉት አትጠጉ፡፡ እሳት ትነካችኋለችና፡፡ ከአላህም ሌላ ጠባቂዎች የሏችሁም፡፡ ከዚያም አትረድዱም፡፡

وَلَا تَرۡكَنُوٓاْ إِلَى ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ فَتَمَسَّكُمُ ٱلنَّارُ وَمَا لَكُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ مِنۡ أَوۡلِيَآءَ ثُمَّ لَا تُنصَرُونَ ١١٣

114. ሶላትንም በቀን ጫፎች ከሌሊትም ክፍሎች ፈጽም፡፡ መልካም ሥራዎች ኀጢአቶችን ያስወገድዳሉና፡፡ ይህ ለተገሳጮች ግሳጼ ነው፡፡

وَأَقِمِ ٱلصَّلَوٰةَ طَرَفَيِ ٱلنَّهَارِ وَزُلَفٗا مِّنَ ٱلَّيۡلِۚ إِنَّ ٱلۡحَسَنَٰتِ يُذۡهِبۡنَ ٱلسَّيِّـَٔاتِۚ ذَٰلِكَ ذِكۡرَىٰ لِلذَّٰكِرِينَ ١١٤

115. ታገስም፤ አላህ የበጎ ሠሪዎችን ምንዳ አያጠፋምና፡፡

وَٱصۡبِرۡ فَإِنَّ ٱللَّهَ لَا يُضِيعُ أَجۡرَ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١١٥

116. ከእናንተም በፊት ከነበሩት ከክፍለ ዘመናት ሰዎች ውስጥ በምድር ላይ ከማበላሸት የሚከለክሉ የመልካም ቀሪ ሥራዎች ባለቤቶች ለምን አልነበሩም ግን ከእነሱ ያዳንናቸው ጥቂቶቹ (ከለከሉና ዳኑ)፡፡ እነዚያም የበደሉት ሰዎች (አልከለከሉም)፡፡ በእርሱ የተቀማጠሉበትን ተድላ ተከተሉ፡፡ አመጸኞችም ነበሩ፡፡

فَلَوۡلَا كَانَ مِنَ ٱلۡقُرُونِ مِن قَبۡلِكُمۡ أُوْلُواْ بَقِيَّةٖ يَنۡهَوۡنَ عَنِ ٱلۡفَسَادِ فِي ٱلۡأَرۡضِ إِلَّا قَلِيلٗا مِّمَّنۡ أَنجَيۡنَا مِنۡهُمۡۗ وَٱتَّبَعَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مَآ أُتۡرِفُواْ فِيهِ وَكَانُواْ مُجۡرِمِينَ ١١٦

117. ጌታህም ከተሞችን ባለቤቶቻቸው መልካም ሠሪዎች ሆነው ሳሉ በመበደል የሚያጠፋቸው አልነበረም፡፡

وَمَا كَانَ رَبُّكَ لِيُهۡلِكَ ٱلۡقُرَىٰ بِظُلۡمٖ وَأَهۡلُهَا مُصۡلِحُونَ ١١٧

118. ጌታህም በሻ ኖሮ ሰዎችን ሁሉ አንድ ሕዝብ ባደረጋቸው ነበር፡፡ የተለያዩም ከመሆን አይወገዱም፡፡

وَلَوۡ شَآءَ رَبُّكَ لَجَعَلَ ٱلنَّاسَ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗۖ وَلَا يَزَالُونَ مُخۡتَلِفِينَ ١١٨

119. ጌታህ ያዘነለት ብቻ ሲቀር፤ (ከመለያየት አይወገዱም)፡፡ ለዚሁም ፈጠራቸው፡፡ የጌታህም ቃል ገሀነምን ከአጋንንትና ከሰዎች ከሁሉም በእርግጥ እሞላታለሁ በማለት ተፈጸመች፡፡

إِلَّا مَن رَّحِمَ رَبُّكَۚ وَلِذَٰلِكَ خَلَقَهُمۡۗ وَتَمَّتۡ كَلِمَةُ رَبِّكَ لَأَمۡلَأَنَّ جَهَنَّمَ مِنَ ٱلۡجِنَّةِ وَٱلنَّاسِ أَجۡمَعِينَ ١١٩

120. ከመልክተኞቹም ዜናዎች (ተፈላጊውን) ሁሉንም ልብህን በርሱ የምናረካበትን እንተርክልሃለን፡፡ በዚህችም (ሱራ) እውነቱ ነገር ለምእምናን ግሳጼና ማስታወሻ መጥቶልሃል፡፡

وَكُلّٗا نَّقُصُّ عَلَيۡكَ مِنۡ أَنۢبَآءِ ٱلرُّسُلِ مَا نُثَبِّتُ بِهِۦ فُؤَادَكَۚ وَجَآءَكَ فِي هَٰذِهِ ٱلۡحَقُّ وَمَوۡعِظَةٞ وَذِكۡرَىٰ لِلۡمُؤۡمِنِينَ ١٢٠

121. ለእነዚያም ለማያምኑት ባላችሁበት ሁኔታ ላይ ሥሩ፤ እኛ ሠሪዎች ነንና በላቸው፡፡

وَقُل لِّلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ ٱعۡمَلُواْ عَلَىٰ مَكَانَتِكُمۡ إِنَّا عَٰمِلُونَ ١٢١

122. ተጠባበቁም እኛ ተጠባባቂዎች ነንና (በላቸው)፡፡

وَٱنتَظِرُوٓاْ إِنَّا مُنتَظِرُونَ ١٢٢

123. በሰማያትና በምድርም ያለው ምስጢር ሁሉ የአላህ ነው፡፡ ነገሩ ሁሉም ወደርሱ ይመለሳል፡፡ ስለዚህ ተገዛው፡፡ በእርሱም ላይ ተጠጋ፡፡ ጌታህም ከሚሠሩት ሁሉ ዘንጊ አይደለም፡፡

وَلِلَّهِ غَيۡبُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَإِلَيۡهِ يُرۡجَعُ ٱلۡأَمۡرُ كُلُّهُۥ فَٱعۡبُدۡهُ وَتَوَكَّلۡ عَلَيۡهِۚ وَمَا رَبُّكَ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ١٢٣

## ሱረቱ ዩሱፍ

## سورة يوسف

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ሊ.ረ (አሊፍ ላም ራ) እነዚህ የገላጩ መጽሐፍ አንቀጾች ናቸው፡፡

الٓرۚ تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱلۡكِتَٰبِ ٱلۡمُبِينِ ١

2. እኛ (ፍቹን) ታውቁ ዘንድ ዐረብኛ ቁርኣን ሲሆን በእርግጥ አወረድነው፡፡

إِنَّآ أَنزَلۡنَٰهُ قُرۡءَٰنًا عَرَبِيّٗا لَّعَلَّكُمۡ تَعۡقِلُونَ ٢

3. እኛ ይህንን ቁርአን ወደ አንተ በማውረዳችን በጣም መልካም ዜናዎችን በአንተ ላይ እንተርክልሃለን፡፡ እነሆ ከእርሱ በፊት (ካለፉት ሕዝቦች ታሪክ) በእርግጥ ከዘንጊዎቹ ነበርክ፡፡

نَحۡنُ نَقُصُّ عَلَيۡكَ أَحۡسَنَ ٱلۡقَصَصِ بِمَآ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانَ وَإِن كُنتَ مِن قَبۡلِهِۦ لَمِنَ ٱلۡغَٰفِلِينَ ٣

4. ዩሱፍ ለአባቱ፡- «አባቴ ሆይ! እኔ ዐስራ አንድ ከዋክብትን ፀሐይንና ጨረቃንም (በሕልሜ) አየሁ፡፡ ለእኔ ሰጋጆች ሆነው አየኋቸው» ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ قَالَ يُوسُفُ لِأَبِيهِ يَٰٓأَبَتِ إِنِّي رَأَيۡتُ أَحَدَ عَشَرَ كَوۡكَبٗا وَٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَ رَأَيۡتُهُمۡ لِي سَٰجِدِينَ ٤

5. (አባቱም) አለ «ልጄ ሆይ! ሕልምህን ለወንድሞችህ አታውራ፡፡ ላንተ ተንኮልን ይሰሩብሃልና፡፡ ሰይጣን ለሰው ግልጽ ጠላት ነውና፡፡»

قَالَ يَٰبُنَيَّ لَا تَقۡصُصۡ رُءۡيَاكَ عَلَىٰٓ إِخۡوَتِكَ فَيَكِيدُواْ لَكَ كَيۡدًاۖ إِنَّ ٱلشَّيۡطَٰنَ لِلۡإِنسَٰنِ عَدُوّٞ مُّبِينٞ ٥

6. «እንደዚሁም (እንዳየኸው) ጌታህ ይመርጥሃል፡፡ ከንግግሮችም ፍች ያስተምርሃል፡፡ ጸጋውንም ከአሁን በፊት በሁለቱ አባቶችህ በኢብራሂምና በኢስሐቅ ላይ እንዳሟላት በአንተ ላይና በያዕቆብ ዘሮችም ላይ ይሞላታል፡፡ ጌታህ ዐዋቂ ጥበበኛ ነውና፡፡»

وَكَذَٰلِكَ يَجۡتَبِيكَ رَبُّكَ وَيُعَلِّمُكَ مِن تَأۡوِيلِ ٱلۡأَحَادِيثِ وَيُتِمُّ نِعۡمَتَهُۥ عَلَيۡكَ وَعَلَىٰٓ ءَالِ يَعۡقُوبَ كَمَآ أَتَمَّهَا عَلَىٰٓ أَبَوَيۡكَ مِن قَبۡلُ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡحَٰقَۚ إِنَّ رَبَّكَ عَلِيمٌ حَكِيمٞ ٦

7. በዩሱፍና በወንድሞቹ (ታሪኮች) ውስጥ ለጠያቂዎች ሁሉ በእርግጥ አስደናቂ ምልክቶች ነበሩ፡፡

۞لَّقَدۡ كَانَ فِي يُوسُفَ وَإِخۡوَتِهِۦٓ ءَايَٰتٞ لِّلسَّآئِلِينَ ٧

8. (ወንድሞቹ) ባሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «እኛ ጭፍሮች ስንሆን ዩሱፍና ወንድሙ (ብንያም) ወደ አባታችን ከእኛ ይበልጥ የተወደዱ ናቸው፡፡ አባታችን በግልጽ ስህተት ውስጥ ነው፡፡

إِذۡ قَالُواْ لَيُوسُفُ وَأَخُوهُ أَحَبُّ إِلَىٰٓ أَبِينَا مِنَّا وَنَحۡنُ عُصۡبَةٌ إِنَّ أَبَانَا لَفِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ٨

9. «ዩሱፍን ግደሉ፡፡ ወይም በ(ሩቅ) ምድር ላይ ጣሉት፡፡ ያባታችሁ ፊት ለእናንተ የግል ይኾናልና፡፡ ከእርሱም በኋላ መልካም ሕዝቦች ትሆናላችሁና» (ተባባሉ)፡፡

ٱقۡتُلُواْ يُوسُفَ أَوِ ٱطۡرَحُوهُ أَرۡضٗا يَخۡلُ لَكُمۡ وَجۡهُ أَبِيكُمۡ وَتَكُونُواْ مِنۢ بَعۡدِهِۦ قَوۡمٗا صَٰلِحِينَ ٩

10. ከእነሱ አንድ ተናጋሪ «ዩሱፍን አትግደሉ ግን በጉድጓድ አዘቅት ጨለማ ውስጥ ጣሉት፤ ከተጓዢዎች አንዱ ያነሳዋልና፡፡ ሠሪዎች ብትኾኑ (በዚሁ ተብቃቁ) አላቸው፡፡

قَالَ قَآئِلٞ مِّنۡهُمۡ لَا تَقۡتُلُواْ يُوسُفَ وَأَلۡقُوهُ فِي غَيَٰبَتِ ٱلۡجُبِّ يَلۡتَقِطۡهُ بَعۡضُ ٱلسَّيَّارَةِ إِن كُنتُمۡ فَٰعِلِينَ ١٠

11. (እነሱም) አሉ «አባታችን ሆይ! በዩሱፍ ላይ ለምን አታምነንም እኛም ለእርሱ በእርግጥ አዛኞች ነን፡፡»

قَالُواْ يَٰٓأَبَانَا مَا لَكَ لَا تَأۡمَ۬نَّا عَلَىٰ يُوسُفَ وَإِنَّا لَهُۥ لَنَٰصِحُونَ ١١

12. «ነገ ከእኛ ጋር ላከውና ይደሰት፤ ይጫወትም፡፡ እኛም ለእርሱ ጠባቂዎች ነን፡፡»

أَرۡسِلۡهُ مَعَنَا غَدٗا يَرۡتَعۡ وَيَلۡعَبۡ وَإِنَّا لَهُۥ لَحَٰفِظُونَ ١٢

13. «እኔ እርሱን (ዩሱፍን) ይዛችሁ መሌዳችሁ በእርግጥ ያሳዝነኛል፡፡ እናንተም ከእርሱ ዘንጊዎች ስትሆኑ ተኩላ ይበላዋል ብዬ እፈራለሁ» አላቸው፡፡

قَالَ إِنِّي لَيَحۡزُنُنِيٓ أَن تَذۡهَبُواْ بِهِۦ وَأَخَافُ أَن يَأۡكُلَهُ ٱلذِّئۡبُ وَأَنتُمۡ عَنۡهُ غَٰفِلُونَ ١٣

14. «እኛ ጭፍራዎች ሆነን ሳለን ተኩላ ቢበላውማ እኛ ያን ጊዜ በእርግጥ ከሳሪዎች ነን» አሉት፡፡

قَالُواْ لَئِنۡ أَكَلَهُ ٱلذِّئۡبُ وَنَحۡنُ عُصۡبَةٌ إِنَّآ إِذٗا لَّخَٰسِرُونَ ١٤

15. እርሱንም ይዘውት በሌዱና በጉድጓዱ ጨለማ አዘቅት ውስጥ እንዲያደርጉት በቆረጡ ጊዜ (ሐሳባቸውን ፈጸሙበት)፡፡ ወደእርሱም እነሱ የማያውቁ ሲሆኑ ይህንን ሥራቸውን በእርግጥ ትነግራቸዋለህ ስንል ላክንበት፡፡

فَلَمَّا ذَهَبُواْ بِهِۦ وَأَجۡمَعُوٓاْ أَن يَجۡعَلُوهُ فِي غَيَٰبَتِ ٱلۡجُبِّۚ وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡهِ لَتُنَبِّئَنَّهُم بِأَمۡرِهِمۡ هَٰذَا وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ١٥

16. አባታቸውንም በምሽት እያለቀሱ መጡት፡፡

وَجَآءُوٓ أَبَاهُمۡ عِشَآءٗ يَبۡكُونَ ١٦

17. «አባታችን ሆይ! እኛ (ለሩጫና ለውርወራ) ልንሽቀዳደም ሌድን፡፡ ዩሱፍንም ዕቃችን ዘንድ ተውነው፡፡ ወዲያውም ተኩላ በላው፡፡ አንተም እውነተኞች ብንሆንም የምታምነን አይደለህም» አሉ፡፡

قَالُواْ يَٰٓأَبَانَآ إِنَّا ذَهَبۡنَا نَسۡتَبِقُ وَتَرَكۡنَا يُوسُفَ عِندَ مَتَٰعِنَا فَأَكَلَهُ ٱلذِّئۡبُۖ وَمَآ أَنتَ بِمُؤۡمِنٖ لَّنَا وَلَوۡ كُنَّا صَٰدِقِينَ ١٧

18. በቀሚሱም ላይ የውሸትን ደም አመጡ፡፡ (አባታቸው) «አይደለም፤ ነፍሶቻችሁ (ውሸት) ነገርን ለእናንተ ሸለሙላችሁ፡፡ ስለዚህ መልካም ትዕግስት (ማድረግ አለብኝ) በምትሉትም ነገር ላይ መታገዣው አላህ ብቻ ነው» አለ፡፡

وَجَآءُو عَلَىٰ قَمِيصِهِۦ بِدَمٖ كَذِبٖۚ قَالَ بَلۡ سَوَّلَتۡ لَكُمۡ أَنفُسُكُمۡ أَمۡرٗاۖ فَصَبۡرٞ جَمِيلٞۖ وَٱللَّهُ ٱلۡمُسۡتَعَانُ عَلَىٰ مَا تَصِفُونَ ١٨

19. መንገደኞችም መጡ፡፡ ውሃ ቀጂያቸውንም ላኩ፡፡ አኮሊውንም (ወደ ጉድጓዱ) ሰደደ «የምስራች! ይህ ወጣት ልጅ ነው» አለ፡፡ ሸቀጥ አድርገውም ደበቁት፡፡ አላህም የሚሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

وَجَآءَتۡ سَيَّارَةٞ فَأَرۡسَلُواْ وَارِدَهُمۡ فَأَدۡلَىٰ دَلۡوَهُۥۖ قَالَ يَٰبُشۡرَىٰ هَٰذَا غُلَٰمٞۚ وَأَسَرُّوهُ بِضَٰعَةٗۚ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِمَا يَعۡمَلُونَ ١٩

20. በርካሽ ዋጋም በሚቆጠሩ ዲርሃሞች ሸጡት፡፡ በእርሱም ከቸልተኞቹ ነበሩ፡፡

وَشَرَوۡهُ بِثَمَنِۭ بَخۡسٖ دَرَٰهِمَ مَعۡدُودَةٖ وَكَانُواْ فِيهِ مِنَ ٱلزَّٰهِدِينَ ٢٠

21. ያም ከምስር የገዛው ሰው ለሚስቱ «መኖሪያውን አክብሪ፡፡ ሊጠቅመን ወይም ልጅ አድርገን ልንይዘው ይከጀላልና» አላት፡፡ እንደዚሁም ለዩሱፍ (ገሾር ልናደርገውና) የሕልሞችንም ፍች ልናስተምረው በምድር ላይ አስመቸነው፡፡ አላህም በነገሩ ላይ አሸናፊ ነው፤ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِي ٱشۡتَرَىٰهُ مِن مِّصۡرَ لِٱمۡرَأَتِهِۦٓ أَكۡرِمِي مَثۡوَىٰهُ عَسَىٰٓ أَن يَنفَعَنَآ أَوۡ نَتَّخِذَهُۥ وَلَدٗاۚ وَكَذَٰلِكَ مَكَّنَّا لِيُوسُفَ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلِنُعَلِّمَهُۥ مِن تَأۡوِيلِ ٱلۡأَحَادِيثِۚ وَٱللَّهُ غَالِبٌ عَلَىٰٓ أَمۡرِهِۦ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٢١

22. ጥንካሬውንም በደረሰ ጊዜ ጥበብንና ዕውቀትን ሰጠነው፡፡ እንደዚሁም መልካም ሠሪዎችን ሁሉ እንመነዳለን፡፡

وَلَمَّا بَلَغَ أَشُدَّهُۥٓ ءَاتَيۡنَٰهُ حُكۡمٗا وَعِلۡمٗاۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٢٢

23. ያቺም እርሱ በቤቷ የነበረባት ሴት ከነፍሱ አባበለችው፡፡ ደጃፎቹንም ዘጋች፤ «ላንተ ተዘጋጅቼልሃለሁና ቶሎ ናም» አለችው፡፡ «በአላህ እጠበቃለሁ እርሱ (የገዛኝ) ጌታዬ ኑሮዬን ያሳመረልኝ ነውና፤ (አልከዳውም)፡፡ እነሆ! በደለኞች አይድኑም» አላት፡፡

وَرَٰوَدَتۡهُ ٱلَّتِي هُوَ فِي بَيۡتِهَا عَن نَّفۡسِهِۦ وَغَلَّقَتِ ٱلۡأَبۡوَٰبَ وَقَالَتۡ هَيۡتَ لَكَۚ قَالَ مَعَاذَ ٱللَّهِۖ إِنَّهُۥ رَبِّيٓ أَحۡسَنَ مَثۡوَايَۖ إِنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٢٣

24. በእርሱም በእርግጥ አሰበች፡፡ በእርሷም አሰበ፤ የጌታውን ማስረጃ ባላየ ኖሮ (የተፈጥሮ ፍላጎቱን ባረካ ነበር፤)፡፡ እንደዚሁ መጥፎ ነገርንና ኀጢአትን ከእርሱ ላይ ልንመልስለት (አስረጃችንን አሳየነው)፡፡ እርሱ ከተመረጡት ባሮቻችን ነውና፡፡

وَلَقَدۡ هَمَّتۡ بِهِۦۖ وَهَمَّ بِهَا لَوۡلَآ أَن رَّءَا بُرۡهَٰنَ رَبِّهِۦۚ كَذَٰلِكَ لِنَصۡرِفَ عَنۡهُ ٱلسُّوٓءَ وَٱلۡفَحۡشَآءَۚ إِنَّهُۥ مِنۡ عِبَادِنَا ٱلۡمُخۡلَصِينَ ﴿٢٤﴾

25. በሩንም ተሽቀዳደሙ ቀሚሱንም ከበስተኋላው ቀደደችው፡፡ ጌታዋንም (ባለቤቷን) እበሩ አጠገብ አገኙት፡፡ (ቀደም ብላ) «በባለቤትህ መጥፎን ያሰበ ሰው ቅጣቱ መታሰር ወይም አሳማሚ ስቃይ እንጂ ሌላ አይደለም» አለችው፡፡

وَٱسۡتَبَقَا ٱلۡبَابَ وَقَدَّتۡ قَمِيصَهُۥ مِن دُبُرٖ وَأَلۡفَيَا سَيِّدَهَا لَدَا ٱلۡبَابِۚ قَالَتۡ مَا جَزَآءُ مَنۡ أَرَادَ بِأَهۡلِكَ سُوٓءًا إِلَّآ أَن يُسۡجَنَ أَوۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿٢٥﴾

26. (ዩሱፍም) «እርሷ ከነፍሴ አባበለችኝ» አለ፡፡ ከቤተሰቦቿም መስካሪ (እንዲህ ሲል) መሰከረ፡፡ «ቀሚሱ ከበስተፊት ተቀድዶ እንደሆነ እውነት ተናገረች፡፡ እርሱም ከውሸታሞቹ ነው፡፡

قَالَ هِيَ رَٰوَدَتۡنِي عَن نَّفۡسِيۚ وَشَهِدَ شَاهِدٞ مِّنۡ أَهۡلِهَآ إِن كَانَ قَمِيصُهُۥ قُدَّ مِن قُبُلٖ فَصَدَقَتۡ وَهُوَ مِنَ ٱلۡكَٰذِبِينَ ﴿٢٦﴾

27. «ቀሚሱም ከበስተኋላ ተቀድዶ እንደሆነ ዋሸች፡፡ እርሱም ከእውነተኞቹ ነው፡፡»

وَإِن كَانَ قَمِيصُهُۥ قُدَّ مِن دُبُرٖ فَكَذَبَتۡ وَهُوَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿٢٧﴾

28. ቀሚሱንም ከበስተኋላ ተቀድዶ ባየ ጊዜ «እርሱ (የተናገርሺው) ከተንኮላችሁ ነው (ሴቶች) ተንኮላችሁ በእርግጥ ብርቱ ነውና» አላት፡፡

فَلَمَّا رَءَا قَمِيصَهُۥ قُدَّ مِن دُبُرٖ قَالَ إِنَّهُۥ مِن كَيۡدِكُنَّۖ إِنَّ كَيۡدَكُنَّ عَظِيمٞ ﴿٢٨﴾

29. «ዩሱፍ ሆይ! ከዚህ (ወሬ) ተከልከል፡፡ ለኃጢአትሽም ማርታን ለምኚ፡፡ አንቺ ከስህተተኞቹ ሆነሻልና» (አለ)፡፡

يُوسُفُ أَعۡرِضۡ عَنۡ هَٰذَاۚ وَٱسۡتَغۡفِرِي لِذَنۢبِكِۖ إِنَّكِ كُنتِ مِنَ ٱلۡخَاطِـِٔينَ ﴿٢٩﴾

30. በከተማው ያሉ ሴቶችም «የዐዚዝ ሚስት ብላቴናዋን ከነፍሱ ታባብለዋለች፡፡ በእውነቱ ፍቅሩ ልቧን መቷታል፡፡ እኛ በግልጽ ስህተት ውስጥ ሆና በእርግጥ እናያታለን» አሉ፡፡

۞وَقَالَ نِسۡوَةٞ فِي ٱلۡمَدِينَةِ ٱمۡرَأَتُ ٱلۡعَزِيزِ تُرَٰوِدُ فَتَىٰهَا عَن نَّفۡسِهِۦۖ قَدۡ شَغَفَهَا حُبًّاۖ إِنَّا لَنَرَىٰهَا فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ﴿٣٠﴾

31. ሀሜታቸውንም በሰማች ጊዜ ወደነሱ ላከችባቸው፡ ፡ ምግብንም ለእነርሱ አዘጋጀችላቸው፡፡ ከእነሱ ለያንዳንዳቸውም ቢላዋን ሰጠች፡፡ በእነሱም ላይ «ውጣ» አለችው፡፡ ባዩትም ጊዜ አደነቁት፡፡ እጆቻቸውንም ቆረጡ፡፡ አላህም ጥራት ይገባው፡፡ ይህ ሰው አይደለም፡፡ ይህ ያማረ መልአክ እንጅ ሌላ አይደለም አሉ፡፡

فَلَمَّا سَمِعَتۡ بِمَكۡرِهِنَّ أَرۡسَلَتۡ إِلَيۡهِنَّ وَأَعۡتَدَتۡ لَهُنَّ مُتَّكَـٔٗا وَءَاتَتۡ كُلَّ وَٰحِدَةٖ مِّنۡهُنَّ سِكِّينٗا وَقَالَتِ ٱخۡرُجۡ عَلَيۡهِنَّۖ فَلَمَّا رَأَيۡنَهُۥٓ أَكۡبَرۡنَهُۥ وَقَطَّعۡنَ أَيۡدِيَهُنَّ وَقُلۡنَ حَٰشَ لِلَّهِ مَا هَٰذَا بَشَرًا إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا مَلَكٞ كَرِيمٞ ﴿٣١﴾

32. «ታዲያ ይህ ያ በርሱ (ፍቅር) የዘለፋችሁኝ ነው፡፡ በእርግጥም ከነፍሱ አባበልኩት፡፡ እምቢ አለም፡፡ የማዘውንም ነገር ባይሠራ በእርግጥ ይታሰራል፡፡ ከወራዶቹም ይሆናል» አለች፡፡

قَالَتۡ فَذَٰلِكُنَّ ٱلَّذِي لُمۡتُنَّنِي فِيهِۖ وَلَقَدۡ رَٰوَدتُّهُۥ عَن نَّفۡسِهِۦ فَٱسۡتَعۡصَمَۖ وَلَئِن لَّمۡ يَفۡعَلۡ مَآ ءَامُرُهُۥ لَيُسۡجَنَنَّ وَلَيَكُونٗا مِّنَ ٱلصَّٰغِرِينَ ﴿٣٢﴾

33. «ጌታዬ ሆይ! ወደርሱ ከሚጠሩኝ ነገር (ከዝሙት) ይልቅ መታሰር ለእኔ የተወደደ ነው፡፡ ተንኮላቸውንም ከእኔ ላይ ባትመልስልኝ ወደነሱ እዘነበላለሁ፡፡ ከስህተተኞቹም እሆናለሁ» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ ٱلسِّجۡنُ أَحَبُّ إِلَيَّ مِمَّا يَدۡعُونَنِيٓ إِلَيۡهِۖ وَإِلَّا تَصۡرِفۡ عَنِّي كَيۡدَهُنَّ أَصۡبُ إِلَيۡهِنَّ وَأَكُن مِّنَ ٱلۡجَٰهِلِينَ ٣٣

34. ጌታውም ጸሎቱን ተቀበለው፡፡ ተንኮላቸውንም ከእርሱ መለሰለት፡፡ እነሆ! እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና፡፡

فَٱسۡتَجَابَ لَهُۥ رَبُّهُۥ فَصَرَفَ عَنۡهُ كَيۡدَهُنَّۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٣٤

35. ከዚያም ማስረጃዎቹን ካዩ በኋላ እስከጊዜ ድረስ እንዲያስሩት ለነሱ ታያቸው፡፡

ثُمَّ بَدَا لَهُم مِّنۢ بَعۡدِ مَا رَأَوُاْ ٱلۡأٓيَٰتِ لَيَسۡجُنُنَّهُۥ حَتَّىٰ حِينٖ ٣٥

36. ከእሱም ጋር ሁለት ጎበዞች እስር ቤቱ ገቡ፡፡ አንደኛቸው «እኔ በህልሜ የወይን ጠጅን ስጠምቅ አየሁ» አለ፡፡ ሌላውም፡- «እኔ በራሴ ላይ እንጀራን ተሸክሜ ከእሱ በራሪ (አሞራ) ስትበላ አየሁ፡፡ ፍቹን ንገረን፡፡ እኛ ከአሳማሪዎች ሆነህ እናይሃለንና» አሉት፡፡

وَدَخَلَ مَعَهُ ٱلسِّجۡنَ فَتَيَانِۖ قَالَ أَحَدُهُمَآ إِنِّيٓ أَرَىٰنِيٓ أَعۡصِرُ خَمۡرٗاۖ وَقَالَ ٱلۡأٓخَرُ إِنِّيٓ أَرَىٰنِيٓ أَحۡمِلُ فَوۡقَ رَأۡسِي خُبۡزٗا تَأۡكُلُ ٱلطَّيۡرُ مِنۡهُۖ نَبِّئۡنَا بِتَأۡوِيلِهِۦٓۖ إِنَّا نَرَىٰكَ مِنَ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٣٦

37. (ዩሱፍም) አለ፡- «ማንኛውም የምትሰሰጡት ምግብ ለናንተ ከመምጣቱ በፊት ፍቹን የምነግራችሁ ቢሆን እንጂ አይመጣላችሁም፡፡ ይኸ ጌታዬ ካሳወቀኝ ነገር ነው፤ እኔ በአላህ የማያምኑን እነርሱም መጨረሻይቱን ዓለም እነርሱ ከሓዲዎች የሆኑትን ሕዝቦች ሃይማኖት ትቻለሁ፡፡

قَالَ لَا يَأۡتِيكُمَا طَعَامٞ تُرۡزَقَانِهِۦٓ إِلَّا نَبَّأۡتُكُمَا بِتَأۡوِيلِهِۦ قَبۡلَ أَن يَأۡتِيَكُمَاۚ ذَٰلِكُمَا مِمَّا عَلَّمَنِي رَبِّيٓۚ إِنِّي تَرَكۡتُ مِلَّةَ قَوۡمٖ لَّا يُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَهُم بِٱلۡأٓخِرَةِ هُمۡ كَٰفِرُونَ ٣٧

38. «የአባቶቼንም የኢብራሂምንና የኢስሐቅን፣ የያዕቆብንም ሃይማኖት ተከትያለሁ፡፡ ለእኛ በአላህ ምንንም ማጋራት አይገባንም ያ (አለማጋራት) በእኛ ላይና በሰዎቹ ላይ የአላህ ችሮታ ነው፡፡ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያመሰግኑም፡፡

وَٱتَّبَعۡتُ مِلَّةَ ءَابَآءِيٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَۚ مَا كَانَ لَنَآ أَن نُّشۡرِكَ بِٱللَّهِ مِن شَيۡءٖۚ ذَٰلِكَ مِن فَضۡلِ ٱللَّهِ عَلَيۡنَا وَعَلَى ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَشۡكُرُونَ ٣٨

39. «የእስር ቤት ጓደኞቼ ሆይ! የተለያዩ አምላኮች ይሻላሉን ወይስ አሸናፊው አንዱ አላህ

يَٰصَٰحِبَيِ ٱلسِّجۡنِ ءَأَرۡبَابٞ مُّتَفَرِّقُونَ خَيۡرٌ أَمِ ٱللَّهُ ٱلۡوَٰحِدُ ٱلۡقَهَّارُ ٣٩

40. «ከእርሱ ሌላ እናንተና አባቶቻችሁ (አማልክት ብላችሁ) የጠራችኋቸውን ስሞች እንጅ አትገዙም፡፡ አላህ በእርሷ ምንም አስረጅ አላወረደም፡፡ ፍርዱ የአላህ እንጅ የሌላ አይደለም፡፡ እርሱን እንጅ ሌላን እንዳትገዙ አዟል፡፡ ይህ ትክክለኛው ሃይማኖት ነው፡፡ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

مَا تَعۡبُدُونَ مِن دُونِهِۦٓ إِلَّآ أَسۡمَآءٗ سَمَّيۡتُمُوهَآ أَنتُمۡ وَءَابَآؤُكُم مَّآ أَنزَلَ ٱللَّهُ بِهَا مِن سُلۡطَٰنٍۚ إِنِ ٱلۡحُكۡمُ إِلَّا لِلَّهِ أَمَرَ أَلَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّآ إِيَّاهُۚ ذَٰلِكَ ٱلدِّينُ ٱلۡقَيِّمُ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٤٠

يَٰصَٰحِبَيِ ٱلسِّجۡنِ أَمَّآ أَحَدُكُمَا فَيَسۡقِي رَبَّهُۥ خَمۡرٗاۖ وَأَمَّا ٱلۡأٓخَرُ فَيُصۡلَبُ فَتَأۡكُلُ ٱلطَّيۡرُ مِن رَّأۡسِهِۦۚ قُضِيَ ٱلۡأَمۡرُ ٱلَّذِي فِيهِ تَسۡتَفۡتِيَانِ ٤١

41. «የወህኒ ቤት ጓደኞቼ ሆይ! አንደኛችሁማ ጌታውን (ንጉሡን) ጠጅ ያጠጣል፡፡ ሌላውማ ይሰቀላል፡፡ ከራሱም በራሪ (አሞራ) ትበላለች፡፡ ያ ፍቹን የምትጠይቁት ነገር ተፈጸመ፤» (አላቸው)፡፡

وَقَالَ لِلَّذِي ظَنَّ أَنَّهُۥ نَاجٖ مِّنۡهُمَا ٱذۡكُرۡنِي عِندَ رَبِّكَ فَأَنسَىٰهُ ٱلشَّيۡطَٰنُ ذِكۡرَ رَبِّهِۦ فَلَبِثَ فِي ٱلسِّجۡنِ بِضۡعَ سِنِينَ ٤٢

42. ለዚያም ከሁለቱ እርሱ የሚድን መሆኑን ለተጠራጠረው እጌታህ ዘንድ አስታውሰኝ አለው፡፡ ጌታውንም ከማስታወስ ሰይጣን አስረሳው፡፡ ለጥቂት ዓመታትም በወህኒ ቤቱ ውስጥ ቆየ፡፡

وَقَالَ ٱلۡمَلِكُ إِنِّيٓ أَرَىٰ سَبۡعَ بَقَرَٰتٖ سِمَانٖ يَأۡكُلُهُنَّ سَبۡعٌ عِجَافٞ وَسَبۡعَ سُنۢبُلَٰتٍ خُضۡرٖ وَأُخَرَ يَابِسَٰتٖۖ يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡمَلَأُ أَفۡتُونِي فِي رُءۡيَٰيَ إِن كُنتُمۡ لِلرُّءۡيَا تَعۡبُرُونَ ٤٣

43. ንጉሡም «እኔ ሰባትን የሰቡ ላሞች ሰባት ከሲታዎች ሲበሏቸው ሰባትንም ለምለም ዘለላዎች ሌሎችንም ደረቆችን (ሲጠመጠሙባቸው በሕልሜ) አያለሁ፡፡ እናንተ ታላላቅ ሰዎች ሆይ! ሕልምን የምትፈቱ እንደሆናችሁ ሕልሜን ፍቱልኝ» አላቸው፡፡

قَالُوٓاْ أَضۡغَٰثُ أَحۡلَٰمٖۖ وَمَا نَحۡنُ بِتَأۡوِيلِ ٱلۡأَحۡلَٰمِ بِعَٰلِمِينَ ٤٤

44. «የሕልሞች ቅዠቶች ናቸው፡፡ እኛም የሕልሞችን ፍች ዐዋቂዎች አይደለንም» አሉት፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِي نَجَا مِنۡهُمَا وَٱدَّكَرَ بَعۡدَ أُمَّةٍ أَنَا۠ أُنَبِّئُكُم بِتَأۡوِيلِهِۦ فَأَرۡسِلُونِ ٤٥

45. ያም ከሁለቱ የዳነውና ከብዙ ጊዜ በኋላ (ዩሱፍን) ያስታወሰው ሰው «እኔ ፍቹን እነግራችኋለሁና ላኩኝ» አለ፤ (ወደ ዩሱፍ ሌደም)፡፡

يُوسُفُ أَيُّهَا ٱلصِّدِّيقُ أَفۡتِنَا فِي سَبۡعِ بَقَرَٰتٖ سِمَانٖ يَأۡكُلُهُنَّ سَبۡعٌ عِجَافٞ وَسَبۡعِ سُنۢبُلَٰتٍ خُضۡرٖ وَأُخَرَ يَابِسَٰتٖ لَّعَلِّيٓ أَرۡجِعُ إِلَى ٱلنَّاسِ لَعَلَّهُمۡ يَعۡلَمُونَ ٤٦

46. «አንተ እውነተኛው ዩሱፍ ሆይ! ሰባትን የሰቡ ላሞች ሰባት ከሲታዎች ላሞች ሲበሉዋቸው ሰባትን ለምለም ዘለላዎችም ሌሎችንም ደረቆች (በነሱ ላይ ሲጠመጠሙባቸው ያየን ሰው ሕልም ፍች) ተችልን፡፡ ያውቁ ዘንድ ወደ ሰዎቹ ልመለስ እከጅላለሁና» (አለው)፡፡

قَالَ تَزۡرَعُونَ سَبۡعَ سِنِينَ دَأَبٗا فَمَا حَصَدتُّمۡ فَذَرُوهُ فِي سُنۢبُلِهِۦٓ إِلَّا قَلِيلٗا مِّمَّا تَأۡكُلُونَ ٤٧

47. (እርሱም) አለ፡- «ሰባትን የተከታተሉ ዓመታት ትዘራላችሁ፡፡ ያጨዳችሁትንም ሁሉ ከምትበሉት ጥቂት በስተቀር በዘለላው ውስጥ ተዉት፡፡

ثُمَّ يَأۡتِي مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ سَبۡعٞ شِدَادٞ يَأۡكُلۡنَ مَا قَدَّمۡتُمۡ لَهُنَّ إِلَّا قَلِيلٗا مِّمَّا تُحۡصِنُونَ ٤٨

48. «ከዚያም ከእነዚያ በኋላ ካደለባችሁት ጥቂት ሲቀር ለእነሱ ያደለባችሁትን ሁሉ የሚበሉ ሰባት የችግር ዓመታት ይመጣሉ፡፡

ثُمَّ يَأۡتِي مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ عَامٞ فِيهِ يُغَاثُ ٱلنَّاسُ وَفِيهِ يَعۡصِرُونَ ٤٩

49. «ከዚያም ከእነዚያ በኋላ ሰዎቹ በርሱ የሚዘነቡበት በርሱም (ወይንን) የሚጨምቁበት ዓመት ይመጣል፡፡»

50. ንጉሡም «እርሱን አምጡልኝ» አለ፡፡ መልክተኛውም (ዩሱፍን) በመጣው ጊዜ «ወደጌታህ ተመለስ፡፡ የዚያንም እጆቻቸውን የቆረጡትን ሴቶች ሁኔታ ጠይቀው፡፡ ጌታዬ ተንኮላቸውን ዐዋቂ ነውና» አለው፡፡

وَقَالَ ٱلۡمَلِكُ ٱئۡتُونِي بِهِۦۖ فَلَمَّا جَآءَهُ ٱلرَّسُولُ قَالَ ٱرۡجِعۡ إِلَىٰ رَبِّكَ فَسۡـَٔلۡهُ مَا بَالُ ٱلنِّسۡوَةِ ٱلَّٰتِي قَطَّعۡنَ أَيۡدِيَهُنَّۚ إِنَّ رَبِّي بِكَيۡدِهِنَّ عَلِيمٞ ٥٠

51. (ንጉሡም)፡- «ዩሱፍን ከነፍሱ ባባበላችሁት ጊዜ ነገራችሁ ምንድን ነው» አላቸው፡፡ «ለአላህ ጥራት ይገባው፡፡ በእርሱ ላይ ምንም መጥፎን ነገር አላወቅንም» አሉት፡፡ የዐዚዝ ሚስት፡-«አሁን እውነቱ ተገለጸ፡፡ እኔ ከነፍሱ አባበልኩት፡፡ እርሱም ከእውነተኞቹ ነው» አለች፡፡

قَالَ مَا خَطۡبُكُنَّ إِذۡ رَٰوَدتُّنَّ يُوسُفَ عَن نَّفۡسِهِۦۚ قُلۡنَ حَٰشَ لِلَّهِ مَا عَلِمۡنَا عَلَيۡهِ مِن سُوٓءٖۚ قَالَتِ ٱمۡرَأَتُ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡـَٰٔنَ حَصۡحَصَ ٱلۡحَقُّ أَنَا۠ رَٰوَدتُّهُۥ عَن نَّفۡسِهِۦ وَإِنَّهُۥ لَمِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ٥١

52. (ዩሱፍ) «ይህ (ጌታዬ) ሩቅ ሆኖ ሳለ ያልከዳሁት መሆኔን አላህም የከዳተኞችን ተንኮል የማያቃና መሆኑን እንዲያውቅ ነው፤» (አለ)፡፡

ذَٰلِكَ لِيَعۡلَمَ أَنِّي لَمۡ أَخُنۡهُ بِٱلۡغَيۡبِ وَأَنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي كَيۡدَ ٱلۡخَآئِنِينَ ٥٢

53. «ነፍሴንም (ከስሕተት) አላጠራም፡፡ ነፍስ ሁሉ ጌታዬ የጠበቃት ካልሆነች በስተቀር በመጥፎ ነገር በእርግጥ አዛዥ ናትና፡፡ ጌታዬ በጣም መሓሪ አዛኝ ነው» (አለ)፡፡

۞وَمَآ أُبَرِّئُ نَفۡسِيٓۚ إِنَّ ٱلنَّفۡسَ لَأَمَّارَةُۢ بِٱلسُّوٓءِ إِلَّا مَا رَحِمَ رَبِّيٓۚ إِنَّ رَبِّي غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٥٣

54. ንጉሡም «እርሱን አምጡልኝ ለራሴ ግለኛ አደርገዋለሁና» አለ፡፡ ባናገረውም ጊዜ «አንተ ዛሬ እኛ ዘንድ ባለሟል ታማኝ ነህ» አለው፡፡

وَقَالَ ٱلۡمَلِكُ ٱئۡتُونِي بِهِۦٓ أَسۡتَخۡلِصۡهُ لِنَفۡسِيۖ فَلَمَّا كَلَّمَهُۥ قَالَ إِنَّكَ ٱلۡيَوۡمَ لَدَيۡنَا مَكِينٌ أَمِينٞ ٥٤

55. «በምድር ግምጃ ቤቶች ላይ (ሹም) አድርገኝ፡፡ እኔ ጠባቂ አዋቂ ነኝና» አለ፡፡

قَالَ ٱجۡعَلۡنِي عَلَىٰ خَزَآئِنِ ٱلۡأَرۡضِۖ إِنِّي حَفِيظٌ عَلِيمٞ ٥٥

56. እንደዚሁም ለዩሱፍ በምድር ላይ ከእርሷ በፈለገው ስፍራ የሚሰፍር ሲሆን አስመቸነው፡፡ በችሮታችን የምንሻውን ሰው እንለያለን፡፡ የበጎ ሠሪዎችንም ዋጋ አናጠፋም፡፡

وَكَذَٰلِكَ مَكَّنَّا لِيُوسُفَ فِي ٱلۡأَرۡضِ يَتَبَوَّأُ مِنۡهَا حَيۡثُ يَشَآءُۚ نُصِيبُ بِرَحۡمَتِنَا مَن نَّشَآءُۖ وَلَا نُضِيعُ أَجۡرَ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٥٦

57. የመጨረሻይቱም ዓለም ምንዳ ለእነዚያ ላመኑትና ይጠነቀቁ ለነበሩት የበለጠ ነው፡፡

وَلَأَجۡرُ ٱلۡأٓخِرَةِ خَيۡرٞ لِّلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَكَانُواْ يَتَّقُونَ ٥٧

58. የዩሱፍ ወንድሞችም መጡ፡፡ በእርሱም ላይ ገቡ፡፡ እነሱም እርሱን የሳቱት ሲሆኑ ዐወቃቸው፡፡

وَجَآءَ إِخۡوَةُ يُوسُفَ فَدَخَلُواْ عَلَيۡهِ فَعَرَفَهُمۡ وَهُمۡ لَهُۥ مُنكِرُونَ ٥٨

59. (ጉዳያቸውን ፈጽሞ) ስንቃቸውንም ባዘጋጀላቸው ጊዜ አለ፡- «ከአባታችሁ በኩል የሆነውን ወንድማችሁን አምጡልኝ፡፡ እኔ ከአስተናጋጆች ሁሉ በላጭ ስሆን፤ ስፍርን የምሞላ መሆኔን አታዩምን

وَلَمَّا جَهَّزَهُم بِجَهَازِهِمۡ قَالَ ٱئۡتُونِي بِأَخٖ لَّكُم مِّنۡ أَبِيكُمۡۚ أَلَا تَرَوۡنَ أَنِّيٓ أُوفِي ٱلۡكَيۡلَ وَأَنَا۠ خَيۡرُ ٱلۡمُنزِلِينَ ٥٩

60. እርሱንም ባታመጡልኝ እኔ ዘንድ ለእናንተ ስፍር የላችሁም፤ አትቀርቡኝምም፡፡»

فَإِن لَّمۡ تَأۡتُونِي بِهِۦ فَلَا كَيۡلَ لَكُمۡ عِندِي وَلَا تَقۡرَبُونِ ٦٠

61. «ስለእርሱ አባቱን በጥብቅ እንጠይቃለን፡፡ እኛም (ይህንን) በእርግጥ ሠሪዎች ነን» አሉት፡፡

62. ለአሽከሮቹም «ሸቀጣቸውን ወደ ቤተሰቦቻቸው በተመለሱ ጊዜ ያውቋት ዘንድ በየጓዞቻቸው ውስጥ አድርጉላቸው፡፡ ሊመለሱ ይከጀላሉና» አላቸው፡፡

63. ወደ አባታቸውም በተመሰሉ ጊዜ፡- «አባታችን ሆይ! (ወንድማችንን እስከምንወስድ) ስፍር ከእኛ ተከልክሏል፡፡ ስለዚህ ወንድማችንን ከእኛ ጋር ላከው፡፡ ይሰፍርልናልና እኛም ለርሱ ጠባቂዎች ነን» አሉ፡፡

64. «ከአሁን በፊት በወንድሙ ላይ እንዳመንኳችሁ እንጂ በእርሱ ላይ አምናችኋለሁን አላህም በጠባቂነት (ከሁሉ) የበለጠ ነው፡፡ እርሱም ከአዛኞች ሁሉ ይበልጥ አዛኝ ነው፤» አላቸው፡፡

65. ዕቃቸውንም በከፈቱ ጊዜ ሸቀጣቸው ወደእነርሱ ተመልሳ አገኙ፡፡ ፡-«አባታችን ሆይ! ምን እንፈልጋለን ይህቺ ሸቀጣችን ናት፡፡ ወደኛ ተመልሳልናለች፤ (እንረዳባታለን)፡፡ ለቤተሰቦቻችንም እንሸምታለን፡፡ ወንድማችንንም እንጠብቃለን፡፡ የግመልንም ጭነት እንጨምራለን፡፡ ይህ (በንጉሡ ላይ) ቀላል ስፍር ነው» አሉ፡፡

66. «ካልተከበባችሁ በስተቀር እርሱን በእርግጥ የምታመጡልኝ ለመሆናችሁ ከአላህ የሆነን ቃል ኪዳን መተማመኛ እስከምትሰጡኝ ድረስ ከእናንተ ጋር ፈጽሞ አልልከውም» አላቸው፡፡ መተማመኛቸውንም በሰጡት ጊዜ «አላህ በምንለው ሁሉ ላይ ምስክር ነው» አላቸው፡፡

67. አለም «ልጆቼ ሆይ! በአንድ በር አትግቡ፡፡ ግን በተለዩ በሮች ግቡ፡፡ ከአላህም (ፍርድ) በምንም አልጠቅማችሁም፤ (አልመልስላችሁም)፡፡ ፍርዱ የአላህ እንጅ የሌላ አይደለም፡፡ በእርሱ ላይ ተመካሁ፡፡ ተመኪዎችም ሁሉ በእርሱ ብቻ ይመኩ፡፡»

68. አባታቸውም ካዘዛቸው ስፍራ በገቡ ጊዜ ከአላህ (ፍርድ) ምንም ነገር ከነርሱ የሚከለክልላቸው አልነበረም፡፡ ግን በያዕቆብም ነፍስ ውስጥ የነበረች ጉዳይ ናት፡፡ ፈጸማት፡፡ እርሱም ስላሳወቅነው የዕውቀት ባለቤት ነው፤ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

قَالُواْ سَنُرَٰوِدُ عَنۡهُ أَبَاهُ وَإِنَّا لَفَٰعِلُونَ ٦١

وَقَالَ لِفِتۡيَٰنِهِ ٱجۡعَلُواْ بِضَٰعَتَهُمۡ فِي رِحَالِهِمۡ لَعَلَّهُمۡ يَعۡرِفُونَهَآ إِذَا ٱنقَلَبُوٓاْ إِلَىٰٓ أَهۡلِهِمۡ لَعَلَّهُمۡ يَرۡجِعُونَ ٦٢

فَلَمَّا رَجَعُوٓاْ إِلَىٰٓ أَبِيهِمۡ قَالُواْ يَٰٓأَبَانَا مُنِعَ مِنَّا ٱلۡكَيۡلُ فَأَرۡسِلۡ مَعَنَآ أَخَانَا نَكۡتَلۡ وَإِنَّا لَهُۥ لَحَٰفِظُونَ ٦٣

قَالَ هَلۡ ءَامَنُكُمۡ عَلَيۡهِ إِلَّا كَمَآ أَمِنتُكُمۡ عَلَىٰٓ أَخِيهِ مِن قَبۡلُ فَٱللَّهُ خَيۡرٌ حَٰفِظٗاۖ وَهُوَ أَرۡحَمُ ٱلرَّٰحِمِينَ ٦٤

وَلَمَّا فَتَحُواْ مَتَٰعَهُمۡ وَجَدُواْ بِضَٰعَتَهُمۡ رُدَّتۡ إِلَيۡهِمۡۖ قَالُواْ يَٰٓأَبَانَا مَا نَبۡغِيۖ هَٰذِهِۦ بِضَٰعَتُنَا رُدَّتۡ إِلَيۡنَاۖ وَنَمِيرُ أَهۡلَنَا وَنَحۡفَظُ أَخَانَا وَنَزۡدَادُ كَيۡلَ بَعِيرٖۖ ذَٰلِكَ كَيۡلٞ يَسِيرٞ ٦٥

قَالَ لَنۡ أُرۡسِلَهُۥ مَعَكُمۡ حَتَّىٰ تُؤۡتُونِ مَوۡثِقٗا مِّنَ ٱللَّهِ لَتَأۡتُنَّنِي بِهِۦٓ إِلَّآ أَن يُحَاطَ بِكُمۡۖ فَلَمَّآ ءَاتَوۡهُ مَوۡثِقَهُمۡ قَالَ ٱللَّهُ عَلَىٰ مَا نَقُولُ وَكِيلٞ ٦٦

وَقَالَ يَٰبَنِيَّ لَا تَدۡخُلُواْ مِنۢ بَابٖ وَٰحِدٖ وَٱدۡخُلُواْ مِنۡ أَبۡوَٰبٖ مُّتَفَرِّقَةٖۖ وَمَآ أُغۡنِي عَنكُم مِّنَ ٱللَّهِ مِن شَيۡءٍۖ إِنِ ٱلۡحُكۡمُ إِلَّا لِلَّهِۖ عَلَيۡهِ تَوَكَّلۡتُۖ وَعَلَيۡهِ فَلۡيَتَوَكَّلِ ٱلۡمُتَوَكِّلُونَ ٦٧

وَلَمَّا دَخَلُواْ مِنۡ حَيۡثُ أَمَرَهُمۡ أَبُوهُم مَّا كَانَ يُغۡنِي عَنۡهُم مِّنَ ٱللَّهِ مِن شَيۡءٍ إِلَّا حَاجَةٗ فِي نَفۡسِ يَعۡقُوبَ قَضَىٰهَاۚ وَإِنَّهُۥ لَذُو عِلۡمٖ لِّمَا عَلَّمۡنَٰهُ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٦٨

69. በዩሱፍ ላይ በገቡ ጊዜም ወንድሙን ወደርሱ አስጠጋው፡፡ «እነሆ እኔ ወንድምህ ነኝ፡፡ ይሠሩት በነበሩትም ሁሉ አትቆላጭ» አለው፡፡

وَلَمَّا دَخَلُوا۟ عَلَىٰ يُوسُفَ ءَاوَىٰٓ إِلَيْهِ أَخَاهُ ۖ قَالَ إِنِّىٓ أَنَا۠ أَخُوكَ فَلَا تَبْتَئِسْ بِمَا كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ٦٩

70. ዕቃቸውንም ባዘጋጀላቸው ጊዜ፤ ዋንጫይቱን በወንድሙ ዕቃ ውስጥ አደረገ፡፡ ከዚያም «እናንተ ባለ ግመሎች ሆይ! እናንተ በእርግጥ ሌቦች ናችሁ ሲል ጠሪ ተጣራ፡፡»

فَلَمَّا جَهَّزَهُم بِجَهَازِهِمْ جَعَلَ ٱلسِّقَايَةَ فِى رَحْلِ أَخِيهِ ثُمَّ أَذَّنَ مُؤَذِّنٌ أَيَّتُهَا ٱلْعِيرُ إِنَّكُمْ لَسَـٰرِقُونَ ٧٠

71. ወደነሱ ዞረውም «ምንድን ጠፋችሁ» አሉ፡፡

قَالُوا۟ وَأَقْبَلُوا۟ عَلَيْهِم مَّاذَا تَفْقِدُونَ ٧١

72. «የንጉሡ መስፈሪያ ጠፍቶናል፡፡ እርሱንም ላመጣ ሰው የግመል ጭነት አለው፡፡ እኔም በእርሱ ተያዥ ነኝ» አለ፡፡

قَالُوا۟ نَفْقِدُ صُوَاعَ ٱلْمَلِكِ وَلِمَن جَآءَ بِهِۦ حِمْلُ بَعِيرٍ وَأَنَا۠ بِهِۦ زَعِيمٌ ٧٢

73. «በአላህ እንምላለን በምድር ላይ ለማጥፋት እንዳልመጣን በእርግጥ ዐውቃችኋል፡፡ ሌቦችም አልነበርንም» አሉ፡፡

قَالُوا۟ تَٱللَّهِ لَقَدْ عَلِمْتُم مَّا جِئْنَا لِنُفْسِدَ فِى ٱلْأَرْضِ وَمَا كُنَّا سَـٰرِقِينَ ٧٣

74. «ውሸታሞች ብትሆኑ ቅጣቱ ምንድን ነው» አሏቸው፡፡

قَالُوا۟ فَمَا جَزَٰٓؤُهُۥٓ إِن كُنتُمْ كَـٰذِبِينَ ٧٤

75. «ቅጣቱ (በያዕቆብ ሕግ) ዕቃው በጓዙ ውስጥ የተገኘበት ሰው (ራሱ መወሰድ) ነው፡፡ እርሱም ቅጣቱ ነው፡፡ እንደዚሁ በደለኞችን እንቀጣለን» አሉ፡፡

قَالُوا۟ جَزَٰٓؤُهُۥ مَن وُجِدَ فِى رَحْلِهِۦ فَهُوَ جَزَٰٓؤُهُۥ ۚ كَذَٰلِكَ نَجْزِى ٱلظَّـٰلِمِينَ ٧٥

76. (ምርመራውን) ከወንድሙም ዕቃ በፊት በዕቃዎቻቸው ጀመረ፡፡ ከዚያም (ዋንጫይቱን) ከወንድሙ ዕቃ ውስጥ አወጣት፡፡ እንደዚሁ ለዩሱፍ ብልሃትን አስተማርነው፡፡ አላህ ባልሻ ኖሮ በንጉሡ ሕግ ወንድሙን ሊይዝ አይገባውም ነበር፡፡ የምንሻውን ሰው በደረጃዎች ከፍ እናደርጋለን፡፡ ከዕውቀት ባለቤቶች ሁሉ በላይም ዐዋቂ አልለ፡፡

فَبَدَأَ بِأَوْعِيَتِهِمْ قَبْلَ وِعَآءِ أَخِيهِ ثُمَّ ٱسْتَخْرَجَهَا مِن وِعَآءِ أَخِيهِ ۚ كَذَٰلِكَ كِدْنَا لِيُوسُفَ ۖ مَا كَانَ لِيَأْخُذَ أَخَاهُ فِى دِينِ ٱلْمَلِكِ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُ ۚ نَرْفَعُ دَرَجَـٰتٍ مَّن نَّشَآءُ ۗ وَفَوْقَ كُلِّ ذِى عِلْمٍ عَلِيمٌ ٧٦

77. «ቢሰርቅ ከአሁን በፊት የርሱው ወንድም በእርግጥ ሰርቋል» አሉ፡፡ ዩሱፍም (ይህችን ንግግር) በነፍሱ ውስጥ ደበቃት፡፡ ለእነሱም አልገለጣትም፡፡ (በልቡ) «እናንተ ሥራችሁ የከፋ ነው፡፡ አላህም የምትሉትን ሁሉ ይበልጥ ዐዋቂ ነው» አለ፡፡

۞ قَالُوٓا۟ إِن يَسْرِقْ فَقَدْ سَرَقَ أَخٌ لَّهُۥ مِن قَبْلُ ۚ فَأَسَرَّهَا يُوسُفُ فِى نَفْسِهِۦ وَلَمْ يُبْدِهَا لَهُمْ ۚ قَالَ أَنتُمْ شَرٌّ مَّكَانًا ۖ وَٱللَّهُ أَعْلَمُ بِمَا تَصِفُونَ ٧٧

78. አንተ የተከበርከው ሆይ! «ለእርሱ በእርግጥ ታላቅ ሽማግሌ አባት አለው፡፡ ስለዚህ በእርሱ ስፍራ አንደኛችንን ያዝ፡፡ እኛ ከመልካም ሠሪዎች ሆነህ እናይሃለንና» አሉት፡፡

قَالُوا۟ يَـٰٓأَيُّهَا ٱلْعَزِيزُ إِنَّ لَهُۥٓ أَبًا شَيْخًا كَبِيرًا فَخُذْ أَحَدَنَا مَكَانَهُۥٓ ۖ إِنَّا نَرَىٰكَ مِنَ ٱلْمُحْسِنِينَ ٧٨

79. «ዕቃችንን እርሱ ዘንድ ያገኘንበትን ሰው እንጂ ሌላን ከመያዝ በአላህ እንጠብቃለን፡፡ እኛ ያን ጊዜ በእርግጥ በዳዮች ነን» አለ፡፡

قَالَ مَعَاذَ ٱللَّهِ أَن نَّأۡخُذَ إِلَّا مَن وَجَدۡنَا مَتَٰعَنَا عِندَهُۥٓ إِنَّآ إِذٗا لَّظَٰلِمُونَ ﰎ

80. ከርሱም ተስፋን በቆረጡ ጊዜ የሚመካከሩ ሆነው ገለል አሉ፡፡ ታላቃቸው አለ «አባታችሁ በናንተ ላይ ከአላህ የሆነን መታመኛ ኪዳን በእርግጥ የያዘባችሁ መሆኑን ከዚህም በፊት በዩሱፍ ላይ ግፍ የሠራችሁትን አታውቁምን ስለዚህ አባቴ ለእኔ እስከሚፈቅድልኝ ወይም አላህ ለኔ እስከሚፈርድልኝ ድረስ የምስርን ምድር አልለይም፡፡ እርሱም ከፈራጆች ሁሉ በላጭ ነው፡፡

فَلَمَّا ٱسۡتَيۡـَٔسُواْ مِنۡهُ خَلَصُواْ نَجِيّٗاۖ قَالَ كَبِيرُهُمۡ أَلَمۡ تَعۡلَمُوٓاْ أَنَّ أَبَاكُمۡ قَدۡ أَخَذَ عَلَيۡكُم مَّوۡثِقٗا مِّنَ ٱللَّهِ وَمِن قَبۡلُ مَا فَرَّطتُمۡ فِي يُوسُفَۖ فَلَنۡ أَبۡرَحَ ٱلۡأَرۡضَ حَتَّىٰ يَأۡذَنَ لِيٓ أَبِيٓ أَوۡ يَحۡكُمَ ٱللَّهُ لِيۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلۡحَٰكِمِينَ ﰏ

81. «ወደ አባታችሁ ተመለሱ በሉትም፡- አባታችን ሆይ! ልጅህ ሰረቀ፡፡ ባወቅነውም ነገር እንጂ አልመሰከርንም፡፡ ሩቁንም ነገር (ምስጢሩን) ዐዋቂዎች አልነበርንም፡፡

ٱرۡجِعُوٓاْ إِلَىٰٓ أَبِيكُمۡ فَقُولُواْ يَٰٓأَبَانَآ إِنَّ ٱبۡنَكَ سَرَقَ وَمَا شَهِدۡنَآ إِلَّا بِمَا عَلِمۡنَا وَمَا كُنَّا لِلۡغَيۡبِ حَٰفِظِينَ ﰐ

82. «ያችንም በውስጧ የነበርንባትን ከተማ ያችንም በውስጧ የመጣነውን ባለ ግመል ጓድ ጠይቅ፡፡ እኛም በእርግጥ እውነተኞች ነን፡፡»

وَسۡـَٔلِ ٱلۡقَرۡيَةَ ٱلَّتِي كُنَّا فِيهَا وَٱلۡعِيرَ ٱلَّتِيٓ أَقۡبَلۡنَا فِيهَاۖ وَإِنَّا لَصَٰدِقُونَ ﰑ

83. (ያዕቆብ) «አይደለም ነፍሶቻችሁ አንዳች ነገርን ለእናንተ ሸለሙላችሁ፡፡ (ሠራችሁትም)፡፡ መልካምም ትእግስት (ማድረግ) አለብኝ፡፡ እነርሱን (ሦስቱንም) የተሰበሰቡ ሆነው አላህ ሊያመጣልኝ ይከጀላል፡፡ እነሆ እርሱ ዐዋቂ ጥበበኛ ነውና» አላቸው፡፡

قَالَ بَلۡ سَوَّلَتۡ لَكُمۡ أَنفُسُكُمۡ أَمۡرٗاۖ فَصَبۡرٞ جَمِيلٌۖ عَسَى ٱللَّهُ أَن يَأۡتِيَنِي بِهِمۡ جَمِيعًاۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡحَكِيمُ ﰒ

84. ከእነሱም ዘወር አለናኣ«በዩሱፍ ላይ ዋ ሐዘኔ!» አለ፡፡ ዓይኖቹም ከሐዘን (ለቅሶ) የተነሳ ነጡ፡፡ እርሱም በትካዜ የተመላ ነው፡፡

وَتَوَلَّىٰ عَنۡهُمۡ وَقَالَ يَٰٓأَسَفَىٰ عَلَىٰ يُوسُفَ وَٱبۡيَضَّتۡ عَيۡنَاهُ مِنَ ٱلۡحُزۡنِ فَهُوَ كَظِيمٞ ﰓ

85. (እነርሱም) «በአላህ እንምላለን፡፡ ለጥፋት የቀረብክ እስከምትሆን ወይም ከጠፊዎቹ እስከምትሆን ድረስ ዩሱፍን ከማውሳት አትወገድም» አሉ፡፡

قَالُواْ تَٱللَّهِ تَفۡتَؤُاْ تَذۡكُرُ يُوسُفَ حَتَّىٰ تَكُونَ حَرَضًا أَوۡ تَكُونَ مِنَ ٱلۡهَٰلِكِينَ ﰔ

86. «ጭንቀቴንና ሐዘኔንና የማሰሙተው ወደ አላህ ብቻ ነው፡፡ ከአላህም በኩል የማታውቁትን ነገር ዐውቃለሁ» አላቸው፡፡

قَالَ إِنَّمَآ أَشۡكُواْ بَثِّي وَحُزۡنِيٓ إِلَى ٱللَّهِ وَأَعۡلَمُ مِنَ ٱللَّهِ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﰕ

87. «ልጆቼ ሆይ! ሊዱ፤ ከዩሱፍና ከወንድሙም (ወሬ) ተመራመሩ፡፡ ከአላህም እዝነት ተስፋ አትቁረጡ፡፡ እነሆ ከአላህ እዝነት ከሓዲዎች ሕዝቦች እንጂ ተስፋ አይቆርጥም» (አለ)፡፡

يَٰبَنِيَّ ٱذۡهَبُواْ فَتَحَسَّسُواْ مِن يُوسُفَ وَأَخِيهِ وَلَا تَاْيۡـَٔسُواْ مِن رَّوۡحِ ٱللَّهِۖ إِنَّهُۥ لَا يَاْيۡـَٔسُ مِن رَّوۡحِ ٱللَّهِ إِلَّا ٱلۡقَوۡمُ ٱلۡكَٰفِرُونَ ﰖ

88. በእርሱም ላይ በገቡ ጊዜ «አንተ የተከበርከው ሆይ! እኛንም ቤተሰቦቻችንንም ጉዳት ደረሰብን፡፡ ርካሽ ሸቀጥም ይዘን መጥተናል፡፡ ስፍርንም ለኛ ሙላልን፡፡ በኛም ላይ መጽውት አላህ መጽዋቾችን ይመነዳልና» አሉት፡፡

89. «እናንተ የማታውቁ በነበራችሁ ጊዜ በዩሱፍና በወንድሙ ላይ የሰራችሁትን ግፍ ዐወቃችሁን» አላቸው፡፡

90. «አንተ በእርግጥ አንተ ዩሱፍ ነህን» አሉት፡፡ «እኔ ዩሱፍ ነኝ፡፡ ይህም ወንድሜ ነው፡፡ አላህ በኛ ላይ በእርግጥ ለገሰልን፡፡ እነሆ! የሚጠነቀቅና የሚታገስ ሰው (አላህ ይክሰዋል)፡፡ አላህ የበጎ አድራጊዎችን ዋጋ አያጠፋምና» አለ፡፡

91. «በአላህ እንምላለን፡፡ አላህ በኛ ላይ በእርግጥ አበለጠህ፡፡ እኛም በእርግጥ አጥፊዎች ነበርን» አሉ፡፡
92. «ዛሬ በናንተ ላይ ወቀሳ የለባችሁም፡፡ አላህ ለእናንተ ይምራል፡፡ እርሱም ከአዛኞች ሁሉ ይበልጥ አዛኝ ነው» አላቸው፡፤

93. «ይህንን ቀሚሴን ይዛችሁ ሊዱ፡፡ በአባቴ ፊትም ጣሉት የሚያይ ሆኖ ይመጣልና፡፡ ቤተሰቦቻችሁንም ሰብስባችሁ አምጡልኝ» (አላቸው)፡፡

94. ግመል ጫኞቹም (ምስርን) በተለዩ ጊዜ አባታቸው «እኔ የዩሱፍን ሽታ በእርግጥ አገኛለሁ፡፡ ባታቄሉኝ ኖሮ (ታምኑኝ ነበር)» አለ፡፡

95. «በአላህ እንምላለን፡፡ አንተ በእርግጥ በቀድሞው ስህተትህ ውስጥ ነህ» አሉት፡፡
96. አብሳሪውም በመጣ ጊዜ (ቀሚሱን) በፊቱ ላይ ጣለው፡፡ ወዲውም የሚያይ ኾነ፡፡ «እኔ ለእናንተ፡- ከአላህ በኩል የማታውቁትን ዐውቃለሁ አላልኳችሁምን» አላቸው፡፡
97. «አባታችን ሆይ! ለኀጢአቶቻችን ምሕረትን ለምንልን እኛ ጥፋተኞች ነበርንና» አሉ፡፡
98. «ወደፊት ለእናንተ ጌታዬን ምሕረትን እለምንላችኋለሁ፡፡ እነሆ! እርሱ መሓሪው አዛኙ ነውና» አላቸው፡፤

فَلَمَّا دَخَلُواْ عَلَيۡهِ قَالُواْ يَـٰٓأَيُّهَا ٱلۡعَزِيزُ مَسَّنَا وَأَهۡلَنَا ٱلضُّرُّ وَجِئۡنَا بِبِضَٰعَةٖ مُّزۡجَىٰةٖ فَأَوۡفِ لَنَا ٱلۡكَيۡلَ وَتَصَدَّقۡ عَلَيۡنَآۖ إِنَّ ٱللَّهَ يَجۡزِي ٱلۡمُتَصَدِّقِينَ ﴿٨٨﴾

قَالَ هَلۡ عَلِمۡتُم مَّا فَعَلۡتُم بِيُوسُفَ وَأَخِيهِ إِذۡ أَنتُمۡ جَٰهِلُونَ ﴿٨٩﴾

قَالُوٓاْ أَءِنَّكَ لَأَنتَ يُوسُفُۖ قَالَ أَنَا۠ يُوسُفُ وَهَٰذَآ أَخِيۖ قَدۡ مَنَّ ٱللَّهُ عَلَيۡنَآۖ إِنَّهُۥ مَن يَتَّقِ وَيَصۡبِرۡ فَإِنَّ ٱللَّهَ لَا يُضِيعُ أَجۡرَ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ﴿٩٠﴾

قَالُواْ تَٱللَّهِ لَقَدۡ ءَاثَرَكَ ٱللَّهُ عَلَيۡنَا وَإِن كُنَّا لَخَٰطِـِٔينَ ﴿٩١﴾

قَالَ لَا تَثۡرِيبَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡيَوۡمَۖ يَغۡفِرُ ٱللَّهُ لَكُمۡۖ وَهُوَ أَرۡحَمُ ٱلرَّٰحِمِينَ ﴿٩٢﴾

ٱذۡهَبُواْ بِقَمِيصِي هَٰذَا فَأَلۡقُوهُ عَلَىٰ وَجۡهِ أَبِي يَأۡتِ بَصِيرٗا وَأۡتُونِي بِأَهۡلِكُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٩٣﴾

وَلَمَّا فَصَلَتِ ٱلۡعِيرُ قَالَ أَبُوهُمۡ إِنِّي لَأَجِدُ رِيحَ يُوسُفَۖ لَوۡلَآ أَن تُفَنِّدُونِ ﴿٩٤﴾

قَالُواْ تَٱللَّهِ إِنَّكَ لَفِي ضَلَٰلِكَ ٱلۡقَدِيمِ ﴿٩٥﴾

فَلَمَّآ أَن جَآءَ ٱلۡبَشِيرُ أَلۡقَىٰهُ عَلَىٰ وَجۡهِهِۦ فَٱرۡتَدَّ بَصِيرٗاۖ قَالَ أَلَمۡ أَقُل لَّكُمۡ إِنِّيٓ أَعۡلَمُ مِنَ ٱللَّهِ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٩٦﴾

قَالُواْ يَـٰٓأَبَانَا ٱسۡتَغۡفِرۡ لَنَا ذُنُوبَنَآ إِنَّا كُنَّا خَٰطِـِٔينَ ﴿٩٧﴾

قَالَ سَوۡفَ أَسۡتَغۡفِرُ لَكُمۡ رَبِّيٓۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٩٨﴾

99. በዩሱፍ ላይም በገቡ ጊዜ ወላጆቹን ወደርሱ አስጠጋቸው፡፡ «በአላህም ፈቃድ ጥብቆች ስትኾኑ ምስርን ግቡ» አላቸው፡፡

فَلَمَّا دَخَلُواْ عَلَىٰ يُوسُفَ ءَاوَىٰٓ إِلَيۡهِ أَبَوَيۡهِ وَقَالَ ٱدۡخُلُواْ مِصۡرَ إِن شَآءَ ٱللَّهُ ءَامِنِينَ ٩٩

100. ወላጆቹንም በዙፋኑ ላይ አወጣቸው፡፡ ለእርሱም ሰጋጆች ኾነው ወረዱለት፡፡ «አባቴም ሆይ! ይህ ፊት ያየኹት ሕልሜ ፍች ነው፡፡ ጌታ በእርግጥ እውነት አደረጋት፡፡ ከወህኒ ቤትም ባወጣኝና ሰይጣንም በእኔና በወንድሞቼ መካከል ከአበላሸ በኋላ እናንተን ከገጠር ባመጣችሁ ጊዜ በእርግጥ ለኔ መልካም ዋለልኝ፡፡ ጌታዬ ለሚሻው ነገር እዝነቱ ረቂቅ ነው፡፡ እነሆ እሱ ዐዋቂው ጥበበኛው ነው» አለ፡፡

وَرَفَعَ أَبَوَيۡهِ عَلَى ٱلۡعَرۡشِ وَخَرُّواْ لَهُۥ سُجَّدٗاۖ وَقَالَ يَٰٓأَبَتِ هَٰذَا تَأۡوِيلُ رُءۡيَٰيَ مِن قَبۡلُ قَدۡ جَعَلَهَا رَبِّي حَقّٗاۖ وَقَدۡ أَحۡسَنَ بِيٓ إِذۡ أَخۡرَجَنِي مِنَ ٱلسِّجۡنِ وَجَآءَ بِكُم مِّنَ ٱلۡبَدۡوِ مِنۢ بَعۡدِ أَن نَّزَغَ ٱلشَّيۡطَٰنُ بَيۡنِي وَبَيۡنَ إِخۡوَتِيٓۚ إِنَّ رَبِّي لَطِيفٞ لِّمَا يَشَآءُۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡحَكِيمُ ١٠٠

101. «ጌታዬ ሆይ! ከንግሥና በእርግጥ ሰጠኸኝ፡፡ ከሕልሞችም ፍች አስተማርከኝ፡፡ የሰማያትና የምድር ፈጣሪ ሆይ! አንተ በቅርቢቱና በመጨረሻይቱ ዓለም ረዳቴ ነህ፡፡ ሙስሊም ሆኘ ግደለኝ፡፡ በመልካሞቹም አስጠጋኝ» (አለ)፡፡

۞رَبِّ قَدۡ ءَاتَيۡتَنِي مِنَ ٱلۡمُلۡكِ وَعَلَّمۡتَنِي مِن تَأۡوِيلِ ٱلۡأَحَادِيثِۚ فَاطِرَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ أَنتَ وَلِيِّۦ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِۖ تَوَفَّنِي مُسۡلِمٗا وَأَلۡحِقۡنِي بِٱلصَّٰلِحِينَ ١٠١

102. (ሙሐመድ ሆይ) ይህ ወዳንተ የምናወርደው ሲኾን፤ ከሩቅ ወሬዎች ነው፡፡ አንተም እነርሱ (በዩሱፍ) የሚመክሩ ኾነው ነገራቸውን በቆረጡ ጊዜ እነሱ ዘንድ አልነበርክም፡፡

ذَٰلِكَ مِنۡ أَنۢبَآءِ ٱلۡغَيۡبِ نُوحِيهِ إِلَيۡكَۖ وَمَا كُنتَ لَدَيۡهِمۡ إِذۡ أَجۡمَعُوٓاْ أَمۡرَهُمۡ وَهُمۡ يَمۡكُرُونَ ١٠٢

103. አብዛኛዎቹም ሰዎች (ለማመናቸው) ብትጓጓም የሚያምኑ አይደሉም፡፡

وَمَآ أَكۡثَرُ ٱلنَّاسِ وَلَوۡ حَرَصۡتَ بِمُؤۡمِنِينَ ١٠٣

104. በእርሱም (በቁርአን) ላይ ምንም ዋጋ አትጠይቃቸውም፡፡ እርሱ ለዓለማት ግሳጼ እንጂ ሌላ አይደለም፡፡

وَمَا تَسۡـَٔلُهُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۚ إِنۡ هُوَ إِلَّا ذِكۡرٞ لِّلۡعَٰلَمِينَ ١٠٤

105. በሰማያትና በምድርም ካለችው ምልክት ብዙይቱ እነሱ ከርሷ ዘንጊዎች ኾነው በርሷ ላይ ያልፋሉ፡፡

وَكَأَيِّن مِّنۡ ءَايَةٖ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ يَمُرُّونَ عَلَيۡهَا وَهُمۡ عَنۡهَا مُعۡرِضُونَ ١٠٥

106. አብዛኞቻቸውም፤ እነሱ አጋሪዎች ኾነው እንጂ በአላህ አያምኑም፡፡

وَمَا يُؤۡمِنُ أَكۡثَرُهُم بِٱللَّهِ إِلَّا وَهُم مُّشۡرِكُونَ ١٠٦

107. ከአላህ ቅጣት ሸፋኝ አደጋ የምትመጣባቸው ወይም ሰዓቲቱ እነሱ የማያውቁ ሲኾኑ በድንገት የምትመጣባቸው መኾኑዋን አይፈሩምን

أَفَأَمِنُوٓاْ أَن تَأۡتِيَهُمۡ غَٰشِيَةٞ مِّنۡ عَذَابِ ٱللَّهِ أَوۡ تَأۡتِيَهُمُ ٱلسَّاعَةُ بَغۡتَةٗ وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ١٠٧

108. «ይህች መንገዴ ናት፡፡ ወደ አላህ እጠራለሁ፡፡ እኔም የተከተለኝም ሰው በግልጽ ማስረጃ ላይ ነን፡፡ ጥራትም ለአላህ ይገባው፡፡ እኔም ከአጋሪዎቹ አይደለሁም» በል፡፡

قُلۡ هَٰذِهِۦ سَبِيلِيٓ أَدۡعُوٓاْ إِلَى ٱللَّهِۚ عَلَىٰ بَصِيرَةٍ أَنَا۠ وَمَنِ ٱتَّبَعَنِيۖ وَسُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ وَمَآ أَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ١٠٨

109. ካንተ በፊትም ከከተሞች ሰዎች ወደነርሱ ራእይ የምናወርድላቸው የኾኑን ወንዶችን እንጂ አልላክንም፡፡ በምድር ላይ አይኼዱምና የእነዚያን ከእነሱ በፊት የነበሩትን ሰዎች መጨረሻ አይመለከቱምን የመጨረሻይቱም አገር ለእነዚያ ለተጠነቀቁት በእርግጥ የተሻለች ናት፤ አታውቁምን

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ إِلَّا رِجَالٗا نُّوحِيٓ إِلَيۡهِم مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡقُرَىٰٓۗ أَفَلَمۡ يَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَيَنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۗ وَلَدَارُ ٱلۡأٓخِرَةِ خَيۡرٞ لِّلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ﴿١٠٩﴾

110. መልክተኞቹም ተስፋ በቆረጡና እነርሱ በእርግጥ የተዋሹ መኾናቸውን በተጠራጠሩ ጊዜ እርዳታችን መጣላቸው፡፡ (እኛ) የምንሻውም ሰው እንዲድን ተደረገ፡፡ ቅጣታችንም ከአጋሪዎቹ ሕዝቦች ላይ አይመለስም፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا ٱسۡتَيۡـَٔسَ ٱلرُّسُلُ وَظَنُّوٓاْ أَنَّهُمۡ قَدۡ كُذِبُواْ جَآءَهُمۡ نَصۡرُنَا فَنُجِّيَ مَن نَّشَآءُۖ وَلَا يُرَدُّ بَأۡسُنَا عَنِ ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ﴿١١٠﴾

111. በታሪካቸው ውስጥ ለአእምሮ ባለ ቤቶች በእርግጥ መገሰጫ ነበረ፡፡ (ይህ ቁርኣን) የሚቀጣጠፍ ወሬ አይደለም፡፡ ግን ያንን በስተፊቱ ያለውን አረጋጋጭ ለነገርም ሁሉ ገላጭ ለሚያምኑ ሕዝቦችም መሪና ችሮታ ነው፡፡

لَقَدۡ كَانَ فِي قَصَصِهِمۡ عِبۡرَةٞ لِّأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِۗ مَا كَانَ حَدِيثٗا يُفۡتَرَىٰ وَلَٰكِن تَصۡدِيقَ ٱلَّذِي بَيۡنَ يَدَيۡهِ وَتَفۡصِيلَ كُلِّ شَيۡءٖ وَهُدٗى وَرَحۡمَةٗ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ﴿١١١﴾

# ሱረቱ አል-ረዕድ

# سورة الرّعد

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ለ.መ.ረ (አሊፍ ላም ሚም ራ) ይህች (አናቅጽ) ከመጽሐፉ አንቀጾች ናት፡፡ ያም ከጌታህ ወዳንተ የተወረደው እውነት ነው፡፡ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያምኑም፡፡

الٓمٓرۚ تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱلۡكِتَٰبِۗ وَٱلَّذِيٓ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَ ٱلۡحَقُّ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يُؤۡمِنُونَ ﴿١﴾

2. አላህ ያ ሰማያትን የምታዩዋት አዕማድ ሳትኖር ያነሳት ከዚያም በዐርሹ (ዙፋኑ) ላይ (ስልጣኑ) የተደላደለ ፀሐይንና ጨረቃንም የገራ ነው፡፡ ሁሉም ለተወሰነ ጊዜ ይሮጣሉ፡፡ ነገሩን ሁሉ ያስተናብራል፡፡ በጌታችሁ መገናኘት ታረጋግጡ ዘንድ ተዓምራቶችን ይዘረዝራል፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِي رَفَعَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ بِغَيۡرِ عَمَدٖ تَرَوۡنَهَاۖ ثُمَّ ٱسۡتَوَىٰ عَلَى ٱلۡعَرۡشِۖ وَسَخَّرَ ٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَۖ كُلّٞ يَجۡرِي لِأَجَلٖ مُّسَمّٗىۚ يُدَبِّرُ ٱلۡأَمۡرَ يُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّكُم بِلِقَآءِ رَبِّكُمۡ تُوقِنُونَ ﴿٢﴾

3. እርሱም ያ ምድርን የዘረጋ በሷም ተራራዎችንና ወንዞችን ያደረገ በውስጧም ከፍሬዎች ሁሉ ሁለት ሁለት ዓይነቶችን ያደረገ ነው፡፡ ሌሊትን በቀን ይሸፍናል፡፡ በዚህም ውስጥ ለሚያስተነትኑ ሕዝቦች ምልክቶች አሉ፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي مَدَّ ٱلۡأَرۡضَ وَجَعَلَ فِيهَا رَوَٰسِيَ وَأَنۡهَٰرٗاۖ وَمِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِ جَعَلَ فِيهَا زَوۡجَيۡنِ ٱثۡنَيۡنِۖ يُغۡشِي ٱلَّيۡلَ ٱلنَّهَارَۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَتَفَكَّرُونَ ﴿٣﴾

4. በምድርም የተጎራበቱ ቁርጥራጮች አሉ፡፡ ከወይኖችም አትክልቶች አዝርዕቶችም መንታዎችና መንታዎች ያልኾኑ ዘንባባዎችም አሉ፡፡ በአንድ ውሃ ይጠጣሉ፤ (በጣዕምም ይለያያሉ)፡፡ ከፊሉዋንም በከፊሉ ላይ በሚበላው ሰብል እናበልጣለን፡፡ በዚህም ውስጥ ለሚያውቁ ሕዝቦች ተዓምራት አለበት፡፡

وَفِي ٱلۡأَرۡضِ قِطَعٞ مُّتَجَٰوِرَٰتٞ وَجَنَّٰتٞ مِّنۡ أَعۡنَٰبٖ وَزَرۡعٞ وَنَخِيلٞ صِنۡوَانٞ وَغَيۡرُ صِنۡوَانٖ يُسۡقَىٰ بِمَآءٖ وَٰحِدٖ وَنُفَضِّلُ بَعۡضَهَا عَلَىٰ بَعۡضٖ فِي ٱلۡأُكُلِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ٤

5. ብትደነቅም ዐፈር በኾንን ጊዜ እና አዲስ ፍጥረት እንኾናለን ማለታቸው (ታላቅ) ድንቅ ነው፡፡ እነዚህ እነዚያ በጌታቸው የካዱት ናቸው፡፡ እነዚህም እንዛዝላዎች በአንገቶቻቸው ላይ ያሉባቸው ናቸው፡፡ እነዚህም የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

۞وَإِن تَعۡجَبۡ فَعَجَبٞ قَوۡلُهُمۡ أَءِذَا كُنَّا تُرَٰبًا أَءِنَّا لَفِي خَلۡقٖ جَدِيدٍۗ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِرَبِّهِمۡۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ ٱلۡأَغۡلَٰلُ فِيٓ أَعۡنَاقِهِمۡۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِۖ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٥

6. ከእነሱ በፊት የመሰሎቻቸው ቅጣቶች በእርግጥ ያለፉ ሲኾኑ ከመልካሙ በፊት በመጥፎው ያስቸኩሉሃል፡፡ ጌታህም ለሰዎች ከመበደላቸው ጋር በእርግጥ የምህረት ባለቤት ነው፡፡ ጌታህም በእርግጥ ቅጣተ ብርቱ ነው፡፡

وَيَسۡتَعۡجِلُونَكَ بِٱلسَّيِّئَةِ قَبۡلَ ٱلۡحَسَنَةِ وَقَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِهِمُ ٱلۡمَثُلَٰتُۗ وَإِنَّ رَبَّكَ لَذُو مَغۡفِرَةٖ لِّلنَّاسِ عَلَىٰ ظُلۡمِهِمۡۖ وَإِنَّ رَبَّكَ لَشَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٦

7. እነዚያም የካዱት በእርሱ ላይ ከጌታው ተዓምር ለምን አልተወረደለትም ይላሉ፡፡ አንተ አስፈራሪ ብቻ ነህ፡፡ ለሕዝብም ሁሉ መሪ አላቸው፡፡

وَيَقُولُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوۡلَآ أُنزِلَ عَلَيۡهِ ءَايَةٞ مِّن رَّبِّهِۦٓۗ إِنَّمَآ أَنتَ مُنذِرٞۖ وَلِكُلِّ قَوۡمٍ هَادٍ ٧

8. አላህ ሴት ሁሉ የምታረግዘውን ያውቃል፡፡ ማሕጸኖችም የሚያጎድሉትን የሚጨምሩትንም (ያውቃል)፡፡ ነገሩም ሁሉ እርሱ ዘንድ በልክ የተወሰነ ነው፡፤

ٱللَّهُ يَعۡلَمُ مَا تَحۡمِلُ كُلُّ أُنثَىٰ وَمَا تَغِيضُ ٱلۡأَرۡحَامُ وَمَا تَزۡدَادُۚ وَكُلُّ شَيۡءٍ عِندَهُۥ بِمِقۡدَارٍ ٨

9. ሩቁንና ቅርቡን ዐዋቂ ታላቅ የላቀ ነው፡፡

عَٰلِمُ ٱلۡغَيۡبِ وَٱلشَّهَٰدَةِ ٱلۡكَبِيرُ ٱلۡمُتَعَالِ ٩

10. ከእናንተ ውስጥ ቃሉን ዝቅ ያደረገ ሰው በእርሱ የጮኸም ሰው እርሱ በሌሊት ተደባቂም በቀን (ተገልጾ) ኺያጅም የኾነ ሰው (እርሱ ዘንድ) እኩል ነው፡፡

سَوَآءٞ مِّنكُم مَّنۡ أَسَرَّ ٱلۡقَوۡلَ وَمَن جَهَرَ بِهِۦ وَمَنۡ هُوَ مُسۡتَخۡفِۭ بِٱلَّيۡلِ وَسَارِبُۢ بِٱلنَّهَارِ ١٠

11. ለእርሱ (ለሰው) ከስተፊቱም ከኋላውም በአላህ ትዕዛዝ (ከክፉ) የሚጠብቁት ተተካኪዎች (መላእክት) አሉት፡፡ አላህ በሕዝቦች ዘንድ ያለውን ጸጋ በነፍሶቻቸው ያለውን (ኹኔታ) እስከሚለውጡ ድረስ አይለውጥም፡፡ አላህም በሰዎች ላይ ክፉን በሻ ጊዜ ለእርሱ መመለስ የለውም፡፡ ለእነርሱም ከእርሱ ሌላ ምንም ተከላካይ የላቸውም፡፡

لَهُۥ مُعَقِّبَٰتٞ مِّنۢ بَيۡنِ يَدَيۡهِ وَمِنۡ خَلۡفِهِۦ يَحۡفَظُونَهُۥ مِنۡ أَمۡرِ ٱللَّهِۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُغَيِّرُ مَا بِقَوۡمٍ حَتَّىٰ يُغَيِّرُواْ مَا بِأَنفُسِهِمۡۗ وَإِذَآ أَرَادَ ٱللَّهُ بِقَوۡمٖ سُوٓءٗا فَلَا مَرَدَّ لَهُۥۚ وَمَا لَهُم مِّن دُونِهِۦ مِن وَالٍ ١١

12. እርሱ ያ የምትፈሩና የምትከጅሉም ስትሆኑ ብልጭታን የሚያሳያችሁ ከባዶች ደመናዎችንም የሚያስገኝ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي يُرِيكُمُ ٱلۡبَرۡقَ خَوۡفٗا وَطَمَعٗا وَيُنشِئُ ٱلسَّحَابَ ٱلثِّقَالَ ١٢

13. ነጎድጓድም አላህን በማመስገን ያጠራል፡፡ መላእክትም እርሱን ለመፍራት (ያጠሩታል)፡፡ ሙብረቆችንም ይልካል፡፡ እነርሱም (ከሓዲዎች) በአላህ የሚከራከሩ ሲሆኑ በእርሷ የሚሻውን ሰው ይመታል፡፡ እርሱም ኀይለ ብርቱ ነው፡፡

وَيُسَبِّحُ ٱلرَّعۡدُ بِحَمۡدِهِۦ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ مِنۡ خِيفَتِهِۦ وَيُرۡسِلُ ٱلصَّوَٰعِقَ فَيُصِيبُ بِهَا مَن يَشَآءُ وَهُمۡ يُجَٰدِلُونَ فِي ٱللَّهِ وَهُوَ شَدِيدُ ٱلۡمِحَالِ ﴿١٣﴾

14. ለእርሱ (ለአላህ) የእውነት መጥሪያ አለው፡፡ እነዚያም ከእርሱ ሌላ የሚገዙዋቸው (ጣዖታት) ወደ አፉ ይደርስ ዘንድ ወደ ውሃ መዳፎቹን (በሩቅ ሆኖ) እንደሚዘረጋ (ሰው መልስ) እንጂ ለነርሱ በምንም አይመልሱላቸውም፡፡ እርሱም ወደ አፉ ደራሽ አይደለም፡፡ የከሓዲዎችም ጥሪ በከንቱ እንጂ አይደለም፡፡

لَهُۥ دَعۡوَةُ ٱلۡحَقِّۚ وَٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ مِن دُونِهِۦ لَا يَسۡتَجِيبُونَ لَهُم بِشَيۡءٍ إِلَّا كَبَٰسِطِ كَفَّيۡهِ إِلَى ٱلۡمَآءِ لِيَبۡلُغَ فَاهُ وَمَا هُوَ بِبَٰلِغِهِۦۚ وَمَا دُعَآءُ ٱلۡكَٰفِرِينَ إِلَّا فِي ضَلَٰلٖ ﴿١٤﴾

15. በሰማያትና በምድርም ያሉት ሁሉ በውድም ሆነ በግድ ለአላህ ይሰግዳሉ፡ ጥላዎቻቸውም በጧቶችና በሠርኮች ይሰግዳሉ፡፡

وَلِلَّهِ يَسۡجُدُ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ طَوۡعٗا وَكَرۡهٗا وَظِلَٰلُهُم بِٱلۡغُدُوِّ وَٱلۡأٓصَالِ۩ ﴿١٥﴾

16. «የሰማያትና የምድር ጌታ ማን ነው» በላቸው፡፡ «አላህ ነው» በል፡፡ «ለነፍሶቻቸው ጥቅምንም ጉዳትንም የማይችሉን ረዳቶች ከርሱ ሌላ ያዛችሁን» በላቸው፡፡ «ዕውርና የሚያይ ይስተካከላሉን ወይስ ጨለማዎችና ብርሃን ይስተካከላሉን ወይስ ለአላህ እንደርሱ አፈጣጠር የፈጠሩን ተጋሪዎች አደረጉለትና ፍጥረቱ በእነሱ ላይ ተመሳሰለባቸውን» በል፤ «አላህ ሁሉመናውን ፈጣሪ ነው፡፡ እርሱም አንዱ አሸናፊው ነው» በል፡፡

قُلۡ مَن رَّبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ قُلِ ٱللَّهُۚ قُلۡ أَفَٱتَّخَذۡتُم مِّن دُونِهِۦٓ أَوۡلِيَآءَ لَا يَمۡلِكُونَ لِأَنفُسِهِمۡ نَفۡعٗا وَلَا ضَرّٗاۚ قُلۡ هَلۡ يَسۡتَوِي ٱلۡأَعۡمَىٰ وَٱلۡبَصِيرُ أَمۡ هَلۡ تَسۡتَوِي ٱلظُّلُمَٰتُ وَٱلنُّورُۗ أَمۡ جَعَلُواْ لِلَّهِ شُرَكَآءَ خَلَقُواْ كَخَلۡقِهِۦ فَتَشَٰبَهَ ٱلۡخَلۡقُ عَلَيۡهِمۡۚ قُلِ ٱللَّهُ خَٰلِقُ كُلِّ شَيۡءٖ وَهُوَ ٱلۡوَٰحِدُ ٱلۡقَهَّٰرُ ﴿١٦﴾

17. ከሰማይ ውሃን አወረደ፡፡ ሸለቆዎቹም በመጠናቸው ፈሰሱ፡፡ ጎርፉም አስፋፊውን ኮረፋት ተሸከመ፡፡ ለጌጥ ወይም ለዕቃ ፍላጎት በእርሱ ላይ እሳት የሚያነዱበትም (ማዕድን) ብጤው የኾነ ኮረፋት አልለው፡፡ እንደዚሁ አላህ ለእውነትና ለውሸት ምሳሌን ያደርጋል፡፡ ኮረፋቱማ ግብስብስ ኾኖ ይጠፋል፡፡ ለሰዎች የሚጠቅመውማ በምድር ላይ ይቆያል፡፡ እንደዚሁ አላህ ምሳሌዎችን ይገልፃል፡፡

أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَسَالَتۡ أَوۡدِيَةُۢ بِقَدَرِهَا فَٱحۡتَمَلَ ٱلسَّيۡلُ زَبَدٗا رَّابِيٗاۖ وَمِمَّا يُوقِدُونَ عَلَيۡهِ فِي ٱلنَّارِ ٱبۡتِغَآءَ حِلۡيَةٍ أَوۡ مَتَٰعٖ زَبَدٞ مِّثۡلُهُۥۚ كَذَٰلِكَ يَضۡرِبُ ٱللَّهُ ٱلۡحَقَّ وَٱلۡبَٰطِلَۚ فَأَمَّا ٱلزَّبَدُ فَيَذۡهَبُ جُفَآءٗۖ وَأَمَّا مَا يَنفَعُ ٱلنَّاسَ فَيَمۡكُثُ فِي ٱلۡأَرۡضِۚ كَذَٰلِكَ يَضۡرِبُ ٱللَّهُ ٱلۡأَمۡثَالَ ﴿١٧﴾

18. ለእነዚያ ለጌታቸው ለታዘዙት መልካም ነገር (ገነት) አልላቸው፡፡ እነዚያም ለእርሱ ያልታዘዙት ለእነሱ በምድር ያለው ሁሉ ከእርሱም ጋር ብጤው ቢኖራቸው ኖሮ በእርሱ በተበዡበት ነበር፡፡ እነዚያ ለእነሱ ክፉ ምርመራ አለባቸው፡፡ መኖሪያቸውም ገሀነም ናት፡፡ ፍራሻቸውም ከፋች!

لِلَّذِينَ ٱسۡتَجَابُواْ لِرَبِّهِمُ ٱلۡحُسۡنَىٰۚ وَٱلَّذِينَ لَمۡ يَسۡتَجِيبُواْ لَهُۥ لَوۡ أَنَّ لَهُم مَّا فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا وَمِثۡلَهُۥ مَعَهُۥ لَٱفۡتَدَوۡاْ بِهِۦٓۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ سُوٓءُ ٱلۡحِسَابِ وَمَأۡوَىٰهُمۡ جَهَنَّمُۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمِهَادُ ﴿١٨﴾

19. ከጌታህ ወዳንተ የተወረደው እውነት መኾኑን የሚያውቅ ሰው እንደዚያ እርሱ ዕውር እንደኾነው ሰው ነውን የሚገሠጹት የአእምሮ ባለቤቶች ብቻ ናቸው፡፡

20. እነዚያ በአላህ ቃል ኪዳን የሚሞሉ የጠበቀውንም ኪዳን የማያፈርሱ ናቸው፡፡

21. እነዚያም አላህ እንዲቀጠል በእርሱ ያዘዘውን ነገር የሚቀጥሉ ጌታቸውንም የሚያከብሩ መጥፎንም ቁጥጥር የሚፈሩ ናቸው፡፡

22. እነዚያም የጌታቸውን ውዴታ ለመፈለግ የታገሱ፣ ሶላትንም አዘውትረው የሰገዱ፣ እኛ ከሰጠናቸው ሲሳይም በምስጢርም ኾነ በግልጽ የመጸወቱ፣ ክፉውንም ነገር በበጎ የሚገፈትሩ ናቸው፡፡ እነዚያ ለእነሱ መጨረሻይቱ ምስጉን አገር አለቻቸው፡፡

23. (እርሷም) የመኖሪያ ገነቶች ናት፡፡ ይገቡባታል፡፡ ከአባቶቻቸውም፣ ከሚስቶቻቸውም፣ ከዘርያቸውም መልካም የሠራ ሰው (ይገባታል)፡፡ መላእክትም በእነርሱ ላይ ከየደጃፉ ሁሉ ይገባሉ፡፡

24. «ሰላም ለእናንተ ይኹን፡፡ (ይህ ምንዳ) በመታገሳችሁ ነው፡፡ የመጨረሻይቱም አገር ምን ታምር!» (ይሏቸዋል)፡፡

25. እነዚያም የአላህን ቃል ኪዳን ከጠበቀ በኋላ የሚያፈርሱ አላህም እንዲቀጠል በእርሱ ያዘዘውን ነገር የሚቆርጡ በምድርም ላይ የሚያበላሹ እነዚያ ለነሱ እርግማን አለባቸው፡፡ ለእነሱም መጥፎ አገር (ገሀነም) አላቸው፡፡

26. አላህ ለሚሻው ሰው ሲሳይን ያሰፋል፤ ያጠባልም፡፡ (ከሓዲዎች) በቅርቢቱም ሕይወት ተደሰቱ፡፡ የቅርቢቱም ሕይወት በመጨረሻይቱ አንጻር (ትንሽ) መጠቀሚያ እንጂ ምንም አይደለችም፡፡

27. እነዚያም የካዱት «በእርሱ ላይ ከጌታው ተዓምር ለምን አልተወረደም» ይላሉ፡፡ «አላህ የሚሻውን ያጠምማል፡፡ የተመለሰውንም ሰው ወደርሱ ይመራል» በላቸው፡፡

28. (እነሱም) እነዚያ ያመኑ ልቦቻቸውም አላህን በማውሳት የሚረኩ ናቸው፡፡ ንቁ! አላህን በማውሳት ልቦች ይረካሉ፡፡

29. እነዚያ ያመኑትና መልካም ሥራዎችን የሠሩት ለእነሱ ደግ ኑሮ መልካም መመለሻም አላቸው፡፡

۞أَفَمَن يَعۡلَمُ أَنَّمَآ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَ ٱلۡحَقُّ كَمَنۡ هُوَ أَعۡمَىٰٓۚ إِنَّمَا يَتَذَكَّرُ أُوْلُواْ ٱلۡأَلۡبَٰبِ ١٩

ٱلَّذِينَ يُوفُونَ بِعَهۡدِ ٱللَّهِ وَلَا يَنقُضُونَ ٱلۡمِيثَٰقَ ٢٠

وَٱلَّذِينَ يَصِلُونَ مَآ أَمَرَ ٱللَّهُ بِهِۦٓ أَن يُوصَلَ وَيَخۡشَوۡنَ رَبَّهُمۡ وَيَخَافُونَ سُوٓءَ ٱلۡحِسَابِ ٢١

وَٱلَّذِينَ صَبَرُواْ ٱبۡتِغَآءَ وَجۡهِ رَبِّهِمۡ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَأَنفَقُواْ مِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ سِرّٗا وَعَلَانِيَةٗ وَيَدۡرَءُونَ بِٱلۡحَسَنَةِ ٱلسَّيِّئَةَ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عُقۡبَى ٱلدَّارِ ٢٢

جَنَّٰتُ عَدۡنٖ يَدۡخُلُونَهَا وَمَن صَلَحَ مِنۡ ءَابَآئِهِمۡ وَأَزۡوَٰجِهِمۡ وَذُرِّيَّٰتِهِمۡۖ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَدۡخُلُونَ عَلَيۡهِم مِّن كُلِّ بَابٖ ٢٣

سَلَٰمٌ عَلَيۡكُم بِمَا صَبَرۡتُمۡۚ فَنِعۡمَ عُقۡبَى ٱلدَّارِ ٢٤

وَٱلَّذِينَ يَنقُضُونَ عَهۡدَ ٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ مِيثَٰقِهِۦ وَيَقۡطَعُونَ مَآ أَمَرَ ٱللَّهُ بِهِۦٓ أَن يُوصَلَ وَيُفۡسِدُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمُ ٱللَّعۡنَةُ وَلَهُمۡ سُوٓءُ ٱلدَّارِ ٢٥

ٱللَّهُ يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقۡدِرُۚ وَفَرِحُواْ بِٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَمَا ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا فِي ٱلۡأٓخِرَةِ إِلَّا مَتَٰعٞ ٢٦

وَيَقُولُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوۡلَآ أُنزِلَ عَلَيۡهِ ءَايَةٞ مِّن رَّبِّهِۦۚ قُلۡ إِنَّ ٱللَّهَ يُضِلُّ مَن يَشَآءُ وَيَهۡدِيٓ إِلَيۡهِ مَنۡ أَنَابَ ٢٧

ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَتَطۡمَئِنُّ قُلُوبُهُم بِذِكۡرِ ٱللَّهِۗ أَلَا بِذِكۡرِ ٱللَّهِ تَطۡمَئِنُّ ٱلۡقُلُوبُ ٢٨

ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ طُوبَىٰ لَهُمۡ وَحُسۡنُ مَـَٔابٖ ٢٩

30. እንደዚሁ ከበፊትዋ ብዙ ሕዝቦች በእርግጥ ያለፉ ወደኾነችው ሕዝብ እነርሱ በአልረሕማን የሚክዱ ሲኾኑ ያንን ወደ አንተ ያወረድነውን ቁርኣን በእነርሱ ላይ ታነብላቸው ዘንድ ላክንህ፡፡ «እርሱ (አልረሕማን) ጌታዬ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ በርሱ ላይ ተጠጋሁ፡፡ መመለሻየም ወደርሱ ብቻ ነው» በላቸው፡፡

كَذَٰلِكَ أَرۡسَلۡنَٰكَ فِيٓ أُمَّةٖ قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِهَآ أُمَمٞ لِّتَتۡلُوَاْ عَلَيۡهِمُ ٱلَّذِيٓ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ وَهُمۡ يَكۡفُرُونَ بِٱلرَّحۡمَٰنِۚ قُلۡ هُوَ رَبِّي لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ عَلَيۡهِ تَوَكَّلۡتُ وَإِلَيۡهِ مَتَابِ ٣٠

31. ቁርኣንም በእርሱ ተራራዎች በተነዱበት ወይም በእርሱ ምድር በተቆራረጠችበት ወይም በእርሱ ሙታን እንዲናገሩ በተደረጉበት ኖሮ (የመካ ከሓዲዎች ባላመኑ ነበር)፡፡ በእውነቱ ነገሩ ሁሉ የአላህ ነው፡፡ እነዚያ ያመኑት ሰዎች እነሆ አላህ በሻ ኖሮ ሰዎችን በመላ በእርግጥ ይመራቸው እንደነበረ አያውቁምን እነዚያም የካዱት በሥራቸው ምክንያት (አጥፊ) ዐደጋ የምታገኛቸው ከመኾን ወይም የአላህ ቀጠሮ እስኪመጣ በአገራቸው አቅራቢያ (አንተ) የምትሰፍርባቸው ከመኾን አይወገዱም፡፡ አላህ ቀጠሮውን አያፈርስምና፡፡

وَلَوۡ أَنَّ قُرۡءَانٗا سُيِّرَتۡ بِهِ ٱلۡجِبَالُ أَوۡ قُطِّعَتۡ بِهِ ٱلۡأَرۡضُ أَوۡ كُلِّمَ بِهِ ٱلۡمَوۡتَىٰۗ بَل لِّلَّهِ ٱلۡأَمۡرُ جَمِيعًاۗ أَفَلَمۡ يَاْيۡـَٔسِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَن لَّوۡ يَشَآءُ ٱللَّهُ لَهَدَى ٱلنَّاسَ جَمِيعٗاۗ وَلَا يَزَالُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ تُصِيبُهُم بِمَا صَنَعُواْ قَارِعَةٌ أَوۡ تَحُلُّ قَرِيبٗا مِّن دَارِهِمۡ حَتَّىٰ يَأۡتِيَ وَعۡدُ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُخۡلِفُ ٱلۡمِيعَادَ ٣١

32. ከአንተ በፊት በነበሩትም መልክተኞች በእርግጥ ተላግጠባቸዋል፡፡ ለእነዚያም ለካዱት ጊዜን ሰጠኋቸው፡፡ ከዚያም (በቅጣት) ያዝኩዋቸው፡፡ ቅጣቴም እንዴት ነበር!

وَلَقَدِ ٱسۡتُهۡزِئَ بِرُسُلٖ مِّن قَبۡلِكَ فَأَمۡلَيۡتُ لِلَّذِينَ كَفَرُواْ ثُمَّ أَخَذۡتُهُمۡۖ فَكَيۡفَ كَانَ عِقَابِ ٣٢

33. እርሱ በነፍስ ሁሉ ላይ በሠራቸው ሥራ ተጠባባቂ የኾነው (አላህ እንደዚህ እንዳልኾነው ጣዖት ብጤ ነውን) ለአላህም ተጋሪዎችን አደረጉ፡፡ ጥሯቸው «አላህን በምድር ውስጥ የማያውቀው ኖሮ ትነግሩታላችሁን ወይስ ከቃል በግልጽ (ፍቺ በሌለው ከንቱ ቃል ተጋሪዎች በማለት ትጠሩዋቸዋላችሁን)» በላቸው፡፡ በእውነቱ ለእነዚያ ለካዱት ተንኮላቸው ተሸለመላቸው፡፡ ከእውነቱ መንገድም ታገዱ፡፡ አላህም ያጠመመው ሰው ለእርሱ ምንም አቅኚ የለውም፡፡

أَفَمَنۡ هُوَ قَآئِمٌ عَلَىٰ كُلِّ نَفۡسِۭ بِمَا كَسَبَتۡۗ وَجَعَلُواْ لِلَّهِ شُرَكَآءَ قُلۡ سَمُّوهُمۡۚ أَمۡ تُنَبِّـُٔونَهُۥ بِمَا لَا يَعۡلَمُ فِي ٱلۡأَرۡضِ أَم بِظَٰهِرٖ مِّنَ ٱلۡقَوۡلِۗ بَلۡ زُيِّنَ لِلَّذِينَ كَفَرُواْ مَكۡرُهُمۡ وَصُدُّواْ عَنِ ٱلسَّبِيلِۗ وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِنۡ هَادٖ ٣٣

34. ለእነሱ በቅርቢቱ ሕይወት ቅጣት አላቸው፡፡ የመጨረሻይቱም (ዓለም) ቅጣት በጣም የበረታ ነው፡፡ ለእነሱም ከአላህ (ቅጣት) ምንም ጠባቂ የላቸውም፡፡

لَّهُمۡ عَذَابٞ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَعَذَابُ ٱلۡأٓخِرَةِ أَشَقُّۖ وَمَا لَهُم مِّنَ ٱللَّهِ مِن وَاقٖ ٣٤

35. ያች ጥንቁቆቹ ተስፋ የተሰጧት ገነት ምጣኔዋ (እንደሚነገራችሁ ነው)፡፡ ከሥርዋ ወንዞች ይፈስሳሉ፡፡ ምግቧ (ሁልጊዜ) የማይቋረጥ፤ ነው፡፡ ጥላዋም (እንደዚሁ)፡፡ ይህች የእነዚያ የተጠነቀቁት መጨረሻ ናት፡፡ የከሃዲዎችም መጨረሻ እሳት ናት፡፡

۞مَّثَلُ ٱلۡجَنَّةِ ٱلَّتِي وُعِدَ ٱلۡمُتَّقُونَۖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۖ أُكُلُهَا دَآئِمٞ وَظِلُّهَاۚ تِلۡكَ عُقۡبَى ٱلَّذِينَ ٱتَّقَواْۚ وَّعُقۡبَى ٱلۡكَٰفِرِينَ ٱلنَّارُ ٣٥

36. እነዚያም መጽሐፉን የሰጠናቸው ወዳንተ በተወረደው ይደሰታሉ፡፡ ከአሕዛብም ከፊሉን የሚክዱ ሰዎች አልሉ፡፡ «እኔ የታዘዝኩት አላህን ብቻ እንድገዛ በእርሱም እንደዳላጋራ ነው፡፡ ወደእርሱ እጠራለሁ፤ መመለሻዬም ወደእርሱ ነው» በላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يَفۡرَحُونَ بِمَآ أُنزِلَ إِلَيۡكَۖ وَمِنَ ٱلۡأَحۡزَابِ مَن يُنكِرُ بَعۡضَهُۥۚ قُلۡ إِنَّمَآ أُمِرۡتُ أَنۡ أَعۡبُدَ ٱللَّهَ وَلَآ أُشۡرِكَ بِهِۦٓۚ إِلَيۡهِ أَدۡعُواْ وَإِلَيۡهِ مَـَٔابِ ٣٦

37. እንደዚሁ በዐረብኛ የተነገረ ፍትሕ ሲኾን አወረድነው፡፡ ዕውቀቱ ከመጣልህም በኋላ ዝንባሌዎቻቸውን ብትከተል ከአላህ ቅጣት ምንም ረዳትም ጠባቂም የለህም፡፡

وَكَذَٰلِكَ أَنزَلۡنَٰهُ حُكۡمًا عَرَبِيّٗاۚ وَلَئِنِ ٱتَّبَعۡتَ أَهۡوَآءَهُم بَعۡدَ مَا جَآءَكَ مِنَ ٱلۡعِلۡمِ مَا لَكَ مِنَ ٱللَّهِ مِن وَلِيّٖ وَلَا وَاقٖ ٣٧

38. ከአንተ በፊትም መልክተኞችን በእርግጥ ልከናል፡፡ ለእነርሱም ሚስቶችንና ልጆችን አድርገናል፡፡ ለማንኛውም መልክተኛ በአላህ ፈቃድ እንጂ ተዓምር ሊያመጣ አይገባውም፡፡ ለጊዜው ሁሉ ጽሑፍ አለው፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا رُسُلٗا مِّن قَبۡلِكَ وَجَعَلۡنَا لَهُمۡ أَزۡوَٰجٗا وَذُرِّيَّةٗۚ وَمَا كَانَ لِرَسُولٍ أَن يَأۡتِيَ بِـَٔايَةٍ إِلَّا بِإِذۡنِ ٱللَّهِۗ لِكُلِّ أَجَلٖ كِتَابٞ ٣٨

39. አላህ የሚሻውን ያብሳል፤ ያጸድቃልም፡፡ የመጽሐፉ መሠረትም እርሱ ዘንድ ነው፡፡

يَمۡحُواْ ٱللَّهُ مَا يَشَآءُ وَيُثۡبِتُۖ وَعِندَهُۥٓ أُمُّ ٱلۡكِتَٰبِ ٣٩

40. የዚያንም ያስፈራራናቸውን ከፊሉን ብናሳይህ (መልካም ነው)፡፡ ወይም ብንገድልህ (ወቀሳ የለብህም)፡፡ በአንተ ላይ ያለብህ ማድረስ ብቻ ነው፡፡ ምርመራውም በኛ ላይ ነው፡፤

وَإِن مَّا نُرِيَنَّكَ بَعۡضَ ٱلَّذِي نَعِدُهُمۡ أَوۡ نَتَوَفَّيَنَّكَ فَإِنَّمَا عَلَيۡكَ ٱلۡبَلَٰغُ وَعَلَيۡنَا ٱلۡحِسَابُ ٤٠

41. እኛ ምድርን ከጫፎችዋ የምናጎድላት ኾነን የምንመጣባት መኾናችንን አላዩምን አላህም ይፈርዳል፡ ፡ ለፍርዱም ገልባጭ የለውም፡፡ እርሱም ምርመራው ፈጣን ነው፡፡

أَوَلَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّا نَأۡتِي ٱلۡأَرۡضَ نَنقُصُهَا مِنۡ أَطۡرَافِهَاۚ وَٱللَّهُ يَحۡكُمُ لَا مُعَقِّبَ لِحُكۡمِهِۦۚ وَهُوَ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ٤١

42. እነዚያም ከእነሱ በፊት የነበሩት በእርግጥ መከሩ፡፡ አዘንግቶም የመያዙ ዘዴ በሙሉ የአላህ ነው፡፡ ነፍስ ሁሉ የምትሠራውን ያውቃል፡፡ ከሓዲዎችም የመጨረሻይቱ አገር ለማን እንደምትኾን ወደፊት ያውቃሉ፡፡

وَقَدۡ مَكَرَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ فَلِلَّهِ ٱلۡمَكۡرُ جَمِيعٗاۖ يَعۡلَمُ مَا تَكۡسِبُ كُلُّ نَفۡسٖۗ وَسَيَعۡلَمُ ٱلۡكُفَّٰرُ لِمَنۡ عُقۡبَى ٱلدَّارِ ٤٢

43. እነዚያም የካዱት ሰዎች «መልክተኛ አይደለህም» ይላሉ፡፡ «በእኔና በእናንተ መካከል መስካሪ በአላህና እርሱ ዘንድ የመጽሐፉ ዕውቀት ባለው ሰው በቃ» በላቸው፡፡

وَيَقُولُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَسۡتَ مُرۡسَلٗاۚ قُلۡ كَفَىٰ بِٱللَّهِ شَهِيدَۢا بَيۡنِي وَبَيۡنَكُمۡ وَمَنۡ عِندَهُۥ عِلۡمُ ٱلۡكِتَٰبِ ٤٣

# ሱረቱ ኢብራሂም

# سورة إبراهيم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ሊ.ረ (አሊፍ ላም ራ፤ ይህ ቁርአን) ሰዎችን በጌታቸው ፈቃድ ከጨለማዎች ወደ ብርሃን አሸናፊ ምስጉን ወደ ኾነው:: ጌታ መንገድ ታወጣ ዘንድ ወዳንተ ያወረድነው መጽሐፍ ነው::

الٓرۚ كِتَٰبٌ أَنزَلۡنَٰهُ إِلَيۡكَ لِتُخۡرِجَ ٱلنَّاسَ مِنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِ بِإِذۡنِ رَبِّهِمۡ إِلَىٰ صِرَٰطِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَمِيدِ ١

2. አላህ ያ በሰማያት ያለው በምድርም ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ የኾነ ነው፤ ለከሓዲዎችም ከብርቱ ቅጣት ወዮላቸው::

ٱللَّهِ ٱلَّذِي لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۗ وَوَيۡلٞ لِّلۡكَٰفِرِينَ مِنۡ عَذَابٖ شَدِيدٍ ٢

3. እነዚያ የቅርቢቱን ሕይወት ከመጨረሻይቱ ሕይወት ይበልጥ የሚወዱ ከአላህም መንገድ የሚያግዱ መጥመሟንም የሚፈልጉዋት ናቸው:: እነዚያ በሩቅ ስሕተት ውስጥ ናቸው::

ٱلَّذِينَ يَسۡتَحِبُّونَ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا عَلَى ٱلۡأٓخِرَةِ وَيَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَيَبۡغُونَهَا عِوَجًاۚ أُوْلَٰٓئِكَ فِي ضَلَٰلِۭ بَعِيدٖ ٣

4. ከመልክተኛ ማንኛውንም ለእነርሱ ያብራራላቸው ዘንድ በወገኖቹ ቋንቋ እንጂ በሌላ አልላክንም:: አላህም የሚሻውን ያጠማል:: የሚሻውንም ያቀናል:: እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው::

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا مِن رَّسُولٍ إِلَّا بِلِسَانِ قَوۡمِهِۦ لِيُبَيِّنَ لَهُمۡۖ فَيُضِلُّ ٱللَّهُ مَن يَشَآءُ وَيَهۡدِي مَن يَشَآءُۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٤

5. ሙሳንም ወገኖችህን ከጨለማዎች ወደ ብርሃን አውጣ አላህንም ቀኖች አስገንዝባቸው በማለት በተዓምራታችን በእርግጥ ላክነው:: በዚህ ውስጥ በብዙ ታጋሽና በብዙ አመስጋኝ ለኾኑት ሁሉ በእርግጥ ተዓምራቶች አሉ::

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا مُوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَآ أَنۡ أَخۡرِجۡ قَوۡمَكَ مِنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِ وَذَكِّرۡهُم بِأَيَّىٰمِ ٱللَّهِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّكُلِّ صَبَّارٖ شَكُورٖ ٥

6. ሙሳም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፤ ከፈርዖን ቤተሰቦች መጥፎን ቅጣት የሚያቀምሱዋችሁ ወንዶች ልጆቻችሁንም የሚያርዱ ሴቶቻችሁንም የሚተዉ ሲኾኑ በአዳንናችሁ ጊዜ በእናንተ ላይ (የዋለላችሁን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ:: በዚህም ከጌታችሁ የኾነ ታላቅ ፈተና አለበት::

وَإِذۡ قَالَ مُوسَىٰ لِقَوۡمِهِ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَةَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ إِذۡ أَنجَىٰكُم مِّنۡ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ يَسُومُونَكُمۡ سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِ وَيُذَبِّحُونَ أَبۡنَآءَكُمۡ وَيَسۡتَحۡيُونَ نِسَآءَكُمۡۚ وَفِي ذَٰلِكُم بَلَآءٞ مِّن رَّبِّكُمۡ عَظِيمٞ ٦

7. ጌታችሁም «ብታመሰግኑ በእርግጥ እጨምርላችኋለሁ ብትክዱም (እቀጣችኋለሁ) ቅጣቴ በእርግጥ ብርቱ ነውና» በማለት ባስታወቀ ጊዜ (አስታውሱ)::

وَإِذۡ تَأَذَّنَ رَبُّكُمۡ لَئِن شَكَرۡتُمۡ لَأَزِيدَنَّكُمۡۖ وَلَئِن كَفَرۡتُمۡ إِنَّ عَذَابِي لَشَدِيدٞ ٧

8. ሙሳም አለ «እናንተም በምድር ያለውም ሁሉ በመላ ብትክዱ አላህ በእርግጥ ተብቃቂ ምስጉን ነው:: »

وَقَالَ مُوسَىٰٓ إِن تَكۡفُرُوٓاْ أَنتُمۡ وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا فَإِنَّ ٱللَّهَ لَغَنِيٌّ حَمِيدٌ ٨

9. የእነዚያ ከናንተ በፊት የነበሩት የኑሕ ሕዝቦች የዓድም የሰሙድም የእነዚያም ከእነሱ በኋላ የነበሩት ከአላህ በስተቀር ሌላ የማያውቃቸው (ሕዝቦች) ወሬ አልመጣላችሁምን መልክተኞቻቸው በማስረጃዎች መጧቸው፡፡ እጆቻቸውንም (በቁጭት ሊነክሱ) ወደ አፎቻቸው መለሱ፡፡ አሉም «እኛ እናንተ በርሱ በተላካችሁበት ነገር ካድን እኛም ወደርሱ ከምትጠሩን ነገር አወላዋይ በኾነ ጥርጣሬ ውስጥ ነን፡፡»

أَلَمْ يَأْتِكُمْ نَبَؤُا۟ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِكُمْ قَوْمِ نُوحٍ وَعَادٍ وَثَمُودَ وَٱلَّذِينَ مِنۢ بَعْدِهِمْ لَا يَعْلَمُهُمْ إِلَّا ٱللَّهُ ۚ جَآءَتْهُمْ رُسُلُهُم بِٱلْبَيِّنَٰتِ فَرَدُّوٓا۟ أَيْدِيَهُمْ فِىٓ أَفْوَٰهِهِمْ وَقَالُوٓا۟ إِنَّا كَفَرْنَا بِمَآ أُرْسِلْتُم بِهِۦ وَإِنَّا لَفِى شَكٍّ مِّمَّا تَدْعُونَنَآ إِلَيْهِ مُرِيبٍ ﴿٩﴾

10. መልክተኞቻቸው «ከኀጢአቶቻችሁ እንዲምራችሁ ወደ ተወሰነ ጊዜም (ያለ ቅጣት) እንዲያቆያችሁ የሚጠራችሁ ሲኾን ሰማያትንና ምድርን ፈጣሪ በኾነው አላህ (በመኖሩ) ጥርጣሬ አለን» አሏቸው፡፡ (ሕዝቦቹም) «እናንተ ብጤያችን ሰው እንጂ አይደላችሁም አባቶቻችን ይገዙት ከነበሩት ልትከለክሉን ትሻላችሁ፡፡ ግልጽንም አስረጅ (ካመጣችሁት ሌላ) አምጡልን» አሉ፡፡

۞ قَالَتْ رُسُلُهُمْ أَفِى ٱللَّهِ شَكٌّ فَاطِرِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۖ يَدْعُوكُمْ لِيَغْفِرَ لَكُم مِّن ذُنُوبِكُمْ وَيُؤَخِّرَكُمْ إِلَىٰٓ أَجَلٍ مُّسَمًّى ۚ قَالُوٓا۟ إِنْ أَنتُمْ إِلَّا بَشَرٌ مِّثْلُنَا تُرِيدُونَ أَن تَصُدُّونَا عَمَّا كَانَ يَعْبُدُ ءَابَآؤُنَا فَأْتُونَا بِسُلْطَٰنٍ مُّبِينٍ ﴿١٠﴾

11. መልክተኞቻቸው ለእነርሱ አሉ «እኛ ብጤያችሁ ሰው እንጂ ሌላ አይደለንም ግን አላህ ከባሮቹ በሚሻው ሰው ላይ ይለግሳል፡፡ ለእኛም በአላህ ፈቃድ እንጂ ማስረጃን ልናመጣላችሁ አይገባንም፡፡ በአላህም ላይ ምእምናኖች ይጠጉ፡፡

قَالَتْ لَهُمْ رُسُلُهُمْ إِن نَّحْنُ إِلَّا بَشَرٌ مِّثْلُكُمْ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يَمُنُّ عَلَىٰ مَن يَشَآءُ مِنْ عِبَادِهِۦ ۖ وَمَا كَانَ لَنَآ أَن نَّأْتِيَكُم بِسُلْطَٰنٍ إِلَّا بِإِذْنِ ٱللَّهِ ۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلْيَتَوَكَّلِ ٱلْمُؤْمِنُونَ ﴿١١﴾

12. «መንገዳችንንም በእርግጥ የመራን ሲኾን በአላህ ላይ የማንመካ ለእኛ ምን አለን በማሰቃየታችሁም ላይ በእርግጥ እንታገሳለን፡፡ በአላህም ላይ ተመኪዎች ሁሉ ይመኩ፡፡»

وَمَا لَنَآ أَلَّا نَتَوَكَّلَ عَلَى ٱللَّهِ وَقَدْ هَدَىٰنَا سُبُلَنَا ۚ وَلَنَصْبِرَنَّ عَلَىٰ مَآ ءَاذَيْتُمُونَا ۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلْيَتَوَكَّلِ ٱلْمُتَوَكِّلُونَ ﴿١٢﴾

13. እነዚያም የካዱት ለመልክተኞቻቸው «ከምድራችን በእርግጥ እናወጣችኋለን፤ ወይም ወደ ሃይማኖታችን በእርግጥ ትመለሳላችሁ» አሉ፡፡ ወደእነርሱም ጌታቸው እንዲህ ሲል ላከ «ከሓዲዎችን በእርግጥ እናጠፋለን፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ لِرُسُلِهِمْ لَنُخْرِجَنَّكُم مِّنْ أَرْضِنَآ أَوْ لَتَعُودُنَّ فِى مِلَّتِنَا ۖ فَأَوْحَىٰٓ إِلَيْهِمْ رَبُّهُمْ لَنُهْلِكَنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٣﴾

14. «ከእነሱም በኋላ ምድሪቱን በእርግጥ እናስቀምጣችኋለን፡፡ ይኽ በፊቴ መቆሙን ለሚፈራ ዛቻዬንም ለሚፈራ ሰው ነው፡፡»

وَلَنُسْكِنَنَّكُمُ ٱلْأَرْضَ مِنۢ بَعْدِهِمْ ۚ ذَٰلِكَ لِمَنْ خَافَ مَقَامِى وَخَافَ وَعِيدِ ﴿١٤﴾

15. እርዳታንም (ከአላህ) ፈለጉ፤ (ተረዱም)፡፡ ጨካኝ ሞገደኛ የኾነም ሁሉ አፈረ፡፡

وَٱسْتَفْتَحُوا۟ وَخَابَ كُلُّ جَبَّارٍ عَنِيدٍ ﴿١٥﴾

16. ከስተፊቱ ገሀነም አለበት፡፡ እኻ ከኾነም ውሃ ይጋታል፡፡

مِّن وَرَآئِهِۦ جَهَنَّمُ وَيُسْقَىٰ مِن مَّآءٍ صَدِيدٍ ﴿١٦﴾

17. ይጎነጨዋል፤ ሊውጠውም አይቀርብም፡፡ ሞትም ከየስፍራው ሁሉ ይመጣበታል፤ እርሱም የሚሞት አይደለም፡፡ ከስተፊቱም ከባድ ቅጣት አለ፡፡

يَتَجَرَّعُهُۥ وَلَا يَكَادُ يُسِيغُهُۥ وَيَأْتِيهِ ٱلْمَوْتُ مِن كُلِّ مَكَانٍ وَمَا هُوَ بِمَيِّتٍ ۖ وَمِن وَرَآئِهِۦ عَذَابٌ غَلِيظٌ ﴿١٧﴾

18. የእነዚያ በጌታቸው የካዱት ሰዎች ምሳሌ (መልካም) ሥራዎቻቸው በነፋሻ ቀን ነፋስ በርሱ እንደ በረታችበት አመድ ነው፡፡ በሠሩት ሥራ በምንም ላይ (ሊጠቀሙ) አይችሉም፡፡ ይህ እርሱ ሩቅ ጥፋት ነው፡፡

مَّثَلُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِرَبِّهِمۡۖ أَعۡمَٰلُهُمۡ كَرَمَادٍ ٱشۡتَدَّتۡ بِهِ ٱلرِّيحُ فِي يَوۡمٍ عَاصِفٖۖ لَّا يَقۡدِرُونَ مِمَّا كَسَبُواْ عَلَىٰ شَيۡءٖۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلضَّلَٰلُ ٱلۡبَعِيدُ ١٨

19. አላህ ሰማያትንና ምድርን በእውነት የፈጠረ መኾኑን አታይምን ቢሻ ያጠፋችኋል፡፡ አዲስ ፍጡርንም ያመጣል፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ بِٱلۡحَقِّۚ إِن يَشَأۡ يُذۡهِبۡكُمۡ وَيَأۡتِ بِخَلۡقٖ جَدِيدٖ ١٩

20. ይህም በአላህ ላይ አስቸጋሪ አይደለም፡፡

وَمَا ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ بِعَزِيزٖ ٢٠

21. የተሰበሰቡም ኾነው ለአላህ ይገለጻሉ፡፡ (ሐሳበ) ደካማዎቹም (ተከታዮች) ለእነዚያ ለኮሩት «እኛ ለእናንተ ተከታዮች ነበርን፤ እናንተ ከአላህ ቅጣት ከኛ ላይ አንዳችን ነገር ተከላካዮች ናችሁን» ይላሉ፡፡ (አስከታዮቹም) «አላህ ባቀናን ኖሮ በእርግጥ በመራናችሁ ነበር» ይሏቸዋል፡፡ «ብንበሳጭ ወይም ብንታገስም በእኛ ላይ እኩል ነው፡፡ ለእኛ ምንም መጠጊያ የለንም» ይላሉ፡፡

وَبَرَزُواْ لِلَّهِ جَمِيعٗا فَقَالَ ٱلضُّعَفَٰٓؤُاْ لِلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُوٓاْ إِنَّا كُنَّا لَكُمۡ تَبَعٗا فَهَلۡ أَنتُم مُّغۡنُونَ عَنَّا مِنۡ عَذَابِ ٱللَّهِ مِن شَيۡءٖۚ قَالُواْ لَوۡ هَدَىٰنَا ٱللَّهُ لَهَدَيۡنَٰكُمۡۖ سَوَآءٌ عَلَيۡنَآ أَجَزِعۡنَآ أَمۡ صَبَرۡنَا مَا لَنَا مِن مَّحِيصٖ ٢١

22. ነገሩም በተፈጸመ ጊዜ ሰይጣን ይላቸዋል «አላህ እውነተኛውን ቃል ኪዳን ገባላችሁ፡፡ ቃል ኪዳንም ገባሁላችሁ፤ አፈረስኩባችሁም፡፡ ለእኔም በእናንተ ላይ ምንም ስልጣን አልበረኝም፡፡ ግን ጠራኋችሁ፡፡ ለእኔም ታዘዛችሁ፡፡ ስለዚህ አትውቀሱኝ፤ ነፍሶቻችሁንም ውቀሱ፡፡ እኔ የምረዳችሁ አይደለሁም፡፡ እናንተም የምትረዱኝ አይደላችሁም፡፡ እኔ ከአሁን በፊት ለአላህ ተጋሪ በአደረጋችሁት ነገር ካድኩ፡፡ በዳዮቹ ለእነርሱ በእርግጥ አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡»

وَقَالَ ٱلشَّيۡطَٰنُ لَمَّا قُضِيَ ٱلۡأَمۡرُ إِنَّ ٱللَّهَ وَعَدَكُمۡ وَعۡدَ ٱلۡحَقِّ وَوَعَدتُّكُمۡ فَأَخۡلَفۡتُكُمۡۖ وَمَا كَانَ لِيَ عَلَيۡكُم مِّن سُلۡطَٰنٍ إِلَّآ أَن دَعَوۡتُكُمۡ فَٱسۡتَجَبۡتُمۡ لِيۖ فَلَا تَلُومُونِي وَلُومُوٓاْ أَنفُسَكُمۖ مَّآ أَنَا۠ بِمُصۡرِخِكُمۡ وَمَآ أَنتُم بِمُصۡرِخِيَّ إِنِّي كَفَرۡتُ بِمَآ أَشۡرَكۡتُمُونِ مِن قَبۡلُۗ إِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٢٢

23. እነዚያም ያመኑና መልካም ሥራዎችን የሠሩ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ በጌታቸው ፈቃድ እንዲገቡ ይደረጋሉ፡፡ በውስጣቸው መከባበሪያቸው ሰላም (ለእናንተ ይኹን መባባል) ነው፡፡

وَأُدۡخِلَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا بِإِذۡنِ رَبِّهِمۡۖ تَحِيَّتُهُمۡ فِيهَا سَلَٰمٌ ٢٣

24. አላህ መልካምን ቃል ሥርዋ (በምድር ውስጥ) የተደላደለች ቅርንጫፍዋም ወደ ሰማይ (የረዘመች) እንደሆነች መልካም ዛፍ አድርጎ ምሳሌን እንዴት እንደገለጸ አላየኽምን

أَلَمۡ تَرَ كَيۡفَ ضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلٗا كَلِمَةٗ طَيِّبَةٗ كَشَجَرَةٖ طَيِّبَةٍ أَصۡلُهَا ثَابِتٞ وَفَرۡعُهَا فِي ٱلسَّمَآءِ ٢٤

25. ምግቧን (ፍሬዋን) በጌታዋ ፈቃድ በየጊዜው ትሰጣለች፡፡ አላህም ለሰዎች ይገሰጹ ዘንድ ምሳሌዎችን ይገልጻል፡፡

تُؤۡتِيٓ أُكُلَهَا كُلَّ حِينِۭ بِإِذۡنِ رَبِّهَاۗ وَيَضۡرِبُ ٱللَّهُ ٱلۡأَمۡثَالَ لِلنَّاسِ لَعَلَّهُمۡ يَتَذَكَّرُونَ ٢٥

26. የመጥፎም ቃል ምሳሌ ከምድር በላይ የተጎለሰሰች ለእርሷ ምንም መደላደል የሌላት እንደኾነች መጥፎ ዛፍ ነው፡፡

وَمَثَلُ كَلِمَةٍ خَبِيثَةٖ كَشَجَرَةٍ خَبِيثَةٍ ٱجۡتُثَّتۡ مِن فَوۡقِ ٱلۡأَرۡضِ مَا لَهَا مِن قَرَارٖ ٢٦

27. አላህ እነዚያን ያመኑትን በቅርቢቱም ሕይወት በመጨረሻይቱም (በመቃብር) በተረጋገጠው ቃል ላይ ያረጋቸዋል፡፡ ከሓዲዎችንም አላህ ያሳስታቸዋል፡፡ አላህም የሚሻውን ይሠራል፡፡

يُثَبِّتُ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱلۡقَوۡلِ ٱلثَّابِتِ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَفِي ٱلۡأٓخِرَةِۖ وَيُضِلُّ ٱللَّهُ ٱلظَّٰلِمِينَۚ وَيَفۡعَلُ ٱللَّهُ مَا يَشَآءُ ٢٧

28. ወደእነዚያ የአላህን ጸጋ በክህደት ወደ ለወጡት ሕዝቦቻቸውንም በጥፋት አገር ወዳሰፈሩት (ወደ ቁረይሾች) አላየህምን

۞أَلَمۡ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ بَدَّلُواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ كُفۡرٗا وَأَحَلُّواْ قَوۡمَهُمۡ دَارَ ٱلۡبَوَارِ ٢٨

29. (አገሪቱም) የሚገቧት ስትኾን ገሀነም ናት፡፡ ምን ትከፋም መርጊያ!

جَهَنَّمَ يَصۡلَوۡنَهَاۖ وَبِئۡسَ ٱلۡقَرَارُ ٢٩

30. ለአላህም ከመንገዱ ያሳስቱ ዘንድ ባላንጣዎችን አደረጉለት፡፡ «(ጥቂትን) ተጠቀሙ መመለሻችሁም ወደ እሳት ነው» በላቸው፡፡

وَجَعَلُواْ لِلَّهِ أَندَادٗا لِّيُضِلُّواْ عَن سَبِيلِهِۦۗ قُلۡ تَمَتَّعُواْ فَإِنَّ مَصِيرَكُمۡ إِلَى ٱلنَّارِ ٣٠

31. ለእነዚያ ላመኑት ባሮቼ በእርሱ ውስጥ ሽያጭና ወዳጅነት የሌለበት ቀን ከመምጣቱ በፊት ሶላትን በደንቡ ይሰግዳሉ፡፡ ከሰጠናቸውም ሲሳይ በምስጢርም በግልጽም ይለግሳሉ፡፡ (ስገዱ ለግሱም) በላቸው፡፡

قُل لِّعِبَادِيَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ يُقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَيُنفِقُواْ مِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ سِرّٗا وَعَلَانِيَةٗ مِّن قَبۡلِ أَن يَأۡتِيَ يَوۡمٞ لَّا بَيۡعٞ فِيهِ وَلَا خِلَٰلٌ ٣١

32. አላህ ያ ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ ከሰማይም ውሃን ያወረደ በእርሱም ከፍሬዎች ሲሳይን ለእናንተ ያወጣ መርከቦችንም በፈቃዱ በባሕር ላይ ይንሻለሉ ዘንድ ለናንተ የገራ ወንዞችንም ለናንተ የገራ ነው፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَأَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَخۡرَجَ بِهِۦ مِنَ ٱلثَّمَرَٰتِ رِزۡقٗا لَّكُمۡۖ وَسَخَّرَ لَكُمُ ٱلۡفُلۡكَ لِتَجۡرِيَ فِي ٱلۡبَحۡرِ بِأَمۡرِهِۦۖ وَسَخَّرَ لَكُمُ ٱلۡأَنۡهَٰرَ ٣٢

33. ፀሐይንና ጨረቃንም ዘወትር ኼያጆች ሲኾኑ ለእናንተ የገራ ሌሊትንና ቀንንም ለእናንተ የገራላችሁ ነው፡፡

وَسَخَّرَ لَكُمُ ٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَ دَآئِبَيۡنِۖ وَسَخَّرَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ ٣٣

34. ከለመናችሁትም ሁሉ የሰጣችሁ ነው፡፡ የአላህንም ጸጋ ብትቆጥሩ አትዘልቋትም፡፡ ሰው በጣም በደለኛ ከሓዲ ነው፡፡

وَءَاتَىٰكُم مِّن كُلِّ مَا سَأَلۡتُمُوهُۚ وَإِن تَعُدُّواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ لَا تُحۡصُوهَآۗ إِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ لَظَلُومٞ كَفَّارٞ ٣٤

35. ኢብራሂምም ባለ ጊዜ (አስታውስ) «ጌታዬ ሆይ! ይህንን አገር (መካን) ጸጥተኛ አድርገው፡፡ እኔንም ልጆቼንም ጣዖታትን ከመገዛት አርቀን፡፡

وَإِذۡ قَالَ إِبۡرَٰهِيمُ رَبِّ ٱجۡعَلۡ هَٰذَا ٱلۡبَلَدَ ءَامِنٗا وَٱجۡنُبۡنِي وَبَنِيَّ أَن نَّعۡبُدَ ٱلۡأَصۡنَامَ ٣٥

36. «ጌታዬ ሆይ! እነርሱ (ጣዖታት) ከሰዎች ብዙዎችን አሳስተዋልና፡፡ የተከተለኝም ሰው እርሱ ከኔ ነው፡፡ ትእዛዜንም የጣሰ ሰው አንተ መሓሪ አዛኝ ነህ፡፡

رَبِّ إِنَّهُنَّ أَضۡلَلۡنَ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِۖ فَمَن تَبِعَنِي فَإِنَّهُۥ مِنِّيۖ وَمَنۡ عَصَانِي فَإِنَّكَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٣٦

37. «ጌታችን ሆይ! እኔ አዝመራ በሌለው ሸለቆ ውስጥ በተከበረው ቤት (በካዕባ) አጠገብ ከዘሮቼ አስቀመጥኩ፡፡ ጌታችን ሆይ! ሶላትን ያቋቁሙ ዘንድ (አስቀመጥኳቸው)፡፡ ከሰዎችም ልቦችን ወደእነሱ የሚናፍቁ አድርግ፡፡ ያመሰግኑህም ዘንድ ከፍሬዎች ስጣቸው፡፡

رَّبَّنَآ إِنِّيٓ أَسۡكَنتُ مِن ذُرِّيَّتِي بِوَادٍ غَيۡرِ ذِي زَرۡعٍ عِندَ بَيۡتِكَ ٱلۡمُحَرَّمِ رَبَّنَا لِيُقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ فَٱجۡعَلۡ أَفۡـِٔدَةٗ مِّنَ ٱلنَّاسِ تَهۡوِيٓ إِلَيۡهِمۡ وَٱرۡزُقۡهُم مِّنَ ٱلثَّمَرَٰتِ لَعَلَّهُمۡ يَشۡكُرُونَ ٣٧

38. «ጌታችን ሆይ! አንተ የምንደብቀውንም የምንገልጸውንም ሁሉ በእርግጥ ታውቃለህ፡፡ በአላህም ላይ በምድርም በሰማይም ምንም ነገር አይደበቅም፡፡

رَبَّنَآ إِنَّكَ تَعۡلَمُ مَا نُخۡفِي وَمَا نُعۡلِنُۗ وَمَا يَخۡفَىٰ عَلَى ٱللَّهِ مِن شَيۡءٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فِي ٱلسَّمَآءِ ٣٨

39. «ለእዚያ ከሽምግልና በኋላ ኢስማዒልን ኢስሐቅንም ለእኔ ለሰጠኝ አላህ ምስጋና ይገባው፡፡ ጌታዬ ልመናን በእርግጥ ሰሚ ነውና፡፡

ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ ٱلَّذِي وَهَبَ لِي عَلَى ٱلۡكِبَرِ إِسۡمَٰعِيلَ وَإِسۡحَٰقَۚ إِنَّ رَبِّي لَسَمِيعُ ٱلدُّعَآءِ ٣٩

40. «ጌታዬ ሆይ! ሰላትን አዘውትሬ የምሰግድ አድርገኝ፡፡ ከዘሮቼም (አድርግ)፡፡ ጌታችን ሆይ! ጸሎቴንም ተቀበለኝ፤

رَبِّ ٱجۡعَلۡنِي مُقِيمَ ٱلصَّلَوٰةِ وَمِن ذُرِّيَّتِيۚ رَبَّنَا وَتَقَبَّلۡ دُعَآءِ ٤٠

41. «ጌታችን ሆይ! ለእኔም ለወላቼም ለምእመናንም ሁሉ ምርመራ በሚደረግበት ቀን ማር፡፡»

رَبَّنَا ٱغۡفِرۡ لِي وَلِوَٰلِدَيَّ وَلِلۡمُؤۡمِنِينَ يَوۡمَ يَقُومُ ٱلۡحِسَابُ ٤١

42. አላህንም በደለኞች ከሚሠሩት ግፍ ዘንጊ አድርገህ አታስብ፡፡ የሚያቆያቸው ዓይኖች በእርሱ እስከሚፈጡበት ቀን ድረስ ብቻ ነው፡፡

وَلَا تَحۡسَبَنَّ ٱللَّهَ غَٰفِلًا عَمَّا يَعۡمَلُ ٱلظَّٰلِمُونَۚ إِنَّمَا يُؤَخِّرُهُمۡ لِيَوۡمٖ تَشۡخَصُ فِيهِ ٱلۡأَبۡصَٰرُ ٤٢

43. (ወደ ጠሪው መልአክ) ቸኳዮች ራሶቻቸውን አንጋጣጮች ኾነው (ዓይኖቻቸው ይፈጣሉ)፡፡ ዓይኖቻቸው ወደነርሱ አይመለሱም፡፡ ልቦቻቸውም ባዶዎች ናቸው፡፡

مُهۡطِعِينَ مُقۡنِعِي رُءُوسِهِمۡ لَا يَرۡتَدُّ إِلَيۡهِمۡ طَرۡفُهُمۡۖ وَأَفۡـِٔدَتُهُمۡ هَوَآءٞ ٤٣

44. ሰዎችንም ቅጣቱ የሚመጣባቸውን ቀን አስፈራራቸው፡፡ እነዚያም የበደሉት «ጌታችን ሆይ! ወደ ቅርብ ጊዜ ድረስ አቆየን፡፡ ጥሪህን እንቀበላለንና መልክተኞቹንም እንከተላለንና» ይላሉ፡፡ «ከአሁን በፊት (በምድረ ዓለም) ለእናንተ ምንም መወገድ የላችሁም በማለት የማላችሁ አልነበራችሁምን» (ይባላሉ)፡፡

وَأَنذِرِ ٱلنَّاسَ يَوۡمَ يَأۡتِيهِمُ ٱلۡعَذَابُ فَيَقُولُ ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ رَبَّنَآ أَخِّرۡنَآ إِلَىٰٓ أَجَلٖ قَرِيبٖ نُّجِبۡ دَعۡوَتَكَ وَنَتَّبِعِ ٱلرُّسُلَۗ أَوَلَمۡ تَكُونُوٓاْ أَقۡسَمۡتُم مِّن قَبۡلُ مَا لَكُم مِّن زَوَالٖ ٤٤

45. «በእነዚያም ነፍሶቻቸውን በበደሉት ሰዎች መኖሪያ ውስጥ ተቀመጣችሁ፡፡ በእነሱም እንዴት እንደሠራንባቸው ለእናንተ ተገለጸላችሁ፡፡ ለእናንተም ምሳሌዎችን ገለጽንላችሁ፡፡»

وَسَكَنتُمۡ فِي مَسَٰكِنِ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ وَتَبَيَّنَ لَكُمۡ كَيۡفَ فَعَلۡنَا بِهِمۡ وَضَرَبۡنَا لَكُمُ ٱلۡأَمۡثَالَ ٤٥

وَقَدۡ مَكَرُواْ مَكۡرَهُمۡ وَعِندَ ٱللَّهِ مَكۡرُهُمۡ وَإِن كَانَ مَكۡرُهُمۡ لِتَزُولَ مِنۡهُ ٱلۡجِبَالُ ﴿٤٦﴾

46. (በነቢዩ ላይ) ሴራቸውንም በእርግጥ አሴሩ፡፡ ሴራቸውም (ቅጣቱ) አላህ ዘንድ ነው፡፡ ሴራቸውም ኮረብታዎች (ሕግጋቶች) በእርሱ የሚወገዱበት አልነበረም፡፡

فَلَا تَحۡسَبَنَّ ٱللَّهَ مُخۡلِفَ وَعۡدِهِۦ رُسُلَهُۥٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٞ ذُو ٱنتِقَامٖ ﴿٤٧﴾

47. አላህንም መልክተኞቹን (የገባላቸውን) ቃል ኪዳኑን አፍራሽ አድርገህ አታስብ፡፡ አላህ አሸናፊ የመበቀል ባለቤት ነው፡፡

يَوۡمَ تُبَدَّلُ ٱلۡأَرۡضُ غَيۡرَ ٱلۡأَرۡضِ وَٱلسَّمَٰوَٰتُۖ وَبَرَزُواْ لِلَّهِ ٱلۡوَٰحِدِ ٱلۡقَهَّارِ ﴿٤٨﴾

48. ምድር በሌላ ምድር የምትለወጥበትን ሰማያትም (እንደዚሁ) አንድ አሸናፊ ለኾነው አላህም (ፍጡራን ሁሉ) የሚገለጹበት ቀን (አስታውሱ)፡፡

وَتَرَى ٱلۡمُجۡرِمِينَ يَوۡمَئِذٖ مُّقَرَّنِينَ فِي ٱلۡأَصۡفَادِ ﴿٤٩﴾

49. አመጸኞችንም በዚያ ቀን በሰንሰለቶች ተቆራኝተው ታያቸዋለህ፡፡

سَرَابِيلُهُم مِّن قَطِرَانٖ وَتَغۡشَىٰ وُجُوهَهُمُ ٱلنَّارُ ﴿٥٠﴾

50. ቀሚሶቻቸው ከካትራም ናቸው፡፡ ፊቶቻቸውንም እሳት ትሸፍናቸዋለች፡፡

لِيَجۡزِيَ ٱللَّهُ كُلَّ نَفۡسٖ مَّا كَسَبَتۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ﴿٥١﴾

51. አላህ ነፍስን ሁሉ የሠራችውን ይመነዳ ዘንድ (ይህንን አደረገ)፡፡ አላህ ምርመራው ፈጣን ነው፡፡

هَٰذَا بَلَٰغٞ لِّلنَّاسِ وَلِيُنذَرُواْ بِهِۦ وَلِيَعۡلَمُوٓاْ أَنَّمَا هُوَ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞ وَلِيَذَّكَّرَ أُوْلُواْ ٱلۡأَلۡبَٰبِ ﴿٥٢﴾

52. ይህ (ቁርኣን) ለሰዎች ገላጭ ነው፡፡ (ሊመከሩበት)፣ በእርሱም ሊስፈራሩበት፣ እርሱም አንድ አምላክ ብቻ መኾኑን ሊያውቁበት፣ የአእምሮ ባለቤቶችም ሊገሰፁበት (የተወረደ) ነው፡፡

## ሱረቱ አል ሒጅር

## سورة الحجر

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

الٓرۚ تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱلۡكِتَٰبِ وَقُرۡءَانٖ مُّبِينٖ ﴿١﴾

1. አ.ለ.ረ (አሊፍ ላም ራ) ይህች (አናቅጽ) ከመጽሐፉ አንቀጾችና ገላጭ ከኾነው ቁርኣን ናት፡፡

رُّبَمَا يَوَدُّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوۡ كَانُواْ مُسۡلِمِينَ ﴿٢﴾

2. እነዚያ የካዱት (በትንሣኤ ቀን) ሙስሊሞች በኾኑ ኖሩ በብዛት ይመኛሉ፡፡

3. ተዋቸው ይብሉ፤ ይጠቀሙም፡፡ ተስፋም ያዘናጋቸው፡፡ በእርግጥም (መጥፎ ፍጻሜያቸውን) ያውቃሉ፡፡

ذَرۡهُمۡ يَأۡكُلُواْ وَيَتَمَتَّعُواْ وَيُلۡهِهِمُ ٱلۡأَمَلُۖ فَسَوۡفَ يَعۡلَمُونَ ٣

4. ማንኛይቱንም ከተማ ለእርሷ የተወሰነ መጽሐፍ (ጊዜያት) ያላት ኾና እንጂ አላጠፋንም፡፡

وَمَآ أَهۡلَكۡنَا مِن قَرۡيَةٍ إِلَّا وَلَهَا كِتَابٞ مَّعۡلُومٞ ٤

5. ማንኛይቱም ሕዝብ ጊዜዋን ምንም አትቀድምም፡፡ (ከእርሱ) አይቆዩምም፡፡

مَّا تَسۡبِقُ مِنۡ أُمَّةٍ أَجَلَهَا وَمَا يَسۡتَـٔۡخِرُونَ ٥

6. «አንተ ያ በእርሱ ላይ ቁርኣን የተወረደለት ሆይ! አንተ በእርግጥ ዕብድ ነህ» አሉም፡፡

وَقَالُواْ يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِي نُزِّلَ عَلَيۡهِ ٱلذِّكۡرُ إِنَّكَ لَمَجۡنُونٞ ٦

7. «ከእውነተኞቹ እንደ ኾንክ በመላእክት (መስካሪ) ለምን አትመጣንም» (አሉ)፡፡

لَّوۡ مَا تَأۡتِينَا بِٱلۡمَلَـٰٓئِكَةِ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّـٰدِقِينَ ٧

8. መላእክትን በእውነት (በቅጣት) እንጂ አናወርድም፡፡ ያን ጊዜም የሚቆዩ አይደሉም፡፡

مَا نُنَزِّلُ ٱلۡمَلَـٰٓئِكَةَ إِلَّا بِٱلۡحَقِّ وَمَا كَانُوٓاْ إِذٗا مُّنظَرِينَ ٨

9. እኛ ቁርኣንን እኛው አወረድነው፡፡ እኛም ለእርሱ ጠባቂዎቹ ነን፡፡

إِنَّا نَحۡنُ نَزَّلۡنَا ٱلذِّكۡرَ وَإِنَّا لَهُۥ لَحَٰفِظُونَ ٩

10. ከአንተም በፊት በነበሩት በመጀመሪያዎቹ ሕዝቦች ውስጥ (መልክተኞችን) በእርግጥ ልከናል፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ فِي شِيَعِ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٠

11. ማንኛውም መልእክተኛ በእርሱ የሚያላግጡበት ኾነው እንጅ አይመጣቸውም ነበር፡፡

وَمَا يَأۡتِيهِم مِّن رَّسُولٍ إِلَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ١١

12. እንደዚሁ (ማስተባበልን) በአመጸኞቹ ልቦች ውስጥ እናገባዋለን፡፡

كَذَٰلِكَ نَسۡلُكُهُۥ فِي قُلُوبِ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ١٢

13. በእርሱ አያምኑበትም፡፡ የቀድሞዎቹም ድርጊት በእርግጥ አልፋለች፤ (እንደጠፉ ይጠፋሉ)፡፡

لَا يُؤۡمِنُونَ بِهِۦ وَقَدۡ خَلَتۡ سُنَّةُ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٣

14. በእነርሱም ላይ ከሰማይ ደጃፍን በከፈትንላቸውና በእርሱ ሲወጡ በዋሉ ኖሮ፤

وَلَوۡ فَتَحۡنَا عَلَيۡهِم بَابٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ فَظَلُّواْ فِيهِ يَعۡرُجُونَ ١٤

15. «የተዘጉት ዓይኖቻችን ናቸው፡፡ እንዲያውም እኛ የተደገመብን ሰዎች ነን» ባሉ ነበር፡፡

لَقَالُوٓاْ إِنَّمَا سُكِّرَتۡ أَبۡصَٰرُنَا بَلۡ نَحۡنُ قَوۡمٞ مَّسۡحُورُونَ ١٥

16. በሰማይም ላይ ቡርጆችን በእርግጥ አድርገናል፡፡ ለተመልካቾችም (በከዋክብት) አጊጠናታል፡፡

وَلَقَدۡ جَعَلۡنَا فِي ٱلسَّمَآءِ بُرُوجٗا وَزَيَّنَّـٰهَا لِلنَّـٰظِرِينَ ١٦

17. ከተባረረ ሰይጣንም ሁሉ ጠብቀናታል፡፡

وَحَفِظۡنَـٰهَا مِن كُلِّ شَيۡطَٰنٖ رَّجِيمٍ ١٧

18. ግን (ወሬ) መስማትን የሚሰርቅ ወዲያውኑ አብሪ ችቦ ይከተለዋል፡፡ (ያቃጥለዋል)፡፡

إِلَّا مَنِ ٱسۡتَرَقَ ٱلسَّمۡعَ فَأَتۡبَعَهُۥ شِهَابٞ مُّبِينٞ ١٨

19. ምድርንም ዘረጋናት፡፡ በውስጧም ኮረብታዎችን ጣልናባት፡፡ በውስጧም (የተለካን) በቃይ ሁሉ አበቀልንባት፡፡

وَٱلۡأَرۡضَ مَدَدۡنَٰهَا وَأَلۡقَيۡنَا فِيهَا رَوَٰسِيَ وَأَنۢبَتۡنَا فِيهَا مِن كُلِّ شَيۡءٖ مَّوۡزُونٖ ١٩

20. በእርሷም ውስጥ ለእናንተ መኖሪያዎችንና ለእርሱ መጋቢዎቹ ያልኾናችሁትንም (እንስሳትን) አደረግንላችሁ፡፡

وَجَعَلۡنَا لَكُمۡ فِيهَا مَعَٰيِشَ وَمَن لَّسۡتُمۡ لَهُۥ بِرَٰزِقِينَ ٢٠

21. መካዚኖቹም (መከፈቻቸው) እኛ ዘንድ ያልሆነ ምንም ነገር የለም፡፡ በተወሰነም ልክ እንጂ አናወርደውም፡፡

وَإِن مِّن شَيۡءٍ إِلَّا عِندَنَا خَزَآئِنُهُۥ وَمَا نُنَزِّلُهُۥٓ إِلَّا بِقَدَرٖ مَّعۡلُومٖ ﴿٢١﴾

22. ነፋሶችንም (ደመናን) ተሸካሚዎች አድርገን ላክን፡፡ ከሰማይም (ከደመና) ዝናብን አወረድን፡፡ እርሱንም አጠጣናችሁ፡፡ እናንተም ለእርሱ አድላቢዎች አይደላችሁም፡፡

وَأَرۡسَلۡنَا ٱلرِّيَٰحَ لَوَٰقِحَ فَأَنزَلۡنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَسۡقَيۡنَٰكُمُوهُ وَمَآ أَنتُمۡ لَهُۥ بِخَٰزِنِينَ ﴿٢٢﴾

23. እኛም ሕያው የምናደርግና የምንገድል እኛው ብቻ ነን፡፡ እኛም (ፍጡርን ሁሉ ) የምንወርስ (ቀሪ) ነን፡፡

وَإِنَّا لَنَحۡنُ نُحۡيِۦ وَنُمِيتُ وَنَحۡنُ ٱلۡوَٰرِثُونَ ﴿٢٣﴾

24. ከእናንተም ተቀዳሚዎቹን በእርግጥ ዐውቀናል፡፡ ወደ ኋላም ቀሪዎቹን በእርግጥ ዐውቀናል፡፡

وَلَقَدۡ عَلِمۡنَا ٱلۡمُسۡتَقۡدِمِينَ مِنكُمۡ وَلَقَدۡ عَلِمۡنَا ٱلۡمُسۡتَـٔۡخِرِينَ ﴿٢٤﴾

25. ጌታህም እርሱ ይሰበስባቸኋል፡፡ እርሱ ጥበበኛ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ هُوَ يَحۡشُرُهُمۡۚ إِنَّهُۥ حَكِيمٌ عَلِيمٞ ﴿٢٥﴾

26. ሰውንም ከሚቅጨለጨል ሸክላ ከሚገማ ጥቁር ጭቃ በእርግጥ ፈጠርነው፡፡

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ مِن صَلۡصَٰلٖ مِّنۡ حَمَإٖ مَّسۡنُونٖ ﴿٢٦﴾

27. ጃንንም (ከሰው) በፊት ከእሳት ነበልባል ፈጠርነው፡፡

وَٱلۡجَآنَّ خَلَقۡنَٰهُ مِن قَبۡلُ مِن نَّارِ ٱلسَّمُومِ ﴿٢٧﴾

28. ጌታህም ለመላእክት ባለጊዜ (አስታውስ)፡፡ እኔ ሰውን ከሚቅጨለጨል ሸክላ ከሚገማ ጭቃ እፈጥራለሁ፡፡

وَإِذۡ قَالَ رَبُّكَ لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ إِنِّي خَٰلِقُۢ بَشَرٗا مِّن صَلۡصَٰلٖ مِّنۡ حَمَإٖ مَّسۡنُونٖ ﴿٢٨﴾

29. (ፍጥረቱን) ባስተካከልኩትና በውስጡ ከመንፈሴ በነፋሁበትም ጊዜ ለእርሱ ሰጋጆች ኾናችሁ ውደቁ፡፡

فَإِذَا سَوَّيۡتُهُۥ وَنَفَخۡتُ فِيهِ مِن رُّوحِي فَقَعُواْ لَهُۥ سَٰجِدِينَ ﴿٢٩﴾

30. መላእክትም መላውም ተሰብስበው ሰገዱ፡፡

فَسَجَدَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ كُلُّهُمۡ أَجۡمَعُونَ ﴿٣٠﴾

31. ኢብሊስ (ዲያብሎስ) ብቻ ሲቀር፡፡ ከሰጋጆቹ ጋር ከመኾን እንቢ አለ፡፡

إِلَّآ إِبۡلِيسَ أَبَىٰٓ أَن يَكُونَ مَعَ ٱلسَّٰجِدِينَ ﴿٣١﴾

32. (አላህም) «ኢብሊስ ሆይ! ከሰጋጆቹ ጋር የማትኾን ላንተ ምን ምክንያት አለህ» አለው፡፡

قَالَ يَٰٓإِبۡلِيسُ مَا لَكَ أَلَّا تَكُونَ مَعَ ٱلسَّٰجِدِينَ ﴿٣٢﴾

33. «ከሚቅጨለጨል ሸክላ ከግም ጭቃ ለፈጠርከው ሰው ልሰግድ አይገባኝም» አለ፡፡

قَالَ لَمۡ أَكُن لِّأَسۡجُدَ لِبَشَرٍ خَلَقۡتَهُۥ مِن صَلۡصَٰلٖ مِّنۡ حَمَإٖ مَّسۡنُونٖ ﴿٣٣﴾

34. (አላህ) አለው «ከርሷም ውጣ፡፡ አንተ የተባረርክ እርጉም ነህና፡፡»

قَالَ فَٱخۡرُجۡ مِنۡهَا فَإِنَّكَ رَجِيمٞ ﴿٣٤﴾

35. «ባንተ ላይም እስከ ፍርዱ ቀን ድረስ እርግማን አለብህ፡፡»

وَإِنَّ عَلَيۡكَ ٱللَّعۡنَةَ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلدِّينِ ﴿٣٥﴾

36. «ጌታዬ ሆይ! እንግዲውያስ (ሰዎች) እስከሚቀሰቀሱበት ቀን ድረስ አቆየኝ» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ فَأَنظِرۡنِيٓ إِلَىٰ يَوۡمِ يُبۡعَثُونَ ﴿٣٦﴾

37. (አላህም) አለ «አንተ ከሚቆዩት ነህ፡፡

قَالَ فَإِنَّكَ مِنَ ٱلۡمُنظَرِينَ ﴿٣٧﴾

38. «እስከታወቀው ወቅት ቀን ድረስ፡፡»

إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡوَقۡتِ ٱلۡمَعۡلُومِ ﴿٣٨﴾

39. (ኢብሊስ) አለ «ጌታዬ ሆይ! እኔን በማጥመምህ ይኹንብኝ ለነርሱ በምድር ላይ (ኀጢአትን) እሸልምላቸዋለሁ፡፡ ሁሉንም አጠማቸዋለሁም፡፡»

قَالَ رَبِّ بِمَآ أَغۡوَيۡتَنِي لَأُزَيِّنَنَّ لَهُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَأُغۡوِيَنَّهُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٣٩﴾

40. «ከነርሱ ፍጹሞቹ ባሮችህ ብቻ ሲቀሩ፡፡»

إِلَّا عِبَادَكَ مِنۡهُمُ ٱلۡمُخۡلَصِينَ ﴿٤٠﴾

41. (አላህም) አለ «ይህ በእኔ ላይ (መጠበቁ የተገባ) ቀጥተኛ መንገድ ነው፡፡»

قَالَ هَٰذَا صِرَٰطٌ عَلَيَّ مُسۡتَقِيمٌ ﴿٤١﴾

42. «እነሆ ባሮቼ በእነሱ ላይ ላንተ ስልጣን የለህም፡፡ ከጠማሞቹ የተከተለህ ሰው ብቻ ሲቀር፡፡»

إِنَّ عِبَادِي لَيۡسَ لَكَ عَلَيۡهِمۡ سُلۡطَٰنٌ إِلَّا مَنِ ٱتَّبَعَكَ مِنَ ٱلۡغَاوِينَ ﴿٤٢﴾

43. «ገሀነምም (ለርሱና ለተከተሉት) ለመላውም በእርግጥ ቀጠሯቸው ናት፡፡

وَإِنَّ جَهَنَّمَ لَمَوۡعِدُهُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٤٣﴾

44. «ለእርሷ ሰባት ደጃፎች አሏት፡፡ ለየደጃፉም ሁሉ ከእነሱ የተከፈለ ፋንታ አለ፡፡

لَهَا سَبۡعَةُ أَبۡوَٰبٖ لِّكُلِّ بَابٖ مِّنۡهُمۡ جُزۡءٞ مَّقۡسُومٌ ﴿٤٤﴾

45. «እነዚያ (ከኀጢአት) የተጠነቀቁት በአትክልቶችና በምንጮች ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُتَّقِينَ فِي جَنَّٰتٖ وَعُيُونٍ ﴿٤٥﴾

46. «ጸጥተኞች ኾናችሁ በሰላም ግቧት (ይባላሉ)፡፡

ٱدۡخُلُوهَا بِسَلَٰمٍ ءَامِنِينَ ﴿٤٦﴾

47. «ባልጋዎችም ላይ ፊት ለፊት የሚቅጣጩ ወንድማማቾች ኾነው በደረቶቻቸው ውስጥ ከቂም ያለውን ሁሉ እናስወግዳለን፡፡

وَنَزَعۡنَا مَا فِي صُدُورِهِم مِّنۡ غِلٍّ إِخۡوَٰنًا عَلَىٰ سُرُرٖ مُّتَقَٰبِلِينَ ﴿٤٧﴾

48. «በእርሷም ውስጥ ድካም አይነካቸውም፡፡ እነሱም ከእርሷ የሚወጡ አይደሉም፡፡»

لَا يَمَسُّهُمۡ فِيهَا نَصَبٞ وَمَا هُم مِّنۡهَا بِمُخۡرَجِينَ ﴿٤٨﴾

49. ባሮቼን እኔ መሐሪው አዛኙ እኔው ብቻ መኾኔን ንገራቸው፡፡

۞نَبِّئۡ عِبَادِيٓ أَنِّيٓ أَنَا ٱلۡغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٤٩﴾

50. ቅጣቴም እርሱ አሳማሚ ቅጣት መኾኑን (ንገራቸው)፡፡

وَأَنَّ عَذَابِي هُوَ ٱلۡعَذَابُ ٱلۡأَلِيمُ ﴿٥٠﴾

51. ከኢብራሂም እንግዶችም (ወሬ) ንገራቸው፡፡

وَنَبِّئۡهُمۡ عَن ضَيۡفِ إِبۡرَٰهِيمَ ﴿٥١﴾

52. በእርሱ ላይ በገቡና ሰላም ባሉት ጊዜ የኾነውን (አስታውስ)፡፡ (እርሱም) «እኛ ከእናንተ ፈሪዎች ነን» አላቸው፡፡

إِذۡ دَخَلُواْ عَلَيۡهِ فَقَالُواْ سَلَٰمٗا قَالَ إِنَّا مِنكُمۡ وَجِلُونَ ﴿٥٢﴾

53. «አትፍራ፤ እኛ ዐዋቂ በኾነ ወንድ ልጅ እናበስርሃለን» አሉት፡፡

قَالُواْ لَا تَوۡجَلۡ إِنَّا نُبَشِّرُكَ بِغُلَٰمٍ عَلِيمٖ ﴿٥٣﴾

54. «እርጅና የደረሰብኝ ከመኾኔ ጋር አበሰራችሁኝን በምን ታበስሩኛላችሁ» አለ፡፡

قَالَ أَبَشَّرۡتُمُونِي عَلَىٰٓ أَن مَّسَّنِيَ ٱلۡكِبَرُ فَبِمَ تُبَشِّرُونَ ﴿٥٤﴾

55. «በእውነት አበሰርንህ፡፡ ከተሰፋ ቆራጮችም አትኹን» አሉ፡፡
56. «ከጠማማዎችም በስተቀር ከጌታው እዝነት ተስፋን የሚቆርጥ ማነው» አለ፡፡
57. «እናንተ መልክተኞች ሆይ! ኧረ ለመኾኑ ነገራችሁ ምንድን ነው» አለ፡፡
58. «እኛ አመጸኞች ወደ ኾኑ ሕዝቦች ተልከናል» አሉት፡፡
59. «የሉጥ ቤተሰቦች ብቻ ሲቀሩ፡፡ (እነርሱን) እኛ ሁላቸውንም በእርግጥ የምናድናቸው ነን፡፡
60. «ሚስቱ ብቻ ስትቀር፡፡ እርሷን (በቅጣቱ ውስጥ) ከሚቀሩት መኾኗን ወሰነናል» (አሉ)፡፡
61. መልክተኞቹም የሉጥን ቤተሰቦች በመጡባቸው ጊዜ፤
62. (ሉጥ) «እናንተ የተሳታችሁ ሕዝቦች ናችሁ» አላቸው፡፡
63. «አይደለም እኛ ሕዝቦችህ በርሱ ይጠራጠሩበት በነበሩት ቅጣት መጣንህ» አሉት፡፡
64. «እውነትንም ይዘን መጣንህ፡፡ እኛም በእርግጥ እውነተኞች ነን፡፡
65. ከቤተሰብህም ጋር በሌሊቱ ከፊል ኺድ፡፡ ከኋላቸውም ተከተል፡፡ ከእናንተም አንድም ሰው ወደ ኋላው አይገላመጥ፡፡ ወደ ታዘዛችሁበትም ስፍራ እለፉ» (አሉት)፡፡
66. ወደርሱም ያንን ትእዛዝ አወረድን፡፡ (እርሱም) የእነዚህ (ሕዝቦች) መጨረሻ ያነጉ ሲኾኑ (ሥራቸው) መቆረጥ ነው፡፡

67. የከተማይቱም ሰዎች የሚበሳሰሩ ኾነው መጡ፡፡

68. (ሉጥም) አለ «እነዚህ እንግዶቼ ናቸውና አታጋልጡኝ፡፡
69. «አላህንም ፍሩ፤ አታሳፍሩኝም፡፡»

70. «ከዓለማት (ማንንም እንዳታስተናግድ) አልከለከልንህምን» አሉት፡፡
71. (ሉጥም) «እነኘህ ሴቶች ልጆቼ ናቸው፡፡ ሠሪዎች ብትኾኑ (አግቧቸው)» አለ፡፡
72. በዕድሜህ እንምላለን እነሱ በእርግጥ በስከራቸው ውስጥ ይዋልላሉ፡፡
73. ጩኸቲቱም ፀሐይ የወጣችባቸው ሲኾኑ ያዘቻቸው፡፡

قَالُواْ بَشَّرۡنَٰكَ بِٱلۡحَقِّ فَلَا تَكُن مِّنَ ٱلۡقَٰنِطِينَ ٥٥

قَالَ وَمَن يَقۡنَطُ مِن رَّحۡمَةِ رَبِّهِۦٓ إِلَّا ٱلضَّآلُّونَ ٥٦

قَالَ فَمَا خَطۡبُكُمۡ أَيُّهَا ٱلۡمُرۡسَلُونَ ٥٧

قَالُوٓاْ إِنَّآ أُرۡسِلۡنَآ إِلَىٰ قَوۡمٖ مُّجۡرِمِينَ ٥٨

إِلَّآ ءَالَ لُوطٍ إِنَّا لَمُنَجُّوهُمۡ أَجۡمَعِينَ ٥٩

إِلَّا ٱمۡرَأَتَهُۥ قَدَّرۡنَآ إِنَّهَا لَمِنَ ٱلۡغَٰبِرِينَ ٦٠

فَلَمَّا جَآءَ ءَالَ لُوطٍ ٱلۡمُرۡسَلُونَ ٦١

قَالَ إِنَّكُمۡ قَوۡمٞ مُّنكَرُونَ ٦٢

قَالُواْ بَلۡ جِئۡنَٰكَ بِمَا كَانُواْ فِيهِ يَمۡتَرُونَ ٦٣

وَأَتَيۡنَٰكَ بِٱلۡحَقِّ وَإِنَّا لَصَٰدِقُونَ ٦٤

فَأَسۡرِ بِأَهۡلِكَ بِقِطۡعٖ مِّنَ ٱلَّيۡلِ وَٱتَّبِعۡ أَدۡبَٰرَهُمۡ وَلَا يَلۡتَفِتۡ مِنكُمۡ أَحَدٞ وَٱمۡضُواْ حَيۡثُ تُؤۡمَرُونَ ٦٥

وَقَضَيۡنَآ إِلَيۡهِ ذَٰلِكَ ٱلۡأَمۡرَ أَنَّ دَابِرَ هَٰٓؤُلَآءِ مَقۡطُوعٞ مُّصۡبِحِينَ ٦٦

وَجَآءَ أَهۡلُ ٱلۡمَدِينَةِ يَسۡتَبۡشِرُونَ ٦٧

قَالَ إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ ضَيۡفِي فَلَا تَفۡضَحُونِ ٦٨

وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَلَا تُخۡزُونِ ٦٩

قَالُوٓاْ أَوَلَمۡ نَنۡهَكَ عَنِ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٧٠

قَالَ هَٰٓؤُلَآءِ بَنَاتِيٓ إِن كُنتُمۡ فَٰعِلِينَ ٧١

لَعَمۡرُكَ إِنَّهُمۡ لَفِي سَكۡرَتِهِمۡ يَعۡمَهُونَ ٧٢

فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلصَّيۡحَةُ مُشۡرِقِينَ ٧٣

74. ላይዋንም ከታችዋ አደረግን፡፡ በእነሱም ላይ የሸክላ ደንጊያዎችን አዘነብንባቸው፡፡

فَجَعَلۡنَا عَٰلِيَهَا سَافِلَهَا وَأَمۡطَرۡنَا عَلَيۡهِمۡ حِجَارَةٗ مِّن سِجِّيلٍ ﴿٧٤﴾

75. በዚህ ውስጥ ለተመልካቾች በእርግጥ መገምገሚያዎች አሉበት፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّلۡمُتَوَسِّمِينَ ﴿٧٥﴾

76. እሷም (ከተማይቱ) በቀጥታ መንገድ ላይ ናት፡፡

وَإِنَّهَا لَبِسَبِيلٖ مُّقِيمٍ ﴿٧٦﴾

77. በዚህ ውስጥ በእርግጥ ለምእምናን መገሰጫ አለ፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٧٧﴾

78. እነሆ የአይከት ሰዎችም በእርግጥ በዳዮች ነበሩ፤

وَإِن كَانَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡأَيۡكَةِ لَظَٰلِمِينَ ﴿٧٨﴾

79. ከነሱም ተበቀልን ሁለቱም (የሉጥና የአይከት ሕዝቦች ከተሞች) በእርግጥ በግልጽ መንገድ ላይ ናቸው፡፡

فَٱنتَقَمۡنَا مِنۡهُمۡ وَإِنَّهُمَا لَبِإِمَامٖ مُّبِينٖ ﴿٧٩﴾

80. የሒጅርም ሰዎች መልክተኞቹን በእርግጥ አስተባበሉ፡፡

وَلَقَدۡ كَذَّبَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡحِجۡرِ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ﴿٨٠﴾

81. ተዓምራታችንንም ሰጠናቸው፡፡ ከእርሷም ዘንጊዎች ነበሩ፡፡

وَءَاتَيۡنَٰهُمۡ ءَايَٰتِنَا فَكَانُواْ عَنۡهَا مُعۡرِضِينَ ﴿٨١﴾

82. ከኮረብታዎችም ቤቶችን ጸጥተኞች ኾነው ይጠርቡ ነበር፡፡

وَكَانُواْ يَنۡحِتُونَ مِنَ ٱلۡجِبَالِ بُيُوتًا ءَامِنِينَ ﴿٨٢﴾

83. ያነጉም ሲኾኑ ጩኸት ያዘቻቸው፤ (ወደሙ)፡፡

فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلصَّيۡحَةُ مُصۡبِحِينَ ﴿٨٣﴾

84. ይሠሩትም የነበሩት ሕንጻ ምንም አልጠቀማቸውም፡፡

فَمَآ أَغۡنَىٰ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ﴿٨٤﴾

85. ሰማያትንና ምድርንም በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ በእውነት እንጂ (በላግጣ) አልፈጠርንም፡፡ ሰዓቲቱም በእርግጥ መጪ ናት፡፡ መልካምንም ይቅርታ አድርግላቸው፡፡

وَمَا خَلَقۡنَا ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَآ إِلَّا بِٱلۡحَقِّۗ وَإِنَّ ٱلسَّاعَةَ لَأٓتِيَةٞۖ فَٱصۡفَحِ ٱلصَّفۡحَ ٱلۡجَمِيلَ ﴿٨٥﴾

86. ጌታህ እርሱ (ያልነበረን) ፈጣሪው ዐዋቂው ነው፡፡

إِنَّ رَبَّكَ هُوَ ٱلۡخَلَّٰقُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿٨٦﴾

87. ከሚደጋገሙ የኾኑን ሰባትንና ታላቁንም ቁርኣን (በሙሉ) በእርግጥ ሰጠንህ፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَٰكَ سَبۡعٗا مِّنَ ٱلۡمَثَانِي وَٱلۡقُرۡءَانَ ٱلۡعَظِيمَ ﴿٨٧﴾

88. ከእነርሱ (ከከሓዲዎች) ብዙዎችን ወገኖች በእርሱ ወደ አጣቀምንበት ጸጋ ዓይኖችህን አትዘርጋ፡፡ በእነሱም ላይ (ባያምኑ) አትዘን፡፡ ክንፍህንም ለምእምናን አለዝብ፡፡

لَا تَمُدَّنَّ عَيۡنَيۡكَ إِلَىٰ مَا مَتَّعۡنَا بِهِۦٓ أَزۡوَٰجٗا مِّنۡهُمۡ وَلَا تَحۡزَنۡ عَلَيۡهِمۡ وَٱخۡفِضۡ جَنَاحَكَ لِلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٨٨﴾

89. በልም «እኔ ግልጽ አስፈራሪው እኔ ነኝ፡፡»

وَقُلۡ إِنِّيٓ أَنَا ٱلنَّذِيرُ ٱلۡمُبِينُ ﴿٨٩﴾

90. (ሰዎችን ለማገድ የመካን በሮች) በተከፋፈሉት ላይ እንደ አወረድነው (በኾነ ቅጣት አስፈራሪያችሁ ነኝ በል)፡፡

كَمَآ أَنزَلۡنَا عَلَى ٱلۡمُقۡتَسِمِينَ ﴿٩٠﴾

91. (እነርሱም) እነዚያ ቁርኣንንን ክፍልፍሎች ያደረጉ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ جَعَلُواْ ٱلۡقُرۡءَانَ عِضِينَ ﴿٩١﴾

92. በጌታህም እንምላለን፡፡ ሁላቸውንም እንጠይቃቸዋለን፤

فَوَرَبِّكَ لَنَسۡـَٔلَنَّهُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٩٢﴾

93. ይሠሩት ከነበሩት ነገር ሁሉ፡፡

عَمَّا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ﴿٩٣﴾

94. የታዘዝከበትንም ነገር በይፋ ግለጽ፡፡ አጋሪዎችንም ተዋቸው፡፡

فَٱصۡدَعۡ بِمَا تُؤۡمَرُ وَأَعۡرِضۡ عَنِ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ﴿٩٤﴾

95. ተሳላቂዎችን ሁሉ እኛ በቅተንሃል፡፡

إِنَّا كَفَيۡنَٰكَ ٱلۡمُسۡتَهۡزِءِينَ ﴿٩٥﴾

96. (እነሱም) እነዚያ ከአላህ ጋር ሌላ አምላክን ያደረጉ ናቸው፡፡ በእርግጥም (ፍጻሜያቸውን) ወደፊት ያውቃሉ፡፡

ٱلَّذِينَ يَجۡعَلُونَ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَۚ فَسَوۡفَ يَعۡلَمُونَ ﴿٩٦﴾

97. አንተም በሚሉት ነገር ልብህ የሚጠብ መኾኑን በእርግጥ እናውቃለን፡፡

وَلَقَدۡ نَعۡلَمُ أَنَّكَ يَضِيقُ صَدۡرُكَ بِمَا يَقُولُونَ ﴿٩٧﴾

98. ጌታህንም ከማመስገን ጋር አጥራው ከሰጋጆቹም ኹን፡፡

فَسَبِّحۡ بِحَمۡدِ رَبِّكَ وَكُن مِّنَ ٱلسَّٰجِدِينَ ﴿٩٨﴾

99. እውነቱም (ሞት) እስኪመጣህ ድረስ ጌታህን ተገዛ፡፡

وَٱعۡبُدۡ رَبَّكَ حَتَّىٰ يَأۡتِيَكَ ٱلۡيَقِينُ ﴿٩٩﴾

## ሱረቱ አል ነሕል

## سورة النحل

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. የአላህ ትዕዛዝ መጣ፤ ስለዚህ አታስቸኩሉት፤ ከማይገባው ሁሉ ጠራ ከሚያጋሩትም ሁሉ ላቀ፤

أَتَىٰٓ أَمۡرُ ٱللَّهِ فَلَا تَسۡتَعۡجِلُوهُۚ سُبۡحَٰنَهُۥ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ﴿١﴾

2. ከባሮቹ በሚሻው ሰው ላይ መላእክትን ከራእይ ጋር በፈቃዱ ያወርዳል (ከሓዲዎችን በቅጣት) አስጠንቅቁ፤ እነሆ ከኔ በቀር ሌላ አምላክ የለም፤ ፍሩኝም ማለትን (አስታውቁ በማለት ያወርዳል)፡፡

يُنَزِّلُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ بِٱلرُّوحِ مِنۡ أَمۡرِهِۦ عَلَىٰ مَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦٓ أَنۡ أَنذِرُوٓاْ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّآ أَنَا۠ فَٱتَّقُونِ ﴿٢﴾

3. ሰማያትንና ምድርን በእውነት ፈጠረ ከሚያጋሩት ሁሉ ጠራ፡፡

خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ بِٱلۡحَقِّۚ تَعَٰلَىٰ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ﴿٣﴾

4. ሰውን ከፍትወት ጠብታ ፈጠረው፡፡ ከዚያም እርሱ ወዲያውኑ (ትንሣኤን በመካድ) ግልጽ ተከራካሪ ይኾናል፡፡

5. ግመልን፣ ከብትን፣ ፍየልንም በርሷ (ብርድ መከላከያ) ሙቀት ጥቅሞችም ያሉባት ስትኾን ለእናንተ ፈጠረላችሁ፡፡ ከርሷም ትበላላችሁ፡፡

6. ለእናንተም በእርሷ ወደ ማረፊያዋ በምትመልሷት ጊዜ በምታሰማሩዋትም ጊዜ ውበት አላችሁ፡፡

7. ጓዞቻችሁንም በነፍሶች ችግር እንጂ ወደማትደርሱበት አገር ትሸከማለች፡፡ ጌታችሁ በእርግጥ ሩኅሩኅ አዛኝ ነውና፡፡

8. ፈረሶችንም፣ በቅሎዎችንም፣ አህዮችንም ልትቀመጡዋቸውና ልታጌጡባቸው (ፈጠረላችሁ)፡፡ የማታውቁትንም ድንቅ ነገር ይፈጥራል፡፡

9. በአላህም ላይ (በችሮታው) ቀጥተኛውን መንገድ መግለጽ አለበት፡፡ ከእርሷም (ከመንገድ) ጠማማ አልለ፡፡ በሻም ኖሮ ሁላችሁንም በእርግጥ ባቀናችሁ ነበር፡፡

10. እርሱ ያ ከሰማይ ውሃን ያወረደ ነው፡፡ ከእርሱ ለእናንተ መጠጥ አላችሁ፡፡ ከእርሱም (እንስሳዎችን) በእርሱ የምታሰማሩበት ዛፍ (ይበቅልበታል)፡፡

11. በእርሱ ለእናንተ አዝመራን፣ (የዘይት) ወይራንም፣ ዘምባባዎችንም (ተምርን)፣ ወይኖችንም፣ ከፍሬዎችም ሁሉ ያበቅልላችኋል፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያስተነትኑ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምርአልለ፡፡

12. ለእናንተም ሌሊትንና ቀንን፣ ፀሐይንና ጨረቃንም ገራላችሁ፡፡ ከዋክብትም በፈቃዱ የተገሩ ናቸው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያውቁ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምራቶች አልሉ፡፡

13. በምድርም ላይ መልኮቹ የተለያዩ ኾኖ ለእናንተ የፈጠረላችሁን ሁሉ (ገራላችሁ)፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚገሰጹ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምር አልለ፡፡

14. እርሱም ያ ባሕርን ከእርሱ እርጥብ ስጋን ልትበሉና ከእርሱም የምትለብሱትን ጌጣጌጥ ታወጡ ዘንድ የገራ ነው፡፡ መርከቦችንም በውስጡ (ውሃውን) ቀዳጆች ኾነው (ሲንሻለሉ) ታያለህ፡፡ ከችሮታው ልትፈልጉና ልታመሰግኑም (ገራላችሁ)፡፡

خَلَقَ ٱلۡإِنسَٰنَ مِن نُّطۡفَةٖ فَإِذَا هُوَ خَصِيمٞ مُّبِينٞ ﴿٤﴾

وَٱلۡأَنۡعَٰمَ خَلَقَهَاۖ لَكُمۡ فِيهَا دِفۡءٞ وَمَنَٰفِعُ وَمِنۡهَا تَأۡكُلُونَ ﴿٥﴾

وَلَكُمۡ فِيهَا جَمَالٌ حِينَ تُرِيحُونَ وَحِينَ تَسۡرَحُونَ ﴿٦﴾

وَتَحۡمِلُ أَثۡقَالَكُمۡ إِلَىٰ بَلَدٖ لَّمۡ تَكُونُواْ بَٰلِغِيهِ إِلَّا بِشِقِّ ٱلۡأَنفُسِۚ إِنَّ رَبَّكُمۡ لَرَءُوفٞ رَّحِيمٞ ﴿٧﴾

وَٱلۡخَيۡلَ وَٱلۡبِغَالَ وَٱلۡحَمِيرَ لِتَرۡكَبُوهَا وَزِينَةٗۚ وَيَخۡلُقُ مَا لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٨﴾

وَعَلَى ٱللَّهِ قَصۡدُ ٱلسَّبِيلِ وَمِنۡهَا جَآئِرٞۚ وَلَوۡ شَآءَ لَهَدَىٰكُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٩﴾

هُوَ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗۖ لَّكُم مِّنۡهُ شَرَابٞ وَمِنۡهُ شَجَرٞ فِيهِ تُسِيمُونَ ﴿١٠﴾

يُنۢبِتُ لَكُم بِهِ ٱلزَّرۡعَ وَٱلزَّيۡتُونَ وَٱلنَّخِيلَ وَٱلۡأَعۡنَٰبَ وَمِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّقَوۡمٖ يَتَفَكَّرُونَ ﴿١١﴾

وَسَخَّرَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ وَٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَۖ وَٱلنُّجُومُ مُسَخَّرَٰتُۢ بِأَمۡرِهِۦٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ﴿١٢﴾

وَمَا ذَرَأَ لَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُخۡتَلِفًا أَلۡوَٰنُهُۥٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّقَوۡمٖ يَذَّكَّرُونَ ﴿١٣﴾

وَهُوَ ٱلَّذِي سَخَّرَ ٱلۡبَحۡرَ لِتَأۡكُلُواْ مِنۡهُ لَحۡمٗا طَرِيّٗا وَتَسۡتَخۡرِجُواْ مِنۡهُ حِلۡيَةٗ تَلۡبَسُونَهَاۖ وَتَرَى ٱلۡفُلۡكَ مَوَاخِرَ فِيهِ وَلِتَبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِهِۦ وَلَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ﴿١٤﴾

15. በምድርም ውስጥ በእናንተ እንዳታረገርግ ተራራዎችን ጣለባት፡፡ ጂረቶችንም፣ መንገዶችንም ትመሩ ዘንድ (አደረገ)፡፡

وَأَلْقَىٰ فِي ٱلْأَرْضِ رَوَٰسِيَ أَن تَمِيدَ بِكُمْ وَأَنْهَٰرًا وَسُبُلًا لَّعَلَّكُمْ تَهْتَدُونَ ﴿١٥﴾

16. ምልክቶችንም (አደረገ)፡፡ በከዋክብትም እነሱ ይምመራሉ፡፡

وَعَلَٰمَٰتٍۚ وَبِٱلنَّجْمِ هُمْ يَهْتَدُونَ ﴿١٦﴾

17. የሚፈጥር እንደማይፈጥር ነውን አትገሰጹምን

أَفَمَن يَخْلُقُ كَمَن لَّا يَخْلُقُۚ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ﴿١٧﴾

18. የአላህንም ጸጋ ብትቆጥሩ አትዘልቋትም፡፡ አላህ በእርግጥ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

وَإِن تَعُدُّواْ نِعْمَةَ ٱللَّهِ لَا تُحْصُوهَآۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَغَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١٨﴾

19. አላህም የምትደብቁትንና የምትገልጹትን ሁሉ ያውቃል፡፡

وَٱللَّهُ يَعْلَمُ مَا تُسِرُّونَ وَمَا تُعْلِنُونَ ﴿١٩﴾

20. እነዚያም ከአላህ ሌላ የምትገዟቸው ምንንም አይፈጥሩም፡፡ እነርሱም ይፈጠራሉ፤

وَٱلَّذِينَ يَدْعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ لَا يَخْلُقُونَ شَيْـًٔا وَهُمْ يُخْلَقُونَ ﴿٢٠﴾

21. ሕያው ያልኾኑ ሙታን ናቸው፡፡ መቼ እንደሚቀሰቀሱም አያውቁም፡፡

أَمْوَٰتٌ غَيْرُ أَحْيَآءٍۖ وَمَا يَشْعُرُونَ أَيَّانَ يُبْعَثُونَ ﴿٢١﴾

22. አምላካችሁ አንድ አምላክ ብቻ ነው፡፡ እነዚያም በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት ልቦቻቸው ከሓዲዎች ናቸው፡፡ እነሱም የኮሩ ናቸው፤ (አያምኑም)፡፡

إِلَٰهُكُمْ إِلَٰهٌ وَٰحِدٌۚ فَٱلَّذِينَ لَا يُؤْمِنُونَ بِٱلْأٓخِرَةِ قُلُوبُهُم مُّنكِرَةٌ وَهُم مُّسْتَكْبِرُونَ ﴿٢٢﴾

23. አላህ የሚደብቁትንና የሚገልጹትን ሁሉ የሚያውቅ ለመኾኑ ጥርጣሬ የለበትም፡፡ እርሱ ኩሩዎችን አይወድም፡፡

لَا جَرَمَ أَنَّ ٱللَّهَ يَعْلَمُ مَا يُسِرُّونَ وَمَا يُعْلِنُونَۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلْمُسْتَكْبِرِينَ ﴿٢٣﴾

24. ለእነርሱም «ጌታችሁ (በሙሐመድ ላይ) ምንን አወረደ» በተባሉ ጊዜ «(እርሱ) የመጀመሪያዎቹ ሕዝቦች ተረቶች ነው» ይላሉ፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُم مَّاذَآ أَنزَلَ رَبُّكُمْ قَالُوٓاْ أَسَٰطِيرُ ٱلْأَوَّلِينَ ﴿٢٤﴾

25. (ይህንንም የሚሉት) በትንሣኤ ቀን ኀጢአቶቻቸውን በሙሉ ከእነዚያም ያለ ዕውቀት ኾነው ከሚያጠሟቸው ሰዎች ኀጢአቶች ከፊሉን ሊሸከሙ ነው፡፡ ንቁ! የሚሸከሙት ኃጢአት ምንኛ ከፋ!

لِيَحْمِلُوٓاْ أَوْزَارَهُمْ كَامِلَةً يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ وَمِنْ أَوْزَارِ ٱلَّذِينَ يُضِلُّونَهُم بِغَيْرِ عِلْمٍۗ أَلَا سَآءَ مَا يَزِرُونَ ﴿٢٥﴾

26. እነዚያ ከእነሱ (ከቁረይሾች) በፊት የነበሩት በእርግጥ መከሩ፡፡ አላህም ሕንጻዎቻቸውን ከመሠረቶቻቸው አፈረሰ፡፡ ጣሪያውም በእነሱ ላይ ከበላያቸው ወደቀባቸው፡፡ ቅጣቱም ከማያውቁት ሥፍራ መጣባቸው፡፡

قَدْ مَكَرَ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ فَأَتَى ٱللَّهُ بُنْيَٰنَهُم مِّنَ ٱلْقَوَاعِدِ فَخَرَّ عَلَيْهِمُ ٱلسَّقْفُ مِن فَوْقِهِمْ وَأَتَىٰهُمُ ٱلْعَذَابُ مِنْ حَيْثُ لَا يَشْعُرُونَ ﴿٢٦﴾

27. ከዚያም በትንሣኤ ቀን ያዋርዳቸዋል፡፡ እነዚያም «በእነሱ (ጉዳይ) ትከራከሩኝ የነበራችሁት ተጋሪዎቼ የት ናቸው» ይላቸዋል፡፡ «እነዚያ ዕውቀትን የተሰጡት ዛሬ ሐፍረቱና ቅጣቱ በእርግጥ በከሓዲዎች ላይ ነው» ይላሉ፡፡

ثُمَّ يَوْمَ ٱلْقِيَـٰمَةِ يُخْزِيهِمْ وَيَقُولُ أَيْنَ شُرَكَآءِىَ ٱلَّذِينَ كُنتُمْ تُشَـٰٓقُّونَ فِيهِمْ ۚ قَالَ ٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ ٱلْعِلْمَ إِنَّ ٱلْخِزْىَ ٱلْيَوْمَ وَٱلسُّوٓءَ عَلَى ٱلْكَـٰفِرِينَ ﴿٢٧﴾

28. (እነርሱ) «እነዚያ ነፍሶቻቸውን በዳይ ኾነው መላእክት የሚገድሏቸው ናቸው፡፡ ከክፉ ሥራ ምንም ነገር የምንሠራም አልነበርን» (ሲሉ) ታዛዥነታቸውን ይገልጻሉ፡፡ «በእውነት አላህ ትሰሩት የነበራችሁትን ነገር ዐዋቂ ነው» (ይባላሉ)፡፡

ٱلَّذِينَ تَتَوَفَّىٰهُمُ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةُ ظَالِمِىٓ أَنفُسِهِمْ ۖ فَأَلْقَوُا۟ ٱلسَّلَمَ مَا كُنَّا نَعْمَلُ مِن سُوٓءٍۭ ۚ بَلَىٰٓ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌۢ بِمَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ﴿٢٨﴾

29. «የገሀነምንም ደጃፎች በውስጧ ዘውታሪዎች ስትኾኑ ግቡ» (ይባላሉ)፡፡ የኩሩዎችም መኖሪያ (ገሀነም) በእርግጥ ከፋች!

فَٱدْخُلُوٓا۟ أَبْوَٰبَ جَهَنَّمَ خَـٰلِدِينَ فِيهَا ۖ فَلَبِئْسَ مَثْوَى ٱلْمُتَكَبِّرِينَ ﴿٢٩﴾

30. ለእነዚያም ለተጠነቀቁት «ጌታችሁ ምንን ነገር አወረደ» ተባሉ፡፡ «መልካምን ነገር» አሉ፡፡ ለእነዚያ ደግ ለሠሩት በዚህች በቅርቢቱ ዓለም መልካም ኑሮ አላቸው፡፡ የመጨረሻይቱም አገር በእርግጥ በላጭ ናት፡፡ የጥንቁቆቹም አገር ምን ታምር!

۞ وَقِيلَ لِلَّذِينَ ٱتَّقَوْا۟ مَاذَآ أَنزَلَ رَبُّكُمْ ۚ قَالُوا۟ خَيْرًا ۗ لِّلَّذِينَ أَحْسَنُوا۟ فِى هَـٰذِهِ ٱلدُّنْيَا حَسَنَةٌ ۚ وَلَدَارُ ٱلْـَٔاخِرَةِ خَيْرٌ ۚ وَلَنِعْمَ دَارُ ٱلْمُتَّقِينَ ﴿٣٠﴾

31. (እርሷም) የሚገቡዋትና በሥርዋ ወንዞች የሚፈሱባት ስትኾን የመኖሪያ አትክልቶች ናት፡፡ ለእነሱም በወስጧ የሚሹት ሁሉ አላቸው፡፡ እንደዚሁ አላህ ጥንቁቆችን ይመነዳል፡፡

جَنَّـٰتُ عَدْنٍ يَدْخُلُونَهَا تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَـٰرُ ۖ لَهُمْ فِيهَا مَا يَشَآءُونَ ۚ كَذَٰلِكَ يَجْزِى ٱللَّهُ ٱلْمُتَّقِينَ ﴿٣١﴾

32. እነዚያ በመልካም ኹኔታ ላይ ኾነው መላእክት «ሰላም በእናንተ ላይ» እያሉ የሚገድሏቸው ናቸው፡፡ «ትሠሩት በነበራችሁት ሥራ ገነትን ግቡ» (ይባላሉ)፡፡

ٱلَّذِينَ تَتَوَفَّىٰهُمُ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةُ طَيِّبِينَ ۙ يَقُولُونَ سَلَـٰمٌ عَلَيْكُمُ ٱدْخُلُوا۟ ٱلْجَنَّةَ بِمَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ﴿٣٢﴾

33. (ከሓዲዎች) መላእክት ወደ እነሱ መምጣትን ወይም የጌታህ ትእዛዝ መምጣቱን እንጂ አይጠባበቁም፡፡ ከእነሱ በፊት የነበሩት እንደዚሁ ሠርተዋል፡፡ አላህም አልበደላቸውም፤ ግን ነፍሶቻቸውን የሚበድሉ ነበሩ፡፡

هَلْ يَنظُرُونَ إِلَّآ أَن تَأْتِيَهُمُ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةُ أَوْ يَأْتِىَ أَمْرُ رَبِّكَ ۚ كَذَٰلِكَ فَعَلَ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ ۚ وَمَا ظَلَمَهُمُ ٱللَّهُ وَلَـٰكِن كَانُوٓا۟ أَنفُسَهُمْ يَظْلِمُونَ ﴿٣٣﴾

34. የሠሩዋቸውም ኀጢአቶች (ቅጣት) አገኛቸው፡፡ በእርሱም ይሳለቁበት የነበሩት ሁሉ በነሱ ላይ ወረደባቸው፡፡

فَأَصَابَهُمْ سَيِّـَٔاتُ مَا عَمِلُوا۟ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُوا۟ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ﴿٣٤﴾

35. እነዚያም (ጣዖታትን) ያጋሩት «አላህ በሻ ኖሮ ከእርሱ ሌላ እኛም አባቶቻችንም ምንንም ባልተገዛን ነበር፤ ያለእርሱም (ትእዛዝ) ምንንም እርም ባላደረግን ነበር አሉ፡፡» እነዚያም ከነሱ በፊት የነበሩት እነደዚሁ ሠሩ፡፡ በመልክተኞቹም ላይ ግልፅ ማድረስ ብቻ እንጂ ሌላ የለባቸውም፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ أَشۡرَكُواْ لَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ مَا عَبَدۡنَا مِن دُونِهِۦ مِن شَيۡءٖ نَّحۡنُ وَلَآ ءَابَآؤُنَا وَلَا حَرَّمۡنَا مِن دُونِهِۦ مِن شَيۡءٖۚ كَذَٰلِكَ فَعَلَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ فَهَلۡ عَلَى ٱلرُّسُلِ إِلَّا ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ٣٥

36. በየሕዝቡም ሁሉ ውስጥ «አላህን ተገዙ፤ ጣዖትንም ራቁ» በማለት መልክተኛን በእርግጥ ልከናል፡፡ ከእነሱም ውስጥ አላህ ያቀናው ሰው አልለ፡፡ ከእነሱም ውስጥ በእርሱ ላይ ጥመት የተረጋገጠበት ሰው አልለ፡፡ በምድርም ላይ ኺዱ፤ የአስተባባዮችም መጨረሻ እንዴት እንደ ነበረ ተመልከቱ፡፡

وَلَقَدۡ بَعَثۡنَا فِي كُلِّ أُمَّةٖ رَّسُولًا أَنِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ وَٱجۡتَنِبُواْ ٱلطَّٰغُوتَۖ فَمِنۡهُم مَّنۡ هَدَى ٱللَّهُ وَمِنۡهُم مَّنۡ حَقَّتۡ عَلَيۡهِ ٱلضَّلَٰلَةُۚ فَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَٱنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُكَذِّبِينَ ٣٦

37. በመቅናታቸው ላይ ብትጓጓ (ምንም ልታደርግ አትችልም)፡፡ አላህ የሚጠመውን ሰው አያቀናውምና፡፡ ለእነሱም ከረዳቶች ምንም የላቸውም፡፡

إِن تَحۡرِصۡ عَلَىٰ هُدَىٰهُمۡ فَإِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي مَن يُضِلُّۖ وَمَا لَهُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٣٧

38. መሓሎቻቸውምን አላህ የሚሞትን ሰው አያስነሳም ሲሉ በአላህ ስም ማሉ፡፡ ሐሰት ነው (ያስነሳቸዋል)፡፡ በእርሱ ላይ ቃል ኪዳን ገብቷል፡፡ አረጋግጧል፤ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

وَأَقۡسَمُواْ بِٱللَّهِ جَهۡدَ أَيۡمَٰنِهِمۡ لَا يَبۡعَثُ ٱللَّهُ مَن يَمُوتُۚ بَلَىٰ وَعۡدًا عَلَيۡهِ حَقّٗا وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٣٨

39. (የሚቀሰቅሳቸውም) ለእነሱ ያንን በእርሱ የሚለያዩበትን ሊገልጽላቸው፤ እነዚያ የካዱትም እነሱ ውሸታሞች የነበሩ መኾናቸውን እንዲያውቁ ነው፡፡

لِيُبَيِّنَ لَهُمُ ٱلَّذِي يَخۡتَلِفُونَ فِيهِ وَلِيَعۡلَمَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَنَّهُمۡ كَانُواْ كَٰذِبِينَ ٣٩

40. ለማንኛውም ነገር (መኾኑን) በሻነው ጊዜ ቃላችን ለእርሱ «ኹን» ማለት ብቻ ነው፤ ወዲውም ይኾናል፡፡

إِنَّمَا قَوۡلُنَا لِشَيۡءٍ إِذَآ أَرَدۡنَٰهُ أَن نَّقُولَ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ٤٠

41. እነዚያም ከተበደሉ በኋላ በአላህ (መንገድ ላይ) የተሰደዱት በቅርቢቱ ዓለም መልካሚቱን አገር (መዲናን) በእርግጥ እናሰፍራቸዋለን፡፡ የመጨረሻይቱም ዓለም ምንዳ ታላቅ ነው፡፡ (ከሓዲዎች) ቢያውቁ ኖሮ (በተከተሏቸው ነበር)፡፡

وَٱلَّذِينَ هَاجَرُواْ فِي ٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ مَا ظُلِمُواْ لَنُبَوِّئَنَّهُمۡ فِي ٱلدُّنۡيَا حَسَنَةٗۖ وَلَأَجۡرُ ٱلۡأٓخِرَةِ أَكۡبَرُۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٤١

42. (እነርሱ) እነዚያ የታገሱት በጌታቸውም ላይ የሚጠጉት ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ صَبَرُواْ وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٤٢

43. ከአንተም በፊት ወደእነሱ ወሕይን (ራእይን) የምናወርድላቸውን ሰዎችን እንጂ ሌላን አልላክንም፡፡ የማታውቁም ብትኾኑ የዕውቀትን ባለቤቶች ጠይቁ፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ إِلَّا رِجَالٗا نُّوحِيٓ إِلَيۡهِمۡۖ فَسۡـَٔلُوٓاْ أَهۡلَ ٱلذِّكۡرِ إِن كُنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ٤٣

44. በግልጽ ማስረጃዎችና በመጻሕፍት (ላክናቸው)፡፡ ወደ አንተም ለሰዎች ወደእነሱ የተወረደውን (ፍቾ) ልትገልጽላቸውና ያስተነትኑም ዘንድ ቁርኣንን አወረድን፡፡

بِٱلۡبَيِّنَٰتِ وَٱلزُّبُرِۗ وَأَنزَلۡنَآ إِلَيۡكَ ٱلذِّكۡرَ لِتُبَيِّنَ لِلنَّاسِ مَا نُزِّلَ إِلَيۡهِمۡ وَلَعَلَّهُمۡ يَتَفَكَّرُونَ ٤٤

45. እነዚያ መጥፎዎችን የዶለቱ አላህ በእነሱ ምድርን የሚገለብጥባቸው ወይም ከማያውቁት ስፍራ ቅጣት የሚመጣባቸው መኾኑን አይፈሩምን

أَفَأَمِنَ ٱلَّذِينَ مَكَرُواْ ٱلسَّيِّـَٔاتِ أَن يَخۡسِفَ ٱللَّهُ بِهِمُ ٱلۡأَرۡضَ أَوۡ يَأۡتِيَهُمُ ٱلۡعَذَابُ مِنۡ حَيۡثُ لَا يَشۡعُرُونَ ﴿٤٥﴾

46. ወይም (ካገር ወደ አገር) በሚዘወሩበት ጊዜ የሚይዛቸው መኾኑን (አይፈሩምን) እነሱም አሸናፊዎች አይደሉም፡፡

أَوۡ يَأۡخُذَهُمۡ فِي تَقَلُّبِهِمۡ فَمَا هُم بِمُعۡجِزِينَ ﴿٤٦﴾

47. ወይም ቀስ በቀስ በማጉደል ላይ የሚይዛቸው መኾኑን (አይፈሩምን) ጌታችሁም በእርግጥ ርኅሩኅ አዛኝ ነው፡፡

أَوۡ يَأۡخُذَهُمۡ عَلَىٰ تَخَوُّفٖ فَإِنَّ رَبَّكُمۡ لَرَءُوفٞ رَّحِيمٌ ﴿٤٧﴾

48. ወደዚያ ከማንኛውም ነገር አላህ ወደ ፈጠረው ጥላዎቹ እነርሱ የተዋረዱ ሲኾኑ ለአላህ ሰጋጆች ኾነው ከቀኝና ከግራዎች ወደሚዘወሩት አላዩምን

أَوَ لَمۡ يَرَوۡاْ إِلَىٰ مَا خَلَقَ ٱللَّهُ مِن شَيۡءٖ يَتَفَيَّؤُاْ ظِلَٰلُهُۥ عَنِ ٱلۡيَمِينِ وَٱلشَّمَآئِلِ سُجَّدٗا لِّلَّهِ وَهُمۡ دَٰخِرُونَ ﴿٤٨﴾

49. ለአላህም በሰማያት ያለው ከተንቀሳቃሽም በምድር ያለው ሁሉ፣ መላእክትም ይሰግዳሉ፡፡ እነርሱም አይኮሩም፡፡

وَلِلَّهِ يَسۡجُدُ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ مِن دَآبَّةٖ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ وَهُمۡ لَا يَسۡتَكۡبِرُونَ ﴿٤٩﴾

50. ጌታቸውን ከበላያቸው ሲኾን ይፈሩታል፡፡ የታዘዙትንም ሁሉ ይሠራሉ፡፡

يَخَافُونَ رَبَّهُم مِّن فَوۡقِهِمۡ وَيَفۡعَلُونَ مَا يُؤۡمَرُونَ۩ ﴿٥٠﴾

51. አላህም አለ «ሁለት አማልክትን አትያዙ፡፡ እርሱ አንድ አምላክ ብቻ ነው፡፡ እኔንም ብቻ ፍሩ፡፡»

۞وَقَالَ ٱللَّهُ لَا تَتَّخِذُوٓاْ إِلَٰهَيۡنِ ٱثۡنَيۡنِۖ إِنَّمَا هُوَ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞ فَإِيَّٰيَ فَٱرۡهَبُونِ ﴿٥١﴾

52. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ ነው፡፡ መገዛትም ዘወትር ሲኾን ለርሱ ብቻ ነው፡፡ ከአላህም ሌላ ያለን ትፈራላችሁን

وَلَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَلَهُ ٱلدِّينُ وَاصِبًاۚ أَفَغَيۡرَ ٱللَّهِ تَتَّقُونَ ﴿٥٢﴾

53. ማንኛውም በእናንተ ላይ ያለው ጸጋ ከአላህ ነው፡፡ ከዚያም ችግር በደረሰባችሁ ጊዜ ወደርሱ ብቻ ትጮሃላችሁ፡፡

وَمَا بِكُم مِّن نِّعۡمَةٖ فَمِنَ ٱللَّهِۖ ثُمَّ إِذَا مَسَّكُمُ ٱلضُّرُّ فَإِلَيۡهِ تَجۡـَٔرُونَ ﴿٥٣﴾

54. ከዚያም ከእናንተ ላይ ችግርን ባነሳላችሁ ጊዜ ከእናንተው የኾኑ ጭፍሮች ወዲያውኑ በጌታቸው (ጣዖትን) ያጋራሉ፡፡

ثُمَّ إِذَا كَشَفَ ٱلضُّرَّ عَنكُمۡ إِذَا فَرِيقٞ مِّنكُم بِرَبِّهِمۡ يُشۡرِكُونَ ﴿٥٤﴾

55. (የሚያጋሩትም) በሰጠናቸው ሊክዱ ነው፡፡ ተጠቀሙም ወደ ፊትም (የሚደርስባችሁን) በእርግጥ ታውቃላችሁ፡፡

لِيَكۡفُرُواْ بِمَآ ءَاتَيۡنَٰهُمۡۚ فَتَمَتَّعُواْ فَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ﴿٥٥﴾

56. ለማያውቁትም (ጣዖታት) ከሰጠናቸው ሲሳይ ፈንታን ያደርጋሉ፡፡ በአላህ እምላለሁ፤ ትቀጣጥፉት ከነበራችሁት ሁሉ በእርግጥ ትጠየቃላችሁ፡፡

وَيَجۡعَلُونَ لِمَا لَا يَعۡلَمُونَ نَصِيبٗا مِّمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡۗ تَٱللَّهِ لَتُسۡـَٔلُنَّ عَمَّا كُنتُمۡ تَفۡتَرُونَ ﴿٥٦﴾

57. ለአላህም (ከመላእክት) ሴቶች ልጆችን ያደርጋሉ፡፡ ጥራት ተገባው፡፡ ለእነርሱም የሚፈልጉትን (ወንዶች ልጆችን) ያደርጋሉ፡፡

وَيَجۡعَلُونَ لِلَّهِ ٱلۡبَنَٰتِ سُبۡحَٰنَهُۥ وَلَهُم مَّا يَشۡتَهُونَ ﴿٥٧﴾

58. አንዳቸውም በሴት ልጅ በተበሰረ ጊዜ እርሱ የተቆጨ ኾኖ ፊቱ ጠቁሮ ይውላል፡፡

وَإِذَا بُشِّرَ أَحَدُهُم بِٱلۡأُنثَىٰ ظَلَّ وَجۡهُهُۥ مُسۡوَدّٗا وَهُوَ كَظِيمٞ ﴿٥٨﴾

59. በእርሱ ከተበሰረበት ነገር መጥፎነት በውርደት ላይ ኾኖ ይያዘውን ወይስ በዐፈር ውስጥ ይደብቀውን (በማለት እያምታታ) ከሰዎች ይደበቃል፡፡ ንቁ! የሚፈርዱት (ፍርድ) ምንኛ ከፋ!

يَتَوَٰرَىٰ مِنَ ٱلۡقَوۡمِ مِن سُوٓءِ مَا بُشِّرَ بِهِۦٓۚ أَيُمۡسِكُهُۥ عَلَىٰ هُونٍ أَمۡ يَدُسُّهُۥ فِي ٱلتُّرَابِۗ أَلَا سَآءَ مَا يَحۡكُمُونَ ﴿٥٩﴾

60. ለእነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም ለማያምኑት መጥፎ ጠባይ አላቸው፡፡ ለአላህም ታላቅ ባሕርይ አለው፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

لِلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ مَثَلُ ٱلسَّوۡءِۖ وَلِلَّهِ ٱلۡمَثَلُ ٱلۡأَعۡلَىٰۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ﴿٦٠﴾

61. አላህም ሰዎችን በበደላቸው በያዛቸው ኖሮ በርሷ (በምድር ላይ) ከተንቀሳቃሽ ምንንም ባልተወ ነበር፡፡ ግን እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ ያቆያቸዋል፡፡ ጊዜያቸውም በመጣ ወቅት አንዲትን ሰዓት አይቆዩም፤ አይቀደሙምም፡፡

وَلَوۡ يُؤَاخِذُ ٱللَّهُ ٱلنَّاسَ بِظُلۡمِهِم مَّا تَرَكَ عَلَيۡهَا مِن دَآبَّةٖ وَلَٰكِن يُؤَخِّرُهُمۡ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗىۖ فَإِذَا جَآءَ أَجَلُهُمۡ لَا يَسۡتَـٔۡخِرُونَ سَاعَةٗ وَلَا يَسۡتَقۡدِمُونَ ﴿٦١﴾

62. ለአላህም የሚጠሉትን ነገር ያደረጋሉ፡፡ ለእነሱም መልካሚቱ (አገር) አለቻቸው በማለት ምላሶቻቸው ውሸትን ይናገራሉ፡፡ ለእነሱ እሳት ያለቻቸው መኾናቸውና እነሱም (ወደርሷ) በቅድሚያ የሚነዱ መኾናቸው ጥርጥር የለበትም፡፡

وَيَجۡعَلُونَ لِلَّهِ مَا يَكۡرَهُونَۚ وَتَصِفُ أَلۡسِنَتُهُمُ ٱلۡكَذِبَ أَنَّ لَهُمُ ٱلۡحُسۡنَىٰۚ لَا جَرَمَ أَنَّ لَهُمُ ٱلنَّارَ وَأَنَّهُم مُّفۡرَطُونَ ﴿٦٢﴾

63. በአላህ እንምላለን፤ ካንተ በፊት ወደ ነበሩት ሕዝቦች በእርግጥ (መልክተኞችን) ልከናል፡፡ ሰይጣንም ለእነርሱ ሥራዎቻቸውን ሸለመላቸው፡፡ እርሱም ዛሬ ረዳታቸው ነው፡፡ ለእነሱም (ኋላ) አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

تَٱللَّهِ لَقَدۡ أَرۡسَلۡنَآ إِلَىٰٓ أُمَمٖ مِّن قَبۡلِكَ فَزَيَّنَ لَهُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ أَعۡمَٰلَهُمۡ فَهُوَ وَلِيُّهُمُ ٱلۡيَوۡمَ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿٦٣﴾

64. ባንተም ላይ መጽሐፉን አላወረድንም፤ ያንን በርሱ የተለያዩበትን ለነርሱ ልታብራራላቸውና ለሚያምኑትም ሕዝቦች መሪና እዝነት ሊኾን እንጂ፡፡

وَمَآ أَنزَلۡنَا عَلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَ إِلَّا لِتُبَيِّنَ لَهُمُ ٱلَّذِي ٱخۡتَلَفُواْ فِيهِ وَهُدٗى وَرَحۡمَةٗ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ﴿٦٤﴾

65. አላህም ከሰማይ ውሃን አወረደ፡፡ በእርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው አደረገ፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚሰሙ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምር አለለ፡፡

وَٱللَّهُ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَحۡيَا بِهِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَآۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّقَوۡمٖ يَسۡمَعُونَ ﴿٦٥﴾

66. ለናንተም በግመል፣ በከብት፣ በፍየል በእርግጥ መገምገሚያ አልላችሁ፡፡ በሆዶቹ ውስጥ ካለው ከፈረስና ከደም መካከል ጥሩ ወተትን ለጠጪዎች ተዋጭ ሲሆን እናጠጣችኋለን፡፡

وَإِنَّ لَكُمۡ فِي ٱلۡأَنۡعَٰمِ لَعِبۡرَةٗۖ نُّسۡقِيكُم مِّمَّا فِي بُطُونِهِۦ مِنۢ بَيۡنِ فَرۡثٖ وَدَمٖ لَّبَنًا خَالِصٗا سَآئِغٗا لِّلشَّٰرِبِينَ ﴿٦٦﴾

67. ከዘምባባዎችና ከወይኖችም ፍሬዎች (እንመግባችኋለን)፡፡ ከእርሱ ጠጅንና መልካም ምግብንም ትሠራላችሁ፡፡ በዚህም ውስጥ ለሚያስቡ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምር አለለ፡፡

وَمِن ثَمَرَٰتِ ٱلنَّخِيلِ وَٱلۡأَعۡنَٰبِ تَتَّخِذُونَ مِنۡهُ سَكَرٗا وَرِزۡقًا حَسَنًاۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ﴿٦٧﴾

68. ጌታህም ወደ ንብ እንዲህ ሲል አስታወቀ «ከተራራዎች፣ ከዛፍም፣ (ሰዎች) ከሚሠሩትም (ቀፎ) ቤቶችን ያዢ፡፡

وَأَوۡحَىٰ رَبُّكَ إِلَى ٱلنَّحۡلِ أَنِ ٱتَّخِذِي مِنَ ٱلۡجِبَالِ بُيُوتٗا وَمِنَ ٱلشَّجَرِ وَمِمَّا يَعۡرِشُونَ ٦٨

69. «ከዚያም ከፍሬዎች ሁሉ ብይ፡፡ የጌታሽንም መንገዶች (ላንቺ) የተገሩ ሲኾኑ ግቢ፡፡» ከሆዶችዋ መልኮቹ የተለያዩ መጠጥ ይወጣል፡፡ በእርሱ ውስጥ ለሰዎች መድኃኒት አለበት፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያስተነትኑ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምር አልለበት፡፡

ثُمَّ كُلِي مِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِ فَٱسۡلُكِي سُبُلَ رَبِّكِ ذُلُلٗاۚ يَخۡرُجُ مِنۢ بُطُونِهَا شَرَابٞ مُّخۡتَلِفٌ أَلۡوَٰنُهُۥ فِيهِ شِفَآءٞ لِّلنَّاسِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّقَوۡمٖ يَتَفَكَّرُونَ ٦٩

70. አላህም ፈጠራችሁ፤ ከዚያም ይገድላችኋል፡፡ ከእናንተም ከዕውቀት በኋላ ምንንም ነገር እንዳያውቅ ወደ ወራዳ ዕድሜ የሚመለስ ሰው አልለ፡፡ አላህ ዐዋቂ ቻይ ነው፡፡

وَٱللَّهُ خَلَقَكُمۡ ثُمَّ يَتَوَفَّىٰكُمۡۚ وَمِنكُم مَّن يُرَدُّ إِلَىٰٓ أَرۡذَلِ ٱلۡعُمُرِ لِكَيۡ لَا يَعۡلَمَ بَعۡدَ عِلۡمٖ شَيۡـًٔاۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٞ قَدِيرٞ ٧٠

71. አላህም ከፊላችሁን በከፊሉ ላይ በሲሳይ አበለጠ፡፡ እነዚያም በላጭ የተደረጉት ሲሳያቸውን እጆቻቸው በያዙዋቸው (ባሮች) ላይ እነሱ በእርሱ ይተካከሉ ዘንድ መላሾች አይደሉም፡፡ ታዲያ በአላህ ጸጋ (ለእርሱ ተጋሪ በማድረግ) ይክዳሉን

وَٱللَّهُ فَضَّلَ بَعۡضَكُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖ فِي ٱلرِّزۡقِۚ فَمَا ٱلَّذِينَ فُضِّلُواْ بِرَآدِّي رِزۡقِهِمۡ عَلَىٰ مَا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُهُمۡ فَهُمۡ فِيهِ سَوَآءٌۚ أَفَبِنِعۡمَةِ ٱللَّهِ يَجۡحَدُونَ ٧١

72. አላህም ከነፍሶቻችሁ (ከጎሶቻችሁ) ለእናንተ ሚስቶችን አደረገ፡፡ ለእናንተም ከሚስቶቻችሁ ወንዶች ልጆችን፣ የልጅ ልጆችንም አደረገላችሁ፡፡ ከመልካሞችም ጸጋዎች ሰጣችሁ፡፡ ታድያ በውሸት (በጣኦት) ያምናሉን በአላህም ጸጋ እነሱ ይክዳሉን

وَٱللَّهُ جَعَلَ لَكُم مِّنۡ أَنفُسِكُمۡ أَزۡوَٰجٗا وَجَعَلَ لَكُم مِّنۡ أَزۡوَٰجِكُم بَنِينَ وَحَفَدَةٗ وَرَزَقَكُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِۚ أَفَبِٱلۡبَٰطِلِ يُؤۡمِنُونَ وَبِنِعۡمَتِ ٱللَّهِ هُمۡ يَكۡفُرُونَ ٧٢

73. ከአላህም ሌላ ከሰማያትም ከምድርም ምንንም ሲሳይ የማይሰጧቸውን (ምንንም) የማይችሉትንም ይግገዛሉ፡፡

وَيَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَمۡلِكُ لَهُمۡ رِزۡقٗا مِّنَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ شَيۡـٔٗا وَلَا يَسۡتَطِيعُونَ ٧٣

74. ለአላህም አምሳያዎችን አታድርጉ፡፡ አላህ (መሳይ እንደሌለው) ያውቃል፡፡ እናንተ ግን አታውቁም፡፡

فَلَا تَضۡرِبُواْ لِلَّهِ ٱلۡأَمۡثَالَۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ وَأَنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ٧٤

75. በምንም ላይ የማይችለውን በይዞታ ያለውን ባሪያና ከእኛ መልካም ሲሳይን የሰጠነውን እርሱም ከእርሱ (ከሰጠነው) በምስጢርና በግልጽ የሚለግሰውን (ነጻ) ሰው አላህ (ለጣዖትና ለርሱ) ምሳሌ አደረገ፡፡ (ሁለቱ) ይተካከላሉን ምስጋና ለአላህ ይኹን፡፡ በእውነቱ አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

۞ضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلًا عَبۡدٗا مَّمۡلُوكٗا لَّا يَقۡدِرُ عَلَىٰ شَيۡءٖ وَمَن رَّزَقۡنَٰهُ مِنَّا رِزۡقًا حَسَنٗا فَهُوَ يُنفِقُ مِنۡهُ سِرّٗا وَجَهۡرًاۖ هَلۡ يَسۡتَوُۥنَۚ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٧٥

76. አላህም ሁለትን ወንዶች (ለከሓዲና ለምእመን) ምሳሌ አደረገ፡፡ አንደኛቸው በምንም ነገር ላይ የማይችል ዲዳ ነው፡፡ እርሱም በጌታው ላይ ሸክም ነው፡፡ ወደ የትም ቢያዞረው በደግ ነገር አይመጣም፡፡ እርሱና ያ እርሱ በቀጥተኛው መንገድ ላይ ኾኖ በማስተካከል የሚያዘው ሰው ይስተካከላሉን

وَضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلٗا رَّجُلَيۡنِ أَحَدُهُمَآ أَبۡكَمُ لَا يَقۡدِرُ عَلَىٰ شَيۡءٖ وَهُوَ كَلٌّ عَلَىٰ مَوۡلَىٰهُ أَيۡنَمَا يُوَجِّههُّ لَا يَأۡتِ بِخَيۡرٍ هَلۡ يَسۡتَوِي هُوَ وَمَن يَأۡمُرُ بِٱلۡعَدۡلِ وَهُوَ عَلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ٧٦

77. በሰማያትና በምድርም ያለው ሩቅ ምስጢር የአላህ ነው፡፡ የሰዓቲቱም ነገር (መምጣቷ) እንደዓይን ቅጽበት እንጂ አይደለም፡፡ ወይ እርሱ ይበልጥ የቀረበ ነው፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَلِلَّهِ غَيۡبُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَمَآ أَمۡرُ ٱلسَّاعَةِ إِلَّا كَلَمۡحِ ٱلۡبَصَرِ أَوۡ هُوَ أَقۡرَبُۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٧٧

78. አላህም ከእናቶቻችሁ ሆዶች ምንም የማታውቁ ሆናችሁ አወጣችሁ፡፡ ታመሰግኑም ዘንድ ለእናንተ መስሚያን ማያዎችንም ልቦችንም አደረገላችሁ፡፡

وَٱللَّهُ أَخۡرَجَكُم مِّنۢ بُطُونِ أُمَّهَٰتِكُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ شَيۡـٔٗا وَجَعَلَ لَكُمُ ٱلسَّمۡعَ وَٱلۡأَبۡصَٰرَ وَٱلۡأَفۡـِٔدَةَ لَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ٧٨

79. ወደ በራሪዎች በሰማይ አየር ውስጥ (ለመብረር) የተገሩ ሲኾኑ (ከመውደቅ) አላህ እንጂ ሌላ የማይዛቸው ኾነው አይመለከቱምን በዚህ ውስጥ ለሚያምኑ ሕዝቦች በእርግጥ ተዓምራቶች አሉ፡፡

أَلَمۡ يَرَوۡاْ إِلَى ٱلطَّيۡرِ مُسَخَّرَٰتٖ فِي جَوِّ ٱلسَّمَآءِ مَا يُمۡسِكُهُنَّ إِلَّا ٱللَّهُۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ٧٩

80. አላህም ከቤቶቻችሁ ለእናንተ መርጊያን አደረገላችሁ፡፡ ከእንስሳዎችም ቆዳዎች በጉዟችሁ ቀን በመቀመጫችሁም ቀን የምታቀልላቸውን ቤቶች ለናንተ አደረገላችሁ፡፡ ከበግዋ ሱፎች፣ ከግመልዋም ጠጉሮች፣ ከፍየልዋም ጠጉሮች የቤት ዕቃዎችን እስከ ጊዜም ድረስ መጠቃቀሚያን (አደረገላችሁ)፡፡

وَٱللَّهُ جَعَلَ لَكُم مِّنۢ بُيُوتِكُمۡ سَكَنٗا وَجَعَلَ لَكُم مِّن جُلُودِ ٱلۡأَنۡعَٰمِ بُيُوتٗا تَسۡتَخِفُّونَهَا يَوۡمَ ظَعۡنِكُمۡ وَيَوۡمَ إِقَامَتِكُمۡ وَمِنۡ أَصۡوَافِهَا وَأَوۡبَارِهَا وَأَشۡعَارِهَآ أَثَٰثٗا وَمَتَٰعًا إِلَىٰ حِينٖ ٨٠

81. አላህም ከፈጠረው ነገር ለእናንተ ጥላዎችን አደረገላችሁ፡፡ ከጋራዎችም ለእናንተ መከለያዎችን አደረገላችሁ፡፡ ሐሩርንም (ብርድንም) የሚጠብቋችሁን ልብሶች የጦራችሁንም አደጋ የሚጠብቋችሁን ጥሩሮች ለእናንተ አደረገላችሁ፡፡ እንደዚሁ ትሰልሙ ዘንድ ጸጋውን በእናንተ ላይ ይሞላል፡፡

وَٱللَّهُ جَعَلَ لَكُم مِّمَّا خَلَقَ ظِلَٰلٗا وَجَعَلَ لَكُم مِّنَ ٱلۡجِبَالِ أَكۡنَٰنٗا وَجَعَلَ لَكُمۡ سَرَٰبِيلَ تَقِيكُمُ ٱلۡحَرَّ وَسَرَٰبِيلَ تَقِيكُم بَأۡسَكُمۡۚ كَذَٰلِكَ يُتِمُّ نِعۡمَتَهُۥ عَلَيۡكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تُسۡلِمُونَ ٨١

82. (ከኢስላም) ቢሸሹም ባንተ ላይ ያለብህ ግልጽ ማድረስ ብቻ ነው፡፡

فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنَّمَا عَلَيۡكَ ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ٨٢

83. የአላህን ጸጋ ያውቃሉ፡፡ ከዚያም ይክዷታል፡፡ አብዛኞቻቸውም ከሓዲዎቹ ናቸው፡፡

يَعۡرِفُونَ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ ثُمَّ يُنكِرُونَهَا وَأَكۡثَرُهُمُ ٱلۡكَٰفِرُونَ ٨٣

84. ከየሕዝቡም ሁሉ መስካሪን የምንቀሰቅስበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ ከዚያም ለእነዚያ ለካዱት (ንግግር) አይፈቀድላቸውም፡፡ እነሱም በወቀሳ አይታለፉም፡፡

وَيَوۡمَ نَبۡعَثُ مِن كُلِّ أُمَّةٖ شَهِيدٗا ثُمَّ لَا يُؤۡذَنُ لِلَّذِينَ كَفَرُواْ وَلَا هُمۡ يُسۡتَعۡتَبُونَ ٨٤

85. እነዚያም የበደሉት ቅጣቱን ባዩ ጊዜ ከእነሱ (ቅጣቱ) አይቀለልላቸውም፡፡ እነሱም ጊዜ አይሰስጡም፡፡

وَإِذَا رَءَا ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ ٱلۡعَذَابَ فَلَا يُخَفَّفُ عَنۡهُمۡ وَلَا هُمۡ يُنظَرُونَ ٨٥

86. እነዚያም ያጋሩት የሚያጋሩዋቸውን ባዩ ጊዜ «ጌታችን ሆይ! እነዚህ ከአንተ ሌላ እንገዛቸው የነበርነው ተጋሪዎቻችን ናቸው» ይላሉ፡፡ (አማልክቶች) «እናንተ በእርግጥ ውሸታሞች ናችሁ» የማለትንም ቃል ወደእነሱ ይጥላሉ፡፡

وَإِذَا رَءَا ٱلَّذِينَ أَشۡرَكُواْ شُرَكَآءَهُمۡ قَالُواْ رَبَّنَا هَٰٓؤُلَآءِ شُرَكَآؤُنَا ٱلَّذِينَ كُنَّا نَدۡعُواْ مِن دُونِكَۖ فَأَلۡقَوۡاْ إِلَيۡهِمُ ٱلۡقَوۡلَ إِنَّكُمۡ لَكَٰذِبُونَ ٨٦

87. (አጋሪዎቹ) በዚያ ቀንም ታዛዥነታቸውን ወደ አላህ ያቀርባሉ፡፡ ይቀጣጥፉት የነበሩትም ሁሉ ከእነርሱ ይጠፉቸዋል፡፡

وَأَلۡقَوۡاْ إِلَى ٱللَّهِ يَوۡمَئِذٍ ٱلسَّلَمَۖ وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ٨٧

88. እነዚያ የካዱ፣ ከአላህም መንገድ የከለከሉ ያጠፉ በነበሩት ምክንያት ቅጣትን በቅጣት ላይ ጨመርንባቸው፡፡

ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ زِدۡنَٰهُمۡ عَذَابٗا فَوۡقَ ٱلۡعَذَابِ بِمَا كَانُواْ يُفۡسِدُونَ ٨٨

89. በየሕዝቡም ሁሉ ውስጥ ከነሳቸው በእነሱ ላይ መስካሪን የምንቀሰቅስበትን አንተንም በእነዚህ (ሕዝቦች) ላይ መስካሪ አድርገን የምናመጣህን ቀን (አስታውስ)፡፡ መጽሐፉንም ለሁሉ ነገር አብራሪ፣ መሪም፣ እዝነትም፣ ለሙስሊሞችም አብሳሪ ኾኖ ባንተ ላይ አወረድነው፡፡

وَيَوۡمَ نَبۡعَثُ فِي كُلِّ أُمَّةٖ شَهِيدًا عَلَيۡهِم مِّنۡ أَنفُسِهِمۡۖ وَجِئۡنَا بِكَ شَهِيدًا عَلَىٰ هَٰٓؤُلَآءِۚ وَنَزَّلۡنَا عَلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَ تِبۡيَٰنٗا لِّكُلِّ شَيۡءٖ وَهُدٗى وَرَحۡمَةٗ وَبُشۡرَىٰ لِلۡمُسۡلِمِينَ ٨٩

90. አላህ በማስተካከል፣ በማሳመርም፣ ለዝምድና ባለቤት በመስጠትም ያዛል፡፡ ከአስከፊም (ከማመንዘር)፣ ከሚጠላም ነገር ሁሉ፣ ከመበደልም ይከለክላል፡፡ ትገነዘቡ ዘንድ ይገስጻችኋል፡፡

۞إِنَّ ٱللَّهَ يَأۡمُرُ بِٱلۡعَدۡلِ وَٱلۡإِحۡسَٰنِ وَإِيتَآيِٕ ذِي ٱلۡقُرۡبَىٰ وَيَنۡهَىٰ عَنِ ٱلۡفَحۡشَآءِ وَٱلۡمُنكَرِ وَٱلۡبَغۡيِۚ يَعِظُكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَذَكَّرُونَ ٩٠

91. ቃል ኪዳንም በገባችሁ ጊዜ በአላህ ቃል ኪዳን ሙሉ፡፡ መሓሎቻችሁንም ከአጠነከራችኋት በኋላ አላህን በእናንተ ላይ በእርግጥ መስካሪ ያደረጋችሁ ስትኾኑ አታፍርሱ፡፡ አላህ የምትሠሩትን ሁሉ ያውቃልና፡፡

وَأَوۡفُواْ بِعَهۡدِ ٱللَّهِ إِذَا عَٰهَدتُّمۡ وَلَا تَنقُضُواْ ٱلۡأَيۡمَٰنَ بَعۡدَ تَوۡكِيدِهَا وَقَدۡ جَعَلۡتُمُ ٱللَّهَ عَلَيۡكُمۡ كَفِيلًاۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ مَا تَفۡعَلُونَ ٩١

92. (ቃል ኪዳናችሁን በማፍረስ አንዲቱ) ሕዝብ እርሷ ከ(ሌላይቱ) ሕዝብ የበዛች ለመኾንዋ በመካከላችሁ መሓሎቻችሁን (ለከዳት) መግቢያ አድርጋችሁ የምትይዙ ስትኾኑ እንደዚያች ፈትልዋን ከጠነከረ በኋላ ትርትሮች አድርጋ እንዳፈረሰችው (ሴት) አትኹኑ፡፡ አላህ በእርሱ ይሞክራችኋል፤ በትንሣኤ ቀንም በእርሱ ትለያዩበት የነበራችሁትን ነገር ለእናንተ በእርግጥ ያብራራላችኋል፡፡

وَلَا تَكُونُواْ كَٱلَّتِي نَقَضَتۡ غَزۡلَهَا مِنۢ بَعۡدِ قُوَّةٍ أَنكَٰثٗا تَتَّخِذُونَ أَيۡمَٰنَكُمۡ دَخَلَۢا بَيۡنَكُمۡ أَن تَكُونَ أُمَّةٌ هِيَ أَرۡبَىٰ مِنۡ أُمَّةٍۚ إِنَّمَا يَبۡلُوكُمُ ٱللَّهُ بِهِۦۚ وَلَيُبَيِّنَنَّ لَكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ مَا كُنتُمۡ فِيهِ تَخۡتَلِفُونَ ٩٢

93. አላህም በሻ ኖሮ አንዲት ሕዝብ ባደረጋችሁ ነበር፡፡ ግን የሚሻውን ሰው ያጠማል፡፡ የሚሻውንም ሰው ያቀናል፡፡ ትሠሩት ከነበራችሁትም ሁሉ በእርግጥ ትጠየቃላችሁ፡፡

وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَجَعَلَكُمۡ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ وَلَٰكِن يُضِلُّ مَن يَشَآءُ وَيَهۡدِي مَن يَشَآءُۚ وَلَتُسۡـَٔلُنَّ عَمَّا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٩٣

94. ጫማዎች ከተደላደሉ በኋላ እንዳይንዳለጡ ከአላህም መንገድ በመከልከላችሁ ምክንያት ቅጣትን እንዳትቀምሱ መሓሎቻችሁን በመካከላችሁ ለክዳት መግቢያ አድርጋችሁ አትያዙ፡፡ ለእናንተም (ያን ጊዜ) ታላቅ ቅጣት አላችሁ፡፡

وَلَا تَتَّخِذُوٓاْ أَيۡمَٰنَكُمۡ دَخَلَۢا بَيۡنَكُمۡ فَتَزِلَّ قَدَمُۢ بَعۡدَ ثُبُوتِهَا وَتَذُوقُواْ ٱلسُّوٓءَ بِمَا صَدَدتُّمۡ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَلَكُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٞ ٩٤

95. በአላህም ቃል ኪዳን ጥቂትን ዋጋ አትግዙ፡፡ የምታውቁ ብትኾኑ አላህ ዘንድ ያለው ምንዳ እርሱ ለእናንተ በላጭ ነውና፡፡

وَلَا تَشۡتَرُواْ بِعَهۡدِ ٱللَّهِ ثَمَنٗا قَلِيلًاۚ إِنَّمَا عِندَ ٱللَّهِ هُوَ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٩٥

96. እናንተ ዘንድ ያለው ሁሉ ያልቃል፡፡ አላህ ዘንድ ያለው ግን (ዘለዓለም) ቀሪ ነው፡፡ እነዚያንም የታገሡትን ይሠሩት በነበሩት በመልካሙ ምንዳቸውን እንመነዳቸዋለን፡፡

مَا عِندَكُمۡ يَنفَدُ وَمَا عِندَ ٱللَّهِ بَاقٖۗ وَلَنَجۡزِيَنَّ ٱلَّذِينَ صَبَرُوٓاْ أَجۡرَهُم بِأَحۡسَنِ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٩٦

97. ከወንድ ወይም ከሴት እርሱ አማኝ ኾኖ በጎን የሰራ መልካም ኑሮን በእርግጥ እናኖረዋለን፡፡ ይሠሩትም ከነበሩት ነገር በመልካሙ ምንዳቸውን እንመነዳቸዋለን፡፡

مَنۡ عَمِلَ صَٰلِحٗا مِّن ذَكَرٍ أَوۡ أُنثَىٰ وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَلَنُحۡيِيَنَّهُۥ حَيَوٰةٗ طَيِّبَةٗۖ وَلَنَجۡزِيَنَّهُمۡ أَجۡرَهُم بِأَحۡسَنِ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٩٧

98. ቁርኣንንም ባነበብህ ጊዜ እርጉም ከኾነው ሰይጣን በአላህ ተጠበቅ፡፡

فَإِذَا قَرَأۡتَ ٱلۡقُرۡءَانَ فَٱسۡتَعِذۡ بِٱللَّهِ مِنَ ٱلشَّيۡطَٰنِ ٱلرَّجِيمِ ٩٨

99. እርሱ በእነዚያ ባመኑትና በጌታቸው ላይ በሚጠጉት ላይ ለእርሱ ስልጣን የለውምና፡፡

إِنَّهُۥ لَيۡسَ لَهُۥ سُلۡطَٰنٌ عَلَى ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٩٩

100. ስልጣኑ በእነዚያ በሚታዘዙት ላይና በእነዚያም እነርሱ በእርሱ (ምክንያት) አጋሪዎች በኾኑት ላይ ብቻ ነው፡፡

إِنَّمَا سُلۡطَٰنُهُۥ عَلَى ٱلَّذِينَ يَتَوَلَّوۡنَهُۥ وَٱلَّذِينَ هُم بِهِۦ مُشۡرِكُونَ ١٠٠

101. በአንቀጽም ስፍራ አንቀጽን በለወጥን ጊዜ አላህም የሚያወርደውን ነገር አዋቂ ነው፡፡ «አንተ ቀጣፊ እንጂ ሌላ አይደለህም» ይላሉ፡፡ በእውነቱ አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

وَإِذَا بَدَّلۡنَآ ءَايَةٗ مَّكَانَ ءَايَةٖ وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا يُنَزِّلُ قَالُوٓاْ إِنَّمَآ أَنتَ مُفۡتَرِۢۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ١٠١

102. እነዚያን ያመኑትን ለማረጋጋት ሙስሊሞቹንም ለመምራትና ለማብሰር (ቁርኣንን) ቅዱሱ መንፈስ (ጂብሪል) እውነተኛ ሲኾን ከጌታህ አወረደው በላቸው፡፡

قُلۡ نَزَّلَهُۥ رُوحُ ٱلۡقُدُسِ مِن رَّبِّكَ بِٱلۡحَقِّ لِيُثَبِّتَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَهُدٗى وَبُشۡرَىٰ لِلۡمُسۡلِمِينَ ١٠٢

103. እነርሱም «እርሱን (ቁርኣንን) የሚያስተምረው ሰው ብቻ ነው» ማለታቸውን በእርግጥ እናውቃለን፡፡ የዚያ ወደርሱ የሚያስጠጉበት ሰው ቋንቋ ዐጀም ነው፡፡ ይህ (ቁርአን) ግን ግልጽ ዐረብኛ ቋንቋ ነው፡፡

وَلَقَدۡ نَعۡلَمُ أَنَّهُمۡ يَقُولُونَ إِنَّمَا يُعَلِّمُهُۥ بَشَرٞۗ لِّسَانُ ٱلَّذِي يُلۡحِدُونَ إِلَيۡهِ أَعۡجَمِيّٞ وَهَٰذَا لِسَانٌ عَرَبِيّٞ مُّبِينٞ ١٠٣

104. እነዚያን በአላህ አንቀጾች የማያምኑትን አላህ አይመራቸውም፤ ለነሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ لَا يَهۡدِيهِمُ ٱللَّهُ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٌ ١٠٤

105. ውሸትን የሚቀጣጥፉት እነዚያ በአላህ አንቀጾች የማያምኑት ብቻ ናቸው፡፡ እነዚያም ውሸታሞቹ እነሱ ብቻ ናቸው፡፡

إِنَّمَا يَفۡتَرِي ٱلۡكَذِبَ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡكَٰذِبُونَ ١٠٥

106. ከእምነቱ በኋላ በአላህ የካደ ሰው (ብርቱ ቅጣት አልለው)፡፡ ልቡ በእምነት የረጋ ኾኖ (በክህደት ቃል በመናገር) የተገደደ ሰው ብቻ ሲቀር፡፡ ግን ልባቸውን በክሕደት የከፈቱ ሰዎች በነሱ ላይ ከአላህ ቁጣ አለባቸው፡፡ ለእነሱም ታላቅ ቅጣት አልላቸው፡፡

مَن كَفَرَ بِٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ إِيمَٰنِهِۦٓ إِلَّا مَنۡ أُكۡرِهَ وَقَلۡبُهُۥ مُطۡمَئِنُّۢ بِٱلۡإِيمَٰنِ وَلَٰكِن مَّن شَرَحَ بِٱلۡكُفۡرِ صَدۡرٗا فَعَلَيۡهِمۡ غَضَبٞ مِّنَ ٱللَّهِ وَلَهُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٞ ١٠٦

107. ይህ (ቅጣት) እነሱ ቅርቢቱን ሕይወት ከመጨረሻይቱ በመምረጣቸው ምክንያትና አላህም ከሓዲዎችን ሕዝቦች የማያቀና በመኾኑ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمُ ٱسۡتَحَبُّواْ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا عَلَى ٱلۡأٓخِرَةِ وَأَنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ١٠٧

108. እነዚያ እነርሱ በልቦቻቸው፣ በዓይኖቻቸውም፣ በጆሮዎቻቸውም ላይ አላህ ያተመባቸው ናቸው፡፡ እነዚያም ዝንጉዎቹ እነሱ ናቸው፡፤

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ طَبَعَ ٱللَّهُ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ وَسَمۡعِهِمۡ وَأَبۡصَٰرِهِمۡۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡغَٰفِلُونَ ١٠٨

109. እነርሱ በመጨረሻይቱ ዓለም ከሳሪዎቹ እነሱ ለመኾናቸው ጥርጥር የለም፡፡

لَا جَرَمَ أَنَّهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ١٠٩

110. ከዚያም ጌታህ ለእነዚያ ከተፈተኑ በኋላ ለተሰደዱት ከዚያም ለታገሉትና ለታገሱት (መሓሪ አዛኝ ነው)፡፡ ጌታህ ከእርሷ (ከፈተናዋ) በኋላ በእርግጥ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

ثُمَّ إِنَّ رَبَّكَ لِلَّذِينَ هَاجَرُواْ مِنۢ بَعۡدِ مَا فُتِنُواْ ثُمَّ جَٰهَدُواْ وَصَبَرُوٓاْ إِنَّ رَبَّكَ مِنۢ بَعۡدِهَا لَغَفُورٞ رَّحِيمٞ ١١٠

111. ነፍስ ሁሉ ከራሷ ላይ የምትከራከር ኾና የምትመጣበትን ነፍስም ሁሉ የሠራችውን (ዋጋ) የምትቀበልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

۞يَوۡمَ تَأۡتِي كُلُّ نَفۡسٖ تُجَٰدِلُ عَن نَّفۡسِهَا وَتُوَفَّىٰ كُلُّ نَفۡسٖ مَّا عَمِلَتۡ وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ١١١

112. አላህ ጸጥተኛ፣ የረካች፣ ሲሳይዋ ሰፊ ኾኖ ከየስፍራው ይመጣላት የነበረችውንና በአላህ ጸጋዎች የካደችውን አላህም ይሠሩት በነበሩት ኃጢአት የረኃብንና የፍርሃትን ቅጣቶች ያቀመሳትን ከተማ (መካን) ምሳሌ አደረገ፡፡

وَضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلٗا قَرۡيَةٗ كَانَتۡ ءَامِنَةٗ مُّطۡمَئِنَّةٗ يَأۡتِيهَا رِزۡقُهَا رَغَدٗا مِّن كُلِّ مَكَانٖ فَكَفَرَتۡ بِأَنۡعُمِ ٱللَّهِ فَأَذَٰقَهَا ٱللَّهُ لِبَاسَ ٱلۡجُوعِ وَٱلۡخَوۡفِ بِمَا كَانُواْ يَصۡنَعُونَ ١١٢

113. ከእነርሱ ውስጥ የኾነ መልክተኛም በእርግጥ መጣላቸው፡፡ አስተባበሉትም፡፡ እነሱም በዳዮች ኾነው ቅጣቱ ያዛቸው፡፡

وَلَقَدۡ جَآءَهُمۡ رَسُولٞ مِّنۡهُمۡ فَكَذَّبُوهُ فَأَخَذَهُمُ ٱلۡعَذَابُ وَهُمۡ ظَٰلِمُونَ ١١٣

114. አላህም ከሰጣችሁ ሲሳይ የተፈቀደ ንጹሕ ሲኾን ብሉ፡፡ የአላህንም ጸጋ እርሱን የምትገዙት ብትሆኑ አመስግኑ፡፡

فَكُلُواْ مِمَّا رَزَقَكُمُ ٱللَّهُ حَلَٰلٗا طَيِّبٗا وَٱشۡكُرُواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ إِن كُنتُمۡ إِيَّاهُ تَعۡبُدُونَ ١١٤

115. በእናንተ ላይ እርም ያደረገው በክትንና ደምን፣ የአሳማንም ስጋ፣ ያንንም (በመታረድ ጊዜ) በእርሱ ከአላህ ስም ሌላ የተነሳበትን ብቻ ነው፡፡ አመጸኛም ወሰን አላፊም ሳይኾን (ለመብላት) የተገደደ ሰው (ይፈቀድለታል)፡፡ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

إِنَّمَا حَرَّمَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡمَيۡتَةَ وَٱلدَّمَ وَلَحۡمَ ٱلۡخِنزِيرِ وَمَآ أُهِلَّ لِغَيۡرِ ٱللَّهِ بِهِۦۖ فَمَنِ ٱضۡطُرَّ غَيۡرَ بَاغٖ وَلَا عَادٖ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ١١٥

116. በአላህም ላይ ውሸትን ልትቀጣጥፉ ምላሶቻችሁ በሚመጥኑት ውሸት «ይህ የተፈቀደ ነው፤ ይህም እርም ነው» አትበሉ፡፡ እነዚያ በአላህ ላይ ውሸትን የሚቀጣጥፉ አይድኑም፡፡

وَلَا تَقُولُواْ لِمَا تَصِفُ أَلۡسِنَتُكُمُ ٱلۡكَذِبَ هَٰذَا حَلَٰلٞ وَهَٰذَا حَرَامٞ لِّتَفۡتَرُواْ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَفۡتَرُونَ عَلَى ٱللَّهِ ٱلۡكَذِبَ لَا يُفۡلِحُونَ ١١٦

117. ጥቂት መጣቀም አላቸው፡፡ ለእነሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

مَتَٰعٞ قَلِيلٞ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ١١٧

118. በእነዚያም ይሁዳውያን በኾኑት ላይ ከአሁን በፊት በአንተ ላይ የተረክነውን ነገር እርም አድርገንባቸዋል፡፡ እኛም አልበደልናቸውም፡፡ ግን ነፍሶቻቸውን ይበድሉ ነበሩ፡፡

وَعَلَى ٱلَّذِينَ هَادُواْ حَرَّمۡنَا مَا قَصَصۡنَا عَلَيۡكَ مِن قَبۡلُۖ وَمَا ظَلَمۡنَٰهُمۡ وَلَٰكِن كَانُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ يَظۡلِمُونَ ١١٨

119. ከዚያም ጌታህ ለእነዚያ በስሕተት መጥፎን ለሠሩና ከዚያም ከዚህ በኋላ ለተጸጸቱ ሥራቸውንም ላበጁ ጌታህ ከእርሷ በኋላ በእርግጥ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

ثُمَّ إِنَّ رَبَّكَ لِلَّذِينَ عَمِلُواْ ٱلسُّوٓءَ بِجَهَٰلَةٖ ثُمَّ تَابُواْ مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ وَأَصۡلَحُوٓاْ إِنَّ رَبَّكَ مِنۢ بَعۡدِهَا لَغَفُورٞ رَّحِيمٞ ١١٩

120. ኢብራሂም ለአላህ ታዛዥ ወደ ቀጥተኛ ሃይማኖት ተዘንባይ ሕዝብ ነበር፡፡ ከአጋሪዎቹም አልነበረም፡፡

إِنَّ إِبۡرَٰهِيمَ كَانَ أُمَّةٗ قَانِتٗا لِّلَّهِ حَنِيفٗا وَلَمۡ يَكُ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ١٢٠

121. ለጸጋዎቹ አመስጋኝ ነበር፤ መረጠው፡፡ ወደ ቀጥተኛውም መንገድ መራው፡፡

شَاكِرٗا لِّأَنۡعُمِهِۚ ٱجۡتَبَىٰهُ وَهَدَىٰهُ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ١٢١

122. በቅርቢቱም ዓለም በጎን ነገር ሰጠነው፡፡ እርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም በእርግጥ ከመልካሞቹ ነው፡፡

وَءَاتَيۡنَٰهُ فِي ٱلدُّنۡيَا حَسَنَةٗۖ وَإِنَّهُۥ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ لَمِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ١٢٢

123. ከዚያም ወደ አንተ የኢብራሂምን ሃይማኖት ቀጥተኛ ሲኾን ተከተል፤ ከአጋሪዎቹም አልነበረም ማለት አወረድን፡፡

ثُمَّ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ أَنِ ٱتَّبِعۡ مِلَّةَ إِبۡرَٰهِيمَ حَنِيفٗاۖ وَمَا كَانَ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ١٢٣

124. ሰንበት (ክልክል) የተደረገው በእነዚያ በእርሱ በተለያዩበት ሰዎች ላይ ብቻ ነው፡፡ ጌታህም በትንሣኤ ቀን ይለያዩበት በነበሩት ነገር በመካከላቸው በእርግጥ ይፈርዳል፡፡

إِنَّمَا جُعِلَ ٱلسَّبۡتُ عَلَى ٱلَّذِينَ ٱخۡتَلَفُواْ فِيهِۚ وَإِنَّ رَبَّكَ لَيَحۡكُمُ بَيۡنَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فِيمَا كَانُواْ فِيهِ يَخۡتَلِفُونَ ١٢٤

125. ወደ ጌታህ መንገድ በብልሃትና በመልካም ግሳጼ (በለዘብታ ቃል) ጥራ፡፡ በዚያችም እርሷ መልካም በኾነችው (ዘዴ) ተከራከራቸው፡፡ ጌታህ እርሱ ከመንገዱ የተሳሳተውን ሰው ዐዋቂ ነው፡፡ እርሱም ቅን የኾኑትን ሰዎች ዐዋቂ ነው፡፡

ٱدۡعُ إِلَىٰ سَبِيلِ رَبِّكَ بِٱلۡحِكۡمَةِ وَٱلۡمَوۡعِظَةِ ٱلۡحَسَنَةِۖ وَجَٰدِلۡهُم بِٱلَّتِي هِيَ أَحۡسَنُۚ إِنَّ رَبَّكَ هُوَ أَعۡلَمُ بِمَن ضَلَّ عَن سَبِيلِهِۦ وَهُوَ أَعۡلَمُ بِٱلۡمُهۡتَدِينَ ١٢٥

126. ብትበቀሉም በርሱ በተቀጣችሁበት ብጤ ተበቀሉ፡፡ ብትታገሱም እርሱ ለታጋሾች በእርግጥ በላጭ ነው፡፡

وَإِنۡ عَاقَبۡتُمۡ فَعَاقِبُواْ بِمِثۡلِ مَا عُوقِبۡتُم بِهِۦۖ وَلَئِن صَبَرۡتُمۡ لَهُوَ خَيۡرٞ لِّلصَّٰبِرِينَ ١٢٦

127. ታገስም፤ መታገስህም በአላህ (ማስቻል) እንጂ አይደለም፡፡ በእነርሱም ላይ (ባያምኑ) አትተከዝ፡፡ (ባንተ ላይ) ከሚመክሩትም ተንኮል በጭንቀት ውስጥ አትኹን፡፡

وَٱصۡبِرۡ وَمَا صَبۡرُكَ إِلَّا بِٱللَّهِۚ وَلَا تَحۡزَنۡ عَلَيۡهِمۡ وَلَا تَكُ فِي ضَيۡقٖ مِّمَّا يَمۡكُرُونَ ١٢٧

128. አላህ ከእነዚያ ከሚፈሩትና ከእነዚያም እነሱ መልካም ሠሪዎች ከኾኑት ጋር ነውና፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ مَعَ ٱلَّذِينَ ٱتَّقَواْ وَّٱلَّذِينَ هُم مُّحۡسِنُونَ ١٢٨

# ሱረቱ አል ኢስራዕ

# سورة الإسراء

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ያ ባሪያውን ከተከበረው መስጊድ ወደዚያ ዙሪያውን ወደ ባረክነው ወደ ሩቁ መስጊድ በሌሊት ውስጥ ያስኼደው (ጌታ) ጥራት ይገባው፡፡ ከተዓምራቶቻችን ልናሳየው (አስኼድነው)፡፡ እነሆ እርሱ (አላህ) ሰሚው ተመልካቹ ነው፡፡

سُبۡحَٰنَ ٱلَّذِيٓ أَسۡرَىٰ بِعَبۡدِهِۦ لَيۡلٗا مِّنَ ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِ إِلَى ٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡأَقۡصَا ٱلَّذِي بَٰرَكۡنَا حَوۡلَهُۥ لِنُرِيَهُۥ مِنۡ ءَايَٰتِنَآۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡبَصِيرُ ١

2. ሙሳንም መጽሐፉን ሰጠነው፡፡ ለእስራኤልም ልጆች መሪ አደረግነው፡፡ ከእኔ ሌላ መጠጊያን አትያዙ፤ (አልናቸውም)፡፡

وَءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡكِتَٰبَ وَجَعَلۡنَٰهُ هُدٗى لِّبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ أَلَّا تَتَّخِذُواْ مِن دُونِي وَكِيلٗا ٢

3. እናንተ ከኑሕ ጋር (በመርከቢቱ) የጫናቸው ዘሮች ሆይ! (አላህን ተገዙ) እርሱ በብዙ አመስጋኝ ባሪያ ነበርና፡፡

ذُرِّيَّةَ مَنۡ حَمَلۡنَا مَعَ نُوحٍۚ إِنَّهُۥ كَانَ عَبۡدٗا شَكُورٗا ٣

4. ወደ እስራኤልም ልጆች በመጽሐፉ ውስጥ (እንዲህ በማለት) አወረድን፡፡ በምድር ላይ በእርግጥ ሁለት ጊዜ ታጠፋላችሁ፡፡ ትልቅንም ኩራት ትኮራላችሁ፡፡

وَقَضَيۡنَآ إِلَىٰ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ فِي ٱلۡكِتَٰبِ لَتُفۡسِدُنَّ فِي ٱلۡأَرۡضِ مَرَّتَيۡنِ وَلَتَعۡلُنَّ عُلُوّٗا كَبِيرٗا ٤

فَإِذَا جَآءَ وَعۡدُ أُولَىٰهُمَا بَعَثۡنَا عَلَيۡكُمۡ عِبَادٗا لَّنَآ أُوْلِي بَأۡسٖ شَدِيدٖ فَجَاسُواْ خِلَٰلَ ٱلدِّيَارِۚ وَكَانَ وَعۡدٗا مَّفۡعُولٗا ٥

5. ከሁለቱ (ጊዜያቶች) የመጀመሪያይቱ ቀጠሮ በመጣም ጊዜ ለእኛ የኾኑን ባሮች የብርቱ ኃይል ባለቤቶች የኾኑትን በእናንተ ላይ እንልካለን፡፡ በቤቶችም መካከል ይመላለሳሉ፤ (ይበረብሩታል፡፡) ይህ ተፈጻሚ ቀጠሮም ነበር፡፡

ثُمَّ رَدَدۡنَا لَكُمُ ٱلۡكَرَّةَ عَلَيۡهِمۡ وَأَمۡدَدۡنَٰكُم بِأَمۡوَٰلٖ وَبَنِينَ وَجَعَلۡنَٰكُمۡ أَكۡثَرَ نَفِيرًا ٦

6. ከዚያም (በኋላ) ለእናንተ በእነሱ ላይ ድልን መለስንላችሁ፡፡ በገንዘቦችና በወንዶች ልጆችም ጨመርንላችሁ፡፡ በወገንም የበዛችሁ አደረግናችሁ፡፡

إِنۡ أَحۡسَنتُمۡ أَحۡسَنتُمۡ لِأَنفُسِكُمۡۖ وَإِنۡ أَسَأۡتُمۡ فَلَهَاۚ فَإِذَا جَآءَ وَعۡدُ ٱلۡأٓخِرَةِ لِيَسُـُٔواْ وُجُوهَكُمۡ وَلِيَدۡخُلُواْ ٱلۡمَسۡجِدَ كَمَا دَخَلُوهُ أَوَّلَ مَرَّةٖ وَلِيُتَبِّرُواْ مَا عَلَوۡاْ تَتۡبِيرًا ٧

7. መልካም ብትሠሩ ለነፍሶቻችሁ መልካምን ሠራችሁ፡፡ መጥፎንም ብትሠሩ በነርሱ (በነፍሶቻችሁ) ላይ ነው፤ (አልን)፡፡ የኋለኛይቱም (ጊዜ) ቀጠሮ በመጣ ጊዜ ፊቶቻችሁን ሊያስከፉ፣ መስጊዱንም በመጀመሪያ ጊዜ እንደገቡት ሊገቡ፣ ያሸነፉትንም ሁሉ (ፈጽመው) ማጥፋትን እንዲያጠፉ (እንልካቸዋለን)፡፡

عَسَىٰ رَبُّكُمۡ أَن يَرۡحَمَكُمۡۚ وَإِنۡ عُدتُّمۡ عُدۡنَاۚ وَجَعَلۡنَا جَهَنَّمَ لِلۡكَٰفِرِينَ حَصِيرًا ٨

8. (በመጽሐፉም አልን) «ብትጸጸቱ፡- ጌታችሁ ሊያዝንላችሁ ይከጀላል፡፡ (ወደ ማጥፋት) ብትመለሱም እንመለሳለን፡፡ ገሀነምንም ለከሓዲዎች ማሰሪያ አደርገናል፡፡

إِنَّ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانَ يَهۡدِي لِلَّتِي هِيَ أَقۡوَمُ وَيُبَشِّرُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٱلَّذِينَ يَعۡمَلُونَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ أَنَّ لَهُمۡ أَجۡرٗا كَبِيرٗا ٩

9. ይህ ቁርአን ወደዚያች እርሷ ቀጥተኛ ወደ ኾነችው መንገድ ይመራል፡፡ እነዚያንም በጎ የሚሠሩትን ምእመናን ለእነሱ ታላቅ ምንዳ ያላቸው መኾኑን ያበስራል፡፡

وَأَنَّ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ أَعۡتَدۡنَا لَهُمۡ عَذَابًا أَلِيمٗا ١٠

10. እነዚያም በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት ለእነሱ አሳማሚ ቅጣትን አዘጋጅተንላቸዋል፤

وَيَدۡعُ ٱلۡإِنسَٰنُ بِٱلشَّرِّ دُعَآءَهُۥ بِٱلۡخَيۡرِۖ وَكَانَ ٱلۡإِنسَٰنُ عَجُولٗا ١١

11. ሰው መልካምን ነገር እንደሚለምን ሁሉ፤ መጥፎንም ነገር ይለምናል፡፡ ሰውም ቸኳላ ነው፡፡

وَجَعَلۡنَا ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ ءَايَتَيۡنِۖ فَمَحَوۡنَآ ءَايَةَ ٱلَّيۡلِ وَجَعَلۡنَآ ءَايَةَ ٱلنَّهَارِ مُبۡصِرَةٗ لِّتَبۡتَغُواْ فَضۡلٗا مِّن رَّبِّكُمۡ وَلِتَعۡلَمُواْ عَدَدَ ٱلسِّنِينَ وَٱلۡحِسَابَۚ وَكُلَّ شَيۡءٖ فَصَّلۡنَٰهُ تَفۡصِيلٗا ١٢

12. ሌሊትንና ቀንንም (ለችሎታችን) ምልክቶች አደረግን፡፡ የሌሊትን ምልክትም አበስን፡፡ የቀንን ምልክትም የምታሳይ አደረግን፡፡ (ይህም የኾነበት) ከጌታችሁ ትርፍን ልትፈልጉ የዓመታትንም ቁጥርና ሒሳብንም ታውቁ ዘንድ ነው፡፡ ነገሩንም ሁሉ ለያይተን ዘረዘርነው፡፡

وَكُلَّ إِنسَٰنٍ أَلۡزَمۡنَٰهُ طَٰٓئِرَهُۥ فِي عُنُقِهِۦۖ وَنُخۡرِجُ لَهُۥ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ كِتَٰبٗا يَلۡقَىٰهُ مَنشُورًا ١٣

13. ሰውንም ሁሉ በራሪውን (ሥራውን) በአንገቱ አስያዝነው፡፡ ለእርሱም በትንሣኤ ቀን የተዘረጋ ኾኖ የሚያገኘው የኾነን መጽሐፍ እናወጣለታለን፡፡

ٱقۡرَأۡ كِتَٰبَكَ كَفَىٰ بِنَفۡسِكَ ٱلۡيَوۡمَ عَلَيۡكَ حَسِيبٗا ١٤

14. «መጽሐፍህን አንብብ፡፡ ዛሬ ባንተ ላይ ተቆጣጣሪነት በነፍስህ በቃ» (ይባላል)፡፡

15. የተመራ ሰው የሚመራው ለራሱ ብቻ ነው፡፡ የተሳሳተም ሰው የሚሳሳተው (ጉዳቱ) በእርሷ ላይ ነው፡፡ ተሸካሚም (ነፍስ) የሌላይቱን ኃጢአት አትሸከምም፡፡ መልዕክተኛንም እስከምንልክ ድረስ የምንቀጣ አይደለንም፡፡

مَّنِ ٱهۡتَدَىٰ فَإِنَّمَا يَهۡتَدِي لِنَفۡسِهِۦۖ وَمَن ضَلَّ فَإِنَّمَا يَضِلُّ عَلَيۡهَاۚ وَلَا تَزِرُ وَازِرَةٞ وِزۡرَ أُخۡرَىٰۗ وَمَا كُنَّا مُعَذِّبِينَ حَتَّىٰ نَبۡعَثَ رَسُولٗا ١٥

16. ከተማንም ለማጥፋት በፈለግን ጊዜ ባለ ጸጋዎችዋን እናዛለን፡፡ በውስጧም ያምጻሉ፡፡ በእርሷም ላይ ቃሉ (ቅጣቱ) ይፈጸምባታል፡፡ ማጥፋትንም እናጠፋታለን፡፡

وَإِذَآ أَرَدۡنَآ أَن نُّهۡلِكَ قَرۡيَةً أَمَرۡنَا مُتۡرَفِيهَا فَفَسَقُواْ فِيهَا فَحَقَّ عَلَيۡهَا ٱلۡقَوۡلُ فَدَمَّرۡنَٰهَا تَدۡمِيرٗا ١٦

17. ከኑሕም በኋላ ከክፍለ ዘመናት ሰዎች ያጠፋናቸው ብዙዎች ናቸው፡፡ የባሮቹንም ኃጢአቶች ውስጠ ዐዋቂ ተመልካች መኾን በጌታህ በቃ፡፡

وَكَمۡ أَهۡلَكۡنَا مِنَ ٱلۡقُرُونِ مِنۢ بَعۡدِ نُوحٖۗ وَكَفَىٰ بِرَبِّكَ بِذُنُوبِ عِبَادِهِۦ خَبِيرَۢا بَصِيرٗا ١٧

18. ቸኳይቱን ዓለም (በሥራው) የሚፈልግ ሰው ለእርሱ በርሷ ውስጥ የሻነውን (ጸጋ) ለምንሻው ሰው እናስቸኩልለታለን፡፡ ከዚያም ለእርሱ ገሀነምን (መኖሪያ) አድርገንለታል፡፡ ተወቃሽ ብራሪ ኾኖ ይገባታል፡፡

مَّن كَانَ يُرِيدُ ٱلۡعَاجِلَةَ عَجَّلۡنَا لَهُۥ فِيهَا مَا نَشَآءُ لِمَن نُّرِيدُ ثُمَّ جَعَلۡنَا لَهُۥ جَهَنَّمَ يَصۡلَىٰهَا مَذۡمُومٗا مَّدۡحُورٗا ١٨

19. መጨረሻይቱንም ዓለም የፈለገ ሰው እርሱ አማኝ ኾኖ ለርሷ (ተገቢ) ሥራዋን የሠራም ሰው እነዚህ ሥራቸው የተመሰገነ ይኾናል፡፡

وَمَنۡ أَرَادَ ٱلۡأٓخِرَةَ وَسَعَىٰ لَهَا سَعۡيَهَا وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَأُوْلَٰٓئِكَ كَانَ سَعۡيُهُم مَّشۡكُورٗا ١٩

20. ሁሉንም እነዚህንና እነዚያን ከጌታህ ስጦታ (በዚህ ዓለም) እንጨምርላቸዋለን፡፡ የጌታህም ስጦታ (በዚች ዓለም) ክልክል አይደለም፡፡

كُلّٗا نُّمِدُّ هَٰٓؤُلَآءِ وَهَٰٓؤُلَآءِ مِنۡ عَطَآءِ رَبِّكَۚ وَمَا كَانَ عَطَآءُ رَبِّكَ مَحۡظُورًا ٢٠

21. ከፊላቸውን በከፊሉ ላይ እንዴት እንዳበለጥን ተመልከት፡፡ የመጨረሻያቱም አገር በማዕረጎች በጣም የከበረችና በመብለጥም የተለቀች ናት፡፡

ٱنظُرۡ كَيۡفَ فَضَّلۡنَا بَعۡضَهُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖۚ وَلَلۡأٓخِرَةُ أَكۡبَرُ دَرَجَٰتٖ وَأَكۡبَرُ تَفۡضِيلٗا ٢١

22. ከአላህ ጋር ሌላን አምላክ አታድርግ የተወቀሰክ ረዳት የሌለህ ትኾናለህና፤

لَّا تَجۡعَلۡ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ فَتَقۡعُدَ مَذۡمُومٗا مَّخۡذُولٗا ٢٢

23. ጌታህም (እንዲህ ሲል) አዘዘ፡- እርሱን እንጂ ሌላን አትገዙ፡፡ በወላጆቻችሁም መልካምን ሥሩ፡፡ በአንተ ዘንድ ኾነው አንዳቸው ወይም ሁለታቸው እርጅናን ቢደርሱ ፎህ አትበላቸው፡፡ አትገላምጣቸውም፡፡ ለእነርሱም መልካምን ቃል ተናገራቸው፡፡

۞وَقَضَىٰ رَبُّكَ أَلَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّآ إِيَّاهُ وَبِٱلۡوَٰلِدَيۡنِ إِحۡسَٰنًاۚ إِمَّا يَبۡلُغَنَّ عِندَكَ ٱلۡكِبَرَ أَحَدُهُمَآ أَوۡ كِلَاهُمَا فَلَا تَقُل لَّهُمَآ أُفّٖ وَلَا تَنۡهَرۡهُمَا وَقُل لَّهُمَا قَوۡلٗا كَرِيمٗا ٢٣

24. ለሁለቱም ከእዝነትህ የመዋረድን ክንፍ ዝቅ አድርግላቸው፡፡ «ጌታዬ ሆይ! በሕፃንነቴ (በርኅራኄ) እንዳሳደጉኝ እዘንልላቸውም» በል፡፡

وَٱخۡفِضۡ لَهُمَا جَنَاحَ ٱلذُّلِّ مِنَ ٱلرَّحۡمَةِ وَقُل رَّبِّ ٱرۡحَمۡهُمَا كَمَا رَبَّيَانِي صَغِيرٗا ٢٤

25. ጌታችሁ በነፍሶቻችሁ ውስጥ ያለውን ሁሉ አዋቂ ነው:: ታዛዦችም ብትኾኑ (በመሳሳትም ብታጠፉ) እርሱ ለተመላሾች መሓሪ ነው::

رَّبُّكُمۡ أَعۡلَمُ بِمَا فِي نُفُوسِكُمۡۚ إِن تَكُونُواْ صَٰلِحِينَ فَإِنَّهُۥ كَانَ لِلۡأَوَّٰبِينَ غَفُورٗا ٢٥

26. ለዝምድና ባለቤትም መብቱን ስጥ:: ለምስኪንና ለመንገደኛም (ስጥ):: ማባከንንም አታባክን::

وَءَاتِ ذَا ٱلۡقُرۡبَىٰ حَقَّهُۥ وَٱلۡمِسۡكِينَ وَٱبۡنَ ٱلسَّبِيلِ وَلَا تُبَذِّرۡ تَبۡذِيرًا ٢٦

27. አባካኞች የሰይጣናት ወንድሞች ናቸውና:: ሰይጣንም ለጌታው ብርቱ ከሓዲ ነው::

إِنَّ ٱلۡمُبَذِّرِينَ كَانُوٓاْ إِخۡوَٰنَ ٱلشَّيَٰطِينِۖ وَكَانَ ٱلشَّيۡطَٰنُ لِرَبِّهِۦ كَفُورٗا ٢٧

28. ከጌታህም የምትከጅላትን ጸጋ ለማጣት ከእነርሱ ብትዞር ለእነሱ ልዝብን ቃል ተናገራቸው::

وَإِمَّا تُعۡرِضَنَّ عَنۡهُمُ ٱبۡتِغَآءَ رَحۡمَةٖ مِّن رَّبِّكَ تَرۡجُوهَا فَقُل لَّهُمۡ قَوۡلٗا مَّيۡسُورٗا ٢٨

29. እጅህንም ወደ አንገትህ የታሰረች አታድርግ:: መዘርጋትንም ሁሉ አትዘርጋት፤ የተወቀስክ የተቆጨኽ ትኾናለህና::

وَلَا تَجۡعَلۡ يَدَكَ مَغۡلُولَةً إِلَىٰ عُنُقِكَ وَلَا تَبۡسُطۡهَا كُلَّ ٱلۡبَسۡطِ فَتَقۡعُدَ مَلُومٗا مَّحۡسُورًا ٢٩

30. ጌታህ ሲሳይን ለሚሻው ሰው ያሰፋል፤ ያጠባልም:: እርሱ በባሮቹ ኹኔታ ውስጠ ዐዋቂ ተመልካች ነውና::

إِنَّ رَبَّكَ يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقۡدِرُۚ إِنَّهُۥ كَانَ بِعِبَادِهِۦ خَبِيرَۢا بَصِيرٗا ٣٠

31. ልጆቻችሁንም ድኽነትን ለመፍራት አትግደሉ:: እኛ እንመግባቸዋለን:: እናንተንም (እንመግባለን):: እነርሱን መግደል ታላቅ ኃጢኣት ነውና::

وَلَا تَقۡتُلُوٓاْ أَوۡلَٰدَكُمۡ خَشۡيَةَ إِمۡلَٰقٖۖ نَّحۡنُ نَرۡزُقُهُمۡ وَإِيَّاكُمۡۚ إِنَّ قَتۡلَهُمۡ كَانَ خِطۡـٔٗا كَبِيرٗا ٣١

32. ዝሙትንም አትቅረቡ:: እርሱ በእርግጥ መጥፎ ሥራ ነውና:: መንገድነቱም ከፋ!

وَلَا تَقۡرَبُواْ ٱلزِّنَىٰٓۖ إِنَّهُۥ كَانَ فَٰحِشَةٗ وَسَآءَ سَبِيلٗا ٣٢

33. ያቺንም አላህ ያወገዘትን ነፍስ ያለ ሕግ አትግደሉ:: የተበደለም ኾኖ የተገደለ ሰው ለዘመዱ (በገዳዩ ላይ) በእርግጥ ስልጣንን አድርገናል:: በመግደልም ወሰንን አይለፍ፤ እርሱ የተረዳ ነውና::

وَلَا تَقۡتُلُواْ ٱلنَّفۡسَ ٱلَّتِي حَرَّمَ ٱللَّهُ إِلَّا بِٱلۡحَقِّۗ وَمَن قُتِلَ مَظۡلُومٗا فَقَدۡ جَعَلۡنَا لِوَلِيِّهِۦ سُلۡطَٰنٗا فَلَا يُسۡرِف فِّي ٱلۡقَتۡلِۖ إِنَّهُۥ كَانَ مَنصُورٗا ٣٣

34. የየቲምንም ገንዘብ የብርታቱን ጊዜ እስኪደርስ ድረስ በዚያች እርሷ መልካም በኾነች ኹኔታ እንጂ አትቅረቡ:: በኪዳናችሁም ሙሉ:: ኪዳን የሚጠየቁበት ነውና::

وَلَا تَقۡرَبُواْ مَالَ ٱلۡيَتِيمِ إِلَّا بِٱلَّتِي هِيَ أَحۡسَنُ حَتَّىٰ يَبۡلُغَ أَشُدَّهُۥۚ وَأَوۡفُواْ بِٱلۡعَهۡدِۖ إِنَّ ٱلۡعَهۡدَ كَانَ مَسۡـُٔولٗا ٣٤

35. በሰፈራችሁም ጊዜ ስፍርን ሙሉ:: በትክክለኛው ሚዛንም መዝኑ:: ይህ መልካም ነገር ነው:: መጨረሻውም ያማረ ነው::

وَأَوۡفُواْ ٱلۡكَيۡلَ إِذَا كِلۡتُمۡ وَزِنُواْ بِٱلۡقِسۡطَاسِ ٱلۡمُسۡتَقِيمِۚ ذَٰلِكَ خَيۡرٞ وَأَحۡسَنُ تَأۡوِيلٗا ٣٥

36. ለአንተም በርሱ ዕውቀት የሌለህን ነገር አትከተል፡፡ መስሚያ፣ ማያም፣ ልብም እነዚህ ሁሉ (ባለቤታቸው) ከእነሱ ተጠያቂ ነውና፡፡

وَلَا تَقۡفُ مَا لَيۡسَ لَكَ بِهِۦ عِلۡمٌۚ إِنَّ ٱلسَّمۡعَ وَٱلۡبَصَرَ وَٱلۡفُؤَادَ كُلُّ أُوْلَٰٓئِكَ كَانَ عَنۡهُ مَسۡـُٔولٗا ٣٦

37. በምድርም ላይ የተንበጣረረክ ሆነህ፤ አትሂድ፡፡ አንተ ፈጽሞ ምድርን አትሰረጉድምና በርዝመትም ፈጽሞ ጋራዎችን አትደርስምና፡፡

وَلَا تَمۡشِ فِي ٱلۡأَرۡضِ مَرَحًاۖ إِنَّكَ لَن تَخۡرِقَ ٱلۡأَرۡضَ وَلَن تَبۡلُغَ ٱلۡجِبَالَ طُولٗا ٣٧

38. ይህ ሁሉ መጥፎው (አሥራ ሁለቱ ክልክሎች) እጌታህ ዘንድ የተጠላ ነው፡፡

كُلُّ ذَٰلِكَ كَانَ سَيِّئُهُۥ عِندَ رَبِّكَ مَكۡرُوهٗا ٣٨

39. ይህ ጌታህ ከጥበቡ ወደ አንተ ካወረደው ነገር ነው፡፡ ከአላህም ጋር ሌላን አምላክ አታድርግ የተወቀስክ የተባረርክ ኾነህ በገሀነም ውስጥ ትጣላለህና፡፡

ذَٰلِكَ مِمَّآ أَوۡحَىٰٓ إِلَيۡكَ رَبُّكَ مِنَ ٱلۡحِكۡمَةِۗ وَلَا تَجۡعَلۡ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ فَتُلۡقَىٰ فِي جَهَنَّمَ مَلُومٗا مَّدۡحُورًا ٣٩

40. ጌታችሁ በወንዶች ልጆች መረጣችሁና ከመላእክት ሴቶችን (ልጆች) ያዘን እናንተ ከባድን ቃል በእርግጥ ትናገራላችሁ፡፡

أَفَأَصۡفَىٰكُمۡ رَبُّكُم بِٱلۡبَنِينَ وَٱتَّخَذَ مِنَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ إِنَٰثًاۚ إِنَّكُمۡ لَتَقُولُونَ قَوۡلًا عَظِيمٗا ٤٠

41. ይገሰጹም ዘንድ በዚህ ቁርኣን ውስጥ ደጋግመን በእርግጥ ገለጽን፡፡ መበርገግንም እንጂ ሌላን አይጨምርላቸውም፡፡

وَلَقَدۡ صَرَّفۡنَا فِي هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ لِيَذَّكَّرُواْ وَمَا يَزِيدُهُمۡ إِلَّا نُفُورٗا ٤١

42. (ሙሐመድ ሆይ) በላቸው «እንደምትሉት ከእርሱ ጋር አማልክት በነበሩ ኖሮ ያን ጊዜ ወደ ዐርሹ ባለቤት መንገድን በፈለጉ ነበር፡፡»

قُل لَّوۡ كَانَ مَعَهُۥٓ ءَالِهَةٞ كَمَا يَقُولُونَ إِذٗا لَّٱبۡتَغَوۡاْ إِلَىٰ ذِي ٱلۡعَرۡشِ سَبِيلٗا ٤٢

43. ጥራት ይገባው፡፡ ከሚሉትም ነገር ሁሉ ከፍ ያለን ልቅና ላቀ፡፡

سُبۡحَٰنَهُۥ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يَقُولُونَ عُلُوّٗا كَبِيرٗا ٤٣

44. ሰባቱ ሰማያትና ምድርም በውስጣቸውም ያለው ሁሉ ለእርሱ ያጠራሉ፡፡ ከነገርም ሁሉ ከማመስገን ጋር የሚያጠራው እንጂ አንድም የለም፡፡ ግን ማጥራታቸውን አታውቁትም፡፡ እርሱ ታጋሽ መሓሪ ነው፡፡

تُسَبِّحُ لَهُ ٱلسَّمَٰوَٰتُ ٱلسَّبۡعُ وَٱلۡأَرۡضُ وَمَن فِيهِنَّۚ وَإِن مِّن شَيۡءٍ إِلَّا يُسَبِّحُ بِحَمۡدِهِۦ وَلَٰكِن لَّا تَفۡقَهُونَ تَسۡبِيحَهُمۡۚ إِنَّهُۥ كَانَ حَلِيمًا غَفُورٗا ٤٤

45. ቁርኣንንም ባነበብክ ጊዜ ባንተና በእነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም በማያምኑት ሰዎች መካከል የሚሸሽግን ግርዶሽ አድርገናል፡፡

وَإِذَا قَرَأۡتَ ٱلۡقُرۡءَانَ جَعَلۡنَا بَيۡنَكَ وَبَيۡنَ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ حِجَابٗا مَّسۡتُورٗا ٤٥

46. እንዳያውቁትም በልቦቻቸው ላይ ሽፋንን በጆሮቻቸውም ውስጥ ድንቁርናን አደረግን፡፡ ጌታህንም ብቻውን ኾኖ በቁርኣን ባወሳኸው ጊዜ የሚሸሹ ኾነው በጀርባዎቻቸው ላይ ይዞራሉ፡፡

وَجَعَلۡنَا عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ أَكِنَّةً أَن يَفۡقَهُوهُ وَفِيٓ ءَاذَانِهِمۡ وَقۡرٗاۚ وَإِذَا ذَكَرۡتَ رَبَّكَ فِي ٱلۡقُرۡءَانِ وَحۡدَهُۥ وَلَّوۡاْ عَلَىٰٓ أَدۡبَٰرِهِمۡ نُفُورٗا ٤٦

47. እኛ ወደ አንተ በሚያዳምጡ ጊዜ እነሱም በሚንሾካሾኩ ጊዜ በዳዮች (እርስ በርሳቸው) የተደገመበትን ሰው እንጂ አትከተሉም በሚሉ ጊዜ በእርሱ የሚያዳምጡበትን ምክንያት ዐዋቂ ነን፡፡

نَّحۡنُ أَعۡلَمُ بِمَا يَسۡتَمِعُونَ بِهِۦٓ إِذۡ يَسۡتَمِعُونَ إِلَيۡكَ وَإِذۡ هُمۡ نَجۡوَىٰٓ إِذۡ يَقُولُ ٱلظَّٰلِمُونَ إِن تَتَّبِعُونَ إِلَّا رَجُلٗا مَّسۡحُورًا ٤٧

48. ምሳሌዎችን ለአንተ እንዴት እንዳደረጉልህና እንደ ተሳሳቱ ተመልከት፡፡ (ወደ እውነቱ ለመድረስ) መንገድንም አይችሉም፡፡

ٱنظُرۡ كَيۡفَ ضَرَبُواْ لَكَ ٱلۡأَمۡثَالَ فَضَلُّواْ فَلَا يَسۡتَطِيعُونَ سَبِيلٗا ٤٨

49. አሉም «እንዴት አጥንቶችና ብስብሶች በኾን ጊዜ እኛ አዲስ ፍጥረት ኾነን በእርግጥ ተቀስቃሾች ነን»

وَقَالُوٓاْ أَءِذَا كُنَّا عِظَٰمٗا وَرُفَٰتًا أَءِنَّا لَمَبۡعُوثُونَ خَلۡقٗا جَدِيدٗا ٤٩

50. በላቸው «ድንጋዮችን ወይም ብረትን ሁኑ»

۞قُلۡ كُونُواْ حِجَارَةً أَوۡ حَدِيدًا ٥٠

51. «ወይም በልቦቻችሁ ውስጥ የሚተልቅን ፍጥረት (ኹኑ መቀስቀሳችሁ አይቀርም)፡፡» «የሚመልሰንም ማነው» ይላሉ፡፡ ያ በመጀመሪያ ጊዜ የፈጠራችሁ ነው» በላቸው፡፡ ወደ አንተም ራሶቻቸውን ይነቀንቃሉ፡፡ «እርሱም መቼ ነው» ይላሉ፡፡ «(እርሱ) ቅርብ ሊኾነን ይቻላል በላቸው፡፡

أَوۡ خَلۡقٗا مِّمَّا يَكۡبُرُ فِي صُدُورِكُمۡۚ فَسَيَقُولُونَ مَن يُعِيدُنَاۖ قُلِ ٱلَّذِي فَطَرَكُمۡ أَوَّلَ مَرَّةٖۚ فَسَيُنۡغِضُونَ إِلَيۡكَ رُءُوسَهُمۡ وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هُوَۖ قُلۡ عَسَىٰٓ أَن يَكُونَ قَرِيبٗا ٥١

52. (እርሱም) የሚጠራችሁና (አላህን) አመስጋኞቹ ኾናችሁ ጥሪውን የምትቀበሉበት ጥቂትንም (ቀኖች) እንጂ ያልቆያችሁ መኾናችሁን የምትጠራጠሩበት ቀን ነው፤ (በላቸው)፡፡

يَوۡمَ يَدۡعُوكُمۡ فَتَسۡتَجِيبُونَ بِحَمۡدِهِۦ وَتَظُنُّونَ إِن لَّبِثۡتُمۡ إِلَّا قَلِيلٗا ٥٢

53. ለባሮቼም በላቸው፡- ያችን እርሷ መልካም የኾነችውን (ቃል) ይናገሩ፡፡ ሰይጣን በመካከላቸው ያበላሻልና፡፡ ሰይጣን ለሰው ግልጽ ጠላት ነውና፡፡

وَقُل لِّعِبَادِي يَقُولُواْ ٱلَّتِي هِيَ أَحۡسَنُۚ إِنَّ ٱلشَّيۡطَٰنَ يَنزَغُ بَيۡنَهُمۡۚ إِنَّ ٱلشَّيۡطَٰنَ كَانَ لِلۡإِنسَٰنِ عَدُوّٗا مُّبِينٗا ٥٣

54. ጌታችሁ በእናንተ (ኹኔታ) ዐዋቂ ነው፡፡ ቢሻ ያዝንላችኋል፤ ወይም ቢሻ ይቀጣችኋል፡፡ በእነሱም ላይ ኃላፊ ኾነህ አላክንህም፡፡ (አታስገድዳቸውም)፡፡

رَّبُّكُمۡ أَعۡلَمُ بِكُمۡۖ إِن يَشَأۡ يَرۡحَمۡكُمۡ أَوۡ إِن يَشَأۡ يُعَذِّبۡكُمۡۚ وَمَآ أَرۡسَلۡنَٰكَ عَلَيۡهِمۡ وَكِيلٗا ٥٤

55. ጌታህም በሰማያትና በምድር ያለውን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡ ከፊሉንም ነቢያት በከፊሉ ላይ በእርግጥ አብልጠናል፡፡ ዳውድንም ዘቡርን ሰጥተነዋል፡፡

وَرَبُّكَ أَعۡلَمُ بِمَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۗ وَلَقَدۡ فَضَّلۡنَا بَعۡضَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ عَلَىٰ بَعۡضٖۖ وَءَاتَيۡنَا دَاوُۥدَ زَبُورٗا ٥٥

56. «እነዚያን ከእርሱ ሌላ (አማልክት) የምትሏቸውን ጥሩ፡፡ ከእናንተም ላይ ጉዳትን ማስወገድን (ወደ ሌላ) ማዞርንም አይችሉም» በላቸው፡፤

قُلِ ٱدۡعُواْ ٱلَّذِينَ زَعَمۡتُم مِّن دُونِهِۦ فَلَا يَمۡلِكُونَ كَشۡفَ ٱلضُّرِّ عَنكُمۡ وَلَا تَحۡوِيلًا ٥٦

57. እነዚያ እነርሱ የሚግገዟቸው ማንኛቸውም (ወደ አላህ) በጣም ቀራቢያቸው ወደ ጌታቸው መቃረቢያን (ሥራ) ይፈልጋሉ፡፡ እዝነቱንም ይከጅላሉ፡፡ ቅጣቱንም ይፈራሉ፡፡ የጌታህ ቅጣት የሚፈራ ነውና፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ يَبۡتَغُونَ إِلَىٰ رَبِّهِمُ ٱلۡوَسِيلَةَ أَيُّهُمۡ أَقۡرَبُ وَيَرۡجُونَ رَحۡمَتَهُۥ وَيَخَافُونَ عَذَابَهُۥٓۚ إِنَّ عَذَابَ رَبِّكَ كَانَ مَحۡذُورٗا ٥٧

58. አንዲትም ከተማ የለችም እኛ ከትንሣኤ ቀን በፊት አጥፊዎችዋ ወይም ብርቱን ቅጣት ቀጪዎችዋ ብንኾን እንጂ፡፡ ይህ በመጽሐፉ የተጻፈ ነው፡፡

وَإِن مِّن قَرۡيَةٍ إِلَّا نَحۡنُ مُهۡلِكُوهَا قَبۡلَ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ أَوۡ مُعَذِّبُوهَا عَذَابٗا شَدِيدٗاۚ كَانَ ذَٰلِكَ فِي ٱلۡكِتَٰبِ مَسۡطُورٗا ٥٨

59. ታምራቶችንም ከመላክ የቀድሞዎቹ ሰዎች በእርሷ ማስተባበልና (መጥፋት) እንጂ ሌላ አልከለከለንም፡፡ ለሰሙድም ግመልን ግልጽ ተዓምር ኾና ሰጠናቸው፡፡ በእርሷም በደሉ፡፡ ተዓምራቶችንም ለማስፈራራት እንጂ አንንልከም፡፡

وَمَا مَنَعَنَآ أَن نُّرۡسِلَ بِٱلۡأٓيَٰتِ إِلَّآ أَن كَذَّبَ بِهَا ٱلۡأَوَّلُونَۚ وَءَاتَيۡنَا ثَمُودَ ٱلنَّاقَةَ مُبۡصِرَةٗ فَظَلَمُواْ بِهَاۚ وَمَا نُرۡسِلُ بِٱلۡأٓيَٰتِ إِلَّا تَخۡوِيفٗا ٥٩

60. ላንተም ጌታህ (ዕውቀቱ) በሰዎቹ ከበበ ባልንህ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ያችንም (በሌሊቱ ጉዞ በዓይንህ) ያሳየንህን ትርዕይት ለሰዎች ፈተና እንጂ አላደረግናትም፡፡ በቁርአንም የተረገመችውን ዛፍ (እንደዚሁ ፈተና እንጂ አላደረግንም)፡፡ እናስፈራራቸዋለንም፤ ታላቅንም ጥመት እንጂ አይጨምርላቸውም፡፡

وَإِذۡ قُلۡنَا لَكَ إِنَّ رَبَّكَ أَحَاطَ بِٱلنَّاسِۚ وَمَا جَعَلۡنَا ٱلرُّءۡيَا ٱلَّتِيٓ أَرَيۡنَٰكَ إِلَّا فِتۡنَةٗ لِّلنَّاسِ وَٱلشَّجَرَةَ ٱلۡمَلۡعُونَةَ فِي ٱلۡقُرۡءَانِۚ وَنُخَوِّفُهُمۡ فَمَا يَزِيدُهُمۡ إِلَّا طُغۡيَٰنٗا كَبِيرٗا ٦٠

61. ለመላእክትም ለአደም ስገዱ ባልናቸው ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ወዲያውም ሰገዱ፤ ኢብሊስ ብቻ ሲቀር፡፡ «ከጭቃ ለፈጠርከው ሰው እሰግዳለሁን» አለ፡፡

وَإِذۡ قُلۡنَا لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ ٱسۡجُدُواْ لِأٓدَمَ فَسَجَدُوٓاْ إِلَّآ إِبۡلِيسَ قَالَ ءَأَسۡجُدُ لِمَنۡ خَلَقۡتَ طِينٗا ٦١

62. «ንገረኝ ይህ ያ በእኔ ላይ ያበለጥከው ነውን እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ ብታቆየኝ ዘሮቹን ጥቂቶች ሲቀሩ ወደ ስህተት በእርግጥ እስባቸዋለሁ» አለ፡፡

قَالَ أَرَءَيۡتَكَ هَٰذَا ٱلَّذِي كَرَّمۡتَ عَلَيَّ لَئِنۡ أَخَّرۡتَنِ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ لَأَحۡتَنِكَنَّ ذُرِّيَّتَهُۥٓ إِلَّا قَلِيلٗا ٦٢

63. (አላህም) አለው «ኺድ፤ ከእነሱም የተከተለህ ገሀነም የተሟላች ቅጣት ስትኾን ፍዳችሁ ናት፡፡

قَالَ ٱذۡهَبۡ فَمَن تَبِعَكَ مِنۡهُمۡ فَإِنَّ جَهَنَّمَ جَزَآؤُكُمۡ جَزَآءٗ مَّوۡفُورٗا ٦٣

64. «ከእነሱ የቻልከውንም ሰው በድምጽህ አታል፡፡ በእነሱም ላይ በፈረሰኞችህ፣ በእግረኞችህም ኾነህ ለልብ፡፡ በገንዘቦቻቸውም፣ በልጆቻቸውም ተጋራቸው፣ ተስፋ ቃልም ግባላቸው፡፡ ሰይጣንም ማታለልን እንጂ ተስፋ ቃልን አይገባላቸውም፡፡

وَٱسۡتَفۡزِزۡ مَنِ ٱسۡتَطَعۡتَ مِنۡهُم بِصَوۡتِكَ وَأَجۡلِبۡ عَلَيۡهِم بِخَيۡلِكَ وَرَجِلِكَ وَشَارِكۡهُمۡ فِي ٱلۡأَمۡوَٰلِ وَٱلۡأَوۡلَٰدِ وَعِدۡهُمۡۚ وَمَا يَعِدُهُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ إِلَّا غُرُورًا ٦٤

65. «ባሮቼ በእነሱ ላይ ፈጽሞ ላንተ ስልጣን የለህም፡፡ መጠጊያም በጌታህ በቃ፡፡»

إِنَّ عِبَادِي لَيۡسَ لَكَ عَلَيۡهِمۡ سُلۡطَٰنٞۚ وَكَفَىٰ بِرَبِّكَ وَكِيلٗا ٦٥

66. ጌታችሁ ያ ከችሮታው ትፈልጉ ዘንድ መርከቦችን በባሕር ላይ ለእናንተ የሚነዳላችሁ ነው፡፡ እነሆ እርሱ ለናንተ አዛኝ ነውና፡፡

رَّبُّكُمُ ٱلَّذِي يُزۡجِي لَكُمُ ٱلۡفُلۡكَ فِي ٱلۡبَحۡرِ لِتَبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِهِۦٓۚ إِنَّهُۥ كَانَ بِكُمۡ رَحِيمٗا ٦٦

67. በባሕሩም ውስጥ ጉዳት ባገኛችሁ ጊዜ የምትጠሩዋቸው (አማልክት) ሁሉ ከእርሱ (ከአላህ) በቀር ይጠፋሉ፡፡ ወደ የብስም በማድረስ ባዳናችሁ ጊዜ (እምነትን) ትተዋላችሁ፡፡ ሰውም በጣም ከሓዲ ነው፡፡

وَإِذَا مَسَّكُمُ ٱلضُّرُّ فِي ٱلۡبَحۡرِ ضَلَّ مَن تَدۡعُونَ إِلَّآ إِيَّاهُۖ فَلَمَّا نَجَّىٰكُمۡ إِلَى ٱلۡبَرِّ أَعۡرَضۡتُمۡۚ وَكَانَ ٱلۡإِنسَٰنُ كَفُورًا ٦٧

68. የየብሱን በኩል (ምድርን) በእናንተ መገልበጡን ወይም ጠጠርን የያዘ ንፋስን በእናንተ ላይ መላኩን ከዚያም ለእናንተ ጠባቂ አለማግኘታችሁን አትፈሩምን

أَفَأَمِنتُمۡ أَن يَخۡسِفَ بِكُمۡ جَانِبَ ٱلۡبَرِّ أَوۡ يُرۡسِلَ عَلَيۡكُمۡ حَاصِبٗا ثُمَّ لَا تَجِدُواْ لَكُمۡ وَكِيلًا ٦٨

69. ወይስ ሌላ ጊዜ ወደ እርሱ (ወደ ባሕር) የሚመልሳችሁ ወዲያውም በእናንተ ላይ ብርቱን ነፋስ የሚልክ በክሕደታችሁም ምክንያት የሚያሰጥማችሁ መኾኑን ከዚያም በኛ ላይ በእርሱ ተከታይን (ረዳትን) ለእናንተ የማታገኙ መኾናችሁን አትፈሩምን

أَمۡ أَمِنتُمۡ أَن يُعِيدَكُمۡ فِيهِ تَارَةً أُخۡرَىٰ فَيُرۡسِلَ عَلَيۡكُمۡ قَاصِفٗا مِّنَ ٱلرِّيحِ فَيُغۡرِقَكُم بِمَا كَفَرۡتُمۡ ثُمَّ لَا تَجِدُواْ لَكُمۡ عَلَيۡنَا بِهِۦ تَبِيعٗا ٦٩

70. የአደምንም ልጆች በእርግጥ (ከሌላው ፍጡር) አከበርናቸው፡፡ በየብስና በባህርም አሳፈርናቸው፡፡ ከመልካሞችም (ሲሳዮች) ሰጠናቸው፡፡ ከፈጠርናቸውም ፍጡሮች በብዙዎቹ ላይ ማብለጥን አበለጥናቸው፡፡

۞وَلَقَدۡ كَرَّمۡنَا بَنِيٓ ءَادَمَ وَحَمَلۡنَٰهُمۡ فِي ٱلۡبَرِّ وَٱلۡبَحۡرِ وَرَزَقۡنَٰهُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ وَفَضَّلۡنَٰهُمۡ عَلَىٰ كَثِيرٖ مِّمَّنۡ خَلَقۡنَا تَفۡضِيلٗا ٧٠

71. ሰዎችን ሁሉ በመሪያቸው የምንጠራበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ መጽሐፉንም በቀኙ የተሰጠ ሰው እነዚያ መጽሐፋቸውን ያነባሉ፡፡ በተምር ፍሬ ስንጥቅ ላይ ያለውን ክር ያክል እንኳ አይበደሉም፡፡

يَوۡمَ نَدۡعُواْ كُلَّ أُنَاسِۭ بِإِمَٰمِهِمۡۖ فَمَنۡ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ بِيَمِينِهِۦ فَأُوْلَٰٓئِكَ يَقۡرَءُونَ كِتَٰبَهُمۡ وَلَا يُظۡلَمُونَ فَتِيلٗا ٧١

72. በዚህችም ዓለም (ልበ) ዕውር የኾነ ሰው እርሱ በመጨረሻይቱም (ዓለም) ይበልጥ ዕውር ነው፡፡ መንገድንም በጣም የተሳሳተ ነው፡፤

وَمَن كَانَ فِي هَٰذِهِۦٓ أَعۡمَىٰ فَهُوَ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ أَعۡمَىٰ وَأَضَلُّ سَبِيلٗا ٧٢

73. እነሆ ከዚያም ወደ አንተ ካወረድነው ሌላን በእኛ ላይ ትዋሽ ዘንድ ሊፈትኑህ በእርግጥ ተቃረቡ፡፡ ያን ጊዜም ወዳጅ አድርገው በያዙህ ነበር፡፡

وَإِن كَادُواْ لَيَفۡتِنُونَكَ عَنِ ٱلَّذِيٓ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ لِتَفۡتَرِيَ عَلَيۡنَا غَيۡرَهُۥۖ وَإِذٗا لَّٱتَّخَذُوكَ خَلِيلٗا ٧٣

74. ባላረጋንህም ኖሮ ወደነሱ ጥቂትን (ዝንባሌ) ልትዘነበል በእርግጥ በተቃረብክ ነበር፡፡

وَلَوۡلَآ أَن ثَبَّتۡنَٰكَ لَقَدۡ كِدتَّ تَرۡكَنُ إِلَيۡهِمۡ شَيۡـٔٗا قَلِيلًا ٧٤

75. ያን ጊዜ የሕይወትን ድርብ (ቅጣት) የሞትንም ድርብ (ቅጣት) ባቀመስንህ ነበር፡፡ ከዚያም ላንተ በኛ ላይ ረዳትን አታገኝም ነበር፡፡

إِذٗا لَّأَذَقۡنَٰكَ ضِعۡفَ ٱلۡحَيَوٰةِ وَضِعۡفَ ٱلۡمَمَاتِ ثُمَّ لَا تَجِدُ لَكَ عَلَيۡنَا نَصِيرٗا ٧٥

76. ከምድሪቱም (ከዓረብ ምድር) ከርሷ ያወጡህ ዘንድ ሊያሸብሩህ በእርግጥ ተቃረቡ፡፡ ያን ጊዜም ከአንተ በኋላ ጥቂትን ጊዜ እንጂ አይቆዩም ነበር፡፡

وَإِن كَادُواْ لَيَسۡتَفِزُّونَكَ مِنَ ٱلۡأَرۡضِ لِيُخۡرِجُوكَ مِنۡهَاۖ وَإِذٗا لَّا يَلۡبَثُونَ خِلَٰفَكَ إِلَّا قَلِيلٗا ٧٦

77. ከመልክተኞቻችን ካንተ በፊት በእርግጥ እንደላክናቸው ሰዎች ልማድ ብጤ (ይጠፉ ነበር)፡፡ ለልማዳችንም መለወጥን አታገኝም፡፡

سُنَّةَ مَن قَدۡ أَرۡسَلۡنَا قَبۡلَكَ مِن رُّسُلِنَاۖ وَلَا تَجِدُ لِسُنَّتِنَا تَحۡوِيلًا ٧٧

78. ሶላትን ከፀሐይ መዘንበል እስከ ሌሊት ጨለማ ድረስ ስገድ፡፡ የጎህንም ሶላት ስገድ፡፡ የጎህ ሶላት (መላእክት) የሚጣዱት ነውና፡፡

أَقِمِ ٱلصَّلَوٰةَ لِدُلُوكِ ٱلشَّمۡسِ إِلَىٰ غَسَقِ ٱلَّيۡلِ وَقُرۡءَانَ ٱلۡفَجۡرِۖ إِنَّ قُرۡءَانَ ٱلۡفَجۡرِ كَانَ مَشۡهُودٗا ٧٨

79. ከሌሊትም ላንተ ተጨማሪ የኾነችን ሶላት በእርሱ (በቁርኣን) ስገድ፡፡ ጌታህ ምስጉን በኾነ ስፍራ በእርግጥ ያቆምሃል፡፡

وَمِنَ ٱلَّيۡلِ فَتَهَجَّدۡ بِهِۦ نَافِلَةٗ لَّكَ عَسَىٰٓ أَن يَبۡعَثَكَ رَبُّكَ مَقَامٗا مَّحۡمُودٗا ٧٩

80. በልም ጌታዬ ሆይ! የተወደደን ማግባት አግባኝ፡፡ የተወደደንም ማውጣት አውጣኝ፡፡ ለእኔም ከአንተ ዘንድ የተረዳን ስልጣን አድርግልኝ፡፡

وَقُل رَّبِّ أَدۡخِلۡنِي مُدۡخَلَ صِدۡقٖ وَأَخۡرِجۡنِي مُخۡرَجَ صِدۡقٖ وَٱجۡعَل لِّي مِن لَّدُنكَ سُلۡطَٰنٗا نَّصِيرٗا ٨٠

81. በልም «እውነት መጣ ውሸትም ተወገደ፤ እነሆ ውሸት ተወጋጅ ነውና፡፡»

وَقُلۡ جَآءَ ٱلۡحَقُّ وَزَهَقَ ٱلۡبَٰطِلُۚ إِنَّ ٱلۡبَٰطِلَ كَانَ زَهُوقٗا ٨١

82. ከቁርኣንም ለምእመናን መድኀኒትና እዝነት የኾነን እናወርዳለን፡፡ በዳዮችንም ከሳራን እንጂ ሌላ አይጨምርላቸውም፡፡

وَنُنَزِّلُ مِنَ ٱلۡقُرۡءَانِ مَا هُوَ شِفَآءٞ وَرَحۡمَةٞ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ وَلَا يَزِيدُ ٱلظَّٰلِمِينَ إِلَّا خَسَارٗا ٨٢

83. በሰውም ላይ ጸጋችንን በለገስን ጊዜ (ከምስጋና) ይዞራል፡፡ ጎኑንም (ከእውነት) ያርቃል፡፡ ችግርም በነካው ጊዜ ተስፋ ቆራጭ ይኾናል፡፡

وَإِذَآ أَنۡعَمۡنَا عَلَى ٱلۡإِنسَٰنِ أَعۡرَضَ وَنَـَٔا بِجَانِبِهِۦ وَإِذَا مَسَّهُ ٱلشَّرُّ كَانَ يَـُٔوسٗا ٨٣

84. «ሁሉም በሚመስለው መንገዱ ላይ ይሠራል፡፡ ጌታችሁም እርሱ መንገዱ ቀጥተኛ የኾነውን ሰው ዐዋቂ ነው በላቸው፡፡

قُلۡ كُلّٞ يَعۡمَلُ عَلَىٰ شَاكِلَتِهِۦ فَرَبُّكُمۡ أَعۡلَمُ بِمَنۡ هُوَ أَهۡدَىٰ سَبِيلٗا ٨٤

85. ከሩሕም ይጠይቁሃል፡፡ «ሩሕ ከጌታዬ ነገር ነው ከዕውቀትም ጥቂትን እንጂ አልተሰጣችሁም» በላቸው፡
፡

وَيَسۡـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلرُّوحِۖ قُلِ ٱلرُّوحُ مِنۡ أَمۡرِ رَبِّي وَمَآ أُوتِيتُم مِّنَ ٱلۡعِلۡمِ إِلَّا قَلِيلٗا ٨٥

86. ብንሻም ያንን ወዳንተ ያወረድነውን በእርግጥ እናስወግዳለን፡፡ ከዚያም ላንተ በእኛ ላይ በርሱ (ለማስመለስ) ተያገርን አታገኝም፡፡

وَلَئِن شِئۡنَا لَنَذۡهَبَنَّ بِٱلَّذِيٓ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ ثُمَّ لَا تَجِدُ لَكَ بِهِۦ عَلَيۡنَا وَكِيلًا ٨٦

87. ግን ከጌታህ በኾነው እዝነት (ጠበቅነው)፡፡ ችሮታው ባንተ ላይ ታላቅ ነውና፡፤

إِلَّا رَحۡمَةٗ مِّن رَّبِّكَۚ إِنَّ فَضۡلَهُۥ كَانَ عَلَيۡكَ كَبِيرٗا ٨٧

88. «ሰዎችም ጋኔኖችም የዚህን ቁርኣን ብጤ በማምጣት ላይ ቢሰበሰቡ ከፊላቸው ለከፊሉ ረዳት ቢሆንም እንኳ ብጤውን አያመጡም» በላቸው፡፡

قُل لَّئِنِ ٱجۡتَمَعَتِ ٱلۡإِنسُ وَٱلۡجِنُّ عَلَىٰٓ أَن يَأۡتُواْ بِمِثۡلِ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ لَا يَأۡتُونَ بِمِثۡلِهِۦ وَلَوۡ كَانَ بَعۡضُهُمۡ لِبَعۡضٖ ظَهِيرٗا ٨٨

89. በዚህም ቁርኣን ውስጥ ከምሳሌው ሁሉ ለሰዎች በእርግጥ መላለስን፡፡ አብዛኞቹም ሰዎች ክህደትን እንጂ ሌላን እምቢ አሉ፡፡

وَلَقَدۡ صَرَّفۡنَا لِلنَّاسِ فِي هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ مِن كُلِّ مَثَلٖ فَأَبَىٰٓ أَكۡثَرُ ٱلنَّاسِ إِلَّا كُفُورٗا ﴿٨٩﴾

90. አሉም «ለኛ ከምድር ምንጭን እስከምታፈነዳን ለአንተ አናምንም፡፡»

وَقَالُواْ لَن نُّؤۡمِنَ لَكَ حَتَّىٰ تَفۡجُرَ لَنَا مِنَ ٱلۡأَرۡضِ يَنۢبُوعًا ﴿٩٠﴾

91. «ወይም ከዘምባባዎችና ከወይን የኾነች አትክልት ለአንተ እስከምትኖርህና በመካከልዋም ጂረቶችን በብዛት እስከምታንቧቧ፡፡

أَوۡ تَكُونَ لَكَ جَنَّةٞ مِّن نَّخِيلٖ وَعِنَبٖ فَتُفَجِّرَ ٱلۡأَنۡهَٰرَ خِلَٰلَهَا تَفۡجِيرًا ﴿٩١﴾

92. «ወይም እንደምትለው ከሰማይ ቁራጮችን በኛ ላይ እስከምታወድቅ፤ ወይም አላህንና መላእክትን በግልጽ እስከምታመጣ፡፡

أَوۡ تُسۡقِطَ ٱلسَّمَآءَ كَمَا زَعَمۡتَ عَلَيۡنَا كِسَفًا أَوۡ تَأۡتِيَ بِٱللَّهِ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ قَبِيلًا ﴿٩٢﴾

93. «ወይም ከወርቅ የኾነ ቤት ላንተ እስከሚኖርህ፤ ወይም በሰማይ እስከምትወጣ፤ ለመውጣትህም በእኛ ላይ የምናነበው የኾነን መጽሐፍ እስከምታወርድልን ድረስ ፈጽሞ አናምንልህም» (አሉ)፡፡ «ጌታዬ ጥራት ይገባው፤ እኔ ሰው መልክተኛ እንጂ ሌላ አይደለሁም» በላቸው፡፡

أَوۡ يَكُونَ لَكَ بَيۡتٞ مِّن زُخۡرُفٍ أَوۡ تَرۡقَىٰ فِي ٱلسَّمَآءِ وَلَن نُّؤۡمِنَ لِرُقِيِّكَ حَتَّىٰ تُنَزِّلَ عَلَيۡنَا كِتَٰبٗا نَّقۡرَؤُهُۥۗ قُلۡ سُبۡحَانَ رَبِّي هَلۡ كُنتُ إِلَّا بَشَرٗا رَّسُولٗا ﴿٩٣﴾

94. ሰዎችንም መሪ (ቁርኣን) በመጣላቸው ጊዜ ከማመን «አላህ ሰውን መልክተኛ አድርጎ ላከን» ማለታቸው እንጂ ሌላ አልከለከላቸውም፡፡

وَمَا مَنَعَ ٱلنَّاسَ أَن يُؤۡمِنُوٓاْ إِذۡ جَآءَهُمُ ٱلۡهُدَىٰٓ إِلَّآ أَن قَالُوٓاْ أَبَعَثَ ٱللَّهُ بَشَرٗا رَّسُولٗا ﴿٩٤﴾

95. «በምድር ላይ ረግተው የሚኼዱ መላእክት በነበሩ ኖሮ በእነሱ ላይ (ከጎሳቸው) የመልአክን መልክተኛ ባወረድን ነበር» በላቸው፡፡

قُل لَّوۡ كَانَ فِي ٱلۡأَرۡضِ مَلَٰٓئِكَةٞ يَمۡشُونَ مُطۡمَئِنِّينَ لَنَزَّلۡنَا عَلَيۡهِم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ مَلَكٗا رَّسُولٗا ﴿٩٥﴾

96. «በእኔና በእናንተ መካከል መስካሪ በአላህ በቃ፡፡ እርሱ በባሮቹ (ነገር) ውስጥ ዐዋቂ ተመልካች ነውና» በላቸው፡፡

قُلۡ كَفَىٰ بِٱللَّهِ شَهِيدَۢا بَيۡنِي وَبَيۡنَكُمۡۚ إِنَّهُۥ كَانَ بِعِبَادِهِۦ خَبِيرَۢا بَصِيرٗا ﴿٩٦﴾

97. አላህም ያቀናው ሰው ቅኑ እርሱ ብቻ ነው፡፡ ያጠመማቸውም ሰዎች ከእርሱ ሌላ ለእነርሱ ፈጽሞ ረዳት አታገኝላቸውም፡፡ በትንሣኤ ቀንም ዕውሮች፣ ዲዳዎችም ደንቆሮዎችም ኾነው በፊቶቻቸው ላይ (እየተጎተቱ) እንሰበስባቸዋለን፡፡ መኖሪያቸው ገሀነም ናት፡፡ (ነዲድዋ) በደከመች ቁጥር መንቀልቀልን እንጨምርባቸዋለን፡፤

وَمَن يَهۡدِ ٱللَّهُ فَهُوَ ٱلۡمُهۡتَدِۖ وَمَن يُضۡلِلۡ فَلَن تَجِدَ لَهُمۡ أَوۡلِيَآءَ مِن دُونِهِۦۖ وَنَحۡشُرُهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ عَلَىٰ وُجُوهِهِمۡ عُمۡيٗا وَبُكۡمٗا وَصُمّٗاۖ مَّأۡوَىٰهُمۡ جَهَنَّمُۖ كُلَّمَا خَبَتۡ زِدۡنَٰهُمۡ سَعِيرٗا ﴿٩٧﴾

98. ይህ (ቅጣት)፤ እነርሱ በአንቀጾቻችን ስለ ካዱና «አጥንቶችና ብስብሶች በኾን ጊዜ እኛ አዲስ ፍጥረት ኾነን ተቀስቃሾች ነን» ስላሉም ፍዳቸው ነው፡፡

ذَٰلِكَ جَزَآؤُهُم بِأَنَّهُمۡ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَقَالُوٓاْ أَءِذَا كُنَّا عِظَٰمٗا وَرُفَٰتًا أَءِنَّا لَمَبۡعُوثُونَ خَلۡقٗا جَدِيدٗا ﴿٩٨﴾

99. ያ ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ አላህ ብጤያቸውን በመፍጠር ላይ ቻይ መኾኑን በእርሱ ጥርጣሬ የሌለበትም ጊዜ (ለሞትም ለትንሣኤም) ለእነርሱ የወሰነ መኾኑን አላወቁምን በደለኞችም ከክህደት በቀር እምቢ አሉ፡፡

۞أَوَلَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّ ٱللَّهَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ قَادِرٌ عَلَىٰٓ أَن يَخۡلُقَ مِثۡلَهُمۡ وَجَعَلَ لَهُمۡ أَجَلٗا لَّا رَيۡبَ فِيهِ فَأَبَى ٱلظَّٰلِمُونَ إِلَّا كُفُورٗا ٩٩

100. «እናንተ የጌታዬን የችሮታ መካዚኖች ብትይዙ ኖሮ ያን ጊዜ በማውጣታችሁ ማለቋን በመፍራት በጨበጣችሁ ነበር፡፡ ሰውም በጣም ቆጣቢ ነው፡፡»

قُل لَّوۡ أَنتُمۡ تَمۡلِكُونَ خَزَآئِنَ رَحۡمَةِ رَبِّيٓ إِذٗا لَّأَمۡسَكۡتُمۡ خَشۡيَةَ ٱلۡإِنفَاقِۚ وَكَانَ ٱلۡإِنسَٰنُ قَتُورٗا ١٠٠

101. ለሙሳም ግልጽ የኾኑን ዘጠኝ ተዓምራቶች በእርግጥ ሰጠነው፡፡ በመጣቸውም ጊዜ የእስራኤልን ልጆች (ከፈርዖን እንዲለቀቁ) ጠይቅ (አልነው)፡፡ ፈርዖንም «ሙሳ ሆይ! እኔ የተደገሙብህ መኾንህን በእርግጥ እጠረጥራለሁ» አለው፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَىٰ تِسۡعَ ءَايَٰتِۭ بَيِّنَٰتٖۖ فَسۡـَٔلۡ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ إِذۡ جَآءَهُمۡ فَقَالَ لَهُۥ فِرۡعَوۡنُ إِنِّي لَأَظُنُّكَ يَٰمُوسَىٰ مَسۡحُورٗا ١٠١

102. (ሙሳም) «እነዚህን (ተዓምራቶች) መገሰጫዎች ሲኾኑ የሰማያትና የምድር ጌታ እንጂ ሌላ እንዳላወረዳቸው በእርግጥ ዐውቀሃል፡፡ እኔም ፈርዖን ሆይ! የምትጠፋ መኾንህን በእርግጥ እጠረጥርሃለሁ» አለው፡፡

قَالَ لَقَدۡ عَلِمۡتَ مَآ أَنزَلَ هَٰٓؤُلَآءِ إِلَّا رَبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ بَصَآئِرَ وَإِنِّي لَأَظُنُّكَ يَٰفِرۡعَوۡنُ مَثۡبُورٗا ١٠٢

103. ከምድርም ሊቀሰቅሳቸው አሰበ፡፡ እርሱንና ከእርሱ ጋር የነበሩትንም ሰዎች ሁሉንም አሰጠምናቸው፡፡

فَأَرَادَ أَن يَسۡتَفِزَّهُم مِّنَ ٱلۡأَرۡضِ فَأَغۡرَقۡنَٰهُ وَمَن مَّعَهُۥ جَمِيعٗا ١٠٣

104. ከእርሱም በኋላ ለእስራኤል ልጆች «ምድሪቱን ተቀመጡባት የኋለኛይቱም (ሰዓት) ቀጠሮ በመጣ ጊዜ እናንተን የተከማቻችሁ ስትኾኑ እናመጣችኋለን» አልናቸው፡፡

وَقُلۡنَا مِنۢ بَعۡدِهِۦ لِبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱسۡكُنُواْ ٱلۡأَرۡضَ فَإِذَا جَآءَ وَعۡدُ ٱلۡأٓخِرَةِ جِئۡنَا بِكُمۡ لَفِيفٗا ١٠٤

105. (ቁርኣንን) በውነትም አወረድነው፡፡ በእውነትም ወረደ፡፡ አንተንም አብሳሪና አስጠንቃቂ አድርገን እንጂ አልላክንህም፡፡

وَبِٱلۡحَقِّ أَنزَلۡنَٰهُ وَبِٱلۡحَقِّ نَزَلَۗ وَمَآ أَرۡسَلۡنَٰكَ إِلَّا مُبَشِّرٗا وَنَذِيرٗا ١٠٥

106. ቁርኣንንም በሰዎች ላይ በዝግታ ላይ ኾነህ ታነበው ዘንድ ከፋፈልነው፡፡ ቀስ በቀስ ማውረድንም አወረድነው፡፡

وَقُرۡءَانٗا فَرَقۡنَٰهُ لِتَقۡرَأَهُۥ عَلَى ٱلنَّاسِ عَلَىٰ مُكۡثٖ وَنَزَّلۡنَٰهُ تَنزِيلٗا ١٠٦

107. «በእርሱ እመኑ ወይም አትመኑ» በላቸው፤ እነዚያ ከእርሱ በፊት ዕውቀትን የተሰጡት በእነሱ ላይ በተነበበ ጊዜ ሰጋጆች ኾነው በሽንነበቶቻቸው ላይ ይወድቃሉ፤

قُلۡ ءَامِنُواْ بِهِۦٓ أَوۡ لَا تُؤۡمِنُوٓاْۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡعِلۡمَ مِن قَبۡلِهِۦٓ إِذَا يُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ يَخِرُّونَ لِلۡأَذۡقَانِ سُجَّدٗا ١٠٧

108. ይላሉም «ጌታችን ጥራት ይገባው! እነሆ የጌታችን ተስፋ ተፈጻሚ ነው፡፡»

وَيَقُولُونَ سُبۡحَٰنَ رَبِّنَآ إِن كَانَ وَعۡدُ رَبِّنَا لَمَفۡعُولٗا ١٠٨

109. እያለቀሱም በሽንነበቶቻቸው ላይ ይወድቃሉ (አላህን) መፍራትንም ይጨምርላቸዋል፡፡

وَيَخِرُّونَ لِلۡأَذۡقَانِ يَبۡكُونَ وَيَزِيدُهُمۡ خُشُوعٗا۩ ١٠٩

110. «አላህን ጥሩ፤ ወይም አልረሕማንን ጥሩ፤ (ከሁለቱ) ማንኛውንም ብትጠሩ (መልካም ነው)፡፡ ለእርሱ መልካም ስሞች አሉትና» በላቸው፡፡ በስግደትህም (ስታነብ) አትጩህ፡፡ በእርሷም ድምጽህን ዝቅ አታድርግ በዚህም መካከል መንገድን ፈልግ፡፡

قُلِ ٱدْعُوا۟ ٱللَّهَ أَوِ ٱدْعُوا۟ ٱلرَّحْمَٰنَ ۖ أَيًّا مَّا تَدْعُوا۟ فَلَهُ ٱلْأَسْمَآءُ ٱلْحُسْنَىٰ ۚ وَلَا تَجْهَرْ بِصَلَاتِكَ وَلَا تُخَافِتْ بِهَا وَٱبْتَغِ بَيْنَ ذَٰلِكَ سَبِيلًا ﴿١١٠﴾

111. «ምስጋና ለአላህ ለዚያ ልጅን ላልያዘው፣ ለእርሱም በንግሥናው ተጋሪ ለሌለው፣ ለእርሱም ከውርደት ረዳት ለሌለው ይገባው በልም፡፡ ማክበርንም አክብረው፡፡»

وَقُلِ ٱلْحَمْدُ لِلَّهِ ٱلَّذِى لَمْ يَتَّخِذْ وَلَدًا وَلَمْ يَكُن لَّهُۥ شَرِيكٌ فِى ٱلْمُلْكِ وَلَمْ يَكُن لَّهُۥ وَلِىٌّ مِّنَ ٱلذُّلِّ ۖ وَكَبِّرْهُ تَكْبِيرًۢا ﴿١١١﴾

## ሱረቱ አል ከህፍ

## سورة الكهف

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ምስጋና ለአላህ ለዚያ መጽሐፉን በውስጡ መጣመምን ያላደረገበት ሲሆን በባሪያው ላይ ላወረደው ይገባው፡፡

ٱلْحَمْدُ لِلَّهِ ٱلَّذِىٓ أَنزَلَ عَلَىٰ عَبْدِهِ ٱلْكِتَٰبَ وَلَمْ يَجْعَل لَّهُۥ عِوَجَا ۜ ﴿١﴾

2. ቀጥተኛ ሲሆን ከእርሱ ዘንድ የኾነን ብርቱን ቅጣት ሊያስፈራራበት፣ እነዚያንም በጎ ሥራዎችን የሚሠሩትን ምእመናን ለነሱ መልካም ምንዳ ያላቸው መኾኑን ሊያበስርበት፤ (አወረደው)፡፡

قَيِّمًا لِّيُنذِرَ بَأْسًا شَدِيدًا مِّن لَّدُنْهُ وَيُبَشِّرَ ٱلْمُؤْمِنِينَ ٱلَّذِينَ يَعْمَلُونَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ أَنَّ لَهُمْ أَجْرًا حَسَنًا ﴿٢﴾

3. በእርሱ ውስጥ ዘለዓለም የሚቆዩበት ሲኾኑ (ያላቸው መኾኑን)፡፡

مَّٰكِثِينَ فِيهِ أَبَدًا ﴿٣﴾

4. እነዚያንም «አላህ ልጅን ይዟል» ያሉትን ሊያስፈራራበት (አወረደው)፡፡

وَيُنذِرَ ٱلَّذِينَ قَالُوا۟ ٱتَّخَذَ ٱللَّهُ وَلَدًا ﴿٤﴾

5. ለእነሱም ለአባቶቻቸውም በርሱ ምንም እውቀት የላቸውም፡፡ ከአፎቻቸው የምትወጣውን ቃል ምን አከበዳት! ውሸትን እንጂ አይናገሩም፡፡

مَّا لَهُم بِهِۦ مِنْ عِلْمٍ وَلَا لِءَابَآئِهِمْ ۚ كَبُرَتْ كَلِمَةً تَخْرُجُ مِنْ أَفْوَٰهِهِمْ ۚ إِن يَقُولُونَ إِلَّا كَذِبًا ﴿٥﴾

6. በዚህም ንግግር (በቁርኣን) ባያምኑ በፈለጎቻቸው ላይ በቁጭት ነፍስህን አጥፊ ልትሆን ይፈራልሃል፡፡

فَلَعَلَّكَ بَٰخِعٌ نَّفْسَكَ عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِمْ إِن لَّمْ يُؤْمِنُوا۟ بِهَٰذَا ٱلْحَدِيثِ أَسَفًا ﴿٦﴾

7. እኛ ማንኛቸው ሥራው ያማረ መኾኑን ልንፈትናቸው በምድር ላይ ያለን ሁሉ ለእርሷ ጌጥ አደረግን፤

إِنَّا جَعَلْنَا مَا عَلَى ٱلْأَرْضِ زِينَةً لَّهَا لِنَبْلُوَهُمْ أَيُّهُمْ أَحْسَنُ عَمَلًا ﴿٧﴾

8. እኛም በእርሷ ላይ ያለውን (በመጨረሻ) በእርግጥ በቃይ የሌለበት ምልጥ ዐፈር አድራጊዎች ነን፡፡

وَإِنَّا لَجَٰعِلُونَ مَا عَلَيۡهَا صَعِيدٗا جُرُزًا ٨

9. የዋሻውና የሰሌዳው ባለቤቶች ከተዓምራቶቻችን ሲሆኑ ግሩም መሆናቸውን አሰብክን

أَمۡ حَسِبۡتَ أَنَّ أَصۡحَٰبَ ٱلۡكَهۡفِ وَٱلرَّقِيمِ كَانُواْ مِنۡ ءَايَٰتِنَا عَجَبًا ٩

10. ጎበዞቹ ወደ ዋሻው በተጠጉና «ጌታችን ሆይ! ከአንተ ዘንድ እዝነትን ስጠን፤ ለእኛም ከነገራችን ቅንን አዘጋጅልን» ባሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ أَوَى ٱلۡفِتۡيَةُ إِلَى ٱلۡكَهۡفِ فَقَالُواْ رَبَّنَآ ءَاتِنَا مِن لَّدُنكَ رَحۡمَةٗ وَهَيِّئۡ لَنَا مِنۡ أَمۡرِنَا رَشَدٗا ١٠

11. በዋሻውም ውስጥ የተቆጠሩን ዓመታት በጆሮዎቻቸው ላይ መታንባቸው፡፡

فَضَرَبۡنَا عَلَىٰٓ ءَاذَانِهِمۡ فِي ٱلۡكَهۡفِ سِنِينَ عَدَدٗا ١١

12. ከዚያም ከሁለቱ ክፍሎች ለቆዩት ጊዜ ልክ ያረጋገጠው ማንኛው መሆኑን ልናውቅ አስነሳናቸው፡፡

ثُمَّ بَعَثۡنَٰهُمۡ لِنَعۡلَمَ أَيُّ ٱلۡحِزۡبَيۡنِ أَحۡصَىٰ لِمَا لَبِثُوٓاْ أَمَدٗا ١٢

13. እኛ ወሬያቸውን በአንተ ላይ በእውነት እንተርካለን፡፡ እነሱ በጌታቸው ያመኑ ጎበዞች ናቸው፡፡ መመራትንም ጨመርንላቸው፡፡

نَّحۡنُ نَقُصُّ عَلَيۡكَ نَبَأَهُم بِٱلۡحَقِّۚ إِنَّهُمۡ فِتۡيَةٌ ءَامَنُواْ بِرَبِّهِمۡ وَزِدۡنَٰهُمۡ هُدٗى ١٣

14. (በንጉሣቸው ፊት) በቆሙና «ጌታችን የሰማያትና የምድር ጌታ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክን አንገዛም፡፡ ያን ጊዜ (ሌላን ብናመልክ) ወሰን ያለፈን (ንግግር) በእርግጥ ተናገርን፡፡» ባሉ ጊዜ ልቦቻቸውን አጠነከርን፡፡

وَرَبَطۡنَا عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ إِذۡ قَامُواْ فَقَالُواْ رَبُّنَا رَبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ لَن نَّدۡعُوَاْ مِن دُونِهِۦٓ إِلَٰهٗاۖ لَّقَدۡ قُلۡنَآ إِذٗا شَطَطًا ١٤

15. «እነዚህ ሕዝቦቻችን ከእርሱ ሌላ አማልክትን ያዙ፤ (እውነተኞች ከኾኑ) በእነርሱ ላይ ግልጽ ማስረጃን ለምን አያመጡም በአላህም ላይ ውሸትን ከሚቀጣጥፍ ይበልጥ በዳይ ማነው» (አሉ)፡፡

هَٰٓؤُلَآءِ قَوۡمُنَا ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِهِۦٓ ءَالِهَةٗۖ لَّوۡلَا يَأۡتُونَ عَلَيۡهِم بِسُلۡطَٰنِۭ بَيِّنٖۖ فَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبٗا ١٥

16. «እነርሱንና ያንን ከአላህ ሌላ የሚግገዙትን በተለያችሁ ጊዜ ወደ ዋሻው ተጠጉ፡፡ ጌታችሁ ለእናንተ ከችሮታው ይዘረጋላችኋልና፤ ከነገራችሁም ለእናንተ መጠቃቀሚያን ያዘጋጅላችኋል» (ተባባሉ)፡፡

وَإِذِ ٱعۡتَزَلۡتُمُوهُمۡ وَمَا يَعۡبُدُونَ إِلَّا ٱللَّهَ فَأۡوُۥٓاْ إِلَى ٱلۡكَهۡفِ يَنشُرۡ لَكُمۡ رَبُّكُم مِّن رَّحۡمَتِهِۦ وَيُهَيِّئۡ لَكُم مِّنۡ أَمۡرِكُم مِّرۡفَقٗا ١٦

17. ፀሐይንም በወጣች ጊዜ ከዋሻቸው ወደ ቀኝ ጎን ስታዘነብል ታያታለህ፡፡ በገባችም ጊዜ እነርሱ ከእርሱ በሰፊው ስፍራ ውስጥ ኾነው ሳሉ ወደ ግራ በኩል ትተዋቸዋለች፡፡ ይህ ከአላህ ተዓምራቶች ነው፡፡ አላህ የሚያቀናው ሰው ቅኑ እርሱ ብቻ ነው፡፡ የሚያጠመውም ሰው ለርሱ አቅኚን ረዳት አታገኝለትም፡፡

۞وَتَرَى ٱلشَّمۡسَ إِذَا طَلَعَت تَّزَٰوَرُ عَن كَهۡفِهِمۡ ذَاتَ ٱلۡيَمِينِ وَإِذَا غَرَبَت تَّقۡرِضُهُمۡ ذَاتَ ٱلشِّمَالِ وَهُمۡ فِي فَجۡوَةٖ مِّنۡهُۚ ذَٰلِكَ مِنۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِۗ مَن يَهۡدِ ٱللَّهُ فَهُوَ ٱلۡمُهۡتَدِۖ وَمَن يُضۡلِلۡ فَلَن تَجِدَ لَهُۥ وَلِيّٗا مُّرۡشِدٗا ١٧

وَتَحۡسَبُهُمۡ أَيۡقَاظٗا وَهُمۡ رُقُودٞۚ وَنُقَلِّبُهُمۡ ذَاتَ ٱلۡيَمِينِ وَذَاتَ ٱلشِّمَالِۖ وَكَلۡبُهُم بَٰسِطٞ ذِرَاعَيۡهِ بِٱلۡوَصِيدِۚ لَوِ ٱطَّلَعۡتَ عَلَيۡهِمۡ لَوَلَّيۡتَ مِنۡهُمۡ فِرَارٗا وَلَمُلِئۡتَ مِنۡهُمۡ رُعۡبٗا ﴿١٨﴾

18. እነሱም የተኙ ሆነው ሳሉ (ዓይኖቻቸው በመከፈታቸው) ንቁዎች ናቸው ብለህ ታስባቸዋለህ:: ወደ ቀኝ ጎንና ወደ ግራ ጎንም እናገላብጣቸዋለን:: ውሻቸውም ሁለት ክንዶቹን በዋሻው በር ላይ ዘርግቷል:: በእነሱ ላይ ዘልቀህ ብታይ ኖሮ የምትሸሽ ኾነህ በዞርክ ነበር:: ከእነሱም በእርግጥ ፍርሃትን በተመላህ ነበር::

وَكَذَٰلِكَ بَعَثۡنَٰهُمۡ لِيَتَسَآءَلُواْ بَيۡنَهُمۡۚ قَالَ قَآئِلٞ مِّنۡهُمۡ كَمۡ لَبِثۡتُمۡۖ قَالُواْ لَبِثۡنَا يَوۡمًا أَوۡ بَعۡضَ يَوۡمٖۚ قَالُواْ رَبُّكُمۡ أَعۡلَمُ بِمَا لَبِثۡتُمۡ فَٱبۡعَثُوٓاْ أَحَدَكُم بِوَرِقِكُمۡ هَٰذِهِۦٓ إِلَى ٱلۡمَدِينَةِ فَلۡيَنظُرۡ أَيُّهَآ أَزۡكَىٰ طَعَامٗا فَلۡيَأۡتِكُم بِرِزۡقٖ مِّنۡهُ وَلۡيَتَلَطَّفۡ وَلَا يُشۡعِرَنَّ بِكُمۡ أَحَدًا ﴿١٩﴾

19. እንዲሁም በመካከላቸው እንዲጠያየቁ ቀሰቀስናቸው:: ከእነሱ አንድ ተናጋሪ «ምን ያክል ቆያችሁ» አለ:: «አንድን ቀን ወይም የቀንን ከፊል ቆየን» አሉ:: «ጌታችሁ የቆያችሁትን ጊዜ ልክ ዐዋቂ ነው:: ከዚህችም ብራችሁ ጋር አንዳችሁን ወደ ከተማይቱ ላኩ:: ከምግቦቿ የትኛዋ ንጹሕ መሆኗንም ይመልከት:: ከእርሱም (ከንጹሑ) ምግብን ያምጣላችሁ:: ቀስም ይበል:: በእናንተም አንድንም ሰው አያሳውቅ» አሉ::

إِنَّهُمۡ إِن يَظۡهَرُواْ عَلَيۡكُمۡ يَرۡجُمُوكُمۡ أَوۡ يُعِيدُوكُمۡ فِي مِلَّتِهِمۡ وَلَن تُفۡلِحُوٓاْ إِذًا أَبَدٗا ﴿٢٠﴾

20. «እነሱ በእናንተ ላይ ቢዘልቁ ይቀጠቅጧችኋልና:: ወይም ወደ ሃይማኖታቸው ይመልሷችኋል:: ያንጊዜም በፍጹም ፍላጎታችሁን አታገኙም» (ተባባሉ)::

وَكَذَٰلِكَ أَعۡثَرۡنَا عَلَيۡهِمۡ لِيَعۡلَمُوٓاْ أَنَّ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٞ وَأَنَّ ٱلسَّاعَةَ لَا رَيۡبَ فِيهَآ إِذۡ يَتَنَٰزَعُونَ بَيۡنَهُمۡ أَمۡرَهُمۡۖ فَقَالُواْ ٱبۡنُواْ عَلَيۡهِم بُنۡيَٰنٗاۖ رَّبُّهُمۡ أَعۡلَمُ بِهِمۡۚ قَالَ ٱلَّذِينَ غَلَبُواْ عَلَىٰٓ أَمۡرِهِمۡ لَنَتَّخِذَنَّ عَلَيۡهِم مَّسۡجِدٗا ﴿٢١﴾

21. እንደዚሁም የአላህ ቀጠሮ እርግጠኛ መሆኑን ሰዓቲቱም በርሷ ጥርጣሬ የሌለ መሆኑን ያውቁ ዘንድ በእነርሱ ላይ (ሰዎችን) አሳወቅን:: (አማኞቹና ከሓዲዎቹ) ነገራቸውን በመካከላቸው ሲከራከሩ (የሆነውን አስታውስ፤ ከሓዲዎቹ):- «በእነሱ ላይም ግንብን ገንቡ» አሉ:: ጌታቸው በእነሱ ይበልጥ ዐዋቂ ነው:: እነዚያ በነገራቸው ላይ ያሸነፉት (ምእመናን) «በእነሱ ላይ በእርግጥ መስጊድን እንሠራለን» አሉ::

سَيَقُولُونَ ثَلَٰثَةٞ رَّابِعُهُمۡ كَلۡبُهُمۡ وَيَقُولُونَ خَمۡسَةٞ سَادِسُهُمۡ كَلۡبُهُمۡ رَجۡمَۢا بِٱلۡغَيۡبِۖ وَيَقُولُونَ سَبۡعَةٞ وَثَامِنُهُمۡ كَلۡبُهُمۡۚ قُل رَّبِّيٓ أَعۡلَمُ بِعِدَّتِهِم مَّا يَعۡلَمُهُمۡ إِلَّا قَلِيلٞۗ فَلَا تُمَارِ فِيهِمۡ إِلَّا مِرَآءٗ ظَٰهِرٗا وَلَا تَسۡتَفۡتِ فِيهِم مِّنۡهُمۡ أَحَدٗا ﴿٢٢﴾

22. በሩቅ ወርዋሪዎች ሆነው (በጥርጣሬ) «ሦስት ናቸው፤ አራተኛቸው ውሻቸው ነው» ይላሉ:: «አምስት ናቸው፤ ስድስተኛቸው ውሻቸው ነውም» ይላሉ:: «ሰባት ናቸው፤ ስምንተኛቸውም ውሻቸው ነው» ይላሉም:: «ጌታዬ ቁጥራቸውን ዐዋቂ ነው:: ጥቂት (ሰው) እንጂ አያውቃቸውም» በላቸው:: በእነሱም ነገር ግልጽን ክርክር እንጂ (ጠልቀህ) አትከራከር:: በእነሱም ጉዳይ ከነሱ (ከመጽሐፉ ሰዎች) አንድንም አትጠይቅ::

وَلَا تَقُولَنَّ لِشَاْيۡءٍ إِنِّي فَاعِلٞ ذَٰلِكَ غَدًا ﴿٢٣﴾

23. ለማንኛውም ነገር «እኔ ይህንን ነገ ሠሪ ነኝም» አትበል::

إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُۚ وَٱذۡكُر رَّبَّكَ إِذَا نَسِيتَ وَقُلۡ عَسَىٰٓ أَن يَهۡدِيَنِ رَبِّي لِأَقۡرَبَ مِنۡ هَٰذَا رَشَدٗا ﴿٢٤﴾

24. «አላህ የሻ እንደ ሆነ (እሰራዋለሁ)» ብትል እንጂ:: በረሳህም ጊዜ ጌታህን አውሳ:: «ጌታዬም ከዚህ ይበልጥ ለቀጥታ የቀረበን ሊመራኝ ይከጀላል» በላቸው::

25. በዋሻቸውም ውስጥ ሶስት መቶ ዓመታትን ቆዩ፡፡ ዘጠኝንም ጨመሩ፡፡

وَلَبِثُواْ فِي كَهۡفِهِمۡ ثَلَٰثَ مِاْئَةٖ سِنِينَ وَٱزۡدَادُواْ تِسۡعٗا ۝٢٥

26. «አላህ የቆዩትን ልክ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡ የሰማያትና የምድር ምስጢር የእሱ ብቻ ነው፡፡ እርሱ ምን ያይ! ምን ይሰማም! ለእነርሱ ከእርሱ በቀር ምንም ረዳት የላቸውም፡፡ በፍርዱም አንድንም አያጋራም፡፡

قُلِ ٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا لَبِثُواْۖ لَهُۥ غَيۡبُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ أَبۡصِرۡ بِهِۦ وَأَسۡمِعۡۚ مَا لَهُم مِّن دُونِهِۦ مِن وَلِيّٖ وَلَا يُشۡرِكُ فِي حُكۡمِهِۦٓ أَحَدٗا ۝٢٦

27. ከጌታህም መጽሐፍ ወደ አንተ የተወረደውን አንብብ፡፡ ለቃላቶቹ ለዋጭ የላቸውም፡፡ ከእርሱም በቀር መጠጊያን በፍጹም አታገኝም፡፡

وَٱتۡلُ مَآ أُوحِيَ إِلَيۡكَ مِن كِتَابِ رَبِّكَۖ لَا مُبَدِّلَ لِكَلِمَٰتِهِۦ وَلَن تَجِدَ مِن دُونِهِۦ مُلۡتَحَدٗا ۝٢٧

28. ነፍስህንም፤ ከእነዚያ ጌታቸውን ፊቱን (ውዴታውን) የሚሹ ኾነው በጧትና በማታ ከሚግገዙት ጋር አስታግስ፡፡ የቅርቢቱንም ሕይወት ሽልማት የምትሻ ሆነህ ዓይኖችህ ከእነሱ (ወደ ሌላ) አይለፉ፡፡ ልቡንም እኛን ከማስታወስ ያዘነጋነውን ፍላጎቱንም የተከተለውን ነገሩም ሁሉ ወሰን ማለፍ የሆነውን ሰው አትታዘዝ፡፡

وَٱصۡبِرۡ نَفۡسَكَ مَعَ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ رَبَّهُم بِٱلۡغَدَوٰةِ وَٱلۡعَشِيِّ يُرِيدُونَ وَجۡهَهُۥۖ وَلَا تَعۡدُ عَيۡنَاكَ عَنۡهُمۡ تُرِيدُ زِينَةَ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَا تُطِعۡ مَنۡ أَغۡفَلۡنَا قَلۡبَهُۥ عَن ذِكۡرِنَا وَٱتَّبَعَ هَوَىٰهُ وَكَانَ أَمۡرُهُۥ فُرُطٗا ۝٢٨

29. «እውነቱም ከጌታችሁ ነው፡፡ የሻም ሰው ይመን፤ የሻም ሰው ይካድ» በላቸው፡፡ እኛ ለበደለኞች አጥሯ በእነሱ የከበበ የኾነችውን እሳት አዘጋጅተናል፡፡ (ከጥም) እርዳታንም ቢፈልጉ እንደ ዘይት ዝቃጭ ባለ ፊቶችን በሚጠብስ ውሃ ይረዳሉ፡፡ መጠጡ ከፋ! መደገፊያይቱም ምንኛ አስከፋች!

وَقُلِ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكُمۡۖ فَمَن شَآءَ فَلۡيُؤۡمِن وَمَن شَآءَ فَلۡيَكۡفُرۡۚ إِنَّآ أَعۡتَدۡنَا لِلظَّٰلِمِينَ نَارًا أَحَاطَ بِهِمۡ سُرَادِقُهَاۚ وَإِن يَسۡتَغِيثُواْ يُغَاثُواْ بِمَآءٖ كَٱلۡمُهۡلِ يَشۡوِي ٱلۡوُجُوهَۚ بِئۡسَ ٱلشَّرَابُ وَسَآءَتۡ مُرۡتَفَقًا ۝٢٩

30. እነዚያ ያመኑና መልካም ሥራዎችንም የሠሩ እኛ ሥራን ያሳመረን ሰው ምንዳ አናጠፋም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ إِنَّا لَا نُضِيعُ أَجۡرَ مَنۡ أَحۡسَنَ عَمَلًا ۝٣٠

31. እነዚያ ለእነሱ የመኖሪያ ገነቶች ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው አሏቸው፡፡ በእርሷ ውስጥ ከወርቅ የኾኑን አንባሮች ይሸለማሉ፡፡ ከቀጭን ሐርና ከወፍራም ሐርም አረንጓዴን ልብሶች ይለብሳሉ፡፡ በውስጧ በባለ አጎበር አልጋዎች ላይ የተደገፉ ኾነው (ይቀመጣሉ)፡፡ ምንዳቸው ምን ያምር! መደገፊያይቱም ምንኛ አማረች!

أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ جَنَّٰتُ عَدۡنٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهِمُ ٱلۡأَنۡهَٰرُ يُحَلَّوۡنَ فِيهَا مِنۡ أَسَاوِرَ مِن ذَهَبٖ وَيَلۡبَسُونَ ثِيَابًا خُضۡرٗا مِّن سُندُسٖ وَإِسۡتَبۡرَقٖ مُّتَّكِـِٔينَ فِيهَا عَلَى ٱلۡأَرَآئِكِۚ نِعۡمَ ٱلثَّوَابُ وَحَسُنَتۡ مُرۡتَفَقٗا ۝٣١

32. ለእነሱም የሁለትን ሰዎች ምሳሌ ግለጽላቸው፡፡ ለአንደኛቸው (ለከሓዲው) ከወይኖች የኾኑን ሁለት አትክልቶች አደረግንለት፡፡ በዘምባባም አከበብናቸው፡፡ በመካከላቸውም አዝመራን አደረግን፡፡

۞وَٱضۡرِبۡ لَهُم مَّثَلٗا رَّجُلَيۡنِ جَعَلۡنَا لِأَحَدِهِمَا جَنَّتَيۡنِ مِنۡ أَعۡنَٰبٖ وَحَفَفۡنَٰهُمَا بِنَخۡلٖ وَجَعَلۡنَا بَيۡنَهُمَا زَرۡعٗا ۝٣٢

33. ሁለቱም አትክልቶች ሰብላቸውን ሰጡ፡፡ ከእርሱም ምንም አላጎደሉም፡፡ በመካከላቸውም ወንዝን አፈሰስን፡፡

كِلْتَا ٱلْجَنَّتَيْنِ ءَاتَتْ أُكُلَهَا وَلَمْ تَظْلِم مِّنْهُ شَيْـًٔا ۚ وَفَجَّرْنَا خِلَـٰلَهُمَا نَهَرًا ﴿٣٣﴾

34. ለእርሱም (ከአትክልቶቹ ሌላ ፍሬያማ) ሀብት ነበረው፡፡ ለጓደኛውም (ለአማኙ) እርሱ የሚወዳደረው ሲኾን «እኔ ካንተ በገንዘብ ይበልጥ የበዛሁ በወገንም ይበልጥ የበረታሁ ነኝ» አለው፡፡

وَكَانَ لَهُۥ ثَمَرٌ فَقَالَ لِصَـٰحِبِهِۦ وَهُوَ يُحَاوِرُهُۥٓ أَنَا۠ أَكْثَرُ مِنكَ مَالًا وَأَعَزُّ نَفَرًا ﴿٣٤﴾

35. እርሱም ነፍሱን በዳይ ኾኖ ወደ አትክልቱ ገባ፡፡ «ይህች ዘለዓለም ትጠፋለች ብዬ አልጠረጥርም» አለ፡፡

وَدَخَلَ جَنَّتَهُۥ وَهُوَ ظَالِمٌ لِّنَفْسِهِۦ قَالَ مَآ أَظُنُّ أَن تَبِيدَ هَـٰذِهِۦٓ أَبَدًا ﴿٣٥﴾

36. «ሰዓቲቱንም ቋሚ (ኗኝ) ናት ብዬ አልጠረጥርም፡ ፡ (እንደምትለው) ወደ ጌታዬም ብመለስ ከእርሷ የበለጠን መመለሻ በእርግጥ አገኛለሁ» (አለው)፡፡

وَمَآ أَظُنُّ ٱلسَّاعَةَ قَآئِمَةً وَلَئِن رُّدِدتُّ إِلَىٰ رَبِّى لَأَجِدَنَّ خَيْرًا مِّنْهَا مُنقَلَبًا ﴿٣٦﴾

37. ጓደኛው (አማኙ) እርሱ ለእርሱ የሚመላለሰው ሲኾን «በዚያ ከዐፈር፣ ከዚያም ከፍትወት ጠብታ ከፈጠረህ፣ ከዚያም ሰው ባደረገህ (አምላክ) ካድክን» አለው፡፡

قَالَ لَهُۥ صَاحِبُهُۥ وَهُوَ يُحَاوِرُهُۥٓ أَكَفَرْتَ بِٱلَّذِى خَلَقَكَ مِن تُرَابٍ ثُمَّ مِن نُّطْفَةٍ ثُمَّ سَوَّىٰكَ رَجُلًا ﴿٣٧﴾

38. «እኔ ግን እርሱ አላህ ጌታዬ ነው፤ (እላለሁ)፡፡ በጌታዬም አንድንም አላጋራም፡፡

لَّـٰكِنَّا۠ هُوَ ٱللَّهُ رَبِّى وَلَآ أُشْرِكُ بِرَبِّىٓ أَحَدًا ﴿٣٨﴾

39. «አትክልትህንም በገባህ ጊዜ አላህ የሻው ይኾናል፤ በአላህ ቢኾን እንጂ ኀይል የለም፤ አትልም ኖሯልን እኔን በገንዘብም በልጅም ካንተ በጣም ያነስኩ ሆኜ ብታየኝ፡፡

وَلَوْلَآ إِذْ دَخَلْتَ جَنَّتَكَ قُلْتَ مَا شَآءَ ٱللَّهُ لَا قُوَّةَ إِلَّا بِٱللَّهِ ۚ إِن تَرَنِ أَنَا۠ أَقَلَّ مِنكَ مَالًا وَوَلَدًا ﴿٣٩﴾

40. «ጌታዬ ከአትክልትህ የበለጠን ሊሰጠኝ በርሷም (በአትክልትህ) ላይ ከሰማይ መብረቆችን ሊልክባትና የምታንዳልጥ ምልጥ ምድር ልትኾን ይቻላል፡፡

فَعَسَىٰ رَبِّىٓ أَن يُؤْتِيَنِ خَيْرًا مِّن جَنَّتِكَ وَيُرْسِلَ عَلَيْهَا حُسْبَانًا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ فَتُصْبِحَ صَعِيدًا زَلَقًا ﴿٤٠﴾

41. ወይም ውሃው ሠራጊ ሊኾን (ይችላል)፡፡ ያን ጊዜ ለርሱ መፈለግን ፈጽሞ አትችልም» (አለው)፡፡

أَوْ يُصْبِحَ مَآؤُهَا غَوْرًا فَلَن تَسْتَطِيعَ لَهُۥ طَلَبًا ﴿٤١﴾

42. ሀብቱም ተጠፋ፡፡ እርሷ በዳሶቿ ላይ የወደቀች ኾና በእርሷ ባወጣው ገንዘብ ላይ (እየተጸጸተ) መዳፎቹን የሚያገላብጥና «ወይ ጸጸቴ! በጌታዬ አንድም ባላጋራሁ» የሚል ኾነ፡፡

وَأُحِيطَ بِثَمَرِهِۦ فَأَصْبَحَ يُقَلِّبُ كَفَّيْهِ عَلَىٰ مَآ أَنفَقَ فِيهَا وَهِىَ خَاوِيَةٌ عَلَىٰ عُرُوشِهَا وَيَقُولُ يَـٰلَيْتَنِى لَمْ أُشْرِكْ بِرَبِّىٓ أَحَدًا ﴿٤٢﴾

43. ለእርሱም ከአላህ ሌላ የሚረዱት ጭፍሮች አልነበሩትም፡፡ ተረጂም አልነበረም፡፡

وَلَمْ تَكُن لَّهُۥ فِئَةٌ يَنصُرُونَهُۥ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَمَا كَانَ مُنتَصِرًا ﴿٤٣﴾

44. እዚያ ዘንድ (በትንሣኤ ቀን) ስልጣኑ እውነተኛ ለኾነው አላህ ብቻ ነው፡፡ እርሱ በመመንዳት የበለጠ ፍጻሜንም በማሳመር የበለጠ ነው፡፡

هُنَالِكَ ٱلْوَلَـٰيَةُ لِلَّهِ ٱلْحَقِّ ۚ هُوَ خَيْرٌ ثَوَابًا وَخَيْرٌ عُقْبًا ﴿٤٤﴾

45. ለእነሱም የቅርቢቱን ሕይወት ምሳሌ አውሳላቸው፡ ፡ (እርሷ) ከሰማይ እንዳወረድነው ውሃ በእርሱም የምድር በቃይ እንደ ተቀላቀለበት (ከተዋበ በኋላ ደርቆ) ነፋሶችም የሚያበኑት ደቃቅ እንደ ኾነ ብጤ ናት፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَٱضۡرِبۡ لَهُم مَّثَلَ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا كَمَآءٍ أَنزَلۡنَٰهُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ فَٱخۡتَلَطَ بِهِۦ نَبَاتُ ٱلۡأَرۡضِ فَأَصۡبَحَ هَشِيمٗا تَذۡرُوهُ ٱلرِّيَٰحُۗ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ مُّقۡتَدِرًا ٤٥

46. ገንዘብና ወንዶች ልጆች የቅርቢቱ ሕይወት ጌጦች ናቸው፡፡ መልካሞቹም ቀሪዎች (ሥራዎች) እጌታህ ዘንድ በምንዳ በላጭ ናቸው፡፡ በተስፋም በላጭ ናቸው፡፤

ٱلۡمَالُ وَٱلۡبَنُونَ زِينَةُ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَٱلۡبَٰقِيَٰتُ ٱلصَّٰلِحَٰتُ خَيۡرٌ عِندَ رَبِّكَ ثَوَابٗا وَخَيۡرٌ أَمَلٗا ٤٦

47. ተራራዎችንም የምናስኼድበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ ምድርንም ግልጽ ኾና ታያታለህ፡፡ እንሰበስባቸዋለንም፡ ፡ ከእነሱም አንድንም አንተውም፡፡

وَيَوۡمَ نُسَيِّرُ ٱلۡجِبَالَ وَتَرَى ٱلۡأَرۡضَ بَارِزَةٗ وَحَشَرۡنَٰهُمۡ فَلَمۡ نُغَادِرۡ مِنۡهُمۡ أَحَدٗا ٤٧

48. የተሰለፉም ኾነው በጌታህ ላይ ይቀረባሉ፡፡ (ይባላሉም) «በመጀመሪያ ጊዜ እንደ ፈጠርናችሁ (ራቁታችሁን) በእርግጥ መጣችሁን በእውነቱ ለእናንተ (ለመቀስቀሻ) ጊዜን አናደርግም መሰሏችሁ ነበር፡፡»

وَعُرِضُواْ عَلَىٰ رَبِّكَ صَفّٗا لَّقَدۡ جِئۡتُمُونَا كَمَا خَلَقۡنَٰكُمۡ أَوَّلَ مَرَّةِۭۚ بَلۡ زَعَمۡتُمۡ أَلَّن نَّجۡعَلَ لَكُم مَّوۡعِدٗا ٤٨

49. (ለሰው ሁሉ) መጽሐፉም ይቀርባል፡፡ ወዲያውም ከሓዲዎችን በውስጡ ካለው ነገር ፈሪዎች ኾነው ታያቸዋለህ፡፡ «ዋ ጥፋታችን! ለዚህ መጽሐፍ (ከሥራ) ትንሽንም ትልቅንም የቆጠራት ቢኾን እንጂ የማይተወው ምን አለው» ይላሉም፡፡ የሰሩትንም ነገር ሁሉ ቀራቢ ኾኖ ያገኙታል፡፡ ጌታህም አንድንም አይበድልም፡፡

وَوُضِعَ ٱلۡكِتَٰبُ فَتَرَى ٱلۡمُجۡرِمِينَ مُشۡفِقِينَ مِمَّا فِيهِ وَيَقُولُونَ يَٰوَيۡلَتَنَا مَالِ هَٰذَا ٱلۡكِتَٰبِ لَا يُغَادِرُ صَغِيرَةٗ وَلَا كَبِيرَةً إِلَّآ أَحۡصَىٰهَاۚ وَوَجَدُواْ مَا عَمِلُواْ حَاضِرٗاۗ وَلَا يَظۡلِمُ رَبُّكَ أَحَدٗا ٤٩

50. ለመላእክትም ለአደም ስገዱ ባልናቸው ጊዜ (የኾነውን አስታውስ)፡፡ ወዲያውም ሰገዱ፤ ኢብሊስ ብቻ ሲቀር፡፡ ከጋኔን (ጎሳ) ነበር፡፡ ከጌታውም ትእዛዝ ወጣ፡፡ እርሱንና ዘሮቹን እነርሱ ለእናንተ ጠላቶች ሲኾኑ ከእኔ ላይ ረዳቶች አድርጋችሁ ትይዛላችሁን ለበዳዮች ልዋጭነቱ ከፋ!

وَإِذۡ قُلۡنَا لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ ٱسۡجُدُواْ لِأٓدَمَ فَسَجَدُوٓاْ إِلَّآ إِبۡلِيسَ كَانَ مِنَ ٱلۡجِنِّ فَفَسَقَ عَنۡ أَمۡرِ رَبِّهِۦٓۗ أَفَتَتَّخِذُونَهُۥ وَذُرِّيَّتَهُۥٓ أَوۡلِيَآءَ مِن دُونِي وَهُمۡ لَكُمۡ عَدُوُّۢۚ بِئۡسَ لِلظَّٰلِمِينَ بَدَلٗا ٥٠

51. የሰማያትንና የምድርን አፈጣጠር አላሳየኋቸውም፡ ፡ የነፍሶቻቸውንም አፈጣጠር (እንደዚሁ)፡፡ አሳሳቾችንም ረዳቶች አድርጌ የምይዝ አይደለሁም፡፡

۞مَّآ أَشۡهَدتُّهُمۡ خَلۡقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَلَا خَلۡقَ أَنفُسِهِمۡ وَمَا كُنتُ مُتَّخِذَ ٱلۡمُضِلِّينَ عَضُدٗا ٥١

52. «እነዚያንም (አምላክ) የምትሏቸውን ተጋሪዎቼን ጥሩ» የሚልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ ይጠሯቸዋልም ግን አይመልሱላቸውም፡፡ በመካከላቸውም መጥፊያን ስፍራ (ገሀነምን) አደረግን፡፡

وَيَوۡمَ يَقُولُ نَادُواْ شُرَكَآءِيَ ٱلَّذِينَ زَعَمۡتُمۡ فَدَعَوۡهُمۡ فَلَمۡ يَسۡتَجِيبُواْ لَهُمۡ وَجَعَلۡنَا بَيۡنَهُم مَّوۡبِقٗا ٥٢

53. ከሓዲዎችም እሳትን ያያሉ፡፡ እነርሱም በውስጧ ወዳቂዎች መኾናቸውን ያረጋግጣሉ፡፡ ከእርሷም መሸሻን አያገኙም፡፡

وَرَءَا ٱلۡمُجۡرِمُونَ ٱلنَّارَ فَظَنُّوٓاْ أَنَّهُم مُّوَاقِعُوهَا وَلَمۡ يَجِدُواْ عَنۡهَا مَصۡرِفٗا ﴿٥٣﴾

54. በዚህም ቁርኣን ውስጥ ከየምሳሌው ሁሉ ለሰዎች መላልሰን ገለጽን፡፡ ሰውም ከነገሩ ሁሉ ይበልጥ ክርክረ ብዙ ነው፡፡

وَلَقَدۡ صَرَّفۡنَا فِي هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ لِلنَّاسِ مِن كُلِّ مَثَلٖۚ وَكَانَ ٱلۡإِنسَٰنُ أَكۡثَرَ شَيۡءٖ جَدَلٗا ﴿٥٤﴾

55. ሰዎችንም መምሪያ በመጣላቸው ጊዜ ከማመንና ጌታቸውንም ምሕረትን ከመለመን የመጀመሪዎቹ (ሕዝቦች) ልማድ (መጥፋት) ልትመጣባቸው ወይም ቅጣቱ በያይነቱ ሊመጣባቸው (መጠባበቅ) እንጂ ሌላ አልከለከላቸውም፡፡

وَمَا مَنَعَ ٱلنَّاسَ أَن يُؤۡمِنُوٓاْ إِذۡ جَآءَهُمُ ٱلۡهُدَىٰ وَيَسۡتَغۡفِرُواْ رَبَّهُمۡ إِلَّآ أَن تَأۡتِيَهُمۡ سُنَّةُ ٱلۡأَوَّلِينَ أَوۡ يَأۡتِيَهُمُ ٱلۡعَذَابُ قُبُلٗا ﴿٥٥﴾

56. መልክተኞችንም አብሳሪዎችና አስፈራሪዎች ኾነው እንጂ አንልክም፡፡ እነዚያ የካዱትም በውሸት እውነቱን በእሱ ሊያበላሹ ይከራከራሉ፡፡ አንቀጾቼንና በእርሱ የተስፈራሩበትንም ነገር ማላገጫ አድርገው ያዙ፡፡

وَمَا نُرۡسِلُ ٱلۡمُرۡسَلِينَ إِلَّا مُبَشِّرِينَ وَمُنذِرِينَۚ وَيُجَٰدِلُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِٱلۡبَٰطِلِ لِيُدۡحِضُواْ بِهِ ٱلۡحَقَّۖ وَٱتَّخَذُوٓاْ ءَايَٰتِي وَمَآ أُنذِرُواْ هُزُوٗا ﴿٥٦﴾

57. በጌታውም አንቀጾች ከተገሰጸና ከእርሷ ከዞረ እጆቹም ያስቀደሙትን ነገር ከረሳ ሰው ይበልጥ በዳይ ማነው እኛ በልቦቻቸው ላይ እንዳያውቁት ሺፋኖችን በጆሮዎቻቸውም ውስጥ ድንቁርናን አደረግን፡፡ ወደ መመራትም ብትጠራቸው ያን ጊዜ ፈጽሞ አይምመሩም፡፡

وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّن ذُكِّرَ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِۦ فَأَعۡرَضَ عَنۡهَا وَنَسِيَ مَا قَدَّمَتۡ يَدَاهُۚ إِنَّا جَعَلۡنَا عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ أَكِنَّةً أَن يَفۡقَهُوهُ وَفِيٓ ءَاذَانِهِمۡ وَقۡرٗاۖ وَإِن تَدۡعُهُمۡ إِلَى ٱلۡهُدَىٰ فَلَن يَهۡتَدُوٓاْ إِذًا أَبَدٗا ﴿٥٧﴾

58. ጌታህም በጣም መሃሪው የእዝነት ባለቤቱ ነው፡፡ በሠሩት ሥራ ቢይዛቸው ኖሮ ቅጣቱን ለእነሱ ባስቸኮለባቸው ነበር፡፡ ግን ለእነሱ ከእርሱ ሌላ መጠጊያን ፈጽሞ የማያገኙበት ቀጠሮ አላቸው፡፡

وَرَبُّكَ ٱلۡغَفُورُ ذُو ٱلرَّحۡمَةِۖ لَوۡ يُؤَاخِذُهُم بِمَا كَسَبُواْ لَعَجَّلَ لَهُمُ ٱلۡعَذَابَۚ بَل لَّهُم مَّوۡعِدٞ لَّن يَجِدُواْ مِن دُونِهِۦ مَوۡئِلٗا ﴿٥٨﴾

59. እነዚህ ከተሞችም በበደሉ ጊዜ አጠፋናቸው፡፡ ለመጥፊያቸውም የተወሰነ ጊዜን አደረግን፡፡

وَتِلۡكَ ٱلۡقُرَىٰٓ أَهۡلَكۡنَٰهُمۡ لَمَّا ظَلَمُواْ وَجَعَلۡنَا لِمَهۡلِكِهِم مَّوۡعِدٗا ﴿٥٩﴾

60. ሙሳም ለወጣቱ «የሁለቱን ባሕሮች መገናኛ እስከምደርስ ወይም ብዙን ጊዜ እስከምኼድ ድረስ (ከመጓዝ) አልወገድም» ያለውን (አስታውስ)፡፡

وَإِذۡ قَالَ مُوسَىٰ لِفَتَىٰهُ لَآ أَبۡرَحُ حَتَّىٰٓ أَبۡلُغَ مَجۡمَعَ ٱلۡبَحۡرَيۡنِ أَوۡ أَمۡضِيَ حُقُبٗا ﴿٦٠﴾

61. የሁለቱን መገናኛ በደረሱም ጊዜ ዐሣቸውን ረሱ፡፡ (ዐሣው) መንገዱንም በባህሩ ውስጥ ቀዳዳ አድርጎ ያዘ፡፡

فَلَمَّا بَلَغَا مَجۡمَعَ بَيۡنِهِمَا نَسِيَا حُوتَهُمَا فَٱتَّخَذَ سَبِيلَهُۥ فِي ٱلۡبَحۡرِ سَرَبٗا ﴿٦١﴾

62. ባለፉም ጊዜ ለወጣቱ «ምሳችንን ስጠን፡፡ ከዚህ ጉዟችን በእርግጥ ድካምን አግኝተናልና» አለ፡፡

فَلَمَّا جَاوَزَا قَالَ لِفَتَىٰهُ ءَاتِنَا غَدَآءَنَا لَقَدۡ لَقِينَا مِن سَفَرِنَا هَٰذَا نَصَبٗا ﴿٦٢﴾

قَالَ أَرَءَيۡتَ إِذۡ أَوَيۡنَآ إِلَى ٱلصَّخۡرَةِ فَإِنِّي نَسِيتُ ٱلۡحُوتَ وَمَآ أَنسَىٰنِيهُ إِلَّا ٱلشَّيۡطَٰنُ أَنۡ أَذۡكُرَهُۥۚ وَٱتَّخَذَ سَبِيلَهُۥ فِي ٱلۡبَحۡرِ عَجَبٗا ﴿٦٣﴾

63. «አየህን ወደ ቋጥኝዋ በተጠጋን ጊዜ እኔ ዐሣውን ረሳሁ፡፡ ማስታወሱንም ሰይጣን እንጂ ሌላ አላስረሳኝም፡፡ በባሕሩም ውስጥ መንገዱን አስደናቂ (መንገድ) አድርጎ ያዘ» አለ፡፡

قَالَ ذَٰلِكَ مَا كُنَّا نَبۡغِۚ فَٱرۡتَدَّا عَلَىٰٓ ءَاثَارِهِمَا قَصَصٗا ﴿٦٤﴾

64. (ሙሳም) ይህ እንፈልገው የነበርነው ነው አለው፡፡ በፈለጎቻቸውም ላይ እየተከተሉ ተመለሱ፡፡

فَوَجَدَا عَبۡدٗا مِّنۡ عِبَادِنَآ ءَاتَيۡنَٰهُ رَحۡمَةٗ مِّنۡ عِندِنَا وَعَلَّمۡنَٰهُ مِن لَّدُنَّا عِلۡمٗا ﴿٦٥﴾

65. ከባሮቻችንም ከእኛ ዘንድ ችሮታን የሰጠነውን ከእኛም ዘንድ ዕውቀትን ያስተማርነውን አንድን ባሪያ (ኸድርን) አገኙ፡፡

قَالَ لَهُۥ مُوسَىٰ هَلۡ أَتَّبِعُكَ عَلَىٰٓ أَن تُعَلِّمَنِ مِمَّا عُلِّمۡتَ رُشۡدٗا ﴿٦٦﴾

66. ሙሳ ለእርሱ «ከተማርከው ነገር ቀጥተኛን (ዕውቀት) ታስተምረኝ ዘንድ ልከተልህን» አለው፡፡

قَالَ إِنَّكَ لَن تَسۡتَطِيعَ مَعِيَ صَبۡرٗا ﴿٦٧﴾

67. (ባሪያውም) አለ «አንተ ከእኔ ጋር መታገስን በጭራሽ አትችልም፡፡

وَكَيۡفَ تَصۡبِرُ عَلَىٰ مَا لَمۡ تُحِطۡ بِهِۦ خُبۡرٗا ﴿٦٨﴾

68. «በዕውቀትም በእርሱ ባላዳረስከው ነገር ላይ እንዴት ትታገሳለህ»

قَالَ سَتَجِدُنِيٓ إِن شَآءَ ٱللَّهُ صَابِرٗا وَلَآ أَعۡصِي لَكَ أَمۡرٗا ﴿٦٩﴾

69. (ሙሳ) «አላህ የሻ እንደ ኾነ ታጋሽና ላንተ ትዕዛዝን የማልጥስ ኾኜ ታገኘኛለህ» አለው፡፡

قَالَ فَإِنِ ٱتَّبَعۡتَنِي فَلَا تَسۡـَٔلۡنِي عَن شَيۡءٍ حَتَّىٰٓ أُحۡدِثَ لَكَ مِنۡهُ ذِكۡرٗا ﴿٧٠﴾

70. «ብትከተለኝም ለአንተ ከእርሱ ማውሳትን እስከምጀምርልህ ድረስ ከምንም ነገር አትጠይቀኝ» አለው፡፡

فَٱنطَلَقَا حَتَّىٰٓ إِذَا رَكِبَا فِي ٱلسَّفِينَةِ خَرَقَهَاۖ قَالَ أَخَرَقۡتَهَا لِتُغۡرِقَ أَهۡلَهَا لَقَدۡ جِئۡتَ شَيۡـًٔا إِمۡرٗا ﴿٧١﴾

71. ኼዱም፡፡ በመርከቢቱም በተሳፈሩ ጊዜ ቀደዳት፡፡ «ባለ ቤቶቿን ልታሰጥም ቀደድካትን ትልቅ ነገርን በእርግጥ ሠራህ» አለው፡፡

قَالَ أَلَمۡ أَقُلۡ إِنَّكَ لَن تَسۡتَطِيعَ مَعِيَ صَبۡرٗا ﴿٧٢﴾

72. «አንተ ከኔ ጋር ትእግሥትን ፈጽሞ አትችልም አላልኩምን» አለ፡፡

قَالَ لَا تُؤَاخِذۡنِي بِمَا نَسِيتُ وَلَا تُرۡهِقۡنِي مِنۡ أَمۡرِي عُسۡرٗا ﴿٧٣﴾

73. «በረሳሁት ነገር አትያዘኝ፡፡ ከነገሬም ችግርን አታሸክመኝ» አለው፡፡

فَٱنطَلَقَا حَتَّىٰٓ إِذَا لَقِيَا غُلَٰمٗا فَقَتَلَهُۥ قَالَ أَقَتَلۡتَ نَفۡسٗا زَكِيَّةَۢ بِغَيۡرِ نَفۡسٖ لَّقَدۡ جِئۡتَ شَيۡـٔٗا نُّكۡرٗا ﴿٧٤﴾

74. (ወርደው) ተጓዙም፡፡ ወጣትንም ልጅ ባገኙና በገደለው፤ «ጊዜ ያለ ነፍስ (መግደል) ንጹሕን ነፍስ ገደልክን በእርግጥ መጥፎን ነገር ሥራህ» አለው፡፡

۞قَالَ أَلَمۡ أَقُل لَّكَ إِنَّكَ لَن تَسۡتَطِيعَ مَعِيَ صَبۡرٗا ﴿٧٥﴾

75. «አንተ ከኔ ጋር ትእግሥትን ፈጽሞ አትችልም አላልኩህምን» አለ፡፡

قَالَ إِن سَأَلۡتُكَ عَن شَيۡءِۭ بَعۡدَهَا فَلَا تُصَٰحِبۡنِيۖ قَدۡ بَلَغۡتَ مِن لَّدُنِّي عُذۡرٗا ﴿٧٦﴾

76. «ከርሷ (ከአሁኒቱ ጊዜ) በኋላ ከምንም ነገር ብጠይቅህ አትጎዳኘኝ፡፡ ከእኔ የይቅርታን መጨረሻ በእርግጥ ደርሰሃል» አለው፡፡

77. ኼዱም፡፡ ወደ አንዲት ከተማ ሰዎች በመጡም ጊዜ ነዋሪዎቿን ምግብን ጠየቁ፡፡ ከማስተናገዳቸውም እምቢ አሉ፡፡ በእርሷም ውስጥ ለመውደቅ የተቃረበን ግድግዳ አገኙ፡፡ (ኺድር) አቆመውም፡፡ (ሙሳም) «በሻህ ኖሮ በእርሱ ላይ ዋጋን በተቀበልክ ነበር» አለው፡፡

فَٱنطَلَقَا حَتَّىٰٓ إِذَآ أَتَيَآ أَهۡلَ قَرۡيَةٍ ٱسۡتَطۡعَمَآ أَهۡلَهَا فَأَبَوۡاْ أَن يُضَيِّفُوهُمَا فَوَجَدَا فِيهَا جِدَارٗا يُرِيدُ أَن يَنقَضَّ فَأَقَامَهُۥۖ قَالَ لَوۡ شِئۡتَ لَتَّخَذۡتَ عَلَيۡهِ أَجۡرٗا ٧٧

78. (ኺድር) አለ «ይህ በእኔና በአንተ መካከል መለያያ ነው፡፡ በእርሱ ላይ መታገስን ያልቻልክበትን ፍች እነግርሃለሁ፡፡

قَالَ هَٰذَا فِرَاقُ بَيۡنِي وَبَيۡنِكَۚ سَأُنَبِّئُكَ بِتَأۡوِيلِ مَا لَمۡ تَسۡتَطِع عَّلَيۡهِ صَبۡرًا ٧٨

79. «መርከቢቱማ በባሕር ለሚሠሩ ምስኪኖች ነበረች፡፡ ከኋላቸውም መርከብን ሁሉ በቅሚያ የሚይዝ ንጉሥ ነበረና፤ (እንዳይቀማቸው) ላነውራት ፈቀድኩ፡፡

أَمَّا ٱلسَّفِينَةُ فَكَانَتۡ لِمَسَٰكِينَ يَعۡمَلُونَ فِي ٱلۡبَحۡرِ فَأَرَدتُّ أَنۡ أَعِيبَهَا وَكَانَ وَرَآءَهُم مَّلِكٞ يَأۡخُذُ كُلَّ سَفِينَةٍ غَصۡبٗا ٧٩

80. «ወጣቱም ልጅማ ወላጆቹ ምእመናን ነበሩ፡፡ (ቢያድግ) ትእቢትንና ክህደትንም የሚያስገድዳቸው መኾኑን ፈራን፡፡

وَأَمَّا ٱلۡغُلَٰمُ فَكَانَ أَبَوَاهُ مُؤۡمِنَيۡنِ فَخَشِينَآ أَن يُرۡهِقَهُمَا طُغۡيَٰنٗا وَكُفۡرٗا ٨٠

81. «ጌታቸውም በንጹሕነት ከእርሱ በላጭን በእዝነትም ከእርሱ በጣም ቀራቢን ልጅ ሊለውጥላቸው ፈለግን፡፡

فَأَرَدۡنَآ أَن يُبۡدِلَهُمَا رَبُّهُمَا خَيۡرٗا مِّنۡهُ زَكَوٰةٗ وَأَقۡرَبَ رُحۡمٗا ٨١

82. «ግድግዳውማ በከተማይቱ ውስጥ የነበሩ የሁለት የቲሞች ወጣቶች ነበር፡፡ በሥሩም ለእነርሱ የኾነ (የተቀበረ) ድልብ ነበረ፡፡ አባታቸውም መልካም ሰው ነበር፡፡ ጌታህም ለአካለ መጠን እንዲደርሱና ከጌታህ ችሮታ ድልባቸውን እንዲያወጡ ፈቀደ፡፡ በፈቃዴም አልሠራሁትም፡፡ ይህ በእርሱ ላይ መታገስን ያልቻልከው ነገር ፍች ነው» (አለው)፡፡

وَأَمَّا ٱلۡجِدَارُ فَكَانَ لِغُلَٰمَيۡنِ يَتِيمَيۡنِ فِي ٱلۡمَدِينَةِ وَكَانَ تَحۡتَهُۥ كَنزٞ لَّهُمَا وَكَانَ أَبُوهُمَا صَٰلِحٗا فَأَرَادَ رَبُّكَ أَن يَبۡلُغَآ أَشُدَّهُمَا وَيَسۡتَخۡرِجَا كَنزَهُمَا رَحۡمَةٗ مِّن رَّبِّكَۚ وَمَا فَعَلۡتُهُۥ عَنۡ أَمۡرِيۚ ذَٰلِكَ تَأۡوِيلُ مَا لَمۡ تَسۡطِع عَّلَيۡهِ صَبۡرٗا ٨٢

83. ከዙልቀርነይንም ይጠይቁሃል፡፡ «በእናንተ ላይ ከእርሱ ወሬን አነባለሁ፤» በላቸው፡፡

وَيَسۡـَٔلُونَكَ عَن ذِي ٱلۡقَرۡنَيۡنِۖ قُلۡ سَأَتۡلُواْ عَلَيۡكُم مِّنۡهُ ذِكۡرًا ٨٣

84. እኛ ለእርሱ በምድር አስመቸነው፡፡ ከነገሩም ሁሉ (መዳረሻ) መንገድን ሰጠነው፡፡

إِنَّا مَكَّنَّا لَهُۥ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَءَاتَيۡنَٰهُ مِن كُلِّ شَيۡءٖ سَبَبٗا ٨٤

85. መንገድንም (ወደ ምዕራብ) ተከተለ፡፡

فَأَتۡبَعَ سَبَبًا ٨٥

86. ወደ ፀሐይ መግቢያም በደረሰ ጊዜ ጥቁር ጭቃ ባላት ምንጭ ውስጥ ስትጠልቅ አገኛት፡፡ ባጠገቧም ሕዝቦችን አገኘ፡፡ «ዙልቀርነይን ሆይ! ወይም (በመግደል) ትቀጣለህ ወይም በእነርሱ መልካም ነገርን (መማረክን) ትሠራለህ» አልነው፡፤

حَتَّىٰٓ إِذَا بَلَغَ مَغۡرِبَ ٱلشَّمۡسِ وَجَدَهَا تَغۡرُبُ فِي عَيۡنٍ حَمِئَةٖ وَوَجَدَ عِندَهَا قَوۡمٗاۗ قُلۡنَا يَٰذَا ٱلۡقَرۡنَيۡنِ إِمَّآ أَن تُعَذِّبَ وَإِمَّآ أَن تَتَّخِذَ فِيهِمۡ حُسۡنٗا ٨٦

87. «የበደለውን ሰውማ ወደፊት እንቀጣዋለን፡፡ ከዚያም ወደ ጌታው ይመለሳል፡፡ ብርቱንም ቅጣት ይቀጣዋል» አለ፡፡

قَالَ أَمَّا مَن ظَلَمَ فَسَوۡفَ نُعَذِّبُهُۥ ثُمَّ يُرَدُّ إِلَىٰ رَبِّهِۦ فَيُعَذِّبُهُۥ عَذَابٗا نُّكۡرٗا ﴿٨٧﴾

88. «ያመነም ሰውማ መልካምንም ሥራ የሠራ ለእርሱ ከምንዳ በኩል መልካሚቱ (ገነት) አለችው፡፡ ለእርሱም ከትእዛዛችን ገርን ነገር እናዘዋለን» (አለ)፡፡

وَأَمَّا مَنۡ ءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَلَهُۥ جَزَآءً ٱلۡحُسۡنَىٰۖ وَسَنَقُولُ لَهُۥ مِنۡ أَمۡرِنَا يُسۡرٗا ﴿٨٨﴾

89. ከዚያም መንገድን (ወደ ምሥራቅ) ቀጠለ፡፡

ثُمَّ أَتۡبَعَ سَبَبًا ﴿٨٩﴾

90. ወደ ፀሐይ መውጫ በደረሰም ጊዜ ለእነሱ ከበታችዋ መከለያን ባላደረግንላቸው ሕዝቦች ላይ ስትወጣ አገኛት፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا بَلَغَ مَطۡلِعَ ٱلشَّمۡسِ وَجَدَهَا تَطۡلُعُ عَلَىٰ قَوۡمٖ لَّمۡ نَجۡعَل لَّهُم مِّن دُونِهَا سِتۡرٗا ﴿٩٠﴾

91. (ነገሩ) እንደዚሁ ነው፡፡ እርሱም ዘንድ ባለው ነገር ሁሉ በእርግጥ በዕውቀት ከበብን፡፡

كَذَٰلِكَۖ وَقَدۡ أَحَطۡنَا بِمَا لَدَيۡهِ خُبۡرٗا ﴿٩١﴾

92. ከዚያም (ወደ ሰሜን አቅጣጫ) መንገድን ቀጠለ፡፡

ثُمَّ أَتۡبَعَ سَبَبًا ﴿٩٢﴾

93. በሁለቱ ጋራዎችም መካከል በደረሰ ጊዜ በአቅራቢያቸው ንግግርን ለማወቅ የማይቃረቡ ሕዝቦችን አገኘ፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا بَلَغَ بَيۡنَ ٱلسَّدَّيۡنِ وَجَدَ مِن دُونِهِمَا قَوۡمٗا لَّا يَكَادُونَ يَفۡقَهُونَ قَوۡلٗا ﴿٩٣﴾

94. «ዙልቀርነይን ሆይ! የእጁጅና መእጁጅ በምድር ላይ አበላሺዎች ናቸውና በእኛና በእነሱ መካከል ግድብን ታደርግልን ዘንድ ግብርን እናድርግልህን» አሉ፡፡

قَالُواْ يَٰذَا ٱلۡقَرۡنَيۡنِ إِنَّ يَأۡجُوجَ وَمَأۡجُوجَ مُفۡسِدُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَهَلۡ نَجۡعَلُ لَكَ خَرۡجًا عَلَىٰٓ أَن تَجۡعَلَ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَهُمۡ سَدّٗا ﴿٩٤﴾

95. አለ «ጌታዬ በእርሱ ያስመቸኝ ሀብት (ከናንተ ግብር) በላጭ ነው፡፡ ስለዚህ በጉልበት እገዙኝ፡፡ በእናንተና በእነሱ መካከል ብርቱን ግድብ አደርጋለሁና፡፡

قَالَ مَا مَكَّنِّي فِيهِ رَبِّي خَيۡرٞ فَأَعِينُونِي بِقُوَّةٍ أَجۡعَلۡ بَيۡنَكُمۡ وَبَيۡنَهُمۡ رَدۡمًا ﴿٩٥﴾

96. «የብረትን ታላላቅ ቁራጮች ስጡኝ» (አላቸው)፡፡ በሁለቱ ኮረብታዎች (ጫፍ) መካከልም ባስተካከለ ጊዜ አናፉ አላቸው፡፡ (ብረቱን) እሳትም ባደረገው ጊዜ «የቀለጠውን ነሐስ ስጡኝ፤ በርሱ ላይ አፈስበታለሁና» አላቸው፡፡

ءَاتُونِي زُبَرَ ٱلۡحَدِيدِۖ حَتَّىٰٓ إِذَا سَاوَىٰ بَيۡنَ ٱلصَّدَفَيۡنِ قَالَ ٱنفُخُواْۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَعَلَهُۥ نَارٗا قَالَ ءَاتُونِيٓ أُفۡرِغۡ عَلَيۡهِ قِطۡرٗا ﴿٩٦﴾

97. (የእጁጅና መእጁጅ) ሊወጡትም አልቻሉም፡፡ ለእርሱ መሸንቆርንም አልቻሉም፡፡

فَمَا ٱسۡطَٰعُوٓاْ أَن يَظۡهَرُوهُ وَمَا ٱسۡتَطَٰعُواْ لَهُۥ نَقۡبٗا ﴿٩٧﴾

98. «ይህ (ግድብ) ከጌታዬ ችሮታ ነው፡፡ የጌታየም ቀጠሮ በመጣ ጊዜ ትክክል ምድር ያደርገዋል፡፡ የጌታዬም ቀጠሮ ተረጋገጠ ነው» አለ፡፡

قَالَ هَٰذَا رَحۡمَةٞ مِّن رَّبِّيۖ فَإِذَا جَآءَ وَعۡدُ رَبِّي جَعَلَهُۥ دَكَّآءَۖ وَكَانَ وَعۡدُ رَبِّي حَقّٗا ﴿٩٨﴾

۞وَتَرَكۡنَا بَعۡضَهُمۡ يَوۡمَئِذٖ يَمُوجُ فِي بَعۡضٖۖ وَنُفِخَ فِي ٱلصُّورِ فَجَمَعۡنَٰهُمۡ جَمۡعٗا ٩٩

99. በዚያም ቀን ከፊላቸውን በከፊሉ የሚቀላቀሉ አድርገን እንተዋቸዋለን፡፡ በቀንዱም ይነፋል መሰብሰብንም እንሰበስባቸዋለን፡፤

وَعَرَضۡنَا جَهَنَّمَ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡكَٰفِرِينَ عَرۡضًا ١٠٠

100. ገሀነምንም በዚያ ቀን ለከሓዲዎች በጣም ማቅረብን እናቀርባታለን፡፡

ٱلَّذِينَ كَانَتۡ أَعۡيُنُهُمۡ فِي غِطَآءٍ عَن ذِكۡرِي وَكَانُواْ لَا يَسۡتَطِيعُونَ سَمۡعًا ١٠١

101. ለዚያ ዓይኖቻቸው ከግሳጼዬ በሺፋን ውስጥ ለነበሩትና መስማትንም የማይችሉ ለነበሩት (እናቀርባታለን)፡፡

أَفَحَسِبَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَن يَتَّخِذُواْ عِبَادِي مِن دُونِيٓ أَوۡلِيَآءَۚ إِنَّآ أَعۡتَدۡنَا جَهَنَّمَ لِلۡكَٰفِرِينَ نُزُلٗا ١٠٢

102. እነዚያ የካዱት ባሮቼን ከእኔ ሌላ አማልክት አድርገው መያዛቸውን (የማያስቆጣኝ አድርገው) አሰቡን እኛ ገሀነምን ለከሓዲዎች መስተንግዶ አዘጋጅተናል፡፡

قُلۡ هَلۡ نُنَبِّئُكُم بِٱلۡأَخۡسَرِينَ أَعۡمَٰلًا ١٠٣

103. «በሥራዎች በጣም ከሳሪዎቹን እንንገራችሁን» በላቸው፡፡

ٱلَّذِينَ ضَلَّ سَعۡيُهُمۡ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَهُمۡ يَحۡسَبُونَ أَنَّهُمۡ يُحۡسِنُونَ صُنۡعًا ١٠٤

104. እነዚያ እነሱ ሥራን የሚያሳምሩ የሚመስላቸው ሲሆኑ በቅርቢቱ ሕይወት ሥራቸው የጠፋባቸው ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمۡ وَلِقَآئِهِۦ فَحَبِطَتۡ أَعۡمَٰلُهُمۡ فَلَا نُقِيمُ لَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ وَزۡنٗا ١٠٥

105. እነዚያ እነርሱ በጌታቸው ማስረጃዎችና በመገናኘቱ የካዱት ናቸው፡፡ ሥራዎቻቸውም ተበላሹ፡ ፡ ለእነሱም በትንሣኤ ቀን (ጠቃሚ) ሚዛንን አናቆምላቸውም፡፡

ذَٰلِكَ جَزَآؤُهُمۡ جَهَنَّمُ بِمَا كَفَرُواْ وَٱتَّخَذُوٓاْ ءَايَٰتِي وَرُسُلِي هُزُوًا ١٠٦

106. (ነገሩ) ይህ ነው፡፡ በክህደታቸው አንቀጾቼንና መልክተኞቼንም መሳለቂያ አድርገው በመያዛቸው ፍዳቸው ገሀነም ነው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ كَانَتۡ لَهُمۡ جَنَّٰتُ ٱلۡفِرۡدَوۡسِ نُزُلًا ١٠٧

107. እነዚያ ያመኑና መልካም ሥራዎችን የሠሩ የፊርደውስ ገነቶች ለእነሱ መስፈሪያ ናቸው፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَا لَا يَبۡغُونَ عَنۡهَا حِوَلٗا ١٠٨

108. በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ከእርሷ መዛወርን የማይፈልጉ ሲኾኑ፤ (መስፈሪያቸው ነው)፡፡

قُل لَّوۡ كَانَ ٱلۡبَحۡرُ مِدَادٗا لِّكَلِمَٰتِ رَبِّي لَنَفِدَ ٱلۡبَحۡرُ قَبۡلَ أَن تَنفَدَ كَلِمَٰتُ رَبِّي وَلَوۡ جِئۡنَا بِمِثۡلِهِۦ مَدَدٗا ١٠٩

109. «ባሕሩ ለጌታዬ ቃላት (መጻፊያ) ቀለሞችን በሆነ ኖሮ ብጤውን ጭማሪ ብናመጣም እንኳን የጌታዬ ቃላት ከማለቋ በፊት ባሕሩ ባለቀ ነበር» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّمَآ أَنَا۠ بَشَرٞ مِّثۡلُكُمۡ يُوحَىٰٓ إِلَيَّ أَنَّمَآ إِلَٰهُكُمۡ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞۖ فَمَن كَانَ يَرۡجُواْ لِقَآءَ رَبِّهِۦ فَلۡيَعۡمَلۡ عَمَلٗا صَٰلِحٗا وَلَا يُشۡرِكۡ بِعِبَادَةِ رَبِّهِۦٓ أَحَدَۢا ١١٠

110. «እኔ አምላካችሁ አንድ አምላክ ብቻ ነው ማለት ወደኔ የሚወረድልኝ ቢጤያችሁ ሰው ብቻ ነኝ፡፡ የጌታውንም መገናኘት የሚፈልግ ሰው፤ መልካም ሥራን ይሥራ፡፡ በጌታውም መገዛት አንድንም አያጋራ» በላቸው፡፡

# ሱረቱ መርየም

# سورة مريم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ክ.ሀ.የ.ዐ.ጸ (ካፍ ሃ ያ ዓይን ሷድ)

كٓهيعٓصٓ ١

2. (ይህ) ጌታህ ባሪያውን ዘከሪያን በችሮታው ያወሳበት ነው፡፡

ذِكۡرُ رَحۡمَتِ رَبِّكَ عَبۡدَهُۥ زَكَرِيَّآ ٢

3. ጌታውን የምስጢርን ጥሪ በተጣራ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ نَادَىٰ رَبَّهُۥ نِدَآءً خَفِيّٗا ٣

4. አለ «ጌታዬ ሆይ! እኔ አጥንቴ ደከመ፤ ራሴም በሺበት ተንቀለቀለ፤ አንተም በመለመኔ ጌታዬ ሆይ! (ምንጊዜም) ዕድለ ቢስ አልሆንኩም፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّي وَهَنَ ٱلۡعَظۡمُ مِنِّي وَٱشۡتَعَلَ ٱلرَّأۡسُ شَيۡبٗا وَلَمۡ أَكُنۢ بِدُعَآئِكَ رَبِّ شَقِيّٗا ٤

5. «እኔም ከበኋላዬ ዘመዶቼን በእርግጥ ፈራሁ፡፡ ሚስቴም መካን ነበረች ስለዚህ ከአንተ ዘንድ ለኔ ልጅን ስጠኝ፡፡

وَإِنِّي خِفۡتُ ٱلۡمَوَٰلِيَ مِن وَرَآءِي وَكَانَتِ ٱمۡرَأَتِي عَاقِرٗا فَهَبۡ لِي مِن لَّدُنكَ وَلِيّٗا ٥

6. «የሚወርሰኝ ከያዕቆብ ቤተሰቦችም የሚወርስ የሆነን (ልጅ)፡፡ ጌታዬ ሆይ! ተወዳጅም አድርገው፡፡»

يَرِثُنِي وَيَرِثُ مِنۡ ءَالِ يَعۡقُوبَۖ وَٱجۡعَلۡهُ رَبِّ رَضِيّٗا ٦

7. «ዘከሪያ ሆይ! እኛ በወንድ ልጅ ስሙ የሕያ በኾነ ከዚህ በፊት ሞክሼን ባላደረግንለት እናበስርሃለን» (አለው)፡፡

يَٰزَكَرِيَّآ إِنَّا نُبَشِّرُكَ بِغُلَٰمٍ ٱسۡمُهُۥ يَحۡيَىٰ لَمۡ نَجۡعَل لَّهُۥ مِن قَبۡلُ سَمِيّٗا ٧

8. «ጌታዬ ሆይ! ሚስቴ መካን የነበረች ስትኾን እኔም ከእርጅና ድርቀትን በእርግጥ የደረስኩ ስኾን እንዴት ልጅ ይኖረኛል!» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ أَنَّىٰ يَكُونُ لِي غُلَٰمٞ وَكَانَتِ ٱمۡرَأَتِي عَاقِرٗا وَقَدۡ بَلَغۡتُ مِنَ ٱلۡكِبَرِ عِتِيّٗا ٨

9. (ጅብሪል) አለ «(ነገሩ) እንደዚሁ ነው፡፡ ጌታህ፡- ከአሁን በፊት ምንም ያልነበርከውን የፈጠርኩህ ስኾን እርሱ በእኔ ላይ ቀላል ነው» አለ፡፡

قَالَ كَذَٰلِكَ قَالَ رَبُّكَ هُوَ عَلَيَّ هَيِّنٞ وَقَدۡ خَلَقۡتُكَ مِن قَبۡلُ وَلَمۡ تَكُ شَيۡـٔٗا ٩

10. «ጌታዬ ሆይ! (እንግዲያውስ) ለእኔ ምልክትን አድርግልኝ አለ፡፡ ምልክትህ ጤናማ ሆነህ ሳለህ ሦስት ሌሊትን (ከነቀናቸው) ሰዎችን ለማነጋገር አለመቻልህ ነው» አለው፡፡

قَالَ رَبِّ ٱجۡعَل لِّيٓ ءَايَةٗۖ قَالَ ءَايَتُكَ أَلَّا تُكَلِّمَ ٱلنَّاسَ ثَلَٰثَ لَيَالٖ سَوِيّٗا ١٠

11. ከምኩራቡም በሕዝቦቹ ላይ ወጣ፡፡ በ×ትና በማታ (ጌታችሁን) አወድሱ በማለትም ወደነሱ ጠቀሰ፡፡

فَخَرَجَ عَلَىٰ قَوۡمِهِۦ مِنَ ٱلۡمِحۡرَابِ فَأَوۡحَىٰٓ إِلَيۡهِمۡ أَن سَبِّحُواْ بُكۡرَةٗ وَعَشِيّٗا ١١

12. «የሕያ ሆይ! መጽሐፉን በጥብቅ ያዝ!» (አልነው)፡፡ ጥበብንም በሕፃንነቱ ሰጠነው፡፡
13. ከእኛም የሆነን ርኅራኄ ንጽሕናንም (ሰጠነው)፡፡ ጥንቁቅም ነበር፡፡
14. ለወላጆቹም በጎ ሠሪ ነበር፡፡ ትዕቢተኛ አመጸኛም አልነበረም፡፡
15. በተወለደበት ቀንና በሚሞትበትም ቀን፣ ሕያው ሆኖ በሚነሳበትም ቀን ሰላም በእሱ ላይ ይሁን፡፡
16. በመጽሐፉ ውስጥ መርየምንም ከቤተሰቧ ወደ ምሥራቃዊ ስፍራ በተለይች ጊዜ (የሆነውን ታሪኳን) አውሳ፡፡

17. ከእነሱም መጋረጃን አደረገች፡፡ መንፈሳችንምም (ጂብሪልን) ወደርሷ ላክን፡፡ ለእርሷም ትክክለኛ ሰው ሆኖ ተመሰለላት፡፡

18. «እኔ ከአንተ በአልረሕማን እጠበቃለሁ፡፡ ጌታህን ፈሪ እንደ ሆንክ (አትቅረበኝ)» አለች፡፡
19. «እኔ ንጹሕን ልጅ ለአንቺ ልሰጥሽ የጌታሽ መልክተኛ ነኝ» አላት፡፡
20. «(በጋብቻ) ሰው ያልነካኝ ሆኜ አመንዝራም ሳልሆን ለእኔ እንዴት ልጅ ይኖረኛል!» አለች፡፡

21. አላት «(ነገሩ) እንደዚህሽ ነው፡፡» ጌታሽ «እርሱ በእኔ ላይ ገር ነው፡፡ ለሰዎችም ታምር ከእኛም ችሮታ ልናደርገው (ይህንን ሠራን) የተፈረደም ነገር ነው» አለ፤ (ነፋባትም)፡፡
22. ወዲያውኑም አረገዘችው፡፡ በእርሱም (በሆዷ ይዛው) ወደ ሩቅ ስፍራ ገለል አለች፡፡
23. ምጡም ወደ ዘንባባይቱ ግንድ አስጠጋት፡፡ «ዋ ምኞቴ! ምነው ከዚህ በፊት በሞትኩ፡፡ ተረስቼም የቀረሁ በሆንኩ» አለች፡፡

24. ከበታቿም እንዲህ ሲል ጠራት «አትዘኚ፡፡ ጌታሽ ከበታችሽ ትንሽን ወንዝ በእርግጥ አድርጓል፡፡
25. «የዘምባባይቱንም ግንድ ወዳንቺ ወዝውዢት ባንቺ ላይ የበሰለን የተምር እሸት ታረግፍልሻለችና፡፡
26. «ብይም፣ ጠጪም፣ ተደሰችም፡፡ እኔ ለአልረሕማን ዝምታን ተስያለሁ፤ ዛሬም ሰውን በፍጹም አላነጋግርም» በይ፡፡

يَٰيَحۡيَىٰ خُذِ ٱلۡكِتَٰبَ بِقُوَّةٖۖ وَءَاتَيۡنَٰهُ ٱلۡحُكۡمَ صَبِيّٗا ١٢

وَحَنَانٗا مِّن لَّدُنَّا وَزَكَوٰةٗۖ وَكَانَ تَقِيّٗا ١٣

وَبَرَّۢا بِوَٰلِدَيۡهِ وَلَمۡ يَكُن جَبَّارًا عَصِيّٗا ١٤

وَسَلَٰمٌ عَلَيۡهِ يَوۡمَ وُلِدَ وَيَوۡمَ يَمُوتُ وَيَوۡمَ يُبۡعَثُ حَيّٗا ١٥

وَٱذۡكُرۡ فِي ٱلۡكِتَٰبِ مَرۡيَمَ إِذِ ٱنتَبَذَتۡ مِنۡ أَهۡلِهَا مَكَانٗا شَرۡقِيّٗا ١٦

فَٱتَّخَذَتۡ مِن دُونِهِمۡ حِجَابٗا فَأَرۡسَلۡنَآ إِلَيۡهَا رُوحَنَا فَتَمَثَّلَ لَهَا بَشَرٗا سَوِيّٗا ١٧

قَالَتۡ إِنِّيٓ أَعُوذُ بِٱلرَّحۡمَٰنِ مِنكَ إِن كُنتَ تَقِيّٗا ١٨

قَالَ إِنَّمَآ أَنَا۠ رَسُولُ رَبِّكِ لِأَهَبَ لَكِ غُلَٰمٗا زَكِيّٗا ١٩

قَالَتۡ أَنَّىٰ يَكُونُ لِي غُلَٰمٞ وَلَمۡ يَمۡسَسۡنِي بَشَرٞ وَلَمۡ أَكُ بَغِيّٗا ٢٠

قَالَ كَذَٰلِكِ قَالَ رَبُّكِ هُوَ عَلَيَّ هَيِّنٞۖ وَلِنَجۡعَلَهُۥٓ ءَايَةٗ لِّلنَّاسِ وَرَحۡمَةٗ مِّنَّاۚ وَكَانَ أَمۡرٗا مَّقۡضِيّٗا ٢١

۞فَحَمَلَتۡهُ فَٱنتَبَذَتۡ بِهِۦ مَكَانٗا قَصِيّٗا ٢٢

فَأَجَآءَهَا ٱلۡمَخَاضُ إِلَىٰ جِذۡعِ ٱلنَّخۡلَةِ قَالَتۡ يَٰلَيۡتَنِي مِتُّ قَبۡلَ هَٰذَا وَكُنتُ نَسۡيٗا مَّنسِيّٗا ٢٣

فَنَادَىٰهَا مِن تَحۡتِهَآ أَلَّا تَحۡزَنِي قَدۡ جَعَلَ رَبُّكِ تَحۡتَكِ سَرِيّٗا ٢٤

وَهُزِّيٓ إِلَيۡكِ بِجِذۡعِ ٱلنَّخۡلَةِ تُسَٰقِطۡ عَلَيۡكِ رُطَبٗا جَنِيّٗا ٢٥

فَكُلِي وَٱشۡرَبِي وَقَرِّي عَيۡنٗاۖ فَإِمَّا تَرَيِنَّ مِنَ ٱلۡبَشَرِ أَحَدٗا فَقُولِيٓ إِنِّي نَذَرۡتُ لِلرَّحۡمَٰنِ صَوۡمٗا فَلَنۡ أُكَلِّمَ ٱلۡيَوۡمَ إِنسِيّٗا ٢٦

27. በእርሱም የተሸከመቺው ሆና ወደ ዘመዶቿ መጣች፡፡ «መርየም ሆይ! ከባድን ነገር በእርግጥ ሠራሽ» አሏት፡፡

فَأَتَتۡ بِهِۦ قَوۡمَهَا تَحۡمِلُهُۥۖ قَالُواْ يَٰمَرۡيَمُ لَقَدۡ جِئۡتِ شَيۡـٔٗا فَرِيّٗا ٢٧

28. «የሃሩን እኅት ሆይ! አባትሽ መጥፎ ሰው አልነበረም፡፡ እናትሽም አመንዝራ አልነበረችም» አሏት፡፡

يَٰٓأُخۡتَ هَٰرُونَ مَا كَانَ أَبُوكِ ٱمۡرَأَ سَوۡءٖ وَمَا كَانَتۡ أُمُّكِ بَغِيّٗا ٢٨

29. ወደርሱም ጠቀሰች፡፡ «በአንቀልባ ያለን ሕጻን እንዴት እናናግራለን!» አሉ፡፡

فَأَشَارَتۡ إِلَيۡهِۖ قَالُواْ كَيۡفَ نُكَلِّمُ مَن كَانَ فِي ٱلۡمَهۡدِ صَبِيّٗا ٢٩

30. (ሕፃኑም) አለ «እኔ የአላህ ባሪያ ነኝ፡፡ መጽሐፍን ሰጥቶኛል ነቢይም አድርጎኛል፡፡»

قَالَ إِنِّي عَبۡدُ ٱللَّهِ ءَاتَىٰنِيَ ٱلۡكِتَٰبَ وَجَعَلَنِي نَبِيّٗا ٣٠

31. «በየትም ስፍራ ብሆን ብሩክ አድርጎኛል፡፡ በሕይወትም እስካለሁ ሶላትን በመስገድ ዘካንም በመስጠት አዞኛል፡፡»

وَجَعَلَنِي مُبَارَكًا أَيۡنَ مَا كُنتُ وَأَوۡصَٰنِي بِٱلصَّلَوٰةِ وَٱلزَّكَوٰةِ مَا دُمۡتُ حَيّٗا ٣١

32. «ለእናቴም ታዛዥ (አድርጎኛል)፡፡ ትዕቢተኛ እምቢተኛም አላደረገኝም፡፡

وَبَرَّۢا بِوَٰلِدَتِي وَلَمۡ يَجۡعَلۡنِي جَبَّارٗا شَقِيّٗا ٣٢

33. «ሰላምም በእኔ ላይ ነው፡፡ በተወለድሁ ቀን፣ በምሞትበትም ቀን፣ ሕያው ኾኜ በምቀሰቀስበትም ቀን፡ ፡»

وَٱلسَّلَٰمُ عَلَيَّ يَوۡمَ وُلِدتُّ وَيَوۡمَ أَمُوتُ وَيَوۡمَ أُبۡعَثُ حَيّٗا ٣٣

34. ይህ የመርየም ልጅ ዒሳ ነው፡፡ ያ በርሱ የሚጠራጠሩበት እውነተኛ ቃል ነው፡፡

ذَٰلِكَ عِيسَى ٱبۡنُ مَرۡيَمَۖ قَوۡلَ ٱلۡحَقِّ ٱلَّذِي فِيهِ يَمۡتَرُونَ ٣٤

35. ለአላህ ልጅን መያዝ አይገባውም፡፡ (ከጉድለት ሁሉ) ጠራ፡፡ ነገርን በሻ ጊዜ ለርሱ የሚለው «ኹን» ነው ወዲያውም ይኾናል፡፡

مَا كَانَ لِلَّهِ أَن يَتَّخِذَ مِن وَلَدٖۖ سُبۡحَٰنَهُۥٓۚ إِذَا قَضَىٰٓ أَمۡرٗا فَإِنَّمَا يَقُولُ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ٣٥

36. (ዒሳ አለ) «አላህም ጌታዬ ጌታችሁም ነውና ተገዙት፡፡ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው፡፡»

وَإِنَّ ٱللَّهَ رَبِّي وَرَبُّكُمۡ فَٱعۡبُدُوهُۚ هَٰذَا صِرَٰطٞ مُّسۡتَقِيمٞ ٣٦

37. ከመካከላቸውም አሕዛቦቹ በእርሱ ነገር ተለያዩ፡፡ ለእነዚያም ለካዱት ሰዎች ከታላቁ ቀን መጋፊጥ ወዮላቸው፡፡

فَٱخۡتَلَفَ ٱلۡأَحۡزَابُ مِنۢ بَيۡنِهِمۡۖ فَوَيۡلٞ لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن مَّشۡهَدِ يَوۡمٍ عَظِيمٍ ٣٧

38. በሚመጡን ቀን ምን ሰሚ ምንስ ተመልካች አደረጋቸው! ግን አመጸኞች ዛሬ (በዚህ ዓለም) በግልጽ ስህተት ውስጥ ናቸው፡፤

أَسۡمِعۡ بِهِمۡ وَأَبۡصِرۡ يَوۡمَ يَأۡتُونَنَاۖ لَٰكِنِ ٱلظَّٰلِمُونَ ٱلۡيَوۡمَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ٣٨

39. እነሱም (አሁን) በዝንጋቴ ላይ ኾነው ሳሉ እነሱም የማያምኑ ሲኾኑ ነገሩ በሚፈረድበት ጊዜ የቁልጭቱን ቀን አስፈራራቸው፡፡

وَأَنذِرۡهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡحَسۡرَةِ إِذۡ قُضِيَ ٱلۡأَمۡرُ وَهُمۡ فِي غَفۡلَةٖ وَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ٣٩

40. እኛ ምድርን በእርሷም ላይ ያለውን ሁሉ እኛ እንወርሳለን፡፡ ወደኛም ይመለሳሉ፡፡

إِنَّا نَحۡنُ نَرِثُ ٱلۡأَرۡضَ وَمَنۡ عَلَيۡهَا وَإِلَيۡنَا يُرۡجَعُونَ ٤٠

41. በመጽሐፉ ውስጥ ኢብራሂምንም አውሳ፡፡ እርሱ በጣም እውነተኛ ነቢይ ነበርና፡፡

وَٱذْكُرْ فِى ٱلْكِتَٰبِ إِبْرَٰهِيمَ ۚ إِنَّهُۥ كَانَ صِدِّيقًا نَّبِيًّا ﴿٤١﴾

42. ለአባቱ ባለ ጊዜ (አስታውስ) «አባቴ ሆይ! የማይሰማንና የማያይን ከአንተም ምንንም የማይጠቅምህን (ጣዖት) ለምን ትግገዛለህ

إِذْ قَالَ لِأَبِيهِ يَٰٓأَبَتِ لِمَ تَعْبُدُ مَا لَا يَسْمَعُ وَلَا يُبْصِرُ وَلَا يُغْنِى عَنكَ شَيْـًٔا ﴿٤٢﴾

43. «አባቴ ሆይ! እኔ ከዕውቀት ያልመጣልህ ነገር በእርግጥ መጥቶልኛልና ተከተለኝ፡፡ ቀጥተኛውን መንገድ እመራሃለሁና፡፡

يَٰٓأَبَتِ إِنِّى قَدْ جَآءَنِى مِنَ ٱلْعِلْمِ مَا لَمْ يَأْتِكَ فَٱتَّبِعْنِىٓ أَهْدِكَ صِرَٰطًا سَوِيًّا ﴿٤٣﴾

44. «አባቴ ሆይ! ሰይጣንን አትግገዛ፡፡ ሰይጣን ለአልረሕማን አመጸኛ ነውና፡፡

يَٰٓأَبَتِ لَا تَعْبُدِ ٱلشَّيْطَٰنَ ۖ إِنَّ ٱلشَّيْطَٰنَ كَانَ لِلرَّحْمَٰنِ عَصِيًّا ﴿٤٤﴾

45. «አባቴ ሆይ! እኔ ከአልረሕማን ቅጣት ሊያገኝህ ለሰይጣንም ጓደኛ ልትኾን እፈራለሁ፡፡»

يَٰٓأَبَتِ إِنِّىٓ أَخَافُ أَن يَمَسَّكَ عَذَابٌ مِّنَ ٱلرَّحْمَٰنِ فَتَكُونَ لِلشَّيْطَٰنِ وَلِيًّا ﴿٤٥﴾

46. (አባቱም) «ኢብራሂም ሆይ! አንተ አምላኮቼን ትተህ የምትዞር ነህን ባትከለከል በእርግጥ እወግርሃለሁ፡፡ ረዥም ጊዜንም ተወኝ» አለ፡፡

قَالَ أَرَاغِبٌ أَنتَ عَنْ ءَالِهَتِى يَٰٓإِبْرَٰهِيمُ ۖ لَئِن لَّمْ تَنتَهِ لَأَرْجُمَنَّكَ ۖ وَٱهْجُرْنِى مَلِيًّا ﴿٤٦﴾

47. «ደህና ኹን፡፡ ወደፊት ከጌታዬ ምሕረትን እለምንልሃለሁ፡፡ እርሱ ለኔ በጣም ርኅሩኅ ነውና» አለ፡ ፡

قَالَ سَلَٰمٌ عَلَيْكَ ۖ سَأَسْتَغْفِرُ لَكَ رَبِّىٓ ۖ إِنَّهُۥ كَانَ بِى حَفِيًّا ﴿٤٧﴾

48. «እናንተንም ከአላህ ሌላ የምትግገዙትንም እርቃለሁ፡፡ ጌታዬንም እግገዛለሁ፡፡ ጌታዬን በመገዛት የማፍር አለመኾኔን እከጅላለሁ፡፡»

وَأَعْتَزِلُكُمْ وَمَا تَدْعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَأَدْعُوا۟ رَبِّى عَسَىٰٓ أَلَّآ أَكُونَ بِدُعَآءِ رَبِّى شَقِيًّا ﴿٤٨﴾

49. እነርሱንም ከአላህ ሌላ የሚግገዙትንም በራቀ ጊዜ ለእርሱ ኢስሐቅንና ያዕቆብን ሰጠነው፡፡ ሁሉንም ነቢይ አደረግንም፡፡

فَلَمَّا ٱعْتَزَلَهُمْ وَمَا يَعْبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَهَبْنَا لَهُۥٓ إِسْحَٰقَ وَيَعْقُوبَ ۖ وَكُلًّا جَعَلْنَا نَبِيًّا ﴿٤٩﴾

50. ለእነሱም ከችሮታችን ሰጠናቸው፡፡ ለእነርሱም ከፍ ያለ ምስጉን ዝናን አደረግንላቸው፡፡

وَوَهَبْنَا لَهُم مِّن رَّحْمَتِنَا وَجَعَلْنَا لَهُمْ لِسَانَ صِدْقٍ عَلِيًّا ﴿٥٠﴾

51. በመጽሐፉ ውስጥ ሙሳንም አውሳ፡፡ እርሱ ምርጥ ነበርና፡፡ መልክተኛ ነቢይም ነበር፡፡

وَٱذْكُرْ فِى ٱلْكِتَٰبِ مُوسَىٰٓ ۚ إِنَّهُۥ كَانَ مُخْلَصًا وَكَانَ رَسُولًا نَّبِيًّا ﴿٥١﴾

52. ከጡር ቀኝ ጎን በኩልም ጠራነው፡፡ ያነጋገርነውም ሲኾን አቀረብነው፡፡

وَنَٰدَيْنَٰهُ مِن جَانِبِ ٱلطُّورِ ٱلْأَيْمَنِ وَقَرَّبْنَٰهُ نَجِيًّا ﴿٥٢﴾

53. ከችሮታችንም ወንድሙን ሃሩንን ነቢይ አድርገን ሰጠነው፡፡

وَوَهَبْنَا لَهُۥ مِن رَّحْمَتِنَآ أَخَاهُ هَٰرُونَ نَبِيًّا ﴿٥٣﴾

54. በመጽሐፉ ኢስማዒልንም አውሳ፡፡ እርሱ ቀጠሮን አክባሪ ነበረና፡፡ መልክተኛ ነቢይም ነበር፡፡

وَٱذۡكُرۡ فِي ٱلۡكِتَٰبِ إِسۡمَٰعِيلَۚ إِنَّهُۥ كَانَ صَادِقَ ٱلۡوَعۡدِ وَكَانَ رَسُولٗا نَّبِيّٗا ﴿٥٤﴾

55. ቤተሰቦቹንም በሶላትና በዘካ ያዝ ነበር፡፡ እጌታውም ዘንድ ተወዳጅ ነበር፡፡

وَكَانَ يَأۡمُرُ أَهۡلَهُۥ بِٱلصَّلَوٰةِ وَٱلزَّكَوٰةِ وَكَانَ عِندَ رَبِّهِۦ مَرۡضِيّٗا ﴿٥٥﴾

56. በመጽሐፉ ኢድሪስንም (ሄኖክን) አውሳ፡፡ እርሱ እውነተኛ ነቢይ ነበርና፡፡

وَٱذۡكُرۡ فِي ٱلۡكِتَٰبِ إِدۡرِيسَۚ إِنَّهُۥ كَانَ صِدِّيقٗا نَّبِيّٗا ﴿٥٦﴾

57. ወደ ከፍተኛም ስፍራ አነሳነው፡፡

وَرَفَعۡنَٰهُ مَكَانًا عَلِيًّا ﴿٥٧﴾

58. እነዚህ (ዐሥሩ) እነዚያ አላህ በእነሱ ላይ የለገሰላቸው ከነቢያት ከአዳም ዘር ከኑሕ ጋር (በመርከቢቱ ላይ) ከጫናቸውም (ዘሮች) ከኢብራሂምና ከእስራኤልም ዘሮች ከመራናቸውና ከመረጥናቸውም የኾኑት የአልረሕማን አንቀጾች በነሱ ላይ በተነበቡ ጊዜ ሰጋጆችና አልቃሾች ኾነው ይወድቃሉ፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ أَنۡعَمَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِم مِّنَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ مِن ذُرِّيَّةِ ءَادَمَ وَمِمَّنۡ حَمَلۡنَا مَعَ نُوحٖ وَمِن ذُرِّيَّةِ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡرَٰٓءِيلَ وَمِمَّنۡ هَدَيۡنَا وَٱجۡتَبَيۡنَآۚ إِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُ ٱلرَّحۡمَٰنِ خَرُّواْۤ سُجَّدٗا وَبُكِيّٗا۩ ﴿٥٨﴾

59. ከእነሱም በኋላ ሶላትን ያጓደሉ (የተዉ) ፍላጎቶችንም የተከተሉ መጥፎ ምትኮች ተተኩ! የገሀነምንም ሸለቆ በእርግጥ ያገኛሉ፡፡

۞فَخَلَفَ مِنۢ بَعۡدِهِمۡ خَلۡفٌ أَضَاعُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَٱتَّبَعُواْ ٱلشَّهَوَٰتِۖ فَسَوۡفَ يَلۡقَوۡنَ غَيًّا ﴿٥٩﴾

60. ግን የተጸጸተና ያመነም በጎንም ሥራ የሠራ ሰው እነዚህ ገነትን ይገባሉ፡፡ አንዳችንም አይበደሉም፡፡

إِلَّا مَن تَابَ وَءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَأُوْلَٰٓئِكَ يَدۡخُلُونَ ٱلۡجَنَّةَ وَلَا يُظۡلَمُونَ شَيۡـٔٗا ﴿٦٠﴾

61. የመኖሪያን ገነቶች ያችን አልረሕማን ለባሮቹ በሩቅ ኾነው ሳሉ ተስፋ ቃል የገባላቸውን (ይገባሉ)፡፡ እርሱ ተስፋው ተፈጻሚ ነውና፤

جَنَّٰتِ عَدۡنٍ ٱلَّتِي وَعَدَ ٱلرَّحۡمَٰنُ عِبَادَهُۥ بِٱلۡغَيۡبِۚ إِنَّهُۥ كَانَ وَعۡدُهُۥ مَأۡتِيّٗا ﴿٦١﴾

62. በእርሷ ሰላምን እንጂ ውድቅን ነገር አይሰሙም፡፡ ለእነሱም በርሷ ውስጥ ጧትም ማታም ሲሳያቸው አላቸው፡፡

لَّا يَسۡمَعُونَ فِيهَا لَغۡوًا إِلَّا سَلَٰمٗاۖ وَلَهُمۡ رِزۡقُهُمۡ فِيهَا بُكۡرَةٗ وَعَشِيّٗا ﴿٦٢﴾

63. ይህች ያቺ ከባሮቻችን ጥንቁቆች ለኾኑት የምናወርሳት ገነት ናት፡፡

تِلۡكَ ٱلۡجَنَّةُ ٱلَّتِي نُورِثُ مِنۡ عِبَادِنَا مَن كَانَ تَقِيّٗا ﴿٦٣﴾

64. (ጂብሪል አለ) «በጌታህም ትእዛዝ እንጅ አንወርድም፡፡ በፊታችን ያለው፣ በኋላችንም ያለው በዚህም መካከል ያለው ሁሉ የርሱ ነው፡፡ ጌታህም ረሺ አይደለም፡፡

وَمَا نَتَنَزَّلُ إِلَّا بِأَمۡرِ رَبِّكَۖ لَهُۥ مَا بَيۡنَ أَيۡدِينَا وَمَا خَلۡفَنَا وَمَا بَيۡنَ ذَٰلِكَۚ وَمَا كَانَ رَبُّكَ نَسِيّٗا ﴿٦٤﴾

65. (እርሱ) የሰማያትና የምድር በሁለቱም መካከል ላለው ሁሉ ጌታ ነውና ተገዛው፡፡ እርሱን በመገዛትም ላይ ታገስ፡፡ ለእርሱ ሞክሼን ታውቃለህን

رَّبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَا فَٱعۡبُدۡهُ وَٱصۡطَبِرۡ لِعِبَٰدَتِهِۦۚ هَلۡ تَعۡلَمُ لَهُۥ سَمِيّٗا ﴿٦٥﴾

66. ሰውም «በሞትኩ ጊዜ ወደፊት ሕያው ኾኜ (ከመቃብር) እወጣለሁን» ይላል፡፡

وَيَقُولُ ٱلۡإِنسَٰنُ أَءِذَا مَا مِتُّ لَسَوۡفَ أُخۡرَجُ حَيًّا ٦٦

67. ሰው ከአሁን በፊት ምንም ነገር ያልነበረ ሲኾን እኛ የፈጠርነው መኾኑን አያስታውስምን

أَوَلَا يَذۡكُرُ ٱلۡإِنسَٰنُ أَنَّا خَلَقۡنَٰهُ مِن قَبۡلُ وَلَمۡ يَكُ شَيۡـٔٗا ٦٧

68. በጌታህ እንምላለን ሰይጣናት ጋር በእርግጥ እንሰበስባቸዋለን፡፡ ከዚያም በገሀነም ዙሪያ የተንበረከኩ ኾነው፤ በእርግጥ እናቀርባቸዋለን፡፡

فَوَرَبِّكَ لَنَحۡشُرَنَّهُمۡ وَٱلشَّيَٰطِينَ ثُمَّ لَنُحۡضِرَنَّهُمۡ حَوۡلَ جَهَنَّمَ جِثِيّٗا ٦٨

69. ከዚያም ከየጭፍሮቹ ሁሉ ከእነርሱ ያንን (እርሱ) በአልረሕማን ላይ በድፍረት በጣም ብርቱ የኾነውን እናወጣለን፡፡

ثُمَّ لَنَنزِعَنَّ مِن كُلِّ شِيعَةٍ أَيُّهُمۡ أَشَدُّ عَلَى ٱلرَّحۡمَٰنِ عِتِيّٗا ٦٩

70. ከዚያም እኛ እነዚያን እነርሱ በእርሷ ለመግባት ተገቢ የኾኑትን እናውቃለን፡፡

ثُمَّ لَنَحۡنُ أَعۡلَمُ بِٱلَّذِينَ هُمۡ أَوۡلَىٰ بِهَا صِلِيّٗا ٧٠

71. ከእናንተም ወደ እርሷ ወራጅ እንጂ አንድም የለም፡፡ (መውረዱም) ጌታህ የፈረደው ግዴታ ነው፡፡

وَإِن مِّنكُمۡ إِلَّا وَارِدُهَاۚ كَانَ عَلَىٰ رَبِّكَ حَتۡمٗا مَّقۡضِيّٗا ٧١

72. ከዚያም እነዚያን የተጠነቀቁትን እናድናለን፡፡ አመጸኞቹንም የተንበረከኩ ኾነው በውስጧ እንተዋቸዋለን፡፡

ثُمَّ نُنَجِّي ٱلَّذِينَ ٱتَّقَواْ وَّنَذَرُ ٱلظَّٰلِمِينَ فِيهَا جِثِيّٗا ٧٢

73. በእነሱም ላይ አንቀጾቻችን ግልጽ መስረጃዎች ኾነው በተነበቡ ጊዜ እነዚያ የካዱት ለእነዚያ ላመኑት «ከሁለቱ ክፍሎች መኖሪያው የሚበልጠውና ሸንጎውም ይበልጥ የሚያምረው ማንኛው ነው» ይላሉ፡፡

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُنَا بَيِّنَٰتٖ قَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لِلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَيُّ ٱلۡفَرِيقَيۡنِ خَيۡرٞ مَّقَامٗا وَأَحۡسَنُ نَدِيّٗا ٧٣

74. ከእነሱም በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች እነሱ በቁሳቁስና በትርኢትም በጣም ያማሩትን ብዙዎችን አጥፍተናል፡፡

وَكَمۡ أَهۡلَكۡنَا قَبۡلَهُم مِّن قَرۡنٍ هُمۡ أَحۡسَنُ أَثَٰثٗا وَرِءۡيٗا ٧٤

75. «በስሕተት ውስጥ የኾነ ሰው አልረሕማን ለእርሱ ማዘግየትን ያዘገየዋል፡፡ የሚዛትባቸውንም ወይም ቅጣቱን ወይም ሰዓቲቱን ባዩ ጊዜ እርሱ ስፍራው መጥፎና ሰራዊቱ ደካማ የኾነው ሰው ማን እንደኾነ በእርግጥ ያውቃሉ» በላቸው፡፡

قُلۡ مَن كَانَ فِي ٱلضَّلَٰلَةِ فَلۡيَمۡدُدۡ لَهُ ٱلرَّحۡمَٰنُ مَدًّاۚ حَتَّىٰٓ إِذَا رَأَوۡاْ مَا يُوعَدُونَ إِمَّا ٱلۡعَذَابَ وَإِمَّا ٱلسَّاعَةَ فَسَيَعۡلَمُونَ مَنۡ هُوَ شَرّٞ مَّكَانٗا وَأَضۡعَفُ جُندٗا ٧٥

76. እነዚያንም የቀኑትን ሰዎች አላህ ቅንነትን ይጨምርላቸዋል፡፡ መልካሞቹ ቀሪዎች (ሥራዎች) እጌታህ ዘንድ በምንዳ በላጭ ናቸው፡፡ በመመለሻም የተሻሉ ናቸው፡፡

وَيَزِيدُ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ٱهۡتَدَوۡاْ هُدٗىۗ وَٱلۡبَٰقِيَٰتُ ٱلصَّٰلِحَٰتُ خَيۡرٌ عِندَ رَبِّكَ ثَوَابٗا وَخَيۡرٞ مَّرَدًّا ٧٦

77. ያንንም በአንቀጾቻችን የካደውን «(በትንሣኤ ቀን) ገንዘብም ልጅም በእርግጥ እሰጣለሁ ያለውንም አየህን»

أَفَرَءَيۡتَ ٱلَّذِي كَفَرَ بِـَٔايَٰتِنَا وَقَالَ لَأُوتَيَنَّ مَالٗا وَوَلَدًا ٧٧

78. ሩቁን ምስጢር ዐወቀን ወይስ አልረሕማን ዘንድ ቃል ኪዳንን ያዘ

أَطَّلَعَ ٱلۡغَيۡبَ أَمِ ٱتَّخَذَ عِندَ ٱلرَّحۡمَٰنِ عَهۡدٗا ٧٨

79. ይከልከል (አይሰጠውም)፡፡ የሚለውን ሁሉ በእርግጥ እንጽፋለን፡፡ ለእርሱም ከቅጣት ጭማሪን እንጨምርለታለን፡፡

كَلَّاۚ سَنَكۡتُبُ مَا يَقُولُ وَنَمُدُّ لَهُۥ مِنَ ٱلۡعَذَابِ مَدّٗا ٧٩

80. (አልለኝ) የሚለውንም ሁሉ እንወርሰዋለን፡፡ ብቻውንም ኾኖ ይመጣናል፡፡

وَنَرِثُهُۥ مَا يَقُولُ وَيَأۡتِينَا فَرۡدٗا ٨٠

81. ከአላህም ሌላ አማልክትን ለእነሱ መከበሪያ (አማላጅ) እንዲኾኑዋቸው ያዙ፡፡

وَٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ ءَالِهَةٗ لِّيَكُونُواْ لَهُمۡ عِزّٗا ٨١

82. ይከልከሉ፤ መገዛታቸውን በእርግጥ ይክዷቸዋል፡፡ በእነሱም ላይ ተቃራኒ ይኾኑባቸዋል፡፡

كَلَّاۚ سَيَكۡفُرُونَ بِعِبَادَتِهِمۡ وَيَكُونُونَ عَلَيۡهِمۡ ضِدًّا ٨٢

83. እኛ ሰይጣናትን በከሓዲዎች ላይ (በመጥፎ ሥራ) ማወባራትን የሚያወባሩዋቸው ሲኾኑ የላክን መኾናችንን አለየህምን

أَلَمۡ تَرَ أَنَّآ أَرۡسَلۡنَا ٱلشَّيَٰطِينَ عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ تَؤُزُّهُمۡ أَزّٗا ٨٣

84. በእነሱም (መቀጣት) ላይ አትቻኮል፡፡ ለእነሱ (ቀንን) መቁጠርን እንቆጥርላቸዋለንና፡፡

فَلَا تَعۡجَلۡ عَلَيۡهِمۡۖ إِنَّمَا نَعُدُّ لَهُمۡ عَدّٗا ٨٤

85. ምእምናንን የተከበሩ ጭፍሮች ኾነው ወደ አልረሕማን የምንሰበስብበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

يَوۡمَ نَحۡشُرُ ٱلۡمُتَّقِينَ إِلَى ٱلرَّحۡمَٰنِ وَفۡدٗا ٨٥

86. ከሓዲዎችንም የተጠሙ ኾነው ወደ ገሀነም የምንነዳበትን (ቀን አስታውስ)፡፡

وَنَسُوقُ ٱلۡمُجۡرِمِينَ إِلَىٰ جَهَنَّمَ وِرۡدٗا ٨٦

87. አልረሕማን ዘንድ ቃል ኪዳንን የያዘ ሰው ቢኾን እንጂ ማማለድን አይችሉም፡፡

لَّا يَمۡلِكُونَ ٱلشَّفَٰعَةَ إِلَّا مَنِ ٱتَّخَذَ عِندَ ٱلرَّحۡمَٰنِ عَهۡدٗا ٨٧

88. «አልረሕማንም ልጅን ያዘ (ወለደ)» አሉ፡፡

وَقَالُواْ ٱتَّخَذَ ٱلرَّحۡمَٰنُ وَلَدٗا ٨٨

89. ከባድ መጥፎን ነገር በእርግጥ አመጣችሁ፡፡

لَّقَدۡ جِئۡتُمۡ شَيۡـًٔا إِدّٗا ٨٩

90. ከእርሱ (ከንግግራቸው) ሰማያት ሊቀደዱ፣ ምድርም ልትሰነጠቅ፣ ጋራዎችም ተንደው ሊወድቁ ይቃረባሉ፡፡

تَكَادُ ٱلسَّمَٰوَٰتُ يَتَفَطَّرۡنَ مِنۡهُ وَتَنشَقُّ ٱلۡأَرۡضُ وَتَخِرُّ ٱلۡجِبَالُ هَدًّا ٩٠

91. ለአልረሕማን ልጅ አልለው ስለአሉ፡፡

أَن دَعَوۡاْ لِلرَّحۡمَٰنِ وَلَدٗا ٩١

92. ለአልረሕማን ልጅን መያዝ አይገባውም፡፡

وَمَا يَنۢبَغِي لِلرَّحۡمَٰنِ أَن يَتَّخِذَ وَلَدًا ٩٢

93. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ (በትንሣኤ ቀን) ለአልራሕማን ባሪያ ኾነው የሚመጡ እንጂ ሌላ አይደሉም፡፡

إِن كُلُّ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ إِلَّآ ءَاتِي ٱلرَّحۡمَٰنِ عَبۡدٗا ٩٣

94. በእርግጥ (በዕውቀቱ) ከቧቸዋል፡፡ መቁጠርንም ቆጥሯቸዋል፡፡

لَّقَدۡ أَحۡصَىٰهُمۡ وَعَدَّهُمۡ عَدّٗا ٩٤

95. ሁሉም በትንሣኤ ቀን ለየብቻ ኾነው ወደርሱ መጪዎች ናቸው፡፡

وَكُلُّهُمۡ ءَاتِيهِ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فَرۡدًا ٩٥

96. እነዚያ ያመኑና በጎ ሥራዎችን የሠሩ አልረሕማን ለእነሱ ውዴታን ይሰጣቸዋል፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ سَيَجۡعَلُ لَهُمُ ٱلرَّحۡمَٰنُ وُدّٗا ٩٦

97. በምላስህም (ቁርኣንን) ያገራነው በእርሱ ጥንቁቆቹን ልታበስርበት በእርሱም ተከራካሪዎችን ሕዝቦች ልታስፈራራበት ነው፡፡

فَإِنَّمَا يَسَّرۡنَٰهُ بِلِسَانِكَ لِتُبَشِّرَ بِهِ ٱلۡمُتَّقِينَ وَتُنذِرَ بِهِۦ قَوۡمٗا لُّدّٗا ٩٧

98. ከእነሱም በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙዎችን አጥፍተናል፡፡ ከእነሱ አንድን እንኳ ታያለህን ወይስ ለእነሱ ሹክሹክታን ትሰማለህን

وَكَمۡ أَهۡلَكۡنَا قَبۡلَهُم مِّن قَرۡنٍ هَلۡ تُحِسُّ مِنۡهُم مِّنۡ أَحَدٍ أَوۡ تَسۡمَعُ لَهُمۡ رِكۡزَۢا ۝٩٨

# ሱረቱ ጣሃ

# سورة طه

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ጠ.ሀ. (ጣ ሃ)

طه ۝١

2. ቁርኣንን ባንተ ላይ እንድትቸገር አላወረድንም፡፡

مَآ أَنزَلۡنَا عَلَيۡكَ ٱلۡقُرۡءَانَ لِتَشۡقَىٰٓ ۝٢

3. ግን አላህን ለሚፈራ ሰው መገሰጫ ይኾን ዘንድ (አወረድነው)፡፡

إِلَّا تَذۡكِرَةٗ لِّمَن يَخۡشَىٰ ۝٣

4. ምድርንና የላይኞዎቹን ሰማያት ከፈጠረ አምላክ ተወረደ፡፡

تَنزِيلٗا مِّمَّنۡ خَلَقَ ٱلۡأَرۡضَ وَٱلسَّمَٰوَٰتِ ٱلۡعُلَى ۝٤

5. (እርሱ) አልረሕማን ነው በዐርሹ ላይ (ስልጣኑ) ተደላደለ፡፡

ٱلرَّحۡمَٰنُ عَلَى ٱلۡعَرۡشِ ٱسۡتَوَىٰ ۝٥

6. በሰማያት ያለው፣ በምድርም ያለው፣ በመካከላቸውም ያለው፣ ከዐፈር በታችም ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ ነው፡፡

لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَا وَمَا تَحۡتَ ٱلثَّرَىٰ ۝٦

7. በንግግር ብትጮህ (አላህ ከጩኸቱ የተብቃቃ ነው)፡ ፡ እርሱ ምስጢርን በጣም የተደበቀንም ያውቃልና፡፡

وَإِن تَجۡهَرۡ بِٱلۡقَوۡلِ فَإِنَّهُۥ يَعۡلَمُ ٱلسِّرَّ وَأَخۡفَى ۝٧

8. አላህ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ ለእርሱ መልካሞች የኾኑ ስሞች አሉት፡፡

ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ لَهُ ٱلۡأَسۡمَآءُ ٱلۡحُسۡنَىٰ ۝٨

9. የሙሳም ወሬ በእርግጥ መጥቶሃል፡፡

وَهَلۡ أَتَىٰكَ حَدِيثُ مُوسَىٰٓ ۝٩

10. እሳትን ባየና ለቤተሰቦቹ፡- (እዚህ) «ቆዩ፤ እኔ እሳትን አየሁ፡፡ ከእርሷ ችቦን ላመጣላችሁ፤ ወይም እሳቲቱ ዘንድ መሪን ላገኝ እከጅላለሁ» ባለጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ رَءَا نَارٗا فَقَالَ لِأَهۡلِهِ ٱمۡكُثُوٓاْ إِنِّيٓ ءَانَسۡتُ نَارٗا لَّعَلِّيٓ ءَاتِيكُم مِّنۡهَا بِقَبَسٍ أَوۡ أَجِدُ عَلَى ٱلنَّارِ هُدٗى ۝١٠

11. በመጣትም ጊዜ «ሙሳ ሆይ» በማለት ተጠራ፡፡

فَلَمَّآ أَتَىٰهَا نُودِيَ يَٰمُوسَىٰٓ ۝١١

12. «እኔ ጌታህ እኔ ነኝ መጫሚያዎችህንም አውልቅ፡፡ አንተ በተቀደሰው ሸለቆ በጡዋ ነህና፡፡

إِنِّيٓ أَنَا۠ رَبُّكَ فَٱخۡلَعۡ نَعۡلَيۡكَ إِنَّكَ بِٱلۡوَادِ ٱلۡمُقَدَّسِ طُوٗى ۝١٢

13. «እኔም መረጥኩህ፤ የሚወረድልህንም ነገር አዳምጥ፡፡

وَأَنَا ٱخۡتَرۡتُكَ فَٱسۡتَمِعۡ لِمَا يُوحَىٰٓ ۝١٣

14. «እኔ አላህ እኔ ነኝ ያለ እኔ አምላክ የለምና ተገዛኝ፡፡ ሶላትንም (በእርሷ) እኔን ለማውሳት ስገድ፡፡

إِنَّنِيٓ أَنَا ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّآ أَنَا۠ فَٱعۡبُدۡنِي وَأَقِمِ ٱلصَّلَوٰةَ لِذِكۡرِيٓ ١٤

15. «ሰዓቲቱ በእርግጥ መጪናት፡፡ ልደብቃት እቃረባለሁ፡፡ ነፍስ ሁሉ በምትሠራው ነገር ትመነዳ ዘንድ (መጭ ናት)፡፡

إِنَّ ٱلسَّاعَةَ ءَاتِيَةٌ أَكَادُ أُخۡفِيهَا لِتُجۡزَىٰ كُلُّ نَفۡسِۭ بِمَا تَسۡعَىٰ ١٥

16. «በእርሷ የማያምነውና ዝንባሌውን የተከተለውም ሰው ከእርሷ አያግድህ ትጠፋለህና፡፤

فَلَا يَصُدَّنَّكَ عَنۡهَا مَن لَّا يُؤۡمِنُ بِهَا وَٱتَّبَعَ هَوَىٰهُ فَتَرۡدَىٰ ١٦

17. «ሙሳ ሆይ! ይህችም በቀኝ እጅህ ያለችው ምንድን ናት» (ተባለ)፡፡

وَمَا تِلۡكَ بِيَمِينِكَ يَٰمُوسَىٰ ١٧

18. «እርሷ በትሬ ናት፡፡ በእርሷ ላይ እደገፍባታለሁ፣ በእርሷም ለፍየሎቼ ቅጠልን አረግፍባታለሁ፣ ለእኔም በእርሷ ሌሎች ጉዳዮች አሉኝ» አለ፡፡

قَالَ هِيَ عَصَايَ أَتَوَكَّؤُاْ عَلَيۡهَا وَأَهُشُّ بِهَا عَلَىٰ غَنَمِي وَلِيَ فِيهَا مَـَٔارِبُ أُخۡرَىٰ ١٨

19. (አላህም) «ሙሳ ሆይ! ጣላት» አለው፡፡

قَالَ أَلۡقِهَا يَٰمُوسَىٰ ١٩

20. ጣላትም፡፡ ወዲያውም እርሷ የምትሮጥ እባብ ኾነች፡፡

فَأَلۡقَىٰهَا فَإِذَا هِيَ حَيَّةٞ تَسۡعَىٰ ٢٠

21. «ያዛት፤ አትፍራም፡፡ ወደ መጀመሪያ ጠባይዋ እንመልሳታለን» አለው፡፡

قَالَ خُذۡهَا وَلَا تَخَفۡۖ سَنُعِيدُهَا سِيرَتَهَا ٱلۡأُولَىٰ ٢١

22. «እጅህንም ወደ ብብትህ አግባ፡፡ ሌላ ተዓምር ስትኾን ያለነውር ነጭ ኾና ትወጣለችና፡፡

وَٱضۡمُمۡ يَدَكَ إِلَىٰ جَنَاحِكَ تَخۡرُجۡ بَيۡضَآءَ مِنۡ غَيۡرِ سُوٓءٍ ءَايَةً أُخۡرَىٰ ٢٢

23. «ከተዓምራቶቻችን ታላቋን እናሳይህ ዘንድ (ይህን ሠራን)፡፡

لِنُرِيَكَ مِنۡ ءَايَٰتِنَا ٱلۡكُبۡرَى ٢٣

24. «ወደ ፈርዖን ኺድ፡፡ እርሱ ወሰን አልፏልና፡፡»

ٱذۡهَبۡ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ إِنَّهُۥ طَغَىٰ ٢٤

25. (ሙሳም) አለ «ጌታዬ ሆይ! ልቤን አስፋልኝ፡፡

قَالَ رَبِّ ٱشۡرَحۡ لِي صَدۡرِي ٢٥

26. «ነገሬንም ለእኔ አግራልኝ፡፡

وَيَسِّرۡ لِيٓ أَمۡرِي ٢٦

27. «ከምላሴም መኮላተፍን ፍታልኝ፡፡

وَٱحۡلُلۡ عُقۡدَةٗ مِّن لِّسَانِي ٢٧

28. «ንግግሬን ያውቃሉና፡፡

يَفۡقَهُواْ قَوۡلِي ٢٨

29. «ከቤተሰቦቼም ለእኔ ረዳትን አድርግልኝ፡፡

وَٱجۡعَل لِّي وَزِيرٗا مِّنۡ أَهۡلِي ٢٩

30. «ሃሩንን ወንድሜን፡፡

هَٰرُونَ أَخِي ٣٠

31. «ኃይሌን በእርሱ አበርታልኝ፡፡

ٱشۡدُدۡ بِهِۦٓ أَزۡرِي ﴿٣١﴾

32. «በነገሬም አጋራው፡፡

وَأَشۡرِكۡهُ فِيٓ أَمۡرِي ﴿٣٢﴾

33. «በብዙ እናጠራህ ዘንድ፡፡

كَيۡ نُسَبِّحَكَ كَثِيرٗا ﴿٣٣﴾

34. «በብዙም እንድናወሳህ፡፡

وَنَذۡكُرَكَ كَثِيرًا ﴿٣٤﴾

35. «አንተ በእኛ ነገር ዐዋቂ ነህና፡፡»

إِنَّكَ كُنتَ بِنَا بَصِيرٗا ﴿٣٥﴾

36. (አላህም) አለ «ሙሳ ሆይ! ልመናህን በእርግጥ ተሰጠህ፡፡

قَالَ قَدۡ أُوتِيتَ سُؤۡلَكَ يَٰمُوسَىٰ ﴿٣٦﴾

37. «በሌላም ጊዜ ባንተ ላይ በእርግጥ ለግሰናል፡፡

وَلَقَدۡ مَنَنَّا عَلَيۡكَ مَرَّةً أُخۡرَىٰٓ ﴿٣٧﴾

38. «ወደናትህ በልብ የሚፈስን ነገር ባሳወቅን ጊዜ፡፡

إِذۡ أَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰٓ أُمِّكَ مَا يُوحَىٰٓ ﴿٣٨﴾

39. «(ሕፃኑን) በሳጥኑ ውስጥ ጣይው፡፡ እርሱንም (ሳጥኑን) በባሕር ላይ ጣይው፡፡ ባሕሩም በዳርቻው ይጣለው፡፡ ለእኔ ጠላት ለእርሱም ጠላት የኾነ ሰው ይይዘዋልና በማለት (ባሳወቅን ጊዜ ለገስንልህ)፡፡ ባንተ ላይም ከእኔ የኾነን መወደድ ጣልኩብህ፡፡ (ልትወደድና) በእኔም ጥበቃ ታድግ ዘንድ፡፡

أَنِ ٱقۡذِفِيهِ فِي ٱلتَّابُوتِ فَٱقۡذِفِيهِ فِي ٱلۡيَمِّ فَلۡيُلۡقِهِ ٱلۡيَمُّ بِٱلسَّاحِلِ يَأۡخُذۡهُ عَدُوّٞ لِّي وَعَدُوّٞ لَّهُۥۚ وَأَلۡقَيۡتُ عَلَيۡكَ مَحَبَّةٗ مِّنِّي وَلِتُصۡنَعَ عَلَىٰ عَيۡنِيٓ ﴿٣٩﴾

40. «እኅትህም በምትኼድና የሚያሳድገውን ሰው ላመላከታችሁን በምትል ጊዜ (መወደድን ጣልኩብህ)፡፡ ወደ እናትህም ዓይንዋ እንዲረጋ (እርሷ) እንዳታዝንም መለስንህ፡፡ ነፍስንም ገደልክ፡፡ ከጭንቅም አዳንንህ፡፡ ፈተናዎችንም ፈተንህ፡፡ በመድየን ቤተሰቦችም ውስጥ (ብዙ) ዓመታትን ተቀመጥክ፡፡ ከዚያም ሙሳ ሆይ! በተወሰነ ጊዜ ላይ መጣህ፡፡

إِذۡ تَمۡشِيٓ أُخۡتُكَ فَتَقُولُ هَلۡ أَدُلُّكُمۡ عَلَىٰ مَن يَكۡفُلُهُۥۖ فَرَجَعۡنَٰكَ إِلَىٰٓ أُمِّكَ كَيۡ تَقَرَّ عَيۡنُهَا وَلَا تَحۡزَنَۚ وَقَتَلۡتَ نَفۡسٗا فَنَجَّيۡنَٰكَ مِنَ ٱلۡغَمِّ وَفَتَنَّٰكَ فُتُونٗاۚ فَلَبِثۡتَ سِنِينَ فِيٓ أَهۡلِ مَدۡيَنَ ثُمَّ جِئۡتَ عَلَىٰ قَدَرٖ يَٰمُوسَىٰ ﴿٤٠﴾

41. «ለነፍሴም (በመልእክቴ) መረጥኩህ፡፡

وَٱصۡطَنَعۡتُكَ لِنَفۡسِي ﴿٤١﴾

42. «አንተም ወንድምህም በተዓምራቶቼ ኺዱ፡፡ እኔንም ከማውሳት አትቦዝኑ፡፡

ٱذۡهَبۡ أَنتَ وَأَخُوكَ بِـَٔايَٰتِي وَلَا تَنِيَا فِي ذِكۡرِي ﴿٤٢﴾

43. «ወደ ፈርዖን ኺዱ፡፡ እርሱ ወሰን አልፏልና፡፡

ٱذۡهَبَآ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ إِنَّهُۥ طَغَىٰ ﴿٤٣﴾

44. «እርሱም ይገሰጽ ወይም ይፈራ ዘንድ፤ ለእርሱ ልዝብን ቃል ተናገሩት፡፡»

فَقُولَا لَهُۥ قَوۡلٗا لَّيِّنٗا لَّعَلَّهُۥ يَتَذَكَّرُ أَوۡ يَخۡشَىٰ ﴿٤٤﴾

45. «ጌታችን ሆይ! እኛ በእኛ ላይ ክፋት በመሥራት መቸኮሉን ወይም ኩራትን መጨመሩን እንፈራለን» አሉ፡፡

قَالَا رَبَّنَآ إِنَّنَا نَخَافُ أَن يَفۡرُطَ عَلَيۡنَآ أَوۡ أَن يَطۡغَىٰ ﴿٤٥﴾

46. (አላህም) አለ «አትፍሩ፡፡ እኔ በእርግጥ ከእናንተ ጋር ነኝና፡፡ እሰማለሁ፤ አያለሁም፡፡

قَالَ لَا تَخَافَآۖ إِنَّنِي مَعَكُمَآ أَسۡمَعُ وَأَرَىٰ ﴿٤٦﴾

47. «ወደርሱም ኺዱ፤ በሉትም፡- ‹እኛ የጌታህ መልክተኞች ነን፡፡› የእስራኤልንም ልጆች ከኛ ጋር ልቀቅ፡፡ አታሰቃያቸውም፡፡ ከጌታህ በኾነው ተዓምር በእርግጥ መጥተንሃልና፡፡ ሰላምም ቀጥታን በተከተለ ሰው ላይ ይኹን፡፡

فَأۡتِيَاهُ فَقُولَآ إِنَّا رَسُولَا رَبِّكَ فَأَرۡسِلۡ مَعَنَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَلَا تُعَذِّبۡهُمۡۖ قَدۡ جِئۡنَٰكَ بِـَٔايَةٖ مِّن رَّبِّكَۖ وَٱلسَّلَٰمُ عَلَىٰ مَنِ ٱتَّبَعَ ٱلۡهُدَىٰٓ ٤٧

48. «እኛ ቅጣቱ ባስተባበለና እምቢ ባለ ሰው ላይ ነው ማለት በእርግጥ ተወረደልን፡፡»

إِنَّا قَدۡ أُوحِيَ إِلَيۡنَآ أَنَّ ٱلۡعَذَابَ عَلَىٰ مَن كَذَّبَ وَتَوَلَّىٰ ٤٨

49. (ፈርዖንም) «ሙሳ ሆይ! ጌታችሁ ማነው» አለ፡፡

قَالَ فَمَن رَّبُّكُمَا يَٰمُوسَىٰ ٤٩

50. «ጌታችን ያ ለፍጥረቱ ነገርን ሁሉ (የሚያስፈልገውን) የሰጠ ከዚያም የመራው ነው» አለው፡፡

قَالَ رَبُّنَا ٱلَّذِيٓ أَعۡطَىٰ كُلَّ شَيۡءٍ خَلۡقَهُۥ ثُمَّ هَدَىٰ ٥٠

51. (ፈርዖንም) «የመጀመሪያይቱ ዘመናት ሕዝቦች ኹኔታ ምንድን ነው» አለ፡፡

قَالَ فَمَا بَالُ ٱلۡقُرُونِ ٱلۡأُولَىٰ ٥١

52. (ሙሳም) «ዕውቀትዋ እጌታዬ ዘንድ በመጽሐፍ የተመዘገበ ነው፡፡ ጌታዬ አይሳሳትም አይረሳምም» አለው፡፡

قَالَ عِلۡمُهَا عِندَ رَبِّي فِي كِتَٰبٖۖ لَّا يَضِلُّ رَبِّي وَلَا يَنسَى ٥٢

53. (እርሱ) ያ ምድርን ለእናንተ ምንጣፍ ያደረገላችሁ፣ በእርሷም ውስጥ ለእናንተ መንገድን ያገራላችሁ፣ ውሃንም ከሰማይ ያወረደ ነው (አለ)፡፡ በርሱም ከተለያየ በቃይ ዓይነቶችን አወጣንላችሁ፡፡

ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ مَهۡدٗا وَسَلَكَ لَكُمۡ فِيهَا سُبُلٗا وَأَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَخۡرَجۡنَا بِهِۦٓ أَزۡوَٰجٗا مِّن نَّبَاتٖ شَتَّىٰ ٥٣

54. ብሉ እንስሳዎቻችሁንም አግጡ፤ (ባዮች ኾነን አወጣንላችሁ)፡፡ በዚህ ውስጥ ለአእምሮ ባለቤቶች በእርግጥ ተዓምራት አለበት፡፡

كُلُواْ وَٱرۡعَوۡاْ أَنۡعَٰمَكُمۡۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّأُوْلِي ٱلنُّهَىٰ ٥٤

55. ከእርሷ (ከምድር) ፈጠርናችሁ፡፡ በእርሷም ውስጥ እንመልሳችኋለን፡፡ ከእርሷም በሌላ ጊዜ እናወጣችኋለን፡፡

۞مِنۡهَا خَلَقۡنَٰكُمۡ وَفِيهَا نُعِيدُكُمۡ وَمِنۡهَا نُخۡرِجُكُمۡ تَارَةً أُخۡرَىٰ ٥٥

56. ተዓምራቶቻችንንም ሁሏንም (ለፈርዖን) በእርግጥ አሳየነው፡፡ አስተባበለም፡፡ እምቢም አለ፡፡

وَلَقَدۡ أَرَيۡنَٰهُ ءَايَٰتِنَا كُلَّهَا فَكَذَّبَ وَأَبَىٰ ٥٦

57. «ከምድራችን በድግምትህ ልታወጣን መጣህብን ሙሳ ሆይ!» አለ፡፡

قَالَ أَجِئۡتَنَا لِتُخۡرِجَنَا مِنۡ أَرۡضِنَا بِسِحۡرِكَ يَٰمُوسَىٰ ٥٧

58. «መሰሉንም ድግምት እናመጣብሃለን፡፡ በእኛና ባንተም መካከል እኛም አንተም የማንጥሰው የኾነ ቀጠሮን በመካከለኛ ስፍራ አድርግልን» አለ፡፡

فَلَنَأۡتِيَنَّكَ بِسِحۡرٖ مِّثۡلِهِۦ فَٱجۡعَلۡ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَكَ مَوۡعِدٗا لَّا نُخۡلِفُهُۥ نَحۡنُ وَلَآ أَنتَ مَكَانٗا سُوٗى ٥٨

59. «ቀጠሯችሁ በማጌጫው ቀን ሰዎቹም በረፋድ በሚሰበሰቡበት ነው» አለ፡፡

قَالَ مَوۡعِدُكُمۡ يَوۡمُ ٱلزِّينَةِ وَأَن يُحۡشَرَ ٱلنَّاسُ ضُحٗى ٥٩

60. ፈርዖንም ዞረ፡፡ ተንኮሉንም ሰበሰበ፡፡ ከዚያም መጣ፡፡

فَتَوَلَّىٰ فِرۡعَوۡنُ فَجَمَعَ كَيۡدَهُۥ ثُمَّ أَتَىٰ ٦٠

61. ሙሳ ለእነሱ አላቸው «ወዮላችሁ በአላህ ላይ ውሸትን አትቅጠፉ፡፡ በቅጣት ያጠፋችኋልና፡፡ የቀጠፈም ሰው በእርግጥ አፈረ፡፡»

قَالَ لَهُم مُّوسَىٰ وَيْلَكُمْ لَا تَفْتَرُوا۟ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا فَيُسْحِتَكُم بِعَذَابٍ ۖ وَقَدْ خَابَ مَنِ ٱفْتَرَىٰ ﴿٦١﴾

62. (ድግምተኞቹ) በመካከላቸውም ነገራቸውን ተጨቃጨቁ፡፡ ውይይትንም ደበቁ፡፡

فَتَنَٰزَعُوٓا۟ أَمْرَهُم بَيْنَهُمْ وَأَسَرُّوا۟ ٱلنَّجْوَىٰ ﴿٦٢﴾

63. «እነዚህ በእርግጥ ደጋሚዎች ናቸው፡፡ ከምድራችሁ በድግምታቸው ሊያወጧችሁ በላጪቱንም መንገዳችሁን ሊያስወግዱባችሁ ይሻሉ» አሉ፡፡

قَالُوٓا۟ إِنْ هَٰذَٰنِ لَسَٰحِرَٰنِ يُرِيدَانِ أَن يُخْرِجَاكُم مِّنْ أَرْضِكُم بِسِحْرِهِمَا وَيَذْهَبَا بِطَرِيقَتِكُمُ ٱلْمُثْلَىٰ ﴿٦٣﴾

64. «ተንኮላችሁንም አጠንክሩ፡፡ ከዚያም ተሰልፋችሁ ኑ፡፡ ዛሬ ያሸነፈም ሰው ምኞቱን አገኘ» (ተባባሉ)፡፡

فَأَجْمِعُوا۟ كَيْدَكُمْ ثُمَّ ٱئْتُوا۟ صَفًّا ۚ وَقَدْ أَفْلَحَ ٱلْيَوْمَ مَنِ ٱسْتَعْلَىٰ ﴿٦٤﴾

65. «ሙሳ ሆይ! ወይ ትጥላለህ ወይም በመጀመሪያ የምንጥል እንኾናለን» (ምረጥ) አሉ፡፡

قَالُوا۟ يَٰمُوسَىٰٓ إِمَّآ أَن تُلْقِىَ وَإِمَّآ أَن نَّكُونَ أَوَّلَ مَنْ أَلْقَىٰ ﴿٦٥﴾

66. «አይደለም ጣሉ» አላቸው፡፡ ወዲያውም ገመዶቻቸውና ዘንጎቻቸው ከድግምታቸው የተነሳ እነርሱ የሚሮጡ (እባቦች) ኾነው ወደርሱ ተመለሱ፡፡

قَالَ بَلْ أَلْقُوا۟ ۖ فَإِذَا حِبَالُهُمْ وَعِصِيُّهُمْ يُخَيَّلُ إِلَيْهِ مِن سِحْرِهِمْ أَنَّهَا تَسْعَىٰ ﴿٦٦﴾

67. ሙሳም በነፍሱ ውስጥ ፍርሃትን አሳደረ፡፡

فَأَوْجَسَ فِى نَفْسِهِۦ خِيفَةً مُّوسَىٰ ﴿٦٧﴾

68. «አትፍራ አንተ የበላዩ አንተ ነህና» አልነው፡፡

قُلْنَا لَا تَخَفْ إِنَّكَ أَنتَ ٱلْأَعْلَىٰ ﴿٦٨﴾

69. «በቀኝ እጅህ ያለቸውንም በትር ጣል፡፡ ያንን የሠሩትን ትውጣለችና፡፡ ያ የሠሩት ሁሉ የድግምተኛ ተንኮል ነውና፡፡ ድግምተኛም በመጣበት ስፍራ ሁሉ አይቀናውም» (አልን)፡፡

وَأَلْقِ مَا فِى يَمِينِكَ تَلْقَفْ مَا صَنَعُوٓا۟ ۖ إِنَّمَا صَنَعُوا۟ كَيْدُ سَٰحِرٍ ۖ وَلَا يُفْلِحُ ٱلسَّاحِرُ حَيْثُ أَتَىٰ ﴿٦٩﴾

70. ድግምተኞቹም ሰጋጆች ኾነው ወደቁ፡፡ «በሃሩንና በሙሳ ጌታ አመንን» አሉ፡፡

فَأُلْقِىَ ٱلسَّحَرَةُ سُجَّدًا قَالُوٓا۟ ءَامَنَّا بِرَبِّ هَٰرُونَ وَمُوسَىٰ ﴿٧٠﴾

71. (ፈርዖንም) «ለእናንተ ሳልፈቅድላችሁ በፊት ለእርሱ አመናችሁን እርሱ በእርግጥ ያ ድግምትን ያስተማራችሁ ትልቃችሁ ነው፡፡ እጆቻችሁንና እግሮቻችሁን በማናጋት (ግራናቀኝን በማፈራረቅ) እቆራርጣችኋለሁ፡፡ በዘምባባም ግንዶች ላይ እሰቅላችኋለሁ፡፡ ማንኛችንም ቅጣቱ በጣም ብርቱ የሚቆይም መኾኑን ታውቃላችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ ءَامَنتُمْ لَهُۥ قَبْلَ أَنْ ءَاذَنَ لَكُمْ ۖ إِنَّهُۥ لَكَبِيرُكُمُ ٱلَّذِى عَلَّمَكُمُ ٱلسِّحْرَ ۖ فَلَأُقَطِّعَنَّ أَيْدِيَكُمْ وَأَرْجُلَكُم مِّنْ خِلَٰفٍ وَلَأُصَلِّبَنَّكُمْ فِى جُذُوعِ ٱلنَّخْلِ وَلَتَعْلَمُنَّ أَيُّنَآ أَشَدُّ عَذَابًا وَأَبْقَىٰ ﴿٧١﴾

72. ከመጡልን ታምራቶች ከዚያም ከፈጠረን(አምላክ) ፈጽሞ አንመርጥህም፤ አንተም የምትፈርደውን ፍረድ፤ የምትፈርደው በዚች በአነስተኛይቱ ሕይወት ብቻ ነው አሉ፡፡

قَالُوا۟ لَن نُّؤْثِرَكَ عَلَىٰ مَا جَآءَنَا مِنَ ٱلْبَيِّنَٰتِ وَٱلَّذِى فَطَرَنَا ۖ فَٱقْضِ مَآ أَنتَ قَاضٍ ۖ إِنَّمَا تَقْضِى هَٰذِهِ ٱلْحَيَوٰةَ ٱلدُّنْيَآ ﴿٧٢﴾

73. «ኃጢአቶቻችንንና ከድግምትም በእርሱ ላይ ያስገደድከንን ለእኛ ይምረን ዘንድ እኛ በጌታችን አምነናል፡፡ አላህም በጣም በላጭ ነው፤ (ቅጣቱም) በጣም የሚዘወትር ነው» አሉ፡፡

74. እነሆ ከሓዲ ኾኖ ወደ ጌታው የሚመጣ ሰው ለእርሱ ገሀነም አለችው፡፡ በውስጧም አይሞትም ሕያውም አይኾን፡፡

75. በጎ ሥራዎችን በእርግጥ የሠራ ምእመን ኾኖ የመጣውም ሰው እነዚያ ለእነሱ ከፍተኛ ደረጃዎች አሏቸው፡፡

76. ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው የመኖሪያ ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ (አሏቸው)፡፡ ይህም የተጥራራ ሰው ምንዳ ነው፡፡

77. ወደ ሙሳም «ባሮቼን ይዘህ በሌሊት ኺድ፡፡ ለእነሱም በባሕር ውስጥ ደረቅ መንገድን አድርግላቸው፡፡ መገኘትን አትፍራ፡፡ (ከመስጠም) አትጨነቅም፡፡» ስንል በእርግጥ ላክንበት፡፡

78. ፈርዖንም ከሰራዊቱ ጋር ኾኖ ተከተላቸው፡፡ ከባህሩም የሚሸፍን ሸፈናቸው፡፡

79. ፈርዖንም ሕዝቦቹን አሳሳታቸው፡፡ ቅኑንም መንገድ አልመራቸውም፡፡

80. የእስራኤል ልጆች ሆይ! ከጠላታችሁ በእርግጥ አዳንናችሁ፡፡ በጡርም ቀኝ ጎን ቀጠሮ አደረግንላችሁ፡፡ በእናንተም ላይ መናንና ድርጭትን አወረድንላችሁ፡፡

81. ከሰጠናችሁ ሲሳይ፤ ከመልካሙ ብሉ፡፡ በእርሱም ወሰንን አትለፉ፡፡ ቁጣዬ በእናንተ ላይ ይወርድባችኋልና፡፡ በእርሱም ላይ ቁጣዬ የሚወርድበት ሰው በእርግጥ ይጠፋል፡፡

82. እኔም ለተጸጸተ፣ ላመነም፣ መልካምንም ለሠራ፣ ከዚያም ለተመራ ሰው በእርግጥ መሓሪ ነኝ፡፡

83. «ሙሳ ሆይ! ከሕዝቦችህ ምን አስቸኮለህም» (ተባለ)፡፡

84. «እነሱ እነዚህ፤ በዱካዬ ላይ ያሉ ናቸው፡፡ ጌታዬ ሆይ! ትወድልንም ዘንድ ወደ አንተ ቸኮልኩ» አለ፡፡

85. (አላህ) «እኛም ከአንተ በኋላ ሰዎችህን በእርግጥ ፈትተን፡፡ ሳምራዊውም አሳሳታቸው» አለው፡፡

إِنَّآ ءَامَنَّا بِرَبِّنَا لِيَغْفِرَ لَنَا خَطَٰيَٰنَا وَمَآ أَكْرَهْتَنَا عَلَيْهِ مِنَ ٱلسِّحْرِ ۗ وَٱللَّهُ خَيْرٌ وَأَبْقَىٰٓ ﴿٧٣﴾

إِنَّهُۥ مَن يَأْتِ رَبَّهُۥ مُجْرِمًا فَإِنَّ لَهُۥ جَهَنَّمَ لَا يَمُوتُ فِيهَا وَلَا يَحْيَىٰ ﴿٧٤﴾

وَمَن يَأْتِهِۦ مُؤْمِنًا قَدْ عَمِلَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فَأُو۟لَٰٓئِكَ لَهُمُ ٱلدَّرَجَٰتُ ٱلْعُلَىٰ ﴿٧٥﴾

جَنَّٰتُ عَدْنٍ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا ۚ وَذَٰلِكَ جَزَآءُ مَن تَزَكَّىٰ ﴿٧٦﴾

وَلَقَدْ أَوْحَيْنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰٓ أَنْ أَسْرِ بِعِبَادِى فَٱضْرِبْ لَهُمْ طَرِيقًا فِى ٱلْبَحْرِ يَبَسًا لَّا تَخَٰفُ دَرَكًا وَلَا تَخْشَىٰ ﴿٧٧﴾

فَأَتْبَعَهُمْ فِرْعَوْنُ بِجُنُودِهِۦ فَغَشِيَهُم مِّنَ ٱلْيَمِّ مَا غَشِيَهُمْ ﴿٧٨﴾

وَأَضَلَّ فِرْعَوْنُ قَوْمَهُۥ وَمَا هَدَىٰ ﴿٧٩﴾

يَٰبَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ قَدْ أَنجَيْنَٰكُم مِّنْ عَدُوِّكُمْ وَوَٰعَدْنَٰكُمْ جَانِبَ ٱلطُّورِ ٱلْأَيْمَنَ وَنَزَّلْنَا عَلَيْكُمُ ٱلْمَنَّ وَٱلسَّلْوَىٰ ﴿٨٠﴾

كُلُوا۟ مِن طَيِّبَٰتِ مَا رَزَقْنَٰكُمْ وَلَا تَطْغَوْا۟ فِيهِ فَيَحِلَّ عَلَيْكُمْ غَضَبِى ۖ وَمَن يَحْلِلْ عَلَيْهِ غَضَبِى فَقَدْ هَوَىٰ ﴿٨١﴾

وَإِنِّى لَغَفَّارٌ لِّمَن تَابَ وَءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحًا ثُمَّ ٱهْتَدَىٰ ﴿٨٢﴾

۞ وَمَآ أَعْجَلَكَ عَن قَوْمِكَ يَٰمُوسَىٰ ﴿٨٣﴾

قَالَ هُمْ أُو۟لَآءِ عَلَىٰٓ أَثَرِى وَعَجِلْتُ إِلَيْكَ رَبِّ لِتَرْضَىٰ ﴿٨٤﴾

قَالَ فَإِنَّا قَدْ فَتَنَّا قَوْمَكَ مِنۢ بَعْدِكَ وَأَضَلَّهُمُ ٱلسَّامِرِىُّ ﴿٨٥﴾

فَرَجَعَ مُوسَىٰٓ إِلَىٰ قَوۡمِهِۦ غَضۡبَٰنَ أَسِفٗاۚ قَالَ يَٰقَوۡمِ أَلَمۡ يَعِدۡكُمۡ رَبُّكُمۡ وَعۡدًا حَسَنًاۚ أَفَطَالَ عَلَيۡكُمُ ٱلۡعَهۡدُ أَمۡ أَرَدتُّمۡ أَن يَحِلَّ عَلَيۡكُمۡ غَضَبٞ مِّن رَّبِّكُمۡ فَأَخۡلَفۡتُم مَّوۡعِدِي ٨٦

86. ሙሳም ወደ ሰዎቹ የተቆጣ ያዘነ ኾኖ ተመለሰ፡፡ «ሕዝቦቼ ሆይ! ጌታችሁ መልካም ተስፋን አልቀጠራችሁምን ቀጠሮው በእናንተ ላይ ረዘመባችሁን» ወይስ በእናንተ ላይ ከጌታችሁ ቅጣት ሊወርድባችሁ ፈለጋችሁና ቀጠሮየን አፈረሳችሁን አላቸው፡፡

قَالُواْ مَآ أَخۡلَفۡنَا مَوۡعِدَكَ بِمَلۡكِنَا وَلَٰكِنَّا حُمِّلۡنَآ أَوۡزَارٗا مِّن زِينَةِ ٱلۡقَوۡمِ فَقَذَفۡنَٰهَا فَكَذَٰلِكَ أَلۡقَى ٱلسَّامِرِيُّ ٨٧

87. «ቀጠሮህን በፈቃዳችን አልጣስንም፡፡ ግን እኛ ከሕዝቦቹ ጌጥ ሸክሞችን ተጫኜን (በእሳት ላይ) ጣልናትም፡፡ ሳምራዊውም እንደዚሁ ጣለ» አሉት፡፡

فَأَخۡرَجَ لَهُمۡ عِجۡلٗا جَسَدٗا لَّهُۥ خُوَارٞ فَقَالُواْ هَٰذَآ إِلَٰهُكُمۡ وَإِلَٰهُ مُوسَىٰ فَنَسِيَ ٨٨

88. ለእነሱም አካል የኾነ ጥጃን ለእርሱ መኳኋር ያለውን አወጣላቸው፡፡ (ተከታዮቹ) «ይህ አምላካችሁ የሙሳም አምላክ ነው ግን ረሳው» አሉም፡፡

أَفَلَا يَرَوۡنَ أَلَّا يَرۡجِعُ إِلَيۡهِمۡ قَوۡلٗا وَلَا يَمۡلِكُ لَهُمۡ ضَرّٗا وَلَا نَفۡعٗا ٨٩

89. ወደእነሱ ንግግርን የማይመልስ ለእነሱም ጉዳትንና ጥቅምን የማይችል መኾኑን አያዩምን

وَلَقَدۡ قَالَ لَهُمۡ هَٰرُونُ مِن قَبۡلُ يَٰقَوۡمِ إِنَّمَا فُتِنتُم بِهِۦۖ وَإِنَّ رَبَّكُمُ ٱلرَّحۡمَٰنُ فَٱتَّبِعُونِي وَأَطِيعُوٓاْ أَمۡرِي ٩٠

90. ሃሩንም ከዚህ በፊት በእርግጥ አላቸው፡- «ሕዝቦቼ ሆይ! (ይህ) በእርሱ የተሞከራችሁበት ብቻ ነው፡፡ ጌታችሁም አልረሕማን ነው፡፡ ተከተሉኝም፡፡ ትዕዛዜንም ስሙ፡፡»

قَالُواْ لَن نَّبۡرَحَ عَلَيۡهِ عَٰكِفِينَ حَتَّىٰ يَرۡجِعَ إِلَيۡنَا مُوسَىٰ ٩١

91. «ሙሳ ወደእኛ እስከሚመለስ በእርሱ (መገዛት) ላይ ከመቆየት ፈጽሞ አንወገድም» አሉ፡፡

قَالَ يَٰهَٰرُونُ مَا مَنَعَكَ إِذۡ رَأَيۡتَهُمۡ ضَلُّوٓاْ ٩٢

92. (ሙሳ) አለ፡- «ሃሩን ሆይ! ተሳስተው ባየሃቸው ጊዜ ምን ከለከልህ

أَلَّا تَتَّبِعَنِۖ أَفَعَصَيۡتَ أَمۡرِي ٩٣

93. «እኔን ከመከተል ትዕዛዜን ጣስክን»

قَالَ يَبۡنَؤُمَّ لَا تَأۡخُذۡ بِلِحۡيَتِي وَلَا بِرَأۡسِيٓۖ إِنِّي خَشِيتُ أَن تَقُولَ فَرَّقۡتَ بَيۡنَ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَلَمۡ تَرۡقُبۡ قَوۡلِي ٩٤

94. «የእናቴ ልጅ ሆይ! ጢሜንም ራሴንም አትያዝ፡፡ እኔ በእስራኤል ልጆች መካከል ለያየህ፤ ቃሌንም አልጠበቅህም ማለትህን ፈራሁ» አለው፡፡

قَالَ فَمَا خَطۡبُكَ يَٰسَٰمِرِيُّ ٩٥

95. (ሙሳ) «ሳምራዊው ሆይ! ነገርህም ምንድን ነው» አለ፡፡

قَالَ بَصُرۡتُ بِمَا لَمۡ يَبۡصُرُواْ بِهِۦ فَقَبَضۡتُ قَبۡضَةٗ مِّنۡ أَثَرِ ٱلرَّسُولِ فَنَبَذۡتُهَا وَكَذَٰلِكَ سَوَّلَتۡ لِي نَفۡسِي ٩٦

96. ያላዩትን ነገር አየሁ፡፡ ከመልክተኛው (ከፈረሱ ኮቴ) ዱካም ጭብጥ አፈርን ዘገንኩ፡፡ (በቅርጹ ላይ) ጣልኳትም፡፡ እንደዚሁም ነፍሴ ሸለመችልኝ» አለ፡፡

97. አለው «ኺድ፤ ላንተም በሕይወትህ (ለአየኸው ሰው ሁሉ) መነካካት የለም ማለት አለህ፡፡ ለአንተም ፈጽሞ የማትጣሰው ቀጠሮ አለህ፡፡ ወደዚያም በእርሱ ላይ ተገዢው ኾነህ ወደ ቆየህበት አምላክህ ተመልከት፡ ፡ በእርግጥ እናቃጥለዋለን፡፡ ከዚያም በባሕሩ ውስጥ መበተንን እንበትነዋለን፡፡»

قَالَ فَٱذْهَبْ فَإِنَّ لَكَ فِى ٱلْحَيَوٰةِ أَن تَقُولَ لَا مِسَاسَ ۖ وَإِنَّ لَكَ مَوْعِدًا لَّن تُخْلَفَهُۥ ۖ وَٱنظُرْ إِلَىٰٓ إِلَٰهِكَ ٱلَّذِى ظَلْتَ عَلَيْهِ عَاكِفًا ۖ لَّنُحَرِّقَنَّهُۥ ثُمَّ لَنَنسِفَنَّهُۥ فِى ٱلْيَمِّ نَسْفًا ﴿٩٧﴾

98. ጌታችሁ ያ ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ የሌለ የኾነው አላህ ብቻ ነው፡፡ እውቀቱ ነገርን ሁሉ አዳረሰ፡፡

إِنَّمَآ إِلَٰهُكُمُ ٱللَّهُ ٱلَّذِى لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ۚ وَسِعَ كُلَّ شَىْءٍ عِلْمًا ﴿٩٨﴾

99. እንደዚሁ በእርግጥ ካለፉት ወሬዎች ባንተ ላይ እንተርካለን፡፡ ከእኛም ዘንድ ቁርኣንን በእርግጥ ሰጠንህ፡፡

كَذَٰلِكَ نَقُصُّ عَلَيْكَ مِنْ أَنۢبَآءِ مَا قَدْ سَبَقَ ۚ وَقَدْ ءَاتَيْنَٰكَ مِن لَّدُنَّا ذِكْرًا ﴿٩٩﴾

100. ከእርሱ ያፈገፈገ ሰው እርሱ በትንሣኤ ቀን ከባድን ቅጣት ይሸከማል፡፡

مَّنْ أَعْرَضَ عَنْهُ فَإِنَّهُۥ يَحْمِلُ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ وِزْرًا ﴿١٠٠﴾

101. በእርሱ ውስጥ ዘውታሪዎች ኾነው (ይሸከማሉ)፡ ፡ በትንሣኤም ቀን ለእነሱ የኾነው ሸክም ከፋ!

خَٰلِدِينَ فِيهِ ۖ وَسَآءَ لَهُمْ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ حِمْلًا ﴿١٠١﴾

102. በቀንዱ በሚነፋ ቀን (ሸክማቸው ከፋ)፤ ከሓዲዎችንም በዚያ ቀን (ዓይኖቻቸው) ሰማያዊዎች ሆነው እንሰበስባቸዋለን፡፡

يَوْمَ يُنفَخُ فِى ٱلصُّورِ ۚ وَنَحْشُرُ ٱلْمُجْرِمِينَ يَوْمَئِذٍ زُرْقًا ﴿١٠٢﴾

103. «ዐሥርን (ቀን) እንጂ አልቆያችሁም» በመባባል በመካከላቸው ይንሾካሾካሉ፡፡

يَتَخَٰفَتُونَ بَيْنَهُمْ إِن لَّبِثْتُمْ إِلَّا عَشْرًا ﴿١٠٣﴾

104. በሐሳብ ቀጥተኛው «አንድን ቀን እንጅ አልቆያችሁም» በሚል ጊዜ የሚሉትን ነገር እኛ ዐዋቂዎች ነን፡፡

نَّحْنُ أَعْلَمُ بِمَا يَقُولُونَ إِذْ يَقُولُ أَمْثَلُهُمْ طَرِيقَةً إِن لَّبِثْتُمْ إِلَّا يَوْمًا ﴿١٠٤﴾

105. ከጋራዎችም ይጠይቁሃል፤ በላቸው «ጌታዬ መበተንን ይበትናቸዋል፡፡

وَيَسْـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلْجِبَالِ فَقُلْ يَنسِفُهَا رَبِّى نَسْفًا ﴿١٠٥﴾

106. «ትክክል ሜዳም ኾና ይተዋታል፡፡

فَيَذَرُهَا قَاعًا صَفْصَفًا ﴿١٠٦﴾

107. «በርሷ ዝቅታና ከፍታን አታይም፡፡»

لَّا تَرَىٰ فِيهَا عِوَجًا وَلَآ أَمْتًا ﴿١٠٧﴾

108. በዚያ ቀን (ለመሰብሰብ) ጠሪውን ለእርሱ መጣመም የሌለውን መከተል ይከተላሉ፡፡ ድምጾችም ለአልረሕማን ጸጥ ይላሉ፡፡ ስለዚህ ሹክሹክታን እንጂ አትሰማም፡፡

يَوْمَئِذٍ يَتَّبِعُونَ ٱلدَّاعِىَ لَا عِوَجَ لَهُۥ ۖ وَخَشَعَتِ ٱلْأَصْوَاتُ لِلرَّحْمَٰنِ فَلَا تَسْمَعُ إِلَّا هَمْسًا ﴿١٠٨﴾

109. በዚያ ቀን ለእርሱ አልረሕማን የፈቀደለትንና ለእርሱም ቃልን የወደደለትን ሰው ቢኾን እንጅ ምልጃ (አንድንም) አትጠቅምም፡፡

يَوْمَئِذٍ لَّا تَنفَعُ ٱلشَّفَٰعَةُ إِلَّا مَنْ أَذِنَ لَهُ ٱلرَّحْمَٰنُ وَرَضِىَ لَهُۥ قَوْلًا ﴿١٠٩﴾

110. በስተፊታቸው ያለውን በስተኋላቸውም ያለውን ሁሉ ያውቃል፡፡ በእርሱም ዕውቀትን አያካብቡም፤ (አያውቁም)፡፡

يَعْلَمُ مَا بَيْنَ أَيْدِيهِمْ وَمَا خَلْفَهُمْ وَلَا يُحِيطُونَ بِهِۦ عِلْمًا ﴿١١٠﴾

111. ፊቶችም ሁሉ ሕያው አስተናባሪ ለኾነው (አላህ) ተዋረዱ፡፡ በደልንም የተሸከመ ሰው በእርግጥ ከሰረ፡፡

۞وَعَنَتِ ٱلۡوُجُوهُ لِلۡحَيِّ ٱلۡقَيُّومِۖ وَقَدۡ خَابَ مَنۡ حَمَلَ ظُلۡمًا ﰮ

112. እርሱ አማኝ ኾኖ ከመልካም ሥራዎችም የሠራ ሰው በደልንም መጉደልንም አይፈራም፡፡

وَمَن يَعۡمَلۡ مِنَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَلَا يَخَافُ ظُلۡمٗا وَلَا هَضۡمٗا ﰯ

113. እንደዚሁም ዐረብኛ ቁርኣን ኾኖ አወረድነው፡፡ አላህንም ይፈሩ ዘንድ ወይም ለእነሱ ግሣጼን ያድስላቸው ዘንድ ከዛቻ ደጋግመን በውስጡ ገለጽን፡፡

وَكَذَٰلِكَ أَنزَلۡنَٰهُ قُرۡءَانًا عَرَبِيّٗا وَصَرَّفۡنَا فِيهِ مِنَ ٱلۡوَعِيدِ لَعَلَّهُمۡ يَتَّقُونَ أَوۡ يُحۡدِثُ لَهُمۡ ذِكۡرٗا ﰰ

114. እውነተኛው ንጉስ አላህም (ከሓዲዎች ከሚሉት) ላቀ፡፡ ወደ አንተ መወረዱም ከመፈጸሙ በፊት በማንበብ አትቸኩል፡፡ «ጌታዬ ሆይ! ዕውቀትንም ጨምርልኝ» በል፡፡

فَتَعَٰلَى ٱللَّهُ ٱلۡمَلِكُ ٱلۡحَقُّۗ وَلَا تَعۡجَلۡ بِٱلۡقُرۡءَانِ مِن قَبۡلِ أَن يُقۡضَىٰٓ إِلَيۡكَ وَحۡيُهُۥۖ وَقُل رَّبِّ زِدۡنِي عِلۡمٗا ﰱ

115. ወደ አደምም ከዚህ በፊት ኪዳንን በእርግጥ አወረድን፡፡ ረሳም፡፡ ለእርሱም ቆራጥነትን አላገኘንለትም፡፡

وَلَقَدۡ عَهِدۡنَآ إِلَىٰٓ ءَادَمَ مِن قَبۡلُ فَنَسِيَ وَلَمۡ نَجِدۡ لَهُۥ عَزۡمٗا ﰲ

116. ለመላእክትም ለአዳም ስገዱ ባልን ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ሰገዱም፤ ኢብሊስ ብቻ ሲቀር እምቢ አለ፡፡

وَإِذۡ قُلۡنَا لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ ٱسۡجُدُواْ لِأٓدَمَ فَسَجَدُوٓاْ إِلَّآ إِبۡلِيسَ أَبَىٰ ﰳ

117. አልንም «አደም ሆይ! ይህ ላንተም ለሚስትህም በእርግጥ ጠላት ነው፡፡ ስለዚህ ከገነት አያውጣችሁ፤ ትለፋለህና፡፡

فَقُلۡنَا يَٰٓـَٔادَمُ إِنَّ هَٰذَا عَدُوّٞ لَّكَ وَلِزَوۡجِكَ فَلَا يُخۡرِجَنَّكُمَا مِنَ ٱلۡجَنَّةِ فَتَشۡقَىٰٓ ﰴ

118. ለአንተ በእርሷ ውስጥ አለመራብና አለመታረዝ አለህ፡፡

إِنَّ لَكَ أَلَّا تَجُوعَ فِيهَا وَلَا تَعۡرَىٰ ﰵ

119. አንተም በርሷ ውስጥ አትጠማም፤ ፀሐይም አትተኮስም፡፡

وَأَنَّكَ لَا تَظۡمَؤُاْ فِيهَا وَلَا تَضۡحَىٰ ﰶ

120. ሰይጣንም ወደርሱ ጎተጎተ «አደም ሆይ! በመዘውተሪያ ዛፍ በማይጠፋ ንግሥናም ላይ ላመላክትህን አለው፡፡

فَوَسۡوَسَ إِلَيۡهِ ٱلشَّيۡطَٰنُ قَالَ يَٰٓـَٔادَمُ هَلۡ أَدُلُّكَ عَلَىٰ شَجَرَةِ ٱلۡخُلۡدِ وَمُلۡكٖ لَّا يَبۡلَىٰ ﰷ

121. ከእርሷም በሉ፡፡ ለእነርሱም ኀፍረተ ገላቸው ተገለጸች፡፡ ከገነትም ቅጠል በላያቸው ላይ ይለጥፉ ጀመር፡፡ አደምም የጌታውን ትእዛዝ (ረስቶ) ጣሰ፡፡ (ከፈለገው መዘውተር) ተሳሳተም፡፡

فَأَكَلَا مِنۡهَا فَبَدَتۡ لَهُمَا سَوۡءَٰتُهُمَا وَطَفِقَا يَخۡصِفَانِ عَلَيۡهِمَا مِن وَرَقِ ٱلۡجَنَّةِۚ وَعَصَىٰٓ ءَادَمُ رَبَّهُۥ فَغَوَىٰ ﰸ

122. ከዚያም ጌታው መረጠው ከእርሱም ጸጸቱን ተቀበለው መራውም፡፡

ثُمَّ ٱجۡتَبَٰهُ رَبُّهُۥ فَتَابَ عَلَيۡهِ وَهَدَىٰ ﰹ

123. አላቸው «ከፊላችሁም ለከፊሉ ጠላት ሲኾን ሁላችሁም ከእርሷ ውረዱ ከእኔም የኾነ መሪ ቢመጣላችሁ መሪየን የተከተለ አይሳሳትም አይቸገርምም፡፡

قَالَ ٱهْبِطَا مِنْهَا جَمِيعًاۢ بَعْضُكُمْ لِبَعْضٍ عَدُوٌّۖ فَإِمَّا يَأْتِيَنَّكُم مِّنِّي هُدًى فَمَنِ ٱتَّبَعَ هُدَايَ فَلَا يَضِلُّ وَلَا يَشْقَىٰ ﴿١٢٣﴾

124. «ከግሣጼዬም የዞረ ሰው ለእርሱ ጠባብ ኑሮ አለው፡፡ በትንሣኤም ቀን ዕውር ኾኖ እንቀሰቅሰዋለን፡፡

وَمَنْ أَعْرَضَ عَن ذِكْرِي فَإِنَّ لَهُۥ مَعِيشَةً ضَنكًا وَنَحْشُرُهُۥ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ أَعْمَىٰ ﴿١٢٤﴾

125. «ጌታዬ ሆይ! ለምን ዕውር አድርገህ አስነሳኸኝ በእርግጥ የማይ የነበርኩ ስኾን» ይላል፡፡

قَالَ رَبِّ لِمَ حَشَرْتَنِيٓ أَعْمَىٰ وَقَدْ كُنتُ بَصِيرًا ﴿١٢٥﴾

126. (ነገሩ) እንደዚሁ ነው፡፡ «ታምራታችን መጣችልህ፡፡ ተውካትም፡፡ እንደዚሁም ዛሬ ትተዋለህ» ይለዋል፡፡

قَالَ كَذَٰلِكَ أَتَتْكَ ءَايَٰتُنَا فَنَسِيتَهَاۖ وَكَذَٰلِكَ ٱلْيَوْمَ تُنسَىٰ ﴿١٢٦﴾

127. እንደዚሁም ያጋራንና በጌታው አንቀጾች ያላመነን ሰው እንቀጣዋለን፡፡ የመጨረሻይቱም ዓለም ቅጣት በጣም ብርቱ ሁልጊዜ ዘውታሪም ነው፡፡

وَكَذَٰلِكَ نَجْزِي مَنْ أَسْرَفَ وَلَمْ يُؤْمِنۢ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِۦۚ وَلَعَذَابُ ٱلْـَٔاخِرَةِ أَشَدُّ وَأَبْقَىٰٓ ﴿١٢٧﴾

128. (ቁረይሾች) ከእነሱ በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙዎችን ያጠፋን መኾናችን በመኖሪያዎቻቸው የሚኼዱ ኾነው ሳሉ ለእነርሱ አልተገለጸላቸውምን በዚህ ውስጥ ለአእምሮ ባለቤቶች በእርግጥ መልክቶች አሉበት፡፡

أَفَلَمْ يَهْدِ لَهُمْ كَمْ أَهْلَكْنَا قَبْلَهُم مِّنَ ٱلْقُرُونِ يَمْشُونَ فِي مَسَٰكِنِهِمْۗ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٍ لِّأُوْلِي ٱلنُّهَىٰ ﴿١٢٨﴾

129. ከጌታህ ያለፈች ቃልና የተወሰነ ጊዜ ባልነበረ ኖሮ (ቅጣቱ አሁኑኑ) የሚይዛቸው ይኾን ነበር፡፡

وَلَوْلَا كَلِمَةٌ سَبَقَتْ مِن رَّبِّكَ لَكَانَ لِزَامًا وَأَجَلٌ مُّسَمًّى ﴿١٢٩﴾

130. በሚሉትም ላይ ታገስ፡፡ ጌታህንም ፀሐይ ከመውጣትዋ በፊት ከመግባትዋም በፊት የምታመሰግን ኾነህ አጥራው፤ (ስገድ)፡፡ ከሌሊት ሰዓቶችም በቀን ጫፎችም አጥራው፡፡ (በሚሰጥህ ምንዳ) ልትወድ ይከጀላልና፡፡

فَٱصْبِرْ عَلَىٰ مَا يَقُولُونَ وَسَبِّحْ بِحَمْدِ رَبِّكَ قَبْلَ طُلُوعِ ٱلشَّمْسِ وَقَبْلَ غُرُوبِهَاۖ وَمِنْ ءَانَآيِٕ ٱلَّيْلِ فَسَبِّحْ وَأَطْرَافَ ٱلنَّهَارِ لَعَلَّكَ تَرْضَىٰ ﴿١٣٠﴾

131. ዓይኖችህንም ከእነርሱ (ከሰዎቹ) ክፍሎችን በእርሱ ልንፈትናቸው ወደ አጣቀምንበት፤ ወደ ቅርቢቱ ሕይወት ጌጦች አትዘርጋ፡፡ የጌታህ ሲሳይም በጣም በላጭ ዘውታሪም ነው፡፡

وَلَا تَمُدَّنَّ عَيْنَيْكَ إِلَىٰ مَا مَتَّعْنَا بِهِۦٓ أَزْوَٰجًا مِّنْهُمْ زَهْرَةَ ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَا لِنَفْتِنَهُمْ فِيهِۚ وَرِزْقُ رَبِّكَ خَيْرٌ وَأَبْقَىٰ ﴿١٣١﴾

132. ቤተሰብህንም በስግደት እዘዝ፡፡ በእርሷም ላይ ዘውትር፤(ጽና)፡፡ ሲሳይን አንጠይቅህም፡፡ እኛ እንሰጥሃለን፡፡ መልካሚቱ መጨረሻም ለጥንቁቆቹ ናት፡ ፡

وَأْمُرْ أَهْلَكَ بِٱلصَّلَوٰةِ وَٱصْطَبِرْ عَلَيْهَاۖ لَا نَسْـَٔلُكَ رِزْقًاۖ نَّحْنُ نَرْزُقُكَۗ وَٱلْعَٰقِبَةُ لِلتَّقْوَىٰ ﴿١٣٢﴾

133. «ከጌታውም በኾነ ተዓምር አይመጣንምን» አሉ በመጀመሪያዎቹ ጽሑፎች ውስጥ ያለችው ማስረጃ አልመጣቻቸውምን

وَقَالُواْ لَوْلَا يَأْتِينَا بِـَٔايَةٍ مِّن رَّبِّهِۦٓۚ أَوَلَمْ تَأْتِهِم بَيِّنَةُ مَا فِي ٱلصُّحُفِ ٱلْأُولَىٰ ﴿١٣٣﴾

134. እኛም ከእርሱ (ከሙሐመድ መላክ) በፊት በቅጣት ባጠፋናቸው ኖሮ «ጌታችን ሆይ! ከመዋረዳችንና ከማፈራችን በፊት አንቀጾችህን እንከተል ዘንድ ወደኛ መልከተኛን አትልክም ነበርን» ባሉ ነበር፡፡

وَلَوۡ أَنَّآ أَهۡلَكۡنَٰهُم بِعَذَابٖ مِّن قَبۡلِهِۦ لَقَالُواْ رَبَّنَا لَوۡلَآ أَرۡسَلۡتَ إِلَيۡنَا رَسُولٗا فَنَتَّبِعَ ءَايَٰتِكَ مِن قَبۡلِ أَن نَّذِلَّ وَنَخۡزَىٰ ﴿١٣٤﴾

135. «ሁሉም ተጠባባቂ ነው፡፡ ተጠባበቁም፡፡ የቀጥታውም መንገድ ባለቤቶች እነማን እንደሆኑ እነማንም እንደ ተመሩ ወደ ፊት ታውቃላችሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ كُلّٞ مُّتَرَبِّصٞ فَتَرَبَّصُواْۖ فَسَتَعۡلَمُونَ مَنۡ أَصۡحَٰبُ ٱلصِّرَٰطِ ٱلسَّوِيِّ وَمَنِ ٱهۡتَدَىٰ ﴿١٣٥﴾

# ሱረቱ አል አንቢያ

# سورة الأنبيا

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ለሰዎች እነርሱ በዝንጋቴ ውስጥ (መሰናዳትን) የተው ኾነው ሳሉ ምርመራቸው ቀረበ፡፡

ٱقۡتَرَبَ لِلنَّاسِ حِسَابُهُمۡ وَهُمۡ فِي غَفۡلَةٖ مُّعۡرِضُونَ ﴿١﴾

2. ከጌታቸው አዲስ የተወረደ ቁርአን አይመጣላቸውም፡፡ እነሱ የሚያላግጡ ሆነው የሚያደምጡት ቢሆኑ እንጂ፡፡

مَا يَأۡتِيهِم مِّن ذِكۡرٖ مِّن رَّبِّهِم مُّحۡدَثٍ إِلَّا ٱسۡتَمَعُوهُ وَهُمۡ يَلۡعَبُونَ ﴿٢﴾

3. ልቦቻቸው ዝንጉዎች ኾነው (የሚያዳምጡት ቢኾኑ እንጅ)፡፡ እነዚያም የበደሉት ሰዎች መንሾካሾክን ደበቁ፡ ፡ «ይህ ብጤያችሁ ሰው እንጅ ሌላ ነውን እናንተም የምታዩ ስትኾኑ ድግምትን ለመቀበል ትመጣላችሁን» (አሉ)፡፡

لَاهِيَةٗ قُلُوبُهُمۡۗ وَأَسَرُّواْ ٱلنَّجۡوَى ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ هَلۡ هَٰذَآ إِلَّا بَشَرٞ مِّثۡلُكُمۡۖ أَفَتَأۡتُونَ ٱلسِّحۡرَ وَأَنتُمۡ تُبۡصِرُونَ ﴿٣﴾

4. (ሙሐመድም) «ጌታዬ ቃልን ሁሉ በሰማይና በምድር ውስጥ ያለ ሲኾን ያውቃል እርሱም ሰሚው ዐዋቂው ነው» አለ፡፡

قَالَ رَبِّي يَعۡلَمُ ٱلۡقَوۡلَ فِي ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿٤﴾

5. «በእውነቱ (ቁርኣኑ) የሕልሞች ቅዠቶች ነው፡፡ ይልቁንም ቀጠፈው እንዲያውም እርሱ ቅኔን ገጣሚ ነው፡፡ የቀድሞዎቹም እንደተላኩ (መልክተኛ ከኾነ) በተዓምር ይምጣብን» አሉ፡፡

بَلۡ قَالُوٓاْ أَضۡغَٰثُ أَحۡلَٰمِۭ بَلِ ٱفۡتَرَىٰهُ بَلۡ هُوَ شَاعِرٞ فَلۡيَأۡتِنَا بِـَٔايَةٖ كَمَآ أُرۡسِلَ ٱلۡأَوَّلُونَ ﴿٥﴾

6. ከእነሱ በፊት ያጠፋናት ከተማ አላመነችም፡፡ ታዲያ እነሱ ያምናሉን

مَآ ءَامَنَتۡ قَبۡلَهُم مِّن قَرۡيَةٍ أَهۡلَكۡنَٰهَآۖ أَفَهُمۡ يُؤۡمِنُونَ ﴿٦﴾

7. ከአንተም በፊት ወደእነሱ የምናወርድላቸው የኾነን ሰዎችን እንጂ ሌላን አላክንም፡፡ የማታውቁም ብትኾኑ የመጽሐፉን ባለቤቶች ጠይቁ፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا قَبۡلَكَ إِلَّا رِجَالٗا نُّوحِيٓ إِلَيۡهِمۡۖ فَسۡـَٔلُوٓاْ أَهۡلَ ٱلذِّكۡرِ إِن كُنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ﴿٧﴾

8. ምግብን የማይበሉ አካልም አላደረግናቸውም፡፡ ዘውታሪዎችም አልነበሩም፡፡

وَمَا جَعَلۡنَٰهُمۡ جَسَدٗا لَّا يَأۡكُلُونَ ٱلطَّعَامَ وَمَا كَانُواْ خَٰلِدِينَ ٨

9. ከዚያም ቀጠሮን ሞላንላቸው፡፡ አዳንናቸውም፡፡ የምንሻውንም ሰው (አዳን)፡፡ ወሰን አላፊዎቹንም አጠፋን፡፡

ثُمَّ صَدَقۡنَٰهُمُ ٱلۡوَعۡدَ فَأَنجَيۡنَٰهُمۡ وَمَن نَّشَآءُ وَأَهۡلَكۡنَا ٱلۡمُسۡرِفِينَ ٩

10. ክብራችሁ በውስጡ ያለበትን መጽሐፍ ወደእናንተ በእርግጥ አወረድን፡፡ አታውቁምን

لَقَدۡ أَنزَلۡنَآ إِلَيۡكُمۡ كِتَٰبٗا فِيهِ ذِكۡرُكُمۡۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ١٠

11. በዳይም ከነበረች ከተማ ያጠፋናትና ከኋላዋም ሌሎችን ሕዝቦች ያስገኘነው ብዙ ናት፡፡

وَكَمۡ قَصَمۡنَا مِن قَرۡيَةٖ كَانَتۡ ظَالِمَةٗ وَأَنشَأۡنَا بَعۡدَهَا قَوۡمًا ءَاخَرِينَ ١١

12. ቅጣታችንም በተሰማቸው ጊዜ እነርሱ ወዲያውኑ ከእርሷ (ለመሸሽ) ይገሠግሣሉ፡፡

فَلَمَّآ أَحَسُّواْ بَأۡسَنَآ إِذَا هُم مِّنۡهَا يَرۡكُضُونَ ١٢

13. አትገሥግሡ፤ ትለመኑም ይኾናልና፡፡ በእርሱ ወደ ተቀማጠላችሁበት ጸጋ ወደ መኖሪያዎቻችሁም ተመለሱ (ይባላሉ)፡፡

لَا تَرۡكُضُواْ وَٱرۡجِعُوٓاْ إِلَىٰ مَآ أُتۡرِفۡتُمۡ فِيهِ وَمَسَٰكِنِكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تُسۡـَٔلُونَ ١٣

14. «ዋ ጥፋታችን! እኛ በእርግጥ በዳዮች ነበርን» ይላሉ፡፡

قَالُواْ يَٰوَيۡلَنَآ إِنَّا كُنَّا ظَٰلِمِينَ ١٤

15. የታጨዱ ሬሳዎችም እስካደረግናቸው ድረስ ይህቺ ጠሪያቸው ከመኾን አልተወገደችም፡፡

فَمَا زَالَت تِّلۡكَ دَعۡوَىٰهُمۡ حَتَّىٰ جَعَلۡنَٰهُمۡ حَصِيدًا خَٰمِدِينَ ١٥

16. ሰማይንና ምድርን በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ ቀላጆች ኾነን አልፈጠርንም፡፡

وَمَا خَلَقۡنَا ٱلسَّمَآءَ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَا لَٰعِبِينَ ١٦

17. መጫወቻን (ሚስትና ልጅን) ልንይዝ በሻን ኖሮ ከእኛ ዘንድ በያዝነው ነበር፡፡ (ግን) ሠሪዎች አይደለንም፡፡

لَوۡ أَرَدۡنَآ أَن نَّتَّخِذَ لَهۡوٗا لَّٱتَّخَذۡنَٰهُ مِن لَّدُنَّآ إِن كُنَّا فَٰعِلِينَ ١٧

18. በእርግጥ እውነትን በውሸት ላይ እንጥላለን፡፡ አንጎሉን ያፈርሰዋልም፡፡ ወዲያውም እርሱ ጠፊ ነው፡፡ ለእናንተም ከዚያ (ሚስትና ልጅ አለው በማለት) ከምትመጥኑት ነገር ብርቱ ቅጣት አላችሁ፤ (ወዮላችሁ)፡፡

بَلۡ نَقۡذِفُ بِٱلۡحَقِّ عَلَى ٱلۡبَٰطِلِ فَيَدۡمَغُهُۥ فَإِذَا هُوَ زَاهِقٞۚ وَلَكُمُ ٱلۡوَيۡلُ مِمَّا تَصِفُونَ ١٨

19. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉም የእርሱ ነው፡፡ እርሱ ዘንድ ያሉትም (መላእክት) እርሱን ከመገዛት አይኮሩም፡፡ አይሰለቹምም፡፡

وَلَهُۥ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَمَنۡ عِندَهُۥ لَا يَسۡتَكۡبِرُونَ عَنۡ عِبَادَتِهِۦ وَلَا يَسۡتَحۡسِرُونَ ١٩

20. በሌሊትና በቀንም ያጠሩታል፤ አያርፉም፡፡

يُسَبِّحُونَ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ لَا يَفۡتُرُونَ ٢٠

21. ይልቁንም ከምድር የኾኑን እነርሱ ሙታንን የሚያስነሱን አማልክት ያዙን (የለም)፡፡

أَمِ ٱتَّخَذُوٓاْ ءَالِهَةٗ مِّنَ ٱلۡأَرۡضِ هُمۡ يُنشِرُونَ ٢١

22. በሁለቱ (በሰማያትና በምድር) ውስጥ ከአላህ ሌላ አማልክት በነበሩ ኖሮ በተበላሹ ነበር፡፡ የዐርሹ ጌታ አላህም ከሚሉት ሁሉ ጠራ፡፡

لَوۡ كَانَ فِيهِمَآ ءَالِهَةٌ إِلَّا ٱللَّهُ لَفَسَدَتَاۚ فَسُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ رَبِّ ٱلۡعَرۡشِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿٢٢﴾

23. ከሚሠራው ሁሉ አይጠየቅም፡፡ እነርሱ (ፍጥረቶቹ) ግን ይጠየቃሉ፡፡

لَا يُسۡـَٔلُ عَمَّا يَفۡعَلُ وَهُمۡ يُسۡـَٔلُونَ ﴿٢٣﴾

24. ይልቁንም ከእርሱ ሌላ አማልክትን ያዙን «አስረጃችሁን አምጡ፡፡ ይህ (ቁርኣን) እኔ ዘንድ ያለው ሕዝብ መገሰጫ ከእኔ በፊትም የነበሩት ሕዝቦች መገሰጫ ነው» በላቸው፡፡ በውነቱ አብዛኞቻቸው እውነቱን አያውቁም፡፡ ስለዚህ እነሱ እምቢተኞች ናቸው፡፡

أَمِ ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِهِۦٓ ءَالِهَةٗۖ قُلۡ هَاتُواْ بُرۡهَٰنَكُمۡۖ هَٰذَا ذِكۡرُ مَن مَّعِيَ وَذِكۡرُ مَن قَبۡلِيۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٱلۡحَقَّۖ فَهُم مُّعۡرِضُونَ ﴿٢٤﴾

25. ከአንተ በፊትም እነሆ ከእኔ ሌላ አምላክ የለምና ተገዙኝ በማለት ወደርሱ የምናወርድለት ቢኾን እንጅ ከመልክተኛ አንድንም አልላክንም፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ مِن رَّسُولٍ إِلَّا نُوحِيٓ إِلَيۡهِ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّآ أَنَا۠ فَٱعۡبُدُونِ ﴿٢٥﴾

26. «አልረሕማንም (ከመላእክት) ልጅን ያዘ» አሉ፡፡ ጥራት ተገባው፡፡ አይደለም (መላእክት) የተከበሩ ባሮች ናቸው፡፡

وَقَالُواْ ٱتَّخَذَ ٱلرَّحۡمَٰنُ وَلَدٗاۗ سُبۡحَٰنَهُۥۚ بَلۡ عِبَادٞ مُّكۡرَمُونَ ﴿٢٦﴾

27. በንግግር አይቀድሙትም፤ (ያላለውን አይሉም)፡፡ እነርሱም በትእዛዙ ይሠራሉ፡፡

لَا يَسۡبِقُونَهُۥ بِٱلۡقَوۡلِ وَهُم بِأَمۡرِهِۦ يَعۡمَلُونَ ﴿٢٧﴾

28. በፊታቸው ያለውንና በኋላቸው ያለውንም ሁሉ ያውቃል፡፡ ለወደደውም ሰው እንጅ ለሌላው አያማልዱም፡፡ እነርሱም እርሱን ከመፍራታቸው የተነሳ ተጨናቂዎች ናቸው፡፡

يَعۡلَمُ مَا بَيۡنَ أَيۡدِيهِمۡ وَمَا خَلۡفَهُمۡ وَلَا يَشۡفَعُونَ إِلَّا لِمَنِ ٱرۡتَضَىٰ وَهُم مِّنۡ خَشۡيَتِهِۦ مُشۡفِقُونَ ﴿٢٨﴾

29. ከእነሱም «እኔ ከእርሱ ሌላ አምላክ ነኝ» የሚል ያንን ገሀነምን እንመነዳዋለን፡፡ እንደዚሁ በዳዮችን እንመነዳለን፡፡

۞وَمَن يَقُلۡ مِنۡهُمۡ إِنِّيٓ إِلَٰهٞ مِّن دُونِهِۦ فَذَٰلِكَ نَجۡزِيهِ جَهَنَّمَۚ كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٢٩﴾

30. እነዚያም የካዱት ሰማያትና ምድር የተጣበቁ የነበሩና የለያየናቸው መኾናችንን አያውቁምን ሕያው የኾነንም ነገር ሁሉ ከውሃ ፈጠርን፡፡ አያምኑምን

أَوَلَمۡ يَرَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَنَّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ كَانَتَا رَتۡقٗا فَفَتَقۡنَٰهُمَاۖ وَجَعَلۡنَا مِنَ ٱلۡمَآءِ كُلَّ شَيۡءٍ حَيٍّۚ أَفَلَا يُؤۡمِنُونَ ﴿٣٠﴾

31. በምድርም ውስጥ በእነሱ እንዳታረገርግ ጋራዎችን አደረግን፡፡ ይመሩም ዘንድ በእርሷ ውስጥ ሰፋፊ መንገዶችን አደረግን፡፡

وَجَعَلۡنَا فِي ٱلۡأَرۡضِ رَوَٰسِيَ أَن تَمِيدَ بِهِمۡ وَجَعَلۡنَا فِيهَا فِجَاجٗا سُبُلٗا لَّعَلَّهُمۡ يَهۡتَدُونَ ﴿٣١﴾

32. ሰማይንም (ከመውደቅ) የተጠበቀ ጣራ አደረግን፡፡ እነርሱም ከተዓምራቶቿ ዘንጊዎች ናቸው፡፡

وَجَعَلۡنَا ٱلسَّمَآءَ سَقۡفٗا مَّحۡفُوظٗاۖ وَهُمۡ عَنۡ ءَايَٰتِهَا مُعۡرِضُونَ ﴿٣٢﴾

33. እርሱም ሌሊትንና ቀንን፣ ፀሐይንና ጨረቃንም የፈጠረ ነው፡፡ ሁሉም በፈለካቸው ውስጥ ይዋኛሉ፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ وَٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَۖ كُلّٞ فِي فَلَكٖ يَسۡبَحُونَ ﴿٣٣﴾

34. (ሙሐመድ ሆይ!) ካንተ በፊት ለማንም ሰው ዘለዓለም መኖርን አላደረግንም፡፡ ታዲያ ብትሞት እነሱ ዘውታሪዎች ናቸውን

وَمَا جَعَلۡنَا لِبَشَرٖ مِّن قَبۡلِكَ ٱلۡخُلۡدَۖ أَفَإِيْن مِّتَّ فَهُمُ ٱلۡخَٰلِدُونَ ٣٤

35. ነፍስ ሁሉ ሞትን ቀማሽ ናት፡፡ ለመፈተንም በክፉም በበጎም እንሞክራችኋለን፡፡ ወደኛም ትመለሳላችሁ፡፡

كُلُّ نَفۡسٖ ذَآئِقَةُ ٱلۡمَوۡتِۗ وَنَبۡلُوكُم بِٱلشَّرِّ وَٱلۡخَيۡرِ فِتۡنَةٗۖ وَإِلَيۡنَا تُرۡجَعُونَ ٣٥

36. እነዚያም የካዱት ሰዎች ባዩህ ጊዜ መሳለቂያ አድርገው እንጂ አይይዙህም፡፡ እነሱ በአልረሕማን መወሳት እነርሱ ከሓዲዎች ሲሆኑ «ያ አማልክቶቻችሁን (በክፉ) የሚያነሳው ይህ ነውን» (ይላሉ)፡፡

وَإِذَا رَءَاكَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِن يَتَّخِذُونَكَ إِلَّا هُزُوًا أَهَٰذَا ٱلَّذِي يَذۡكُرُ ءَالِهَتَكُمۡ وَهُم بِذِكۡرِ ٱلرَّحۡمَٰنِ هُمۡ كَٰفِرُونَ ٣٦

37. ሰው ቸኳይ ሆኖ ተፈጠረ፡፡ ተዓምራቶቼን በእርግጥ አሳያችኋለሁና አታቻኩሉኝ፡፡

خُلِقَ ٱلۡإِنسَٰنُ مِنۡ عَجَلٖۚ سَأُوْرِيكُمۡ ءَايَٰتِي فَلَا تَسۡتَعۡجِلُونِ ٣٧

38. «ይህ ቀጠሮም መቼ ነው እውነተኞች ከኾናችሁ (አምጡት)» ይላሉ፡፡

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلۡوَعۡدُ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٣٨

39. እነዚያ የካዱት ከፊቶቻቸውና ከጀርባዎቻቸው ላይ እሳትን የማይከለክሉበትን እነሱም የማይረዳዱበትን ጊዜ ቢያውቁ ኖሮ (ይህንን አይሉም ነበር)፡፡

لَوۡ يَعۡلَمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ حِينَ لَا يَكُفُّونَ عَن وُجُوهِهِمُ ٱلنَّارَ وَلَا عَن ظُهُورِهِمۡ وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ٣٩

40. ይልቁንም (ሰዓቲቱ) በድንገት ትመጣቸዋለች፤ ታዋልላቸዋለችም፡፡ መመለሷንም አይችሉም፡፡ እነሱም አይቆዩም፡፡

بَلۡ تَأۡتِيهِم بَغۡتَةٗ فَتَبۡهَتُهُمۡ فَلَا يَسۡتَطِيعُونَ رَدَّهَا وَلَا هُمۡ يُنظَرُونَ ٤٠

41. ከአንተ በፊትም የነበሩት መልክተኞች በእርግጥ ተቀለደባቸው፡፡ በእነዚያም ከእነሱ ይቀልዱ በነበሩት በርሱ ይሳለቁበት የነበሩት (ቅጣት) ሰፈረባቸው፡፡

وَلَقَدِ ٱسۡتُهۡزِئَ بِرُسُلٖ مِّن قَبۡلِكَ فَحَاقَ بِٱلَّذِينَ سَخِرُواْ مِنۡهُم مَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ٤١

42. «ከአልረሕማን (ቅጣት) በሌሊትና በቀን የሚጠብቃችሁ ማነው» በላቸው፡፡ በእውነቱ እነሱ ከጌታቸው ግሳጼ (ከቁርአን) ዘንጊዎች ናቸው፡፡

قُلۡ مَن يَكۡلَؤُكُم بِٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِ مِنَ ٱلرَّحۡمَٰنِۚ بَلۡ هُمۡ عَن ذِكۡرِ رَبِّهِم مُّعۡرِضُونَ ٤٢

43. ለእነሱ ከእኛ ሌላ የምትከላከልላቸው አማልክት አለቻቸውን ነፍሶቻቸውን መርዳትን አይችሉም፡፡ እነርሱም (ከሓዲዎቹ) ከእኛ አይጠበቁም፡፡

أَمۡ لَهُمۡ ءَالِهَةٞ تَمۡنَعُهُم مِّن دُونِنَاۚ لَا يَسۡتَطِيعُونَ نَصۡرَ أَنفُسِهِمۡ وَلَا هُم مِّنَّا يُصۡحَبُونَ ٤٣

44. በእውነት እነዚህንና አባቶቻቸውን በእነሱ ላይ ዕድሜ እስከ ረዘመባቸው ድረስ አጣቀምናቸው፡፡ (ተታለሉም)፡፡ እኛ ምድርን ከጫፎችዋ የምናጎላት ኾነን ስንመጣባት አያዩምን እነሱ አሸናፊዎች ናቸውን

بَلۡ مَتَّعۡنَا هَٰٓؤُلَآءِ وَءَابَآءَهُمۡ حَتَّىٰ طَالَ عَلَيۡهِمُ ٱلۡعُمُرُۗ أَفَلَا يَرَوۡنَ أَنَّا نَأۡتِي ٱلۡأَرۡضَ نَنقُصُهَا مِنۡ أَطۡرَافِهَآۚ أَفَهُمُ ٱلۡغَٰلِبُونَ ٤٤

45. «የማስፈራራችሁ በተወረደልኝ ብቻ ነው፡፡ ግን ደንቆሮዎች በሚስፈራሩ ጊዜ ጥሪን አይሰሙም» በላቸው፡፡

قُلْ إِنَّمَآ أُنذِرُكُم بِٱلْوَحْىِ ۚ وَلَا يَسْمَعُ ٱلصُّمُّ ٱلدُّعَآءَ إِذَا مَا يُنذَرُونَ ﴿٤٥﴾

46. ከጌታህ ቅጣትም ወላፈን ብትነካቸው «ዋ ጥፋታችን! እኛ በዳዮች ነበርን» ይላሉ፡፡

وَلَئِن مَّسَّتْهُمْ نَفْحَةٌ مِّنْ عَذَابِ رَبِّكَ لَيَقُولُنَّ يَٰوَيْلَنَآ إِنَّا كُنَّا ظَٰلِمِينَ ﴿٤٦﴾

47. በትንሣኤም ቀን ትክክለኛ ሚዛኖችን እናቆማለን፡፡ ማንኛይቱም ነፍስ ምንንም አትበደልም፡፡ (ሥራው) የሰናፍጭ ቅንጣት ያክል ቢኾንም እርሷን እናመጣታለን፡፡ ተቆጣጣሪዎችም በኛ በቃ፡፡

وَنَضَعُ ٱلْمَوَٰزِينَ ٱلْقِسْطَ لِيَوْمِ ٱلْقِيَٰمَةِ فَلَا تُظْلَمُ نَفْسٌ شَيْـًٔا ۖ وَإِن كَانَ مِثْقَالَ حَبَّةٍ مِّنْ خَرْدَلٍ أَتَيْنَا بِهَا ۗ وَكَفَىٰ بِنَا حَٰسِبِينَ ﴿٤٧﴾

48. ለሙሳና ለሃሩንም እውነትንና ውሸትን የሚለይን ብርሃንንም ለጥንቁቆችም መገሰጫን በእርግጥ ሰጠናቸው፡፡

وَلَقَدْ ءَاتَيْنَا مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ٱلْفُرْقَانَ وَضِيَآءً وَذِكْرًا لِّلْمُتَّقِينَ ﴿٤٨﴾

49. ለእነዚያ ጌታቸውን በሩቅ ለሚፈሩት እነሱም ከሰዓቲቱ ተጨናቂዎች ለኾኑ (መገሰጫን ሰጠን)፡፡

ٱلَّذِينَ يَخْشَوْنَ رَبَّهُم بِٱلْغَيْبِ وَهُم مِّنَ ٱلسَّاعَةِ مُشْفِقُونَ ﴿٤٩﴾

50. ይህም (ቁርኣን) ያወረድነው የኾነ ብሩክ መገሰጫ ነው፡፡ ታዲያ እናንተ ለእርሱ ከሓዲዎች ናችሁን

وَهَٰذَا ذِكْرٌ مُّبَارَكٌ أَنزَلْنَٰهُ ۚ أَفَأَنتُمْ لَهُۥ مُنكِرُونَ ﴿٥٠﴾

51. ለኢብራሂምም ከዚያ በፊት ቅን መንገዱን በእርግጥ ሰጠነው፡፡ እኛም በእርሱ (ተገቢነት) ዐዋቂዎች ነበርን፡፡

۞ وَلَقَدْ ءَاتَيْنَآ إِبْرَٰهِيمَ رُشْدَهُۥ مِن قَبْلُ وَكُنَّا بِهِۦ عَٰلِمِينَ ﴿٥١﴾

52. ለአባቱና ለሕዝቦቹ «ይህቺ ቅርጻ ቅርጽ ያቺ እናንተ ለእርሷ ተገገዢዎች የኾናችሁት ምንድን ናት» ባለ ጊዜ (መራነው)፡፡

إِذْ قَالَ لِأَبِيهِ وَقَوْمِهِۦ مَا هَٰذِهِ ٱلتَّمَاثِيلُ ٱلَّتِىٓ أَنتُمْ لَهَا عَٰكِفُونَ ﴿٥٢﴾

53. «አባቶቻችንን ለእርሷ ተገገዢዎች ኾነው አገኘን» አሉት፡፡

قَالُوا۟ وَجَدْنَآ ءَابَآءَنَا لَهَا عَٰبِدِينَ ﴿٥٣﴾

54. «እናንተም አባቶቻችሁም በእርግጥ በግልጽ ስህተት ውስጥ ነበራችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ لَقَدْ كُنتُمْ أَنتُمْ وَءَابَآؤُكُمْ فِى ضَلَٰلٍ مُّبِينٍ ﴿٥٤﴾

55. «በምሩ መጣህልን ወይንስ አንተ ከሚቀልዱት ነህ» አሉት፡፡

قَالُوٓا۟ أَجِئْتَنَا بِٱلْحَقِّ أَمْ أَنتَ مِنَ ٱللَّٰعِبِينَ ﴿٥٥﴾

56. «አይደለም ጌታችሁ የሰማያትና የምድር ጌታ ያ የፈጠራቸው ነው፡፡ እኔም በዚህ ላይ ከመስካሪዎቹ ነኝ» አለ፡፡

قَالَ بَل رَّبُّكُمْ رَبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ٱلَّذِى فَطَرَهُنَّ وَأَنَا۠ عَلَىٰ ذَٰلِكُم مِّنَ ٱلشَّٰهِدِينَ ﴿٥٦﴾

57. «በአላህም እምላለሁ ዞሪዎች ኾናችሁ ከሄዳችሁ በኋላ ጣዖቶቻችሁን ተንኮል እሠራባቸዋለሁ» (አለ)፡፡

وَتَٱللَّهِ لَأَكِيدَنَّ أَصْنَٰمَكُم بَعْدَ أَن تُوَلُّوا۟ مُدْبِرِينَ ﴿٥٧﴾

58. (ዘወር ሲሉ) ስብርብሮችም አደረጋቸው፡፡ ለእነሱ የኾነ አንድ ታላቅ (ጣዖት) ብቻ ሲቀር ወደርሱ ይመለሱ ዘንድ (እርሱን ተወው)፡፡

فَجَعَلَهُمْ جُذَٰذًا إِلَّا كَبِيرًا لَّهُمْ لَعَلَّهُمْ إِلَيْهِ يَرْجِعُونَ ﴿٥٨﴾

59. «በአማልክቶቻችን ይህንን የሠራ ማነው እርሱ በእርግጥ ከበደለኞች ነው» አሉ፡፡

قَالُواْ مَن فَعَلَ هَٰذَا بِـَٔالِهَتِنَآ إِنَّهُۥ لَمِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٥٩

60. «ኢብራሂም የሚባል ጎበዝ (በመጥፎ) ሲያነሳቸው ሰምተናል» ተባባሉ፡፡

قَالُواْ سَمِعۡنَا فَتٗى يَذۡكُرُهُمۡ يُقَالُ لَهُۥٓ إِبۡرَٰهِيمُ ٦٠

61. «ይመሰክሩበት ዘንድ በሰዎቹ ዓይን (ፊት) ላይ አምጡት» አሉ፡፡

قَالُواْ فَأۡتُواْ بِهِۦ عَلَىٰٓ أَعۡيُنِ ٱلنَّاسِ لَعَلَّهُمۡ يَشۡهَدُونَ ٦١

62. «ኢብራሂም ሆይ! በአማልክቶቻችን ይህንን የሠራህ አንተ ነህን» አሉት፡፡

قَالُوٓاْ ءَأَنتَ فَعَلۡتَ هَٰذَا بِـَٔالِهَتِنَا يَٰٓإِبۡرَٰهِيمُ ٦٢

63. «አይደለም ይህ ታላቃቸው ሠራው፡፡ ይናገሩም እንደ ኾነ ጠይቋቸው» አለ፡፡

قَالَ بَلۡ فَعَلَهُۥ كَبِيرُهُمۡ هَٰذَا فَسۡـَٔلُوهُمۡ إِن كَانُواْ يَنطِقُونَ ٦٣

64. ወደ ነፍሶቻቸውም ተመለሱ፡፡ «እናንተ (በመጠየቃችሁ) በዳዮቹ እናንተው ናችሁም» ተባባሉ፡ ፡

فَرَجَعُوٓاْ إِلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡ فَقَالُوٓاْ إِنَّكُمۡ أَنتُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٦٤

65. ከዚያም በራሶቻቸው ላይ ተገለበጡ፡፡ «እነዚህ የሚናገሩ አለመኾናቸውን በእርግጥ ዐውቀሃል፤» (አሉ)፡፡

ثُمَّ نُكِسُواْ عَلَىٰ رُءُوسِهِمۡ لَقَدۡ عَلِمۡتَ مَا هَٰٓؤُلَآءِ يَنطِقُونَ ٦٥

66. «ታዲያ ለእናንተ ምንም የማይጠቅማችሁንና የማይጎዳችሁን ነገር ከአላህ ሌላ ትገዛላችሁን» አላቸው፡፡

قَالَ أَفَتَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَنفَعُكُمۡ شَيۡـٔٗا وَلَا يَضُرُّكُمۡ ٦٦

67. «ፎህ! ለእናንተ ከአላህ ሌላ ለምትገዙትም ነገር፤ አታውቁምን» (አለ)፡፡

أُفّٖ لَّكُمۡ وَلِمَا تَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ٦٧

68. «ሠሪዎች እንደ ኾናችሁ አቃጥሉት፡፡ አማልክቶቻችሁንም እርዱ» አሉ፡፡ (በእሳት ላይ ጣሉትም)፡፡

قَالُواْ حَرِّقُوهُ وَٱنصُرُوٓاْ ءَالِهَتَكُمۡ إِن كُنتُمۡ فَٰعِلِينَ ٦٨

69. «እሳት ሆይ! በኢብራሂም ላይ ቀዝቃዛ፤ ሰላምም ሁኚ» አልን፡፡

قُلۡنَا يَٰنَارُ كُونِي بَرۡدٗا وَسَلَٰمًا عَلَىٰٓ إِبۡرَٰهِيمَ ٦٩

70. በእርሱም ተንኮልን አሰቡ፡፡ በጣም ከሳሪዎችም አደረግናቸው፡፡

وَأَرَادُواْ بِهِۦ كَيۡدٗا فَجَعَلۡنَٰهُمُ ٱلۡأَخۡسَرِينَ ٧٠

71. እርሱንና ሉጥንም ወደዚያች፤ በውስጧ ለዓለማት በረከትን ወደ አደረግንባት ምድር (በመውሰድ) አዳን፡፡

وَنَجَّيۡنَٰهُ وَلُوطًا إِلَى ٱلۡأَرۡضِ ٱلَّتِي بَٰرَكۡنَا فِيهَا لِلۡعَٰلَمِينَ ٧١

72. ለእርሱም ኢስሐቅን ያዕቆብንም ተጨማሪ አድርገን ሰጠነው፡፡ ሁሉንም መልካሞች አደረግን፡፤

وَوَهَبۡنَا لَهُۥٓ إِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ نَافِلَةٗۖ وَكُلّٗا جَعَلۡنَا صَٰلِحِينَ ٧٢

73. በትዕዛዛችንም ወደ በጎ ሥራ የሚመሩ መሪዎች አደረግናቸው፡፡ ወደእነሱም መልካም ሥራዎችን መሥራትን፣ ሶላትንም መስገድን፣ ዘካንም መስጠትን አወረድን፡፡ ለእኛ ተገዢዎችም ነበሩ፡፡

وَجَعَلۡنَٰهُمۡ أَئِمَّةٗ يَهۡدُونَ بِأَمۡرِنَا وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡهِمۡ فِعۡلَ ٱلۡخَيۡرَٰتِ وَإِقَامَ ٱلصَّلَوٰةِ وَإِيتَآءَ ٱلزَّكَوٰةِۖ وَكَانُواْ لَنَا عَٰبِدِينَ ٧٣

74. ሉጥንም ፍርድንና ዕውቀትን ሰጠነው፡፡ ከዚያችም መጥፎ ሥራዎችን ትሠራ ከነበረችው ከተማ አዳንነው፡፡ እነሱ ክፉ ሰዎች አመጸኞች ነበሩና፡፡

وَلُوطًا ءَاتَيْنَٰهُ حُكْمًا وَعِلْمًا وَنَجَّيْنَٰهُ مِنَ ٱلْقَرْيَةِ ٱلَّتِي كَانَت تَّعْمَلُ ٱلْخَبَٰٓئِثَۚ إِنَّهُمْ كَانُوا۟ قَوْمَ سَوْءٍ فَٰسِقِينَ ﴿٧٤﴾

75. በችሮታችንም ውስጥ አገባነው፡፡ እርሱ ከመልካሞቹ ነውና፡፡

وَأَدْخَلْنَٰهُ فِي رَحْمَتِنَآۖ إِنَّهُۥ مِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿٧٥﴾

76. ኑሕንም ከዚያ በፊት (ጌታውን) በጠራ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ለእርሱም (ጥሪውን) ተቀበልነው፡፡ እርሱንም ቤተሰቦቹንም ከከባድ ጭንቅ አዳን፡፡

وَنُوحًا إِذْ نَادَىٰ مِن قَبْلُ فَٱسْتَجَبْنَا لَهُۥ فَنَجَّيْنَٰهُ وَأَهْلَهُۥ مِنَ ٱلْكَرْبِ ٱلْعَظِيمِ ﴿٧٦﴾

77. ከነዚያም በታምራቶቻችን ከአስተባበሉት ሕዝቦች (ተንኮል) ጠበቅነው፡፡ እነሱ ክፉ ሕዝቦች አመጸኞች ነበሩና፡፡ ሁሉንም አሰጠምናቸውም፡፡

وَنَصَرْنَٰهُ مِنَ ٱلْقَوْمِ ٱلَّذِينَ كَذَّبُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَآۚ إِنَّهُمْ كَانُوا۟ قَوْمَ سَوْءٍ فَأَغْرَقْنَٰهُمْ أَجْمَعِينَ ﴿٧٧﴾

78. ዳውድንና ሱለይማንንም በአዝመራው ነገር በሚፈርዱ ጊዜ የሕዝቦቹ ፍየሎች ሌሊት በርሱ ውስጥ በተሰማሩ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ፍርዳቸውንም ዐዋቂዎች ነበርን፡፡

وَدَاوُۥدَ وَسُلَيْمَٰنَ إِذْ يَحْكُمَانِ فِي ٱلْحَرْثِ إِذْ نَفَشَتْ فِيهِ غَنَمُ ٱلْقَوْمِ وَكُنَّا لِحُكْمِهِمْ شَٰهِدِينَ ﴿٧٨﴾

79. ለሱለይማንም (ትክክለኛይቱን ፍርድ) አሳወቅናት፡፡ ለሁሉም ጥበብንና ዕውቀትን ሰጠን፡፡ ተራራዎችን ከዳውድ ጋር የሚያወድሱ ሲኾኑ ገራን፡፡ አእዋፍንም (እንደዚሁ ገራን)፡፡ ሠሪዎችም ነበርን፡፡

فَفَهَّمْنَٰهَا سُلَيْمَٰنَۚ وَكُلًّا ءَاتَيْنَا حُكْمًا وَعِلْمًاۚ وَسَخَّرْنَا مَعَ دَاوُۥدَ ٱلْجِبَالَ يُسَبِّحْنَ وَٱلطَّيْرَۚ وَكُنَّا فَٰعِلِينَ ﴿٧٩﴾

80. የብረት ልብስንም ሥራ ለእናንተ ከጦራችሁ ትጠብቃችሁ ዘንድ አስተማርነው፡፡ እናንተ አመስጋኞች ናችሁን

وَعَلَّمْنَٰهُ صَنْعَةَ لَبُوسٍ لَّكُمْ لِتُحْصِنَكُم مِّنۢ بَأْسِكُمْۖ فَهَلْ أَنتُمْ شَٰكِرُونَ ﴿٨٠﴾

81. ለሱለይማንም ነፋስን በኀይል የምትነፍስ በትዕዛዙ ወደዚያች በእርሷ ውስጥ በረከትን ወደ አደረግንባት ምድር (ወደ ሻም) የምትፈስ ስትኾን (ገራንለት)፡፡ በነገሩ ሁሉም ዐዋቂዎች ነበርን፡፡

وَلِسُلَيْمَٰنَ ٱلرِّيحَ عَاصِفَةً تَجْرِي بِأَمْرِهِۦٓ إِلَى ٱلْأَرْضِ ٱلَّتِي بَٰرَكْنَا فِيهَاۚ وَكُنَّا بِكُلِّ شَيْءٍ عَٰلِمِينَ ﴿٨١﴾

82. ከሰይጣናትም ለእርሱ (ሉልን ለማውጣት) የሚጠልሙንና ከዚያም ሌላ ያለን ሥራ የሚሠሩን (ገራንለት)፡፡ ለእነሱም ተጠባባቂዎች ነበርን፡፡

وَمِنَ ٱلشَّيَٰطِينِ مَن يَغُوصُونَ لَهُۥ وَيَعْمَلُونَ عَمَلًا دُونَ ذَٰلِكَۖ وَكُنَّا لَهُمْ حَٰفِظِينَ ﴿٨٢﴾

83. አዩብንም (ኢዮብን) ጌታውን «እኔ መከራ አገኘኝ አንተም ከአዛኞች ሁሉ ይበልጥ አዛኝ ነህ» ሲል በተጣራ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

۞ وَأَيُّوبَ إِذْ نَادَىٰ رَبَّهُۥٓ أَنِّي مَسَّنِيَ ٱلضُّرُّ وَأَنتَ أَرْحَمُ ٱلرَّٰحِمِينَ ﴿٨٣﴾

84. ለእርሱም ጥሪውን ተቀበልነው፡፡ ከጉዳትም በእርሱ ላይ የነበረውን ሁሉ አስወገድን፡፡ ቤተሰቦቹንም ከእነሱም ጋር መሰላቸውን ከእኛ ዘንድ ለችሮታና ለተገዢዎች ለማስገንዘብ ሰጠነው፡፡

فَٱسْتَجَبْنَا لَهُۥ فَكَشَفْنَا مَا بِهِۦ مِن ضُرٍّۖ وَءَاتَيْنَٰهُ أَهْلَهُۥ وَمِثْلَهُم مَّعَهُمْ رَحْمَةً مِّنْ عِندِنَا وَذِكْرَىٰ لِلْعَٰبِدِينَ ﴿٨٤﴾

85. ኢስማዒልንም ኢድሪስንም ዙልኪፍልንም (አስታውስ)፡፡ ሁሉም ከታጋሾቹ ናቸው፡፡

وَإِسْمَٰعِيلَ وَإِدْرِيسَ وَذَا ٱلْكِفْلِۖ كُلٌّ مِّنَ ٱلصَّٰبِرِينَ ﴿٨٥﴾

86. ከችሮታችንም ውስጥ አገባናቸው፡፡ እነሱ ከመልካሞቹ ናቸውና፡፡

وَأَدۡخَلۡنَٰهُمۡ فِي رَحۡمَتِنَآۖ إِنَّهُم مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿٨٦﴾

87. የዓሳውንም ባለቤት ተቆጥቶ በኼደ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ በእርሱም ላይ ፈጽሞ የማንፈርድበት መኾናችንን ጠረጠረ፡፡ (ዓሳም ዋጠው)፡፡ በጨለማዎችም ውስጥ ኾኖ ከአንተ በቀር ሌላ አምላክ የለም፡፡ ጥራት ይገባህ፡፡ እኔ በእርግጥ ከበዳዮቹ ነበርኩ በማለት ተጣራ፡፡

وَذَا ٱلنُّونِ إِذ ذَّهَبَ مُغَٰضِبٗا فَظَنَّ أَن لَّن نَّقۡدِرَ عَلَيۡهِ فَنَادَىٰ فِي ٱلظُّلُمَٰتِ أَن لَّآ إِلَٰهَ إِلَّآ أَنتَ سُبۡحَٰنَكَ إِنِّي كُنتُ مِنَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٨٧﴾

88. ለርሱም ጥሪውን ተቀበልነው፡፡ ከጭንቅም አዳነው፡፡ እንደዚሁም ምእመናንን እናድናለን፡፡

فَٱسۡتَجَبۡنَا لَهُۥ وَنَجَّيۡنَٰهُ مِنَ ٱلۡغَمِّۚ وَكَذَٰلِكَ نُـۨجِي ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٨٨﴾

89. ዘከሪያንም «ጌታዬ ሆይ! ብቻዬን አትተወኝ፡፡ አንተም ከወራሾች ሁሉ በላጭ ነህ ሲል» ጌታውን በተጣራ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

وَزَكَرِيَّآ إِذۡ نَادَىٰ رَبَّهُۥ رَبِّ لَا تَذَرۡنِي فَرۡدٗا وَأَنتَ خَيۡرُ ٱلۡوَٰرِثِينَ ﴿٨٩﴾

90. ለእርሱም ጥሪውን ተቀበልነው፡፡ ለእርሱም የሕያን ሰጠነው፡፡ ለእርሱም ሚስቱን አበጀንለት፡፡ እነርሱ በበጎ ሥራዎች የሚቻኮሉ ከጃዮችና ፈሪዎች ኾነው የሚለምኑንም ነበሩ፡፡ ለእኛ ተዋራጆችም ነበሩ፡፡

فَٱسۡتَجَبۡنَا لَهُۥ وَوَهَبۡنَا لَهُۥ يَحۡيَىٰ وَأَصۡلَحۡنَا لَهُۥ زَوۡجَهُۥٓۚ إِنَّهُمۡ كَانُواْ يُسَٰرِعُونَ فِي ٱلۡخَيۡرَٰتِ وَيَدۡعُونَنَا رَغَبٗا وَرَهَبٗاۖ وَكَانُواْ لَنَا خَٰشِعِينَ ﴿٩٠﴾

91. ያችንም ብልቷን የጠበቀቺውን በርሷም ውስጥ ከመንፈሳችን የነፋንባትን እርሷንም ልጅዋንም (እንደዚሁ) ለዓለማት ተዓምር ያደረግናትን (መርየምን አስታውስ)፡፡

وَٱلَّتِيٓ أَحۡصَنَتۡ فَرۡجَهَا فَنَفَخۡنَا فِيهَا مِن رُّوحِنَا وَجَعَلۡنَٰهَا وَٱبۡنَهَآ ءَايَةٗ لِّلۡعَٰلَمِينَ ﴿٩١﴾

92. ይህች (ሕግጋት) አንዲት መንገድ ስትሆን በእርግጥ ሃይማኖታችሁ ናት፡፡ እኔም ጌታችሁ ነኝና ተገዙኝ፡፡

إِنَّ هَٰذِهِۦٓ أُمَّتُكُمۡ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ وَأَنَا۠ رَبُّكُمۡ فَٱعۡبُدُونِ ﴿٩٢﴾

93. በሃይማኖታቸውም ነገር በመካከላቸው ተለያዩ፡፡ ሁሉም ወደኛ ተመላሾች ናቸው፡፡

وَتَقَطَّعُوٓاْ أَمۡرَهُم بَيۡنَهُمۡۖ كُلٌّ إِلَيۡنَا رَٰجِعُونَ ﴿٩٣﴾

94. እርሱ ያመነ ኾኖ ከበጎ ሥራዎች ማንኛውንም የሚሠራም ሰው፤ ምንዳውን አይነፈግም፡፡ እኛም ለእርሱ መዝጋቢዎች ነን፡፡

فَمَن يَعۡمَلۡ مِنَ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَلَا كُفۡرَانَ لِسَعۡيِهِۦ وَإِنَّا لَهُۥ كَٰتِبُونَ ﴿٩٤﴾

95. ባጠፋናትም ከተማ ላይ እነሱ (ወደኛ) የማይመለሱ መኾናቸው እብለት ነው፤ (ይመለሳሉ)፡፡

وَحَرَٰمٌ عَلَىٰ قَرۡيَةٍ أَهۡلَكۡنَٰهَآ أَنَّهُمۡ لَا يَرۡجِعُونَ ﴿٩٥﴾

96. የእጁጅና መእጁጅም እነርሱ ከየተረተሩ የሚንደረደሩ ሲኾኑ (ግድባቸው) በተከፈተች ጊዜ፥

حَتَّىٰٓ إِذَا فُتِحَتۡ يَأۡجُوجُ وَمَأۡجُوجُ وَهُم مِّن كُلِّ حَدَبٖ يَنسِلُونَ ﴿٩٦﴾

97. እውነተኛውም ቀጠሮ በቀረበ ጊዜ፥ ያን ጊዜ እነሆ የእነዚያ የካዱት ሰዎች ዓይኖች ይፈጥጣሉ፡፡ «ዋ ጥፋታችን! ከዚህ (ቀን) በእርግጥ በዝንጋቴ ላይ ነበርን፤ በእውነትም በዳዮች ነበርን» (ይላሉ)፡፡

وَٱقۡتَرَبَ ٱلۡوَعۡدُ ٱلۡحَقُّ فَإِذَا هِيَ شَٰخِصَةٌ أَبۡصَٰرُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يَٰوَيۡلَنَا قَدۡ كُنَّا فِي غَفۡلَةٖ مِّنۡ هَٰذَا بَلۡ كُنَّا ظَٰلِمِينَ ﴿٩٧﴾

98. እናንተ ከአላህ ሌላ የምትግገዟቸውም (ጣዖታት) የገሀነም ማገዶዎች ናችሁ፡፡ እናንተ ለእርሷ ወራጆች ናችሁ፡፡

إِنَّكُمۡ وَمَا تَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ حَصَبُ جَهَنَّمَ أَنتُمۡ لَهَا وَٰرِدُونَ ٩٨

99. እነዚህ (ጣዖታት) አማልክት በነበሩ ኖሮ አይገቧዋትም ነበር፡፡ ግን ሁሉም በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

لَوۡ كَانَ هَٰٓؤُلَآءِ ءَالِهَةٗ مَّا وَرَدُوهَاۖ وَكُلّٞ فِيهَا خَٰلِدُونَ ٩٩

100. ለእነርሱ በእርሷ ውስጥ መንሰቅሰቅ አላቸው፡፡ እነርሱም በውስጧ (ምንንም) አይሰሙም፡፡

لَهُمۡ فِيهَا زَفِيرٞ وَهُمۡ فِيهَا لَا يَسۡمَعُونَ ١٠٠

101. እነዚያ ከእኛ መልካሚ ቃል ለእነርሱ ያለፈችላቸው እነዚያ ከርሷ የተራቁ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ سَبَقَتۡ لَهُم مِّنَّا ٱلۡحُسۡنَىٰٓ أُوْلَٰٓئِكَ عَنۡهَا مُبۡعَدُونَ ١٠١

102. ድምጽዋን አይሰሙም፡፡ እነርሱም ነፍሶቻቸው በሚሹት ነገር ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

لَا يَسۡمَعُونَ حَسِيسَهَاۖ وَهُمۡ فِي مَا ٱشۡتَهَتۡ أَنفُسُهُمۡ خَٰلِدُونَ ١٠٢

103. ታላቁ ድንጋጤ አያስተክዛቸውም፡፡ መላእክትም ይህ ያ ትቀጠሩ የነበራችሁት ቀናችሁ ነው፤ እያሉ ይቀበሏቸዋል፡፡

لَا يَحۡزُنُهُمُ ٱلۡفَزَعُ ٱلۡأَكۡبَرُ وَتَتَلَقَّىٰهُمُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ هَٰذَا يَوۡمُكُمُ ٱلَّذِي كُنتُمۡ تُوعَدُونَ ١٠٣

104. ለመጽሐፎች የኾኑ ገጾች እንደሚጠቀለሉ ሰማይን የምንጠቀልልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ የመጀመሪያን ፍጥረት እንደ ጀመርን እንመልሰዋለን፡፡ (መፈጸሙ) በእኛ ላይ የኾነን ቀጠሮ ቀጠርን፡፡ እኛ (የቀጠርነውን) ሠሪዎች ነን፡፡

يَوۡمَ نَطۡوِي ٱلسَّمَآءَ كَطَيِّ ٱلسِّجِلِّ لِلۡكُتُبِۚ كَمَا بَدَأۡنَآ أَوَّلَ خَلۡقٖ نُّعِيدُهُۥۚ وَعۡدًا عَلَيۡنَآۚ إِنَّا كُنَّا فَٰعِلِينَ ١٠٤

105. ምድንም መልካሞቹ ባሮቼ ይወርሷታል ማለትን ከመጽሐፉ (ከተጠበቀው ሰሌዳ) በኋላ በመጽሐፎቹ በእርግጥ ጽፈናል፡፡

وَلَقَدۡ كَتَبۡنَا فِي ٱلزَّبُورِ مِنۢ بَعۡدِ ٱلذِّكۡرِ أَنَّ ٱلۡأَرۡضَ يَرِثُهَا عِبَادِيَ ٱلصَّٰلِحُونَ ١٠٥

106. በዚህ (ቁርኣን) ውስጥ ለተገዢዎች ሕዝቦች በቂነት አለለ፡፡

إِنَّ فِي هَٰذَا لَبَلَٰغٗا لِّقَوۡمٍ عَٰبِدِينَ ١٠٦

107. (ሙሐመድ ሆይ!) ለዓለማትም እዝነት አድርገን እንጅ አልላክንህም፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَٰكَ إِلَّا رَحۡمَةٗ لِّلۡعَٰلَمِينَ ١٠٧

108. «ያ ወደኔ የሚወረደው አምላካችሁ አንድ አምላክ ብቻ ነው ማለት ነው፤ ታዲያ እናንተ ፍጹም ታዛዦች ናችሁን» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّمَا يُوحَىٰٓ إِلَيَّ أَنَّمَآ إِلَٰهُكُمۡ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞۖ فَهَلۡ أَنتُم مُّسۡلِمُونَ ١٠٨

109. እምቢም ቢሉ (በማወቅ) በእኩልነት ላይ ኾነን (የታዘዝኩትን) አስታውቅኋችሁ፡፡ «የምትስፈራሩበትም ነገር ቅርብ ወይም ሩቅ መኾኑን አላውቅም፤» በላቸው፡፡

فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَقُلۡ ءَاذَنتُكُمۡ عَلَىٰ سَوَآءٖۖ وَإِنۡ أَدۡرِيٓ أَقَرِيبٌ أَم بَعِيدٞ مَّا تُوعَدُونَ ١٠٩

110. እርሱ ከንግግር ጩኸትን ያውቃል፡፡ የምትደብቁትንም ሁሉ ያውቃል፡፡

إِنَّهُۥ يَعۡلَمُ ٱلۡجَهۡرَ مِنَ ٱلۡقَوۡلِ وَيَعۡلَمُ مَا تَكۡتُمُونَ ١١٠

111. እርሱም (ቅጣትን ማቆየት) ምናልባት ለእናንተ ፈተናና እስከ ጊዜው መጠቃቀሚያ እንደሆነም አላውቅም፤ (በላቸው)፡፡

وَإِنۡ أَدۡرِي لَعَلَّهُۥ فِتۡنَةٞ لَّكُمۡ وَمَتَٰعٌ إِلَىٰ حِينٖ ﴿١١١﴾

112. «ጌታዬ ሆይ! በእውነት ፍረድ፤ ጌታችንም እጅግ በጣም ሩኅሩኅ በምትሉት ነገር ላይ መታገዣ ነው» አለ፡፡

قَٰلَ رَبِّ ٱحۡكُم بِٱلۡحَقِّۗ وَرَبُّنَا ٱلرَّحۡمَٰنُ ٱلۡمُسۡتَعَانُ عَلَىٰ مَا تَصِفُونَ ﴿١١٢﴾

# ሱረቱ አል ሐጅ

# سورة الحج

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. እናንተ ሰዎች ሆይ! ጌታችሁን ፍሩ የሰዓቲቱ እንቅጥቃጤ በጣም ከባድ ነገር ነውና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ٱتَّقُواْ رَبَّكُمۡۚ إِنَّ زَلۡزَلَةَ ٱلسَّاعَةِ شَيۡءٌ عَظِيمٞ ﴿١﴾

2. በምታዩዋት ቀን አጥቢ ሁሉ ከአጠባችው ልጅ ትፈዝዛለች፡፡ የእርግዝና ባለቤት የኾነችም ሁሉ እርጉዟን ትጨነግፋለች፡፡ ሰዎቹንም (በድንጋጤ ብርታት) የሰከሩ ኾነው ታያለህ፡፡ እነርሱም (ከመጠጥ) የሰከሩ አይደሉም፡፡ ግን የአላህ ቅጣት ብርቱ ነው፡፡

يَوۡمَ تَرَوۡنَهَا تَذۡهَلُ كُلُّ مُرۡضِعَةٍ عَمَّآ أَرۡضَعَتۡ وَتَضَعُ كُلُّ ذَاتِ حَمۡلٍ حَمۡلَهَا وَتَرَى ٱلنَّاسَ سُكَٰرَىٰ وَمَا هُم بِسُكَٰرَىٰ وَلَٰكِنَّ عَذَابَ ٱللَّهِ شَدِيدٞ ﴿٢﴾

3. ከሰዎቹም ያለ ዕውቀት በአላህ ነገር የሚከራከር፤ ሞገደኛ ሰይጣንንም ሁሉ የሚከተል ሰው አልለ፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يُجَٰدِلُ فِي ٱللَّهِ بِغَيۡرِ عِلۡمٖ وَيَتَّبِعُ كُلَّ شَيۡطَٰنٖ مَّرِيدٖ ﴿٣﴾

4. እነሆ! የተከተለውን ሰው እርሱ ያጠመዋል፡፡ ወደ ነዳጅ እሳት ስቃይም ይመራዋል ማለት በርሱ ላይ ተጽፏል፡፡

كُتِبَ عَلَيۡهِ أَنَّهُۥ مَن تَوَلَّاهُ فَأَنَّهُۥ يُضِلُّهُۥ وَيَهۡدِيهِ إِلَىٰ عَذَابِ ٱلسَّعِيرِ ﴿٤﴾

5. እናንተ ሰዎች ሆይ! ከመቀስቀስ በመጠራጠር ውስጥ እንደ ሆናችሁ (አፈጣጠራችሁን ተመልከቱ)፡፡ እኛም ከዐፈር ፈጠርናችሁ፣ ከዚያም ከፍትወት ጠብታ፣ ከዚያም ከረጋ ደም፣ ከዚያም ከቁራጭ ሥጋ፣ ፍጥረትዋ ሙሉ ከሆነችና ሙሉ ካልሆነች (ቿሎታችንን) ለናንተ ልንገልጽላችሁ ፈጠርናችሁ፡፡ የምንሻውንም እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ በማሕፀን ውስጥ እናረጋዋለን፡፡ ከዚያም ሕፃን ሆናችሁ እናወጣችኋለን፡፡ ከዚያም ሙሉ ጥንካሪያችሁን ትደርሱ ዘንድ (እናሳድጋችኋለን)፡፡ ከእናንተም የሚሞት ሰው አልለ፡፡ ከእናንተም ከዕውቀት በኋላ ምንንም እንዳያውቅ ወደ ወራዳ ዕድሜ የሚመለስ ሰው አልለ፡፡ ምድርንም ደረቅ ሆና ታያታለህ፡፡ በእርሷም ላይ ውሃን ባወረድን ጊዜ ትላወሳለች፡፡ ትነፋፋለችም፡፡ ውበት ካለው ጎሳ ሁሉ ታበቅላለችም፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِن كُنتُمْ فِى رَيْبٍ مِّنَ ٱلْبَعْثِ فَإِنَّا خَلَقْنَـٰكُم مِّن تُرَابٍ ثُمَّ مِن نُّطْفَةٍ ثُمَّ مِنْ عَلَقَةٍ ثُمَّ مِن مُّضْغَةٍ مُّخَلَّقَةٍ وَغَيْرِ مُخَلَّقَةٍ لِّنُبَيِّنَ لَكُمْ ۚ وَنُقِرُّ فِى ٱلْأَرْحَامِ مَا نَشَآءُ إِلَىٰٓ أَجَلٍ مُّسَمًّى ثُمَّ نُخْرِجُكُمْ طِفْلًا ثُمَّ لِتَبْلُغُوٓا۟ أَشُدَّكُمْ ۖ وَمِنكُم مَّن يُتَوَفَّىٰ وَمِنكُم مَّن يُرَدُّ إِلَىٰٓ أَرْذَلِ ٱلْعُمُرِ لِكَيْلَا يَعْلَمَ مِنۢ بَعْدِ عِلْمٍ شَيْـًٔا ۚ وَتَرَى ٱلْأَرْضَ هَامِدَةً فَإِذَآ أَنزَلْنَا عَلَيْهَا ٱلْمَآءَ ٱهْتَزَّتْ وَرَبَتْ وَأَنۢبَتَتْ مِن كُلِّ زَوْجٍۭ بَهِيجٍ ﴿٥﴾

6. ይህ አላህ እርሱ መኖሩ የተረጋገጠ፣ እርሱም ሙታንን ሕያው የሚያደርግ፣ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ በመሆኑ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلْحَقُّ وَأَنَّهُۥ يُحْىِ ٱلْمَوْتَىٰ وَأَنَّهُۥ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٦﴾

7. ሰዓቲቱም መጪ ፣ በእርሷ ፈጽሞ ጥርጣሬ የሌለባት በመሆኗ፣ አላህም በመቃብሮች ውስጥ ያለን ሁሉ የሚቀሰቅስ በመሆኑ ነው፡፡

وَأَنَّ ٱلسَّاعَةَ ءَاتِيَةٌ لَّا رَيْبَ فِيهَا وَأَنَّ ٱللَّهَ يَبْعَثُ مَن فِى ٱلْقُبُورِ ﴿٧﴾

8. ከሰዎችም ውስጥ ያለ ዕውቀት፣ ያለ ማስረጃም፣ ያለ አብራሪ መጽሐፍም በአላህ ነገር የሚከራከር ሰው አልለ፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يُجَـٰدِلُ فِى ٱللَّهِ بِغَيْرِ عِلْمٍ وَلَا هُدًى وَلَا كِتَـٰبٍ مُّنِيرٍ ﴿٨﴾

9. ጎኑን ያጠፈ ሆኖ ከአላህ መንገድ ሊያሳስት (ይከራከራል)፡፡ በቅርቢቱ ዓለም ለእርሱ ውርደት አልለው፡፡ በትንሳኤ ቀንም አቃጣይን ቅጣት እናቀምሰዋለን፡፡

ثَانِىَ عِطْفِهِۦ لِيُضِلَّ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ ۖ لَهُۥ فِى ٱلدُّنْيَا خِزْىٌ ۖ وَنُذِيقُهُۥ يَوْمَ ٱلْقِيَـٰمَةِ عَذَابَ ٱلْحَرِيقِ ﴿٩﴾

10. ይህ እጆችህ ባስቀደሙት ኀጢአት አላህም ለባሮቹ ፈጽሞ በዳይ ባለመሆኑ ነው (ይባላል)፡፡

ذَٰلِكَ بِمَا قَدَّمَتْ يَدَاكَ وَأَنَّ ٱللَّهَ لَيْسَ بِظَلَّـٰمٍ لِّلْعَبِيدِ ﴿١٠﴾

11. ከሰዎችም (ከሃይማኖት) በጫፍ ላይ ሆኖ አላህን የሚግገዛ ሰው አልለ፡፡ ታዲያ መልካም ነገር ቢያገኘው በእርሱ ይረጋል፡፡ መከራም ብታገኘው በፊቱ ላይ ይገለበጣል፡፡ የቅርቢቱን ዓለምም የመጨረሻይቱንም ከሰረ፡፡ ይህ እርሱ ግልጽ ከሳራ ነው፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَعْبُدُ ٱللَّهَ عَلَىٰ حَرْفٍ ۖ فَإِنْ أَصَابَهُۥ خَيْرٌ ٱطْمَأَنَّ بِهِۦ ۖ وَإِنْ أَصَابَتْهُ فِتْنَةٌ ٱنقَلَبَ عَلَىٰ وَجْهِهِۦ خَسِرَ ٱلدُّنْيَا وَٱلْـَٔاخِرَةَ ۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلْخُسْرَانُ ٱلْمُبِينُ ﴿١١﴾

12. ከአላህ ሌላ የማይጎዳውንና የማይጠቅመውን ይግገዛል፡፡ ይህ እርሱ (ከእውነት) የራቀ ስህተት ነው፡፡

يَدْعُوا۟ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَضُرُّهُۥ وَمَا لَا يَنفَعُهُۥ ۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلضَّلَـٰلُ ٱلْبَعِيدُ ﴿١٢﴾

13. ያንን ከጥቅሙ ይልቅ ጉዳቱ የሚቀርብን ይግገዛል፡ ፡ ረዳቱ ምንኛ ከፋ!

يَدۡعُواْ لَمَن ضَرُّهُۥٓ أَقۡرَبُ مِن نَّفۡعِهِۦۚ لَبِئۡسَ ٱلۡمَوۡلَىٰ وَلَبِئۡسَ ٱلۡعَشِيرُ ١٣

14. አላህ እነዚያን ያመኑትንና መልካም ሥራዎችን የሠሩትን በሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች ያገባቸዋል፡፡ አላህ የሚሻውን ነገር በእርግጥ ይሠራል፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ يُدۡخِلُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَفۡعَلُ مَا يُرِيدُ ١٤

15. አላህ (መልክተኛውን) በቅርቢቱም በመጨረሻይቱም ዓለም አይረዳውም ብሎ የሚያስብ ሰው ገመድን ወደ ሰማይ ይዘርጋ፡፡ ከዚያም (ትንፋሹ እስኪቆረጥ) ይታነቅ፡፡ ተንኮሉ የሚያስቆጨውን ነገር ያስወግድለት እንደሆነም ይመልከት፡፡

مَن كَانَ يَظُنُّ أَن لَّن يَنصُرَهُ ٱللَّهُ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ فَلۡيَمۡدُدۡ بِسَبَبٍ إِلَى ٱلسَّمَآءِ ثُمَّ لۡيَقۡطَعۡ فَلۡيَنظُرۡ هَلۡ يُذۡهِبَنَّ كَيۡدُهُۥ مَا يَغِيظُ ١٥

16. እንደዚሁም (ቁርኣንን) የተብራሩ አንቀጾች አድርገን አወረድነው፡፡ አላህም የሚሻውን ሰው ይመራል፡፡

وَكَذَٰلِكَ أَنزَلۡنَٰهُ ءَايَٰتِۭ بَيِّنَٰتٖ وَأَنَّ ٱللَّهَ يَهۡدِي مَن يُرِيدُ ١٦

17. እነዚያ ያመኑት፣ እነዚያም ይሁዳውያን የሆኑ፣ ሳቢያኖችም፣ ክርስቲያኖችም፣ መጁሶችም እነዚያም (ጣዖታትን በአላህ) ያጋሩ አላህ በትንሣኤ ቀን በመካከላቸው በፍርድ ይለያል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ በእርግጥ ዐዋቂ ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَٱلَّذِينَ هَادُواْ وَٱلصَّٰبِـِٔينَ وَٱلنَّصَٰرَىٰ وَٱلۡمَجُوسَ وَٱلَّذِينَ أَشۡرَكُوٓاْ إِنَّ ٱللَّهَ يَفۡصِلُ بَيۡنَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ شَهِيدٌ ١٧

18. አላህ በሰማያት ያለው ሁሉ፣ በምድርም ያለው ሁሉ፣ ፀሐይና ጨረቃም፣ ከዋክብትም፣ ተራራዎችም፣ ዛፎችም፣ ተንቀሳቃሾችም ከሰዎች ብዙዎችም፣ ለርሱ የሚሰግዱለት መሆኑን አታውቁምን ብዙውም በርሱ ላይ ቅጣት ተረጋገጠበት፡፡ አላህ የሚያዋርደውም ሰው ለእርሱ ምንም አክባሪ የለውም፡፡ አላህ የሻውን ይሠራልና፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ يَسۡجُدُۤ لَهُۥ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ وَٱلشَّمۡسُ وَٱلۡقَمَرُ وَٱلنُّجُومُ وَٱلۡجِبَالُ وَٱلشَّجَرُ وَٱلدَّوَآبُّ وَكَثِيرٞ مِّنَ ٱلنَّاسِۖ وَكَثِيرٌ حَقَّ عَلَيۡهِ ٱلۡعَذَابُۗ وَمَن يُهِنِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِن مُّكۡرِمٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَفۡعَلُ مَا يَشَآءُ۩ ١٨

19. እነዚህ በጌታቸው የተከራከሩ ሁለት ባላጋራዎች ናቸው፡፡ እነዚያም የካዱት ለእነርሱ የእሳት ልብሶች ተለክተውላቸዋል፡፡ ከራሶቻቸው በላይ የፈላ ውሃ ይምቧቧቸዋል፡፡

۞هَٰذَانِ خَصۡمَانِ ٱخۡتَصَمُواْ فِي رَبِّهِمۡۖ فَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ قُطِّعَتۡ لَهُمۡ ثِيَابٞ مِّن نَّارٖ يُصَبُّ مِن فَوۡقِ رُءُوسِهِمُ ٱلۡحَمِيمُ ١٩

20. በሆዶቻቸው ውስጥ ያሉ ቆዳዎቻቸውም በእርሱ ይቀለጣሉ፡፡

يُصۡهَرُ بِهِۦ مَا فِي بُطُونِهِمۡ وَٱلۡجُلُودُ ٢٠

21. ለእነሱም (መቅጫ) ከብረት የሆኑ መዶሻዎች አሉሉ፡፡

وَلَهُم مَّقَٰمِعُ مِنۡ حَدِيدٖ ٢١

22. ከጭንቀት ብርታት የተነሳ ከእርሷ ለመውጣት በፈለጉ ቁጥር ከእርሷ ውስጥ እንዲመለሱ ይደረጋሉ፡፡ «በጣም የሚያቃጥልንም ቅጣት ቅመሱ» (ይባላሉ)፡፡

كُلَّمَآ أَرَادُوٓاْ أَن يَخۡرُجُواْ مِنۡهَا مِنۡ غَمٍّ أُعِيدُواْ فِيهَا وَذُوقُواْ عَذَابَ ٱلۡحَرِيقِ ٢٢

23. አላህ እነዚያን ያመኑትንና መልካም ሥራዎችን የሠሩትን ሰዎች በሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈስሱባቸውን ገነቶች ያገባቸዋል፡፡ በእርሷ ውስጥ ከወርቅ የሆኑን አንባሮችና ሉልን ይሸለማሉ፡፡ በእርሷ ውስጥ ልብሶቻቸውም ሐር ናቸው፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ يُدۡخِلُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ يُحَلَّوۡنَ فِيهَا مِنۡ أَسَاوِرَ مِن ذَهَبٖ وَلُؤۡلُؤٗاۖ وَلِبَاسُهُمۡ فِيهَا حَرِيرٞ ﴿٢٣﴾

24. ከንግግርም ወደ መልካሙ ተመሩ፡፡ ወደ ምስጉንም መንገድ ተመሩ፡፡

وَهُدُوٓاْ إِلَى ٱلطَّيِّبِ مِنَ ٱلۡقَوۡلِ وَهُدُوٓاْ إِلَىٰ صِرَٰطِ ٱلۡحَمِيدِ ﴿٢٤﴾

25. እነዚያ የካዱ ከአላህም መንገድና ከዚያም ለሰዎች በውስጡ ነዋሪ ለሆኑትም፣ ከሩቅ ለሚመጡትም እኩል ካደረግነው ከተከበረው መስጊድ (ሰዎችን) የሚከለክሉ (አሳማሚን ቅጣት እናቀምሳቸዋለን)፡፡ በእርሱም ውስጥ (ከትክክለኛ መንገድ) በመዘንበል በዳይ ሆኖ (ማንኛውንም ነገር) የሚፈልግ ሰው ከአሳማሚ ቅጣት እናቀምሰዋለን፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَيَصُدُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَٱلۡمَسۡجِدِ ٱلۡحَرَامِ ٱلَّذِي جَعَلۡنَٰهُ لِلنَّاسِ سَوَآءً ٱلۡعَٰكِفُ فِيهِ وَٱلۡبَادِۚ وَمَن يُرِدۡ فِيهِ بِإِلۡحَادِۭ بِظُلۡمٖ نُّذِقۡهُ مِنۡ عَذَابٍ أَلِيمٖ ﴿٢٥﴾

26. ለኢብራሂምም የቤቱን (የካዕባን) ስፍራ መመለሻ ባደረግንለት ጊዜ «በእኔ ምንንም አታጋራ፣ ቤቴንም ለሚዞሩትና ለሚቆሙበት ለሚያጎነብሱትና በግንባራቸውም ለሚደፉት ንጹሕ አድርግላቸው» (ባልነው ጊዜ አስታውስ)፡፡

وَإِذۡ بَوَّأۡنَا لِإِبۡرَٰهِيمَ مَكَانَ ٱلۡبَيۡتِ أَن لَّا تُشۡرِكۡ بِي شَيۡـٔٗا وَطَهِّرۡ بَيۡتِيَ لِلطَّآئِفِينَ وَٱلۡقَآئِمِينَ وَٱلرُّكَّعِ ٱلسُّجُودِ ﴿٢٦﴾

27. (አልነውም)፡- በሰዎችም ውስጥ በሐጅ ትዕዛዝ ጥራ፡፡ እግረኞች ከየሩቅ መንገድ በሚመጡ ከሲታ ግመሎችም ሁሉ ላይ ሆነው ይመጡሃልና፡፡

وَأَذِّن فِي ٱلنَّاسِ بِٱلۡحَجِّ يَأۡتُوكَ رِجَالٗا وَعَلَىٰ كُلِّ ضَامِرٖ يَأۡتِينَ مِن كُلِّ فَجٍّ عَمِيقٖ ﴿٢٧﴾

28. ለእነሱ የሆኑ ጥቅሞችን ይጣዱ ዘንድ በታወቁ ቀኖችም ውስጥ ከለማዳ እንስሳዎች በሰጣቸው ሲሳይ ላይ የአላህን ስም ያወሱ ዘንድ (ይመጡሃል)፡፡ ከርሷም ብሉ፡፡ ችግረኛ ድሃንም አብሉ፡፡

لِّيَشۡهَدُواْ مَنَٰفِعَ لَهُمۡ وَيَذۡكُرُواْ ٱسۡمَ ٱللَّهِ فِيٓ أَيَّامٖ مَّعۡلُومَٰتٍ عَلَىٰ مَا رَزَقَهُم مِّنۢ بَهِيمَةِ ٱلۡأَنۡعَٰمِۖ فَكُلُواْ مِنۡهَا وَأَطۡعِمُواْ ٱلۡبَآئِسَ ٱلۡفَقِيرَ ﴿٢٨﴾

29. ከዚያም (እንደ ጠጉርና ጥፍር ያሉትን) ትርፍ አካላቸውንና ዕድፋቸውን ያስወግዱ፡፡ ስለቶቻቸውንም ይሙሉ፤ በጥንታዊውም ቤት ይዙሩ፡፡

ثُمَّ لۡيَقۡضُواْ تَفَثَهُمۡ وَلۡيُوفُواْ نُذُورَهُمۡ وَلۡيَطَّوَّفُواْ بِٱلۡبَيۡتِ ٱلۡعَتِيقِ ﴿٢٩﴾

30. (ነገሩ) ይህ ነው፡፡ የአላህንም ሕግጋት የሚያከብር ሰው እርሱ ጌታው ዘንድ ለእርሱ በጣም የተሻለ ነው፡፡ የቤት እንስሳትም (ግመል ከብት በግና ፍየል) በናንተ ላይ (እርም መሆኑ) ከሚነበብላችሁ በስተቀር ለእናንተ ተፈቅዳላችኋለች፡፡ ከጣዖታትም ርክሰት ተጠንቀቁ፡፡ ሐሰትንም ቃል ራቁ፡፡

ذَٰلِكَۖ وَمَن يُعَظِّمۡ حُرُمَٰتِ ٱللَّهِ فَهُوَ خَيۡرٞ لَّهُۥ عِندَ رَبِّهِۦۗ وَأُحِلَّتۡ لَكُمُ ٱلۡأَنۡعَٰمُ إِلَّا مَا يُتۡلَىٰ عَلَيۡكُمۡۖ فَٱجۡتَنِبُواْ ٱلرِّجۡسَ مِنَ ٱلۡأَوۡثَٰنِ وَٱجۡتَنِبُواْ قَوۡلَ ٱلزُّورِ ﴿٣٠﴾

حُنَفَآءَ لِلَّهِ غَيۡرَ مُشۡرِكِينَ بِهِۦۚ وَمَن يُشۡرِكۡ بِٱللَّهِ فَكَأَنَّمَا خَرَّ مِنَ ٱلسَّمَآءِ فَتَخۡطَفُهُ ٱلطَّيۡرُ أَوۡ تَهۡوِي بِهِ ٱلرِّيحُ فِي مَكَانٖ سَحِيقٖ ٣١

31. ለአላህ ታዛዦች በእርሱ የማታገሩ ሆናችሁ (ከሐሰት ራቁ)፡፡ በአላህም የሚያጋራ ሰው፤ ከሰማይ እንደ ወደቀና በራሪ እንደምትነጥቀው፣ ወይም ነፋስ እርሱን በሩቅ ስፍራ እንደምትጥለው ብጤ ነው፡፡

ذَٰلِكَۖ وَمَن يُعَظِّمۡ شَعَٰٓئِرَ ٱللَّهِ فَإِنَّهَا مِن تَقۡوَى ٱلۡقُلُوبِ ٣٢

32. (ነገሩ) ይህ ነው፡፡ የአላህንም የሃይማኖት ምልክቶች የሚያከብር ሰው እርሷ ከልቦች የኾነች ጥንቃቄ ናት፡፡

لَكُمۡ فِيهَا مَنَٰفِعُ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗى ثُمَّ مَحِلُّهَآ إِلَى ٱلۡبَيۡتِ ٱلۡعَتِيقِ ٣٣

33. ለእናንተ በእርሷ እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ ጥቅሞች አሏችሁ፡፡ ከዚያም (የማረጃ) ስፍራዋ እጥንታዊው ቤት አጠገብ ነው፡፡

وَلِكُلِّ أُمَّةٖ جَعَلۡنَا مَنسَكٗا لِّيَذۡكُرُواْ ٱسۡمَ ٱللَّهِ عَلَىٰ مَا رَزَقَهُم مِّنۢ بَهِيمَةِ ٱلۡأَنۡعَٰمِۗ فَإِلَٰهُكُمۡ إِلَٰهٞ وَٰحِدٞ فَلَهُۥٓ أَسۡلِمُواْۗ وَبَشِّرِ ٱلۡمُخۡبِتِينَ ٣٤

34. ለሕዝብም ሁሉ (ወደ አላህ) መስዋዕት ማቅረብን ደነገግን፡፡ ከቤት እንስሳት በሰጣቸው ሲሳይ ላይ የአላህን ስም ብቻ ያወሱ ዘንድ (አዘዝናቸው)፡፡ አምላካችሁም አንድ አምላክ ብቻ ነው፡፡ ለእርሱም ብቻ ታዘዙ፡፡ ለአላህ ተዋራጆችንም አብስራቸው፡፡

ٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِرَ ٱللَّهُ وَجِلَتۡ قُلُوبُهُمۡ وَٱلصَّٰبِرِينَ عَلَىٰ مَآ أَصَابَهُمۡ وَٱلۡمُقِيمِي ٱلصَّلَوٰةِ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ٣٥

35. እነዚያን አላህ በተወሳ ጊዜ ልቦቻቸው የሚጨነቁትን፣ በደረሰባቸውም (መከራ) ላይ ታጋሾችን፣ ሶላትንም አስተካክለው ሰጋጆችን፣ ከሰጠናቸውም ሲሳይ የሚለግሱትን (አብስር)፡፡

وَٱلۡبُدۡنَ جَعَلۡنَٰهَا لَكُم مِّن شَعَٰٓئِرِ ٱللَّهِ لَكُمۡ فِيهَا خَيۡرٞۖ فَٱذۡكُرُواْ ٱسۡمَ ٱللَّهِ عَلَيۡهَا صَوَآفَّۖ فَإِذَا وَجَبَتۡ جُنُوبُهَا فَكُلُواْ مِنۡهَا وَأَطۡعِمُواْ ٱلۡقَانِعَ وَٱلۡمُعۡتَرَّۚ كَذَٰلِكَ سَخَّرۡنَٰهَا لَكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ٣٦

36. ግመሎችንም ለእናንተ ከአላህ ሃይማኖት ምልክቶች አደረግናቸው፡፡ በእርሷ ለእናንተ መልካም ጥቅም አላችሁ፡፡ በእርሷም ላይ (ስታርዷት) በሶስት እግሮችዋ ቆማ የተሰለፈች ሆና የአላህን ስም አውሱ፡፡ ጎኖቻቸውም በወደቁ ጊዜ ከእርሷ ብሉ፡፡ ለማኙንም ለልመና የሚያገዳድምንም አብሉ፡፡ እንደዚሁ ታመሰግኑ ዘንድ ለእናንተ ገራናት፡፡

لَن يَنَالَ ٱللَّهَ لُحُومُهَا وَلَا دِمَآؤُهَا وَلَٰكِن يَنَالُهُ ٱلتَّقۡوَىٰ مِنكُمۡۚ كَذَٰلِكَ سَخَّرَهَا لَكُمۡ لِتُكَبِّرُواْ ٱللَّهَ عَلَىٰ مَا هَدَىٰكُمۡۗ وَبَشِّرِ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٣٧

37. አላህን ሥጋዎቿም ደሞቿም ፈጽሞ አይደርሰውም፡ ፡ ግን ከእናንተ የሆነው ፍራቻ ይደርሰዋል፡፡ እንደዚሁ አላህን በመራችሁ ላይ ልታከብሩት ለእናንተ ገራት፡፡ በጎ ሠሪዎችንም አብስር፡፡

۞إِنَّ ٱللَّهَ يُدَٰفِعُ عَنِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ كُلَّ خَوَّانٖ كَفُورٍ ٣٨

38. አላህ ከእነዚያ ካመኑት ላይ ይከላከልላቸዋል፡፡ አላህ ከዳተኛን ውለታቢስን ሁሉ አይወድም፡፡

أُذِنَ لِلَّذِينَ يُقَٰتَلُونَ بِأَنَّهُمۡ ظُلِمُواْۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ نَصۡرِهِمۡ لَقَدِيرٌ ٣٩

39. ለእነዚያ ለሚገደሉት (ምእመናን) እነርሱ የተበደሉ በመኾናቸው (መጋደል) ተፈቀደላቸው፡፡ አላህም እነርሱን በመርዳት ላይ በእርግጥ ቻይ ነው፡፡

40. ለእነዚያ «ጌታችን አላህ ነው» ከማለታቸው በስተቀር ያለ አግባብ ከአገራቸው የተባረሩ ለሆኑት (ተፈቀደ)፡፡ አላህ ሰዎችን ከፊላቸውን በከፊሉ መገፍተሩ ባልነበረ ኖሮ ገዳማት፣ ቤተክርስቲያኖችም፣ ምኩራቦችም በውስጣቸው የአላህ ስም በብዛት የሚወሳባቸው መስጊዶችም፤ በተፈረሱ ነበር፡፡ አላህም ሃይማኖቱን የሚረዳውን ሰው በእርግጥ ይረዳዋል፡፡ አላህ ብርቱ አሸናፊ ነውና፡፡

ٱلَّذِينَ أُخۡرِجُواْ مِن دِيَٰرِهِم بِغَيۡرِ حَقٍّ إِلَّآ أَن يَقُولُواْ رَبُّنَا ٱللَّهُۗ وَلَوۡلَا دَفۡعُ ٱللَّهِ ٱلنَّاسَ بَعۡضَهُم بِبَعۡضٖ لَّهُدِّمَتۡ صَوَٰمِعُ وَبِيَعٞ وَصَلَوَٰتٞ وَمَسَٰجِدُ يُذۡكَرُ فِيهَا ٱسۡمُ ٱللَّهِ كَثِيرٗاۗ وَلَيَنصُرَنَّ ٱللَّهُ مَن يَنصُرُهُۥٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَقَوِيٌّ عَزِيزٌ ٤٠

41. (እነርሱም) እነዚያ በምድር ላይ ብናስመቻቸው ሶላትን እንደሚገባ የሚያስተካክሉ፣ ዘካንም የሚሰጡ፣ በደግ ነገርም የሚያዝዙ፣ ከመጥፎ ነገርም የሚከለክሉ ናቸው፡፡ የነገሮቹም ሁሉ መጨረሻ ወደ አላህ ነው፡፡

ٱلَّذِينَ إِن مَّكَّنَّٰهُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ أَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَوُاْ ٱلزَّكَوٰةَ وَأَمَرُواْ بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَنَهَوۡاْ عَنِ ٱلۡمُنكَرِۗ وَلِلَّهِ عَٰقِبَةُ ٱلۡأُمُورِ ٤١

42. ቢያስተባብሉህም ከእነሱ በፊት የኑሕ ሕዝቦች ዓድና ሰሙድም በእርግጥ አስተባብለዋል፡፡

وَإِن يُكَذِّبُوكَ فَقَدۡ كَذَّبَتۡ قَبۡلَهُمۡ قَوۡمُ نُوحٖ وَعَادٞ وَثَمُودُ ٤٢

43. የኢብራሂምም ሕዝቦች የሉጥም ሕዝቦች (አስተባብለዋል)፡፡

وَقَوۡمُ إِبۡرَٰهِيمَ وَقَوۡمُ لُوطٖ ٤٣

44. የመድየንም ሰዎች (አስተባብለዋል)፡፡ ሙሳም ተስተባብሏል፡፡ ለከሓዲዎቹም ጊዜ ሰጠኋቸው፡፡ ከዚያም ያዝቸው፡፡ ጥላቻዬም እንዴት ነበረ!

وَأَصۡحَٰبُ مَدۡيَنَۖ وَكُذِّبَ مُوسَىٰۖ فَأَمۡلَيۡتُ لِلۡكَٰفِرِينَ ثُمَّ أَخَذۡتُهُمۡۖ فَكَيۡفَ كَانَ نَكِيرِ ٤٤

45. ከከተማም እርሷ በደለኛ ሆና ያጠፋናትና እርሷ በጣሪያዎቿ ላይ ወዳቂ የሆነችው ብዙ ናት፡፡ ከተራቆተችም የውሃ ጉድጓድ ከተገነባም ሕንፃ (ያጠፋነው ብዙ ነው)፡፡

فَكَأَيِّن مِّن قَرۡيَةٍ أَهۡلَكۡنَٰهَا وَهِيَ ظَالِمَةٞ فَهِيَ خَاوِيَةٌ عَلَىٰ عُرُوشِهَا وَبِئۡرٖ مُّعَطَّلَةٖ وَقَصۡرٖ مَّشِيدٍ ٤٥

46. ለእነርሱም በእነርሱ የሚያውቁባቸው ልቦች ወይም በእነርሱ የሚሰሙባቸው ጆሮች ይኖሯቸው ዘንድ በምድር ላይ አይሄዱምን እነሆ ዓይኖች አይታወሩም ግን እነዚያ በደረቶች ውስጥ ያሉት ልቦች ይታወራሉ፡፡

أَفَلَمۡ يَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَتَكُونَ لَهُمۡ قُلُوبٞ يَعۡقِلُونَ بِهَآ أَوۡ ءَاذَانٞ يَسۡمَعُونَ بِهَاۖ فَإِنَّهَا لَا تَعۡمَى ٱلۡأَبۡصَٰرُ وَلَٰكِن تَعۡمَى ٱلۡقُلُوبُ ٱلَّتِي فِي ٱلصُّدُورِ ٤٦

47. አላህም ቀጠሮውን በፍጹም የማይጥስ ሲሆን በቅጣት ያቻኩሉሃል፡፡ እጌታህም ዘንድ አንዱ ቀን ከምትቆጥሩት (ቀን) እንደ ሺሕ ዓመት ነው፡፡

وَيَسۡتَعۡجِلُونَكَ بِٱلۡعَذَابِ وَلَن يُخۡلِفَ ٱللَّهُ وَعۡدَهُۥۚ وَإِنَّ يَوۡمًا عِندَ رَبِّكَ كَأَلۡفِ سَنَةٖ مِّمَّا تَعُدُّونَ ٤٧

48. ከከተማ እርሷ በዳይ ሆና ለእርሷ ጊዜ የሰጠኋትና ከዚያም የያዝኳት ብዙ ናት፡፡ መመለሻም ወደኔ ብቻ ነው፡፡

وَكَأَيِّن مِّن قَرۡيَةٍ أَمۡلَيۡتُ لَهَا وَهِيَ ظَالِمَةٞ ثُمَّ أَخَذۡتُهَا وَإِلَيَّ ٱلۡمَصِيرُ ٤٨

49. «እናንተ ሰዎች ሆይ! እኔ ለእናንተ ግልጽ አስጠንቃቂ ብቻ ነኝ» በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِنَّمَآ أَنَا۠ لَكُمۡ نَذِيرٞ مُّبِينٞ ٤٩

50. እነዚያም ያመኑ መልካም ሥራዎችንም የሠሩ ለእነርሱ ምህረትና ያማረ ሲሳይ አላቸው፡፡

فَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَرِزۡقٞ كَرِيمٞ ٥٠

51. እነዚያም የሚያመልጡ መስሏቸው ተዓምራቶቻችንን በመንቀፍ የተጉ እነሱ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ سَعَوۡاْ فِيٓ ءَايَٰتِنَا مُعَٰجِزِينَ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَحِيمِ ٥١

52. ከመልክተኛና ከነቢይም ከአንተ በፊት አንድንም አላክንም ባነበበ (እና ዝም ባለ) ጊዜ ሰይጣን በንባቡ ላይ (ማጥመሚያን ቃል) የሚጥል ቢሆን እንጅ፡፡ ወዲያውም አላህ ሰይጣን የሚጥለውን ያስወግዳል፡፡ ከዚያም አላህ አንቀጾቹን ያጠነክራል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ مِن رَّسُولٖ وَلَا نَبِيٍّ إِلَّآ إِذَا تَمَنَّىٰٓ أَلۡقَى ٱلشَّيۡطَٰنُ فِيٓ أُمۡنِيَّتِهِۦ فَيَنسَخُ ٱللَّهُ مَا يُلۡقِي ٱلشَّيۡطَٰنُ ثُمَّ يُحۡكِمُ ٱللَّهُ ءَايَٰتِهِۦۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٞ ٥٢

53. ሰይጣን የሚጥለውን ነገር ለእነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ በሽታ ላለባቸው ልቦቻቸውም ደረቆች ለሆኑት ፈተና ሊያደርግ (ይጥላል)፡፡ በዳዮችም ከእውነት በራቀ ጭቅጭቅ ውስጥ ናቸው፡፡

لِّيَجۡعَلَ مَا يُلۡقِي ٱلشَّيۡطَٰنُ فِتۡنَةٗ لِّلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ وَٱلۡقَاسِيَةِ قُلُوبُهُمۡۗ وَإِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ لَفِي شِقَاقِۭ بَعِيدٖ ٥٣

54. እነዚያም ዕውቀትን የተሰጡት እርሱ (ቁርኣን) ከጌታህ የኾነ እውነት መኾኑን እንዲያውቁና በእርሱ እንዲያምኑ ልቦቻቸውም ለእርሱ እንዲረኩ (ያጠነክራል)፡፡ አላህም እነዚያን ያመኑትን ወደ ቀጥተኛው መንገድ በእርግጥ መሪ ነው፡፡

وَلِيَعۡلَمَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡعِلۡمَ أَنَّهُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ فَيُؤۡمِنُواْ بِهِۦ فَتُخۡبِتَ لَهُۥ قُلُوبُهُمۡۗ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَهَادِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ٥٤

55. እነዚያ የካዱት ሰዎች ሰዓቲቱ በድንገት እስከምትመጣባቸው ወይም (ከደግ ነገር) መካን የሆነው ቀን ቅጣት እስከሚመጣባቸው ድረስ ከእርሱ (ከቁርኣን) በመጠራጠር ውስጥ ከመሆን አይወገዱም፡፡

وَلَا يَزَالُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فِي مِرۡيَةٖ مِّنۡهُ حَتَّىٰ تَأۡتِيَهُمُ ٱلسَّاعَةُ بَغۡتَةً أَوۡ يَأۡتِيَهُمۡ عَذَابُ يَوۡمٍ عَقِيمٍ ٥٥

56. በዚያ ቀን ንግሥናው የአላህ ብቻ ነው፡፡ በመካከላቸው ይፈርዳል፡፡ እነዚያም ያመኑት መልካም ሥራዎችንም የሠሩት በመደሰቻ ገነቶች ውስጥ ናቸው፡፡

ٱلۡمُلۡكُ يَوۡمَئِذٖ لِّلَّهِ يَحۡكُمُ بَيۡنَهُمۡۚ فَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فِي جَنَّٰتِ ٱلنَّعِيمِ ٥٦

57. እነዚያም የካዱት በአንቀጾቻችንም ያስተባበሉት እነዚያ ለእነርሱ አዋራጅ ቅጣት አላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا فَأُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٞ مُّهِينٞ ٥٧

58. እነዚያም በአላህ ሃይማኖት የተሰደዱ ከዚያም የተገደሉ ወይም የሞቱ አላህ መልካምን ሲሳይ በእርግጥ ይሰጣቸዋል፡፡ አላህም እርሱ ከሰጪዎች ሁሉ በላጭ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ هَاجَرُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ ثُمَّ قُتِلُوٓاْ أَوۡ مَاتُواْ لَيَرۡزُقَنَّهُمُ ٱللَّهُ رِزۡقًا حَسَنٗاۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَهُوَ خَيۡرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ٥٨

59. የሚወዱትን መግቢያ (ገነትን) በእርግጥ ያገባቸዋል፡፡ አላህም በእርግጥ ዐዋቂ ታጋሽ ነው፡፡

لَيُدۡخِلَنَّهُم مُّدۡخَلٗا يَرۡضَوۡنَهُۥۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَعَلِيمٌ حَلِيمٞ ٥٩

60. (ነገሩ) ይህ ነው፡፡ በእሱ በተበደለበትም ብጤ የተበቀለ ሰው ከዚያም በእርሱ ላይ ግፍ የተዋለበት አላህ በእርግጥ ይረዳዋል፡፡ አላህ ይቅር ባይ መሓሪ ነውና፡፡

۞ذَٰلِكَۖ وَمَنۡ عَاقَبَ بِمِثۡلِ مَا عُوقِبَ بِهِۦ ثُمَّ بُغِيَ عَلَيۡهِ لَيَنصُرَنَّهُ ٱللَّهُۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَعَفُوٌّ غَفُورٞ ٦٠

61. ይህ አላህ ሌሊትን በቀን ውስጥ የሚያስገባ ቀንንም በሌሊት ውስጥ የሚያስገባ (ቻይ) አላህም ሰሚ ተመልካች በመሆኑ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ يُولِجُ ٱلَّيۡلَ فِي ٱلنَّهَارِ وَيُولِجُ ٱلنَّهَارَ فِي ٱلَّيۡلِ وَأَنَّ ٱللَّهَ سَمِيعُۢ بَصِيرٞ ٦١

62. ይህ አላህ እርሱ እውነት በመሆኑ ከእርሱም ሌላ የሚግገዙት ነገር እርሱ ፍጹም ውሸት በመሆኑ አላህም እርሱ የሁሉ በላይ ታላቅ በመኾኑ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡحَقُّ وَأَنَّ مَا يَدۡعُونَ مِن دُونِهِۦ هُوَ ٱلۡبَٰطِلُ وَأَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡعَلِيُّ ٱلۡكَبِيرُ ٦٢

63. አላህ ከሰማይ ውሃን ማውረዱንና ምድር የምትለመልም መኾኗን አታይምን አላህ ሩኅሩኅ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَتُصۡبِحُ ٱلۡأَرۡضُ مُخۡضَرَّةًۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَطِيفٌ خَبِيرٞ ٦٣

64. በሰማያት ውስጥ ያለውና በምድር ውስጥ ያለው ሁሉ የርሱ ብቻ ነው፡፡ አላህም እርሱ ተብቃቂው ምስጉኑ ነው፡፡

لَّهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَهُوَ ٱلۡغَنِيُّ ٱلۡحَمِيدُ ٦٤

65. አላህ በምድር ውስጥ ያለን ሁሉ ለእናንተ የገራላችሁ፣ መርከቦችንም በባሕር ውስጥ በፈቃዱ የሚንሻለሉ ሲኾኑ (የገራላችሁ) መኾኑን፣ ሰማይንም በፈቃዱ ካልኾነ በምድር ላይ እንዳትወድቅ የሚይዛት መኾኑን አላየህምን አላህ ለሰዎች በእርግጥ ሩኅሩኅ አዛኝ ነው፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ سَخَّرَ لَكُم مَّا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَٱلۡفُلۡكَ تَجۡرِي فِي ٱلۡبَحۡرِ بِأَمۡرِهِۦ وَيُمۡسِكُ ٱلسَّمَآءَ أَن تَقَعَ عَلَى ٱلۡأَرۡضِ إِلَّا بِإِذۡنِهِۦٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِٱلنَّاسِ لَرَءُوفٞ رَّحِيمٞ ٦٥

66. እርሱም ያ ሕያው ያደረጋችሁ ነው፡፡ ከዚያም ይገድላችኋል፡፡ ከዚያም ሕያው ያደርጋችኋል፡፡ ሰው በእርግጥ በጣም ከሓዲ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَحۡيَاكُمۡ ثُمَّ يُمِيتُكُمۡ ثُمَّ يُحۡيِيكُمۡۗ إِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ لَكَفُورٞ ٦٦

67. ለየሕዝቡ ሁሉ እነሱ የሚሠሩበት የኾነን ሥርዓተ ሃይማኖት አድርገናል፡፡ ስለዚህ በነገሩ አይከራከሩህ፡፡ ወደ ጌታህ መንገድም ጥራ፡፡ አንተ በእርግጥ በቅኑ መንገድ ላይ ነህና፡፡

لِّكُلِّ أُمَّةٖ جَعَلۡنَا مَنسَكًا هُمۡ نَاسِكُوهُۖ فَلَا يُنَٰزِعُنَّكَ فِي ٱلۡأَمۡرِۚ وَٱدۡعُ إِلَىٰ رَبِّكَۖ إِنَّكَ لَعَلَىٰ هُدٗى مُّسۡتَقِيمٖ ٦٧

68. ቢከራከሩህም «አላህ የምትሰሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

وَإِن جَٰدَلُوكَ فَقُلِ ٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا تَعۡمَلُونَ ٦٨

69. አላህ በትንሣኤ ቀን በዚያ በእርሱ ትለያዩበት በነበራችሁት ሁሉ በመካከላችሁ ይፈርዳል፡፡

ٱللَّهُ يَحۡكُمُ بَيۡنَكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فِيمَا كُنتُمۡ فِيهِ تَخۡتَلِفُونَ ٦٩

70. አላህ በሰማይና በምድር ውስጥ ያለን ሁሉ በእርግጥ የሚያውቅ መኾኑን አታውቅምን ይህ በመጽሐፍ ውስጥ (የተመዘገበ) ነው፡፡ ይህ በአላህ ላይ ገር ነው፡፡

أَلَمۡ تَعۡلَمۡ أَنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ مَا فِي ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِۚ إِنَّ ذَٰلِكَ فِي كِتَٰبٍۚ إِنَّ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٞ ٧٠

71. ከአላህ ሌላም በእርሱ ማስረጃን ያላወረደበትን ለእነርሱም በእርሱ ዕውቀት የሌላቸውን ነገር ይግገዛሉ፡ ፡ ለበዳዮችም ምንም ረዳት የላቸውም፡፡

وَيَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَمۡ يُنَزِّلۡ بِهِۦ سُلۡطَٰنٗا وَمَا لَيۡسَ لَهُم بِهِۦ عِلۡمٞۗ وَمَا لِلظَّٰلِمِينَ مِن نَّصِيرٖ ٧١

72. አንቀጾቻችንም የተብራሩ ኾነው በእነሱ ላይ በሚነበቡ ጊዜ በእነዚያ በካዱት ሰዎች ፊቶች ላይ ጥላቻን ታውቃለህ፡፡ በእነዚያ በእነሱ ላይ አንቀጾቻችንን በሚያነቡት ላይ በኃይል ሊዘልሉባቸው ይቃረባሉ፡፡ «ከዚህ ይልቅ የከፋን ነገር ልንገራችሁን» በላቸው፡፡ «(እርሱም) እሳት ናት፡፡ አላህ ለእነዚያ ለካዱት ሰዎች ቀጥሯታል፡፡ ምን ትከፋም መመለሻ!»

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُنَا بَيِّنَٰتٖ تَعۡرِفُ فِي وُجُوهِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱلۡمُنكَرَۖ يَكَادُونَ يَسۡطُونَ بِٱلَّذِينَ يَتۡلُونَ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتِنَاۗ قُلۡ أَفَأُنَبِّئُكُم بِشَرّٖ مِّن ذَٰلِكُمُۚ ٱلنَّارُ وَعَدَهَا ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ٧٢

73. እናንተ ሰዎች ሆይ! አስደናቂ ምሳሌ ተገለጸላችሁ፡፡ ለእርሱም አድምጡት፡፡ እነዚያ ከአላህ ሌላ የምትግገዟቸው (ጣዖታት) ዝንብን ፈጽሞ አይፈጥሩም፡፡ እርሱን (ለመፍጠር) ቢሰበሰቡም እንኳን (አይችሉም)፡፡ አንዳችንም ነገር ዝንቡ ቢነጥቃቸው ከእርሱ አያስጥሉትም፡፡ ፈላጊውም ተፈላጊውም ደከሙ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ضُرِبَ مَثَلٞ فَٱسۡتَمِعُواْ لَهُۥٓۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ لَن يَخۡلُقُواْ ذُبَابٗا وَلَوِ ٱجۡتَمَعُواْ لَهُۥۖ وَإِن يَسۡلُبۡهُمُ ٱلذُّبَابُ شَيۡـٔٗا لَّا يَسۡتَنقِذُوهُ مِنۡهُۚ ضَعُفَ ٱلطَّالِبُ وَٱلۡمَطۡلُوبُ ٧٣

74. አላህን ተገቢ ክብሩን አላከበሩትም፡፡ አላህ በጣም ኃያል አሸናፊ ነው፡፡

مَا قَدَرُواْ ٱللَّهَ حَقَّ قَدۡرِهِۦٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَقَوِيٌّ عَزِيزٌ ٧٤

75. አላህ ከመላእክት ውስጥ መልክተኞችን ይመርጣል፡፡ ከሰዎችም (እንደዚሁ)፤ አላህ ሰሚ ተመልካች ነው፡፡

ٱللَّهُ يَصۡطَفِي مِنَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ رُسُلٗا وَمِنَ ٱلنَّاسِۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعُۢ بَصِيرٞ ٧٥

76. በስተፊታቸው ያለን በስተኋላቸውም ያለን ሁሉ ያውቃል፡፡ ወደ አላህም ነገሮች ሁሉ ይመለሳሉ፡፡

يَعۡلَمُ مَا بَيۡنَ أَيۡدِيهِمۡ وَمَا خَلۡفَهُمۡۚ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرۡجَعُ ٱلۡأُمُورُ ٧٦

77. እናንተ ያመናችሁ ሰዎች ሆይ! (በስግደታችሁ) አጎንብሱ፣ በግንባራችሁም ተደፉ፣ ጌታችሁንም ተገዙ፣ በጎንም ነገር ሥሩ፣ ልትድኑ ይከጀልላችኋልና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱرۡكَعُواْ وَٱسۡجُدُواْۤ وَٱعۡبُدُواْ رَبَّكُمۡ وَٱفۡعَلُواْ ٱلۡخَيۡرَ لَعَلَّكُمۡ تُفۡلِحُونَ۩ ٧٧

78. በአላህም ሃይማኖት ተገቢውን ትግል ታገሉ፡፡ እርሱ መርጧችኋል፡፡ በናንተም ላይ በሃይማኖቱ ውስጥ ምንም ችግር አላደረገባችሁም፡፡ የአባታችሁን የኢብራሂምን ሃይማኖት ተከተሉ፡፡ እርሱ ከዚህ በፊት ሙስሊሞች ብሎ ሰይሟችኋል፡፡ በዚህም (ቁርኣን)፤ መልክተኛው በእናንተ ላይ መስካሪ እንዲሆን እናንተም በሰዎቹ ላይ መስካሪዎች እንድትኾኑ (ሙስሊሞች ብሎ ሰይሟችኋል)፡፡ ሶላትንም አስተካክላችሁ ስገዱ፣ ዘካንም ስጡ፣ በአላህም ተጠበቁ፣ እርሱ ረዳታችሁ ነው፡፡ (እርሱ) ምን ያምር ጠባቂ! ምን ያምርም ረዳት!

وَجَٰهِدُواْ فِي ٱللَّهِ حَقَّ جِهَادِهِۦۚ هُوَ ٱجۡتَبَىٰكُمۡ وَمَا جَعَلَ عَلَيۡكُمۡ فِي ٱلدِّينِ مِنۡ حَرَجٖۚ مِّلَّةَ أَبِيكُمۡ إِبۡرَٰهِيمَۚ هُوَ سَمَّىٰكُمُ ٱلۡمُسۡلِمِينَ مِن قَبۡلُ وَفِي هَٰذَا لِيَكُونَ ٱلرَّسُولُ شَهِيدًا عَلَيۡكُمۡ وَتَكُونُواْ شُهَدَآءَ عَلَى ٱلنَّاسِۚ فَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُواْ ٱلزَّكَوٰةَ وَٱعۡتَصِمُواْ بِٱللَّهِ هُوَ مَوۡلَىٰكُمۡۖ فَنِعۡمَ ٱلۡمَوۡلَىٰ وَنِعۡمَ ٱلنَّصِيرُ ٧٨

# ሱረቱ ሙዕሚኑን

# سورة المؤمنون

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ምእምናን ፍላጎታቸውን ሁሉ በእርግጥ አገኙ (ዳኑ)::

قَدۡ أَفۡلَحَ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ﴿١﴾

2. እነዚያ እነርሱ በስግደታቸው ውስጥ (አላህን) ፈሪዎች::

ٱلَّذِينَ هُمۡ فِي صَلَاتِهِمۡ خَٰشِعُونَ ﴿٢﴾

3. እነዚያም እነርሱ ከውድቅ ንግግር ራቂዎች::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ عَنِ ٱللَّغۡوِ مُعۡرِضُونَ ﴿٣﴾

4. እነዚያም እነርሱ ዘካን ሰጭዎች::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ لِلزَّكَوٰةِ فَٰعِلُونَ ﴿٤﴾

5. እነዚያም እነርሱ ብልቶቻቸውን ጠባቂዎች የሆኑት (አገኙ)::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ لِفُرُوجِهِمۡ حَٰفِظُونَ ﴿٥﴾

6. በሚስቶቻቸው ወይም እጆቻቸው በያዟቸው (ባሪያዎች) ላይ ሲቀር:: እነርሱ (በነዚህ) የማይወቀሱ ናቸውና::

إِلَّا عَلَىٰٓ أَزۡوَٰجِهِمۡ أَوۡ مَا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُهُمۡ فَإِنَّهُمۡ غَيۡرُ مَلُومِينَ ﴿٦﴾

7. ከዚህም ወዲያ የፈለጉ ሰዎች እነዚያ እነርሱ ወሰን አላፊዎች ናቸው::

فَمَنِ ٱبۡتَغَىٰ وَرَآءَ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡعَادُونَ ﴿٧﴾

8. እነዚያም እነርሱ ለአደራዎቻቸውና ለቃል ኪዳናቸው ጠባቂዎች::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ لِأَمَٰنَٰتِهِمۡ وَعَهۡدِهِمۡ رَٰعُونَ ﴿٨﴾

9. እነዚያም እነሱ በስግደቶቻቸው ላይ የሚጠባበቁ የኾኑት (አገኙ)::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ عَلَىٰ صَلَوَٰتِهِمۡ يُحَافِظُونَ ﴿٩﴾

10. እነዚያ ወራሾቹ እነርሱ ናቸው::

أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡوَٰرِثُونَ ﴿١٠﴾

11. እነዚያ ፊርደውስን (ላዕላይ ገነትን)፣ የሚወርሱ ናቸው:: እነርሱ በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው::

ٱلَّذِينَ يَرِثُونَ ٱلۡفِرۡدَوۡسَ هُمۡ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿١١﴾

12. በእርግጥም ሰውን ከነጠረ ጭቃ ፈጠርነው::

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ مِن سُلَٰلَةٖ مِّن طِينٖ ﴿١٢﴾

13. ከዚያም በተጠበቀ መርጊያ ውስጥ የፍትወት ጠብታ አደረግነው::

ثُمَّ جَعَلۡنَٰهُ نُطۡفَةٗ فِي قَرَارٖ مَّكِينٖ ﴿١٣﴾

14. ከዚያም ጠብታዋን (በአርባ ቀን) የረጋ ደም አድርገን ፈጠርን:: የረጋውንም ደም ቁራጭ ሥጋ አድርገን ፈጠርን:: ቁራጪንም ሥጋ አጥንቶች አድርገን ፈጠርን:: አጥንቶቹንም ሥጋን አለበስናቸው:: ከዚያም (ነፍስን በመዝራት) ሌላ ፍጥረትን አድርገን አስገኘነው:: ከሰዓሊዎችም ሁሉ በላጭ የሆነው አላህ ላቀ::

ثُمَّ خَلَقۡنَا ٱلنُّطۡفَةَ عَلَقَةٗ فَخَلَقۡنَا ٱلۡعَلَقَةَ مُضۡغَةٗ فَخَلَقۡنَا ٱلۡمُضۡغَةَ عِظَٰمٗا فَكَسَوۡنَا ٱلۡعِظَٰمَ لَحۡمٗا ثُمَّ أَنشَأۡنَٰهُ خَلۡقًا ءَاخَرَۚ فَتَبَارَكَ ٱللَّهُ أَحۡسَنُ ٱلۡخَٰلِقِينَ ﴿١٤﴾

15. ከዚያም እናንተ ከዚህ በኋላ በእርግጥ ሚቾች ናችሁ::

ثُمَّ إِنَّكُم بَعۡدَ ذَٰلِكَ لَمَيِّتُونَ ﴿١٥﴾

16. ከዚያም እናንተ በትንሣኤ ቀን ትቀሰቀሳላችሁ::

ثُمَّ إِنَّكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ تُبۡعَثُونَ ﴿١٦﴾

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَا فَوۡقَكُمۡ سَبۡعَ طَرَآئِقَ وَمَا كُنَّا عَنِ ٱلۡخَلۡقِ غَٰفِلِينَ ١٧

17. በእርግጥም ከበላያችሁ ሰባትን ሰማያት ፈጠርን፡፡ ከፍጥረቶቹም ዘንጊዎች አይደለንም፡፡

وَأَنزَلۡنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءَۢ بِقَدَرٖ فَأَسۡكَنَّٰهُ فِي ٱلۡأَرۡضِۖ وَإِنَّا عَلَىٰ ذَهَابِۭ بِهِۦ لَقَٰدِرُونَ ١٨

18. ከሰማይም ውሃን በልክ አወረድን፡፡ በምድርም ውስጥ አስቀመጥነው፡፡ እኛም እርሱን በማስወገድ ላይ በእርግጥ ቻዮች ነን፡፡

فَأَنشَأۡنَا لَكُم بِهِۦ جَنَّٰتٖ مِّن نَّخِيلٖ وَأَعۡنَٰبٖ لَّكُمۡ فِيهَا فَوَٰكِهُ كَثِيرَةٞ وَمِنۡهَا تَأۡكُلُونَ ١٩

19. በእርሱም ከዘምባባዎችና ከወይኖች የኾኑን አትክልቶች ለእናንተ አስገኘንላችሁ፡፡ በውስጧ ለእናንተ ብዙ ፍራፍሬዎች አሏችሁ፡፡ ከእርሷም ትበላላችሁ፡፡

وَشَجَرَةٗ تَخۡرُجُ مِن طُورِ سَيۡنَآءَ تَنۢبُتُ بِٱلدُّهۡنِ وَصِبۡغٖ لِّلۡأٓكِلِينَ ٢٠

20. ከሲና ተራራም የምትወጣን ዛፍ በቅባትና ለበይዎችም መባያ በሚኾን (ዘይት) ተቀላቅላ የምትበቅልን (አስገኘንላችሁ)፡፡

وَإِنَّ لَكُمۡ فِي ٱلۡأَنۡعَٰمِ لَعِبۡرَةٗۖ نُّسۡقِيكُم مِّمَّا فِي بُطُونِهَا وَلَكُمۡ فِيهَا مَنَٰفِعُ كَثِيرَةٞ وَمِنۡهَا تَأۡكُلُونَ ٢١

21. ለእናንተም በግመል፣ በከብት፣ በፍየልና በበግ መገምገሚያ አልላችሁ፡፡ በሆዶችዋ ውስጥ ካለው (ወተት) እናጠጣችኋለን፡፡ ለእናንተም በእርሷ ብዙ ጥቅሞች አሏችሁ፡፡ ከእርሷም ትበላላችሁ፡፡

وَعَلَيۡهَا وَعَلَى ٱلۡفُلۡكِ تُحۡمَلُونَ ٢٢

22. በእርሷም ላይ በመርከብም ላይ ትጫናላችሁ፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا نُوحًا إِلَىٰ قَوۡمِهِۦ فَقَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرُهُۥٓۚ أَفَلَا تَتَّقُونَ ٢٣

23. ኑሕንም ወደ ሕዝቦቹ በእርግጥ ላክነው፡፡ ወዲያውም «ሕዝቦቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ ከእርሱ ሌላ ምንም አምላክ የላችሁም፡፡ አትጠነቀቁምን» አላቸው፡፡

فَقَالَ ٱلۡمَلَؤُاْ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن قَوۡمِهِۦ مَا هَٰذَآ إِلَّا بَشَرٞ مِّثۡلُكُمۡ يُرِيدُ أَن يَتَفَضَّلَ عَلَيۡكُمۡ وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَأَنزَلَ مَلَٰٓئِكَةٗ مَّا سَمِعۡنَا بِهَٰذَا فِيٓ ءَابَآئِنَا ٱلۡأَوَّلِينَ ٢٤

24. ከሕዝቦቹም እነዚያ ታላላቆቹ ሰዎች አሉ «ይህ ብጤያችሁ ሰው እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ በእናንተ ላይ መብለጥን ይፈልጋል፡፡ አላህም በሻ ኖሮ መላእክትን ባወረደ ነበር፡፡ ይህንንም (የሚለውን) በመጀመሪያዎቹ አባቶቻችን አልሰማንም፡፡

إِنۡ هُوَ إِلَّا رَجُلُۢ بِهِۦ جِنَّةٞ فَتَرَبَّصُواْ بِهِۦ حَتَّىٰ حِينٖ ٢٥

25. «እርሱ በእርሱ ዕብደት ያለበት ሰው እንጅ ሌላ አይደለም፡፡ በእርሱም እስከ ጊዜ (ሞቱ) ድረስ ተጠባበቁ» (አሉ)፡፡

قَالَ رَبِّ ٱنصُرۡنِي بِمَا كَذَّبُونِ ٢٦

26. (ኑሕም) «ጌታዬ ሆይ! ባስተባበሉኝ ምክንያት እርዳኝ» አለ፡፡

فَأَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡهِ أَنِ ٱصۡنَعِ ٱلۡفُلۡكَ بِأَعۡيُنِنَا وَوَحۡيِنَا فَإِذَا جَآءَ أَمۡرُنَا وَفَارَ ٱلتَّنُّورُ فَٱسۡلُكۡ فِيهَا مِن كُلّٖ زَوۡجَيۡنِ ٱثۡنَيۡنِ وَأَهۡلَكَ إِلَّا مَن سَبَقَ عَلَيۡهِ ٱلۡقَوۡلُ مِنۡهُمۡۖ وَلَا تُخَٰطِبۡنِي فِي ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓاْ إِنَّهُم مُّغۡرَقُونَ ٢٧

27. ወደርሱም (እንዲህ ስንል) ላክን «በተመልካችነታችንና በትእዛዛችንም ታንኳን ሥራ በመጣና እቶኑ በፈለቀ ጊዜ በውስጧ ከሁሉም ሁለት ዓይነቶችን ቤተሰቦችህንም ከነሱ (ጠፊ በመኾን) ቃል ያለፈበት ብቻ ሲቀር፤ አግባ፡፡ በእነዚያም በበደሉት ሰዎች ነገር አታነጋግረኝ፡፡ እነሱ ተሰጣሚዎች ነቸውና፡፡

28. አንተም አብረውህ ካሉት ጋር በታንኳይቱ ላይ በተደላደልክ ጊዜ «ምስጋና ለዚያ ከበደለኞች ሕዝቦች ላዳነን አላህ ይገባው» በል፡፡

فَإِذَا ٱسْتَوَيْتَ أَنتَ وَمَن مَّعَكَ عَلَى ٱلْفُلْكِ فَقُلِ ٱلْحَمْدُ لِلَّهِ ٱلَّذِى نَجَّىٰنَا مِنَ ٱلْقَوْمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٢٨﴾

29. በልም «ጌታዬ ሆይ! ብሩክ የኾነን ማውረድ አውርደኝ፡፡ አንተም ከአውራጆች ሁሉ በላጭ ነህ፡፡»

وَقُل رَّبِّ أَنزِلْنِى مُنزَلًا مُّبَارَكًا وَأَنتَ خَيْرُ ٱلْمُنزِلِينَ ﴿٢٩﴾

30. በዚህ ውስጥ (ለከሃሊነታችን) ምልክቶች አሉሉበት፡፡ እነሆ! (የኑሕን ሰዎች) በእርግጥም ፈትታኞች ነበርን፡፡

إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَٰتٍ وَإِن كُنَّا لَمُبْتَلِينَ ﴿٣٠﴾

31. ከዚያም ከኋላቸው ሌሎችን የክፍለ ዘመን ሕዝቦች አስገኘን፡፡

ثُمَّ أَنشَأْنَا مِنۢ بَعْدِهِمْ قَرْنًا ءَاخَرِينَ ﴿٣١﴾

32. በውስጣቸውም ከእነሱ የኾነን መልክተኛ አላህን ተገዙ ከእርሱ ሌላ አምላክ የላችሁም አትጠነቀቁምን በማለት ላክን፡፡

فَأَرْسَلْنَا فِيهِمْ رَسُولًا مِّنْهُمْ أَنِ ٱعْبُدُوا۟ ٱللَّهَ مَا لَكُم مِّنْ إِلَٰهٍ غَيْرُهُۥٓ ۚ أَفَلَا تَتَّقُونَ ﴿٣٢﴾

33. ከሕዝቦቹም እነዚያ የካዱት በመጨረሻይቱም ቀን መገናኘት ያስተባበሉት በቅርቢቱም ሕይወት ያቀማጠልናቸው ታላላቅ ሰዎች «ይህ ብጤያችሁ ሰው እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ ከርሱ ከምትበሉት ምግብ ይበላል፡፡ ከምትጠጡትም ውሃ ይጠጣል» አሉ፡፡

وَقَالَ ٱلْمَلَأُ مِن قَوْمِهِ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ وَكَذَّبُوا۟ بِلِقَآءِ ٱلْءَاخِرَةِ وَأَتْرَفْنَٰهُمْ فِى ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَا مَا هَٰذَآ إِلَّا بَشَرٌ مِّثْلُكُمْ يَأْكُلُ مِمَّا تَأْكُلُونَ مِنْهُ وَيَشْرَبُ مِمَّا تَشْرَبُونَ ﴿٣٣﴾

34. «ብጤያችሁም የኾነን ሰው ብትታዘዙ እናንተ ያን ጊዜ በእርግጥ የተሞኛችሁ ናችሁ» (አሉ)፡፡

وَلَئِنْ أَطَعْتُم بَشَرًا مِّثْلَكُمْ إِنَّكُمْ إِذًا لَّخَٰسِرُونَ ﴿٣٤﴾

35. «እናንተ በሞታችሁና ዐፈርና አጥንቶችም በኾናችሁ ጊዜ እናንተ (ከመቃብር) ትወጣላችሁ በማለት ያስፈራራችኋልን

أَيَعِدُكُمْ أَنَّكُمْ إِذَا مِتُّمْ وَكُنتُمْ تُرَابًا وَعِظَٰمًا أَنَّكُم مُّخْرَجُونَ ﴿٣٥﴾

36. «ያ የምትስፈራሩበት ነገር ራቀ፤ በጣም ራቀ፡፡

۞ هَيْهَاتَ هَيْهَاتَ لِمَا تُوعَدُونَ ﴿٣٦﴾

37. «እርሷ (ሕይወት) ቅርቢቱ ሕይወታችን እንጂ ሌላ አይደለችም፡፡ እንሞታለን፤ (ልጆቻችን ስለሚተኩ) ሕያውም እንኾናለን፡፡ እኛም ተቀስቃሾች አይደለንም፡፡

إِنْ هِىَ إِلَّا حَيَاتُنَا ٱلدُّنْيَا نَمُوتُ وَنَحْيَا وَمَا نَحْنُ بِمَبْعُوثِينَ ﴿٣٧﴾

38. «እርሱ በአላህ ላይ ውሸትን የቀጠፈ ሰው እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ እኛም ለእርሱ አማኞች አይደለንም» (አሉ)፡፡

إِنْ هُوَ إِلَّا رَجُلٌ ٱفْتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا وَمَا نَحْنُ لَهُۥ بِمُؤْمِنِينَ ﴿٣٨﴾

39. (መልክተኛውም) «ጌታዬ ሆይ! ስላስተባበሉኝ እርዳኝ» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ ٱنصُرْنِى بِمَا كَذَّبُونِ ﴿٣٩﴾

40. (አላህም) «ከጥቂት ጊዜ በኋላ (በጥፋታቸው) በእርግጥ ተጸጻቾች ይኾናሉ» አለው፡፡

قَالَ عَمَّا قَلِيلٍ لَّيُصْبِحُنَّ نَٰدِمِينَ ﴿٤٠﴾

41. ወዲያውም (የጥፋት) ጩኸቲቱ በእውነት ያዘቻቸው፡፡ እንደ ጎርፍ ግብስባሽም አደረግናቸው፡፡ ለበደለኞች ሕዝቦችም (ከእዝነት) መራቅ ተገባቸው፡፡

فَأَخَذَتْهُمُ ٱلصَّيْحَةُ بِٱلْحَقِّ فَجَعَلْنَٰهُمْ غُثَآءً ۚ فَبُعْدًا لِّلْقَوْمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٤١﴾

42. ከዚያም ከእነሱ በኋላ ሌሎችን የክፍለ ዘመናት ሕዝቦች አስገኘን፡፡
43. ማንኛይቱም ሕዝብ ጊዜያዋን አትቀድምም፤ አይቅቆዩምም፡፡
44. ከዚያም መልክተኞቻችንን የሚከታተሉ ኾነው ላክን፡፡ ማንኛይቱንም ሕዝብ መልክተኛዋ በመጣላት ቁጥር አስተባበሉት፡፡ ከፊላቸውንም በከፊሉ (በጥፋት) አስከታተለን፡፡ ወሬዎችም አደረግናቸው፡፡ ለማያምኑም ሕዝቦች (ከእዝነታችን) መራቅ ተገባቸው፡፡

ثُمَّ أَنشَأۡنَا مِنۢ بَعۡدِهِمۡ قُرُونًا ءَاخَرِينَ ﴿٤٢﴾

مَا تَسۡبِقُ مِنۡ أُمَّةٍ أَجَلَهَا وَمَا يَسۡتَـٔۡخِرُونَ ﴿٤٣﴾

ثُمَّ أَرۡسَلۡنَا رُسُلَنَا تَتۡرَاۖ كُلَّ مَا جَآءَ أُمَّةً رَّسُولُهَا كَذَّبُوهُۖ فَأَتۡبَعۡنَا بَعۡضَهُم بَعۡضًا وَجَعَلۡنَٰهُمۡ أَحَادِيثَۚ فَبُعۡدًا لِّقَوۡمٍ لَّا يُؤۡمِنُونَ ﴿٤٤﴾

45. ከዚያም ሙሳንና ወንድሙን ሃሩንን በተዓምራታችንና በግልጽ አስረጅ ላክን፡፡
46. ወደ ፈርዖንና ወደ ጭፍሮቹ (ላክናቸው)፡፡ ኮሩም፡፡ የተንበጣረሩ ሕዝቦችም ነበሩ፡፡
47. «ብጤያችንም ለኾኑ ሁለት ሰዎች ሕዝቦቻቸው ለእኛ ተገዢዎች ኾነው ሳሉ እናምናለን» አሉ፡፡
48. አስተባበሉዋቸውም፡፡ ከጠፊዎቹም ኾኑ፡፡

ثُمَّ أَرۡسَلۡنَا مُوسَىٰ وَأَخَاهُ هَٰرُونَ بِـَٔايَٰتِنَا وَسُلۡطَٰنٖ مُّبِينٍ ﴿٤٥﴾

إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِۦ فَٱسۡتَكۡبَرُواْ وَكَانُواْ قَوۡمًا عَالِينَ ﴿٤٦﴾

فَقَالُوٓاْ أَنُؤۡمِنُ لِبَشَرَيۡنِ مِثۡلِنَا وَقَوۡمُهُمَا لَنَا عَٰبِدُونَ ﴿٤٧﴾

فَكَذَّبُوهُمَا فَكَانُواْ مِنَ ٱلۡمُهۡلَكِينَ ﴿٤٨﴾

49. ሙሳንም (ነገዶቹ) ይምመሩ ዘንድ መጽሐፍን በእርግጥ ሰጠነው፡፡
50. የመርየምን ልጅና እናቱንም ተዓምር አደረግናቸው፡፡ የመደላደልና የምንጭ ባለቤት ወደ ኾነች ከፍተኛ ስፍራም አስጠጋናቸው፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡكِتَٰبَ لَعَلَّهُمۡ يَهۡتَدُونَ ﴿٤٩﴾

وَجَعَلۡنَا ٱبۡنَ مَرۡيَمَ وَأُمَّهُۥٓ ءَايَةٗ وَءَاوَيۡنَٰهُمَآ إِلَىٰ رَبۡوَةٖ ذَاتِ قَرَارٖ وَمَعِينٖ ﴿٥٠﴾

51. እናንተ መልክተኞች ሆይ! ከተፈቀዱት ምግቦች ብሉ፡፡ በጎ ሥራንም ሥሩ፡፡ እኔ የምተሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነኝ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلرُّسُلُ كُلُواْ مِنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ وَٱعۡمَلُواْ صَٰلِحًاۖ إِنِّي بِمَا تَعۡمَلُونَ عَلِيمٞ ﴿٥١﴾

52. ይህችም (በአንድ አምላክ የማመን ሕግጋት) አንድ መንገድ ስትኾን ሃይማኖታችሁ ናት፡፡ እኔም ጌታችሁ ነኝና ፍሩኝ፡፡
53. (ከዚያ ተከታዮቻቸው) የሃይማኖት ነገራቸውንም በመካከላቸው ክፍልፍሎች አድርገው ቆራረጡ፡፡ ሕዝብ ሁሉ እነርሱ ዘንድ ባለው ሃይማኖት ተደሳቾች ናቸው፡፡

وَإِنَّ هَٰذِهِۦٓ أُمَّتُكُمۡ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ وَأَنَا۠ رَبُّكُمۡ فَٱتَّقُونِ ﴿٥٢﴾

فَتَقَطَّعُوٓاْ أَمۡرَهُم بَيۡنَهُمۡ زُبُرٗاۖ كُلُّ حِزۡبِۭ بِمَا لَدَيۡهِمۡ فَرِحُونَ ﴿٥٣﴾

54. እስከ ጊዜያቸውም ድረስ በጥምመታቸው ውስጥ ተዋቸው፡፡
55. ከገንዘብና ከልጆች በእርሱ የምንጨምርላቸውን ያስባሉን
56. በበጎ ነገሮች የምንቻኮልላቸው መኾንን (ያስባሉን) አይደለም፤ (ለማዘንጋት መኾኑን) አያውቁም፡፡
57. እነዚያ እነርሱ ጌታቸውን ከመፍራት የተነሳ ተጨናቂዎች የኾኑት፡፡

فَذَرۡهُمۡ فِي غَمۡرَتِهِمۡ حَتَّىٰ حِينٍ ﴿٥٤﴾

أَيَحۡسَبُونَ أَنَّمَا نُمِدُّهُم بِهِۦ مِن مَّالٖ وَبَنِينَ ﴿٥٥﴾

نُسَارِعُ لَهُمۡ فِي ٱلۡخَيۡرَٰتِۚ بَل لَّا يَشۡعُرُونَ ﴿٥٦﴾

إِنَّ ٱلَّذِينَ هُم مِّنۡ خَشۡيَةِ رَبِّهِم مُّشۡفِقُونَ ﴿٥٧﴾

58. እነዚያም እነርሱ በጌታቸው ተዓምራቶች ከሚያምኑት፡፡

وَٱلَّذِينَ هُم بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمۡ يُؤۡمِنُونَ ﴿٥٨﴾

59. እነዚያም እነርሱ በጌታቸው (ጣዖትን) የማያጋሩት፡ ፡

وَٱلَّذِينَ هُم بِرَبِّهِمۡ لَا يُشۡرِكُونَ ﴿٥٩﴾

60. እነዚያም የሚሰጡትን ነገር እነርሱ ወደ ጌታቸው ተመላሾች መኾናቸውን ልቦቻቸው የሚፈሩ ኾነው የሚሰጡት፡፡

وَٱلَّذِينَ يُؤۡتُونَ مَآ ءَاتَواْ وَّقُلُوبُهُمۡ وَجِلَةٌ أَنَّهُمۡ إِلَىٰ رَبِّهِمۡ رَٰجِعُونَ ﴿٦٠﴾

61. እነዚያ በመልካም ሥራዎች ይጣደፋሉ፡፡ እነሱም ለርሷ ቀዳሚዎች ናቸው፡፡

أُوْلَـٰٓئِكَ يُسَٰرِعُونَ فِي ٱلۡخَيۡرَٰتِ وَهُمۡ لَهَا سَٰبِقُونَ ﴿٦١﴾

62. ማንኛይቱንም ነፍስ ችሎታዋን እንጂ አናስገድዳትም፡፡ እኛም ዘንድ በእውነት የሚናገር መጽሐፍ አልለ፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

وَلَا نُكَلِّفُ نَفۡسًا إِلَّا وُسۡعَهَاۖ وَلَدَيۡنَا كِتَٰبٌ يَنطِقُ بِٱلۡحَقِّ وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ﴿٦٢﴾

63. በእውነቱ (ከሓዲዎች) ልቦቻቸው ከዚያ (መጽሐፍ) በዝንጋቴ ውስጥ ናቸው፡፡ ለእነሱም ከዚህ ሌላ እነሱ ለርሷ ሠሪዎችዋ የኾኑ (መጥፎ) ሥራዎች አሏቸው፡፡

بَلۡ قُلُوبُهُمۡ فِي غَمۡرَةٖ مِّنۡ هَٰذَا وَلَهُمۡ أَعۡمَٰلٞ مِّن دُونِ ذَٰلِكَ هُمۡ لَهَا عَٰمِلُونَ ﴿٦٣﴾

64. ቅምጥሎቻቸውንም በቅጣት በያዝናቸው ጊዜ ወዲያውኑ እነርሱ ይወተውታሉ፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَآ أَخَذۡنَا مُتۡرَفِيهِم بِٱلۡعَذَابِ إِذَا هُمۡ يَجۡـَٔرُونَ ﴿٦٤﴾

65. ዛሬ አትወትውቱ፤ እናንተ ከእኛ ዘንድ አትረዱም፡፡

لَا تَجۡـَٔرُواْ ٱلۡيَوۡمَۖ إِنَّكُم مِّنَّا لَا تُنصَرُونَ ﴿٦٥﴾

66. አንቀጾቼ በእናንተ ላይ በእርግጥ ይነበቡላችሁ ነበር፡፡ በተረከዞቻችሁም ላይ ወደ ኋላችሁ ትመለሱ ነበራችሁ፡፡

قَدۡ كَانَتۡ ءَايَٰتِي تُتۡلَىٰ عَلَيۡكُمۡ فَكُنتُمۡ عَلَىٰٓ أَعۡقَٰبِكُمۡ تَنكِصُونَ ﴿٦٦﴾

67. በእርሱ (በክልሉ ቤት) ኩሩዎች ሌሊት ተጫዋቾች (ቁርኣንንም) የምትተው ኾናችሁ (ትመለሱ ነበራችሁ ይባላሉ)፡፡

مُسۡتَكۡبِرِينَ بِهِۦ سَٰمِرٗا تَهۡجُرُونَ ﴿٦٧﴾

68. (የቁርኣንን) ንግግሩንም አያስተነትኑምን ወይስ ለመጀመሪያዎቹ አባቶቻቸው ያልመጣ ነገር መጣባቸውን

أَفَلَمۡ يَدَّبَّرُواْ ٱلۡقَوۡلَ أَمۡ جَآءَهُم مَّا لَمۡ يَأۡتِ ءَابَآءَهُمُ ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿٦٨﴾

69. ወይስ መልክተኛቸውን አላወቁምን ስለዚህ እነርሱ ለእርሱ ከሓዲዎች ናቸውን

أَمۡ لَمۡ يَعۡرِفُواْ رَسُولَهُمۡ فَهُمۡ لَهُۥ مُنكِرُونَ ﴿٦٩﴾

70. ወይስ በእርሱ ዕብደት አለበት ይላሉን አይደለም፡፡ እውነትን ይዞ መጣላቸው፡፡ አብዛኞቻቸውም እውነትን ጠይዎች ናቸው፡፡

أَمۡ يَقُولُونَ بِهِۦ جِنَّةُۢۚ بَلۡ جَآءَهُم بِٱلۡحَقِّ وَأَكۡثَرُهُمۡ لِلۡحَقِّ كَٰرِهُونَ ﴿٧٠﴾

71. አላህም ዝንባሌዎቻቸውን በተከተለ ኖሮ ሰማያትና ምድር በውስጣቸውም ያለው ሁሉ በእርግጥ በተበላሸ ነበር፡፡ ይልቁንም ክብራቸው ያለበትን ቁርኣን አመጣንላቸው፡፡ እነርሱም ከክብራቸው ዘንጊዎች ናቸው፡፡

وَلَوِ ٱتَّبَعَ ٱلۡحَقُّ أَهۡوَآءَهُمۡ لَفَسَدَتِ ٱلسَّمَٰوَٰتُ وَٱلۡأَرۡضُ وَمَن فِيهِنَّۚ بَلۡ أَتَيۡنَٰهُم بِذِكۡرِهِمۡ فَهُمۡ عَن ذِكۡرِهِم مُّعۡرِضُونَ ﴿٧١﴾

72. ወይስ ግብርን ትጠይቃቸዋለህን የጌታህም ችሮታ በላጭ ነው፡፡ እርሱም ከሰጪዎች ሁሉ በላጭ ነው፡፡

أَمۡ تَسۡـَٔلُهُمۡ خَرۡجٗا فَخَرَاجُ رَبِّكَ خَيۡرٞۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ٧٢

73. አንተም ወደ ቀጥተኛው መንገድ በእርግጥ ትጠራቸዋለህ፡፡

وَإِنَّكَ لَتَدۡعُوهُمۡ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ٧٣

74. እነዚያም በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት ከትክክለኛው መንገድ ተዘንባዮች ናቸው፡፡

وَإِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ عَنِ ٱلصِّرَٰطِ لَنَٰكِبُونَ ٧٤

75. ባዘንንላቸውና ከጉዳትም በእነርሱ ያለውን ባነሳንላቸው ኖሮ በጥመታቸው ውስጥ የሚዋልሉ ኾነው ይዘወትሩ ነበር፡፡

۞وَلَوۡ رَحِمۡنَٰهُمۡ وَكَشَفۡنَا مَا بِهِم مِّن ضُرّٖ لَّلَجُّواْ فِي طُغۡيَٰنِهِمۡ يَعۡمَهُونَ ٧٥

76. በእርግጥም በቅጣት ያዝናቸው፡፡ ታዲያ ለጌታቸው አልተናነሱም፡፡ አይዋደቁምም፡፡

وَلَقَدۡ أَخَذۡنَٰهُم بِٱلۡعَذَابِ فَمَا ٱسۡتَكَانُواْ لِرَبِّهِمۡ وَمَا يَتَضَرَّعُونَ ٧٦

77. በእነሱም ላይ የብርቱ ቅጣት ባለቤት የኾነ ደጃፍን በከፈትንባቸው ጊዜ እነርሱ ያን ጊዜ በእርሱ ተስፋ ቆራጮች ናቸው፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا فَتَحۡنَا عَلَيۡهِم بَابٗا ذَا عَذَابٖ شَدِيدٍ إِذَا هُمۡ فِيهِ مُبۡلِسُونَ ٧٧

78. እርሱም ያ መስሚያዎችንና ማያዎችን ልቦችንም ለእናንተ የፈጠረላችሁ ነው፡፡ ጥቂትን እንጅ አታመሰግኑም፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِيٓ أَنشَأَ لَكُمُ ٱلسَّمۡعَ وَٱلۡأَبۡصَٰرَ وَٱلۡأَفۡـِٔدَةَۚ قَلِيلٗا مَّا تَشۡكُرُونَ ٧٨

79. እርሱም ያ በምድር ውስጥ የበተናችሁ ነው፡፡ ወደርሱም ትሰበሰባላችሁ፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي ذَرَأَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَإِلَيۡهِ تُحۡشَرُونَ ٧٩

80. እርሱም ያ ሕያው የሚያደርግ የሚገድልም ነው፡፡ የሌሊትና የቀን መተካካትም የእርሱ ነው፡፡ አታውቁምን

وَهُوَ ٱلَّذِي يُحۡيِۦ وَيُمِيتُ وَلَهُ ٱخۡتِلَٰفُ ٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ٨٠

81. ይልቁንም (የመካ ከሓዲዎች) የፊተኞቹ ሕዝቦች እንዳሉት ብጤ አሉ፡፡

بَلۡ قَالُواْ مِثۡلَ مَا قَالَ ٱلۡأَوَّلُونَ ٨١

82. «በሞትንና ዐፈርና አጥንቶች በኾን ጊዜ እኛ ተቀስቃሾች ነን» አሉ፡፡

قَالُوٓاْ أَءِذَا مِتۡنَا وَكُنَّا تُرَابٗا وَعِظَٰمًا أَءِنَّا لَمَبۡعُوثُونَ ٨٢

83. «ይህንን እኛም ከእኛ በፊትም የነበሩት አባቶቻችን በእርግጥ ተቀጥረናል፡፡ ይህ የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ተረቶች እንጂ ሌላ አይደለም» (አሉ)፡፡

لَقَدۡ وُعِدۡنَا نَحۡنُ وَءَابَآؤُنَا هَٰذَا مِن قَبۡلُ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّآ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٨٣

84. «ምድርና በውስጥዋ ያለው ሁሉ የማን ነው የምታውቁ ብትኾኑ (ንገሩኝ)» በላቸው፡፡

قُل لِّمَنِ ٱلۡأَرۡضُ وَمَن فِيهَآ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٨٤

85. «በእርግጥ የአላህ ነው» ይሉሃል፡፡ «ታዲያ አትገሰጹምን» በላቸው፡፡

سَيَقُولُونَ لِلَّهِۚ قُلۡ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ٨٥

86. «የሰባቱ ሰማያት ጌታና የታላቁ ዐርሽ ጌታ ማን ነው» በላቸው፡፡

قُلۡ مَن رَّبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ ٱلسَّبۡعِ وَرَبُّ ٱلۡعَرۡشِ ٱلۡعَظِيمِ ٨٦

87. «በእርግጥ አላህ ነው» ይሉሃል፡፡ «እንግዲያ አትፈሩትምን» በላቸው፡፡

سَيَقُولُونَ لِلَّهِۚ قُلۡ أَفَلَا تَتَّقُونَ ٨٧

88. «የነገሩ ሁሉ ግዛት በእጁ የኾነ እርሱ የሚጠብቅ በእርሱ ላይ የማይጠበቅ ማን ነው የምታውቁ እንደኾናችሁ (መልሱልኝ)» በላቸው፡፡

89. «በእርግጥ አላህ ነው» ይሉሃል፡፡ «ታዲያ እንዴት ትታለላላችሁ» በላቸው፡፡

90. ይልቁንም እውነትን አመጣንላቸው፡፡ እነርሱም (በመካዳቸው) ውሸታሞች ናቸው፡፡

91. አላህ ምንም ልጅን አልያዘም (አልወለደም)፡፡ ከእርሱም ጋር አንድም አምላክ የለም፡፡ ያን ጊዜ (ሌላ አምላክ በነበረ) አምላክ ሁሉ በፈጠረው ነገር በተለየ ነበር፡፡ ከፊላቸውም በከፊሉ ላይ በላቀ ነበር፡፡ አላህ ከሚመጥኑት ሁሉ ጠራ፡፡

92. ሩቁንና ቅርቡንም ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡ (በእርሱ) ከሚያጋሩትም ሁሉ ከፍ አለ፡፡

93. (ሙሐመድ ሆይ!) በል «ጌታዬ ሆይ! የሚያስፈራሩበትን (ቅጣት) ብታሳየኝ፡፡

94. «ጌታዬ ሆይ! በበደለኞች ሕዝቦች ውስጥ አታድርገኝ፡፡»

95. እኛም የምናስፈራራቸውን ነገር ልናሳይህ በእርግጥ ቻዮች ነን፡፡

96. በዚያች እርስዋ መልካም በኾነችው (ጠባይ) መጥፎይቱን ነገር ገፍትር፡፡ እኛ የሚሉትን ሁሉ ዐዋቂዎች ነን፡፡

97. በልም «ጌታዬ ሆ! ከሰይጣናት ጉትተጎታዎች በአንተ እጠበቃለሁ፡፡

98. «ባንተም ጌታዬ ሆይ! (በነገሮቼ) ወደእኔ ከመጣዳቸው እጠበቃለሁ፡፡»

99. አንዳቸውንም ሞት በመጣበት ጊዜ እንዲህ ይላል «ጌታዬ ሆይ! (ወደ ምድረ ዓለም) መልሱኝ፡፡

100. «በተውኩት ነገር በጎን ሥራ ልሠራ እከጅላለሁና፡፡» (ይህን ከማለት) ይከልከል፡፡ እርስዋ እርሱ ተናጋሪዋ የኾነች ከንቱ ቃል ናት፡፡ ከስተፊታቸውም እስከሚቀሰቀሱበት ቀን ድረስ ግርዶ አለለ፡፡

101. በቀንዱም በተነፋ ጊዜ በዚያ ቀን በመካከላቸው ዝምድና የለም፡፡ አይጠያየቁምም፡፡

102. ሚዛኖቹም የከበዱለት ሰው እነዚያ እነርሱ ፍላጎታቸውን ያገኙ ናቸው፡፡

قُلْ مَنۢ بِيَدِهِۦ مَلَكُوتُ كُلِّ شَىْءٍ وَهُوَ يُجِيرُ وَلَا يُجَارُ عَلَيْهِ إِن كُنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿٨٨﴾

سَيَقُولُونَ لِلَّهِ ۚ قُلْ فَأَنَّىٰ تُسْحَرُونَ ﴿٨٩﴾

بَلْ أَتَيْنَـٰهُم بِٱلْحَقِّ وَإِنَّهُمْ لَكَـٰذِبُونَ ﴿٩٠﴾

مَا ٱتَّخَذَ ٱللَّهُ مِن وَلَدٍ وَمَا كَانَ مَعَهُۥ مِنْ إِلَـٰهٍ ۚ إِذًا لَّذَهَبَ كُلُّ إِلَـٰهٍۭ بِمَا خَلَقَ وَلَعَلَا بَعْضُهُمْ عَلَىٰ بَعْضٍ ۚ سُبْحَـٰنَ ٱللَّهِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿٩١﴾

عَـٰلِمِ ٱلْغَيْبِ وَٱلشَّهَـٰدَةِ فَتَعَـٰلَىٰ عَمَّا يُشْرِكُونَ ﴿٩٢﴾

قُل رَّبِّ إِمَّا تُرِيَنِّى مَا يُوعَدُونَ ﴿٩٣﴾

رَبِّ فَلَا تَجْعَلْنِى فِى ٱلْقَوْمِ ٱلظَّـٰلِمِينَ ﴿٩٤﴾

وَإِنَّا عَلَىٰٓ أَن نُّرِيَكَ مَا نَعِدُهُمْ لَقَـٰدِرُونَ ﴿٩٥﴾

ٱدْفَعْ بِٱلَّتِى هِىَ أَحْسَنُ ٱلسَّيِّئَةَ ۚ نَحْنُ أَعْلَمُ بِمَا يَصِفُونَ ﴿٩٦﴾

وَقُل رَّبِّ أَعُوذُ بِكَ مِنْ هَمَزَٰتِ ٱلشَّيَـٰطِينِ ﴿٩٧﴾

وَأَعُوذُ بِكَ رَبِّ أَن يَحْضُرُونِ ﴿٩٨﴾

حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَ أَحَدَهُمُ ٱلْمَوْتُ قَالَ رَبِّ ٱرْجِعُونِ ﴿٩٩﴾

لَعَلِّىٓ أَعْمَلُ صَـٰلِحًا فِيمَا تَرَكْتُ ۚ كَلَّآ ۚ إِنَّهَا كَلِمَةٌ هُوَ قَآئِلُهَا ۖ وَمِن وَرَآئِهِم بَرْزَخٌ إِلَىٰ يَوْمِ يُبْعَثُونَ ﴿١٠٠﴾

فَإِذَا نُفِخَ فِى ٱلصُّورِ فَلَآ أَنسَابَ بَيْنَهُمْ يَوْمَئِذٍ وَلَا يَتَسَآءَلُونَ ﴿١٠١﴾

فَمَن ثَقُلَتْ مَوَٰزِينُهُۥ فَأُو۟لَـٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُفْلِحُونَ ﴿١٠٢﴾

103. ሚዛኖቹም የቀለሉበት ሰው እነዚያ እነርሱ ነፍሶቻቸውን ያከሰሩ ናቸው፡፡ በገሀነም ውስጥ ዘመውታሪዎች ናቸው፡፡

وَمَنْ خَفَّتْ مَوَٰزِينُهُۥ فَأُو۟لَـٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓا۟ أَنفُسَهُمْ فِى جَهَنَّمَ خَـٰلِدُونَ ﴿١٠٣﴾

104. ፊቶቻቸውን እሳት ትገርፋቸዋለች፡፡ እነርሱም በእርሷ ውስጥ ከንፈሮቻቸው የተኮማተሩ ናቸው፡፡

تَلْفَحُ وُجُوهَهُمُ ٱلنَّارُ وَهُمْ فِيهَا كَـٰلِحُونَ ﴿١٠٤﴾

105. «አንቀጾቼ በእናንተ ላይ የሚነበቡላችሁና በእነርሱ የምታስተባብሉ አልነበራችሁምን» (ይባላሉ)፡፡

أَلَمْ تَكُنْ ءَايَـٰتِى تُتْلَىٰ عَلَيْكُمْ فَكُنتُم بِهَا تُكَذِّبُونَ ﴿١٠٥﴾

106. ይላሉ «ጌታችን ሆይ! በእኛ ላይ መናጢነታችን አሸነፈችን፡፡ ጠማማዎችም ሕዝቦች ነበርን፡፡

قَالُوا۟ رَبَّنَا غَلَبَتْ عَلَيْنَا شِقْوَتُنَا وَكُنَّا قَوْمًا ضَآلِّينَ ﴿١٠٦﴾

107. «ጌታችን ሆይ! ከእርሷ አውጣን፡፡ (ወደ ክህደት) ብንመለስም እኛ በደዮች ነን፡፡»

رَبَّنَآ أَخْرِجْنَا مِنْهَا فَإِنْ عُدْنَا فَإِنَّا ظَـٰلِمُونَ ﴿١٠٧﴾

108. (አላህም) «ወራዶች ኾናችሁ በውስጥዋ እርጉ፡፡ አታናግሩኝም» ይላቸዋል፡፡

قَالَ ٱخْسَـُٔوا۟ فِيهَا وَلَا تُكَلِّمُونِ ﴿١٠٨﴾

109. እነሆ ከባሮቼ «ጌታችን ሆይ! አምነናልና ማረን፡፡ እዘንልንም አንተም ከአዛኞች ሁሉ ይበልጥ አዛኝ ነህ» የሚሉ ክፍሎች ነበሩ፡፡

إِنَّهُۥ كَانَ فَرِيقٌ مِّنْ عِبَادِى يَقُولُونَ رَبَّنَآ ءَامَنَّا فَٱغْفِرْ لَنَا وَٱرْحَمْنَا وَأَنتَ خَيْرُ ٱلرَّٰحِمِينَ ﴿١٠٩﴾

110. እኔንም ማውሳትን እስካስረሷችሁ ድረስም ማላገጫ አድርጋችሁ ያዛችኋቸው፡፡ በእነርሱም የምትስቁ ነበራችሁ፡፡

فَٱتَّخَذْتُمُوهُمْ سِخْرِيًّا حَتَّىٰٓ أَنسَوْكُمْ ذِكْرِى وَكُنتُم مِّنْهُمْ تَضْحَكُونَ ﴿١١٠﴾

111. እኔ ዛሬ በትዕግስታቸው ምክንያት እነሱ ፍላጎታቸውን የሚያገኙት እነርሱ ብቻ በመኾን መነዳኋቸው፤ (ይላቸዋል)፡፡

إِنِّى جَزَيْتُهُمُ ٱلْيَوْمَ بِمَا صَبَرُوٓا۟ أَنَّهُمْ هُمُ ٱلْفَآئِزُونَ ﴿١١١﴾

112. «በምድር ውስጥ ከዓመታት ቁጥር ስንትን ቆያችሁ» ይላቸዋል፡፡

قَـٰلَ كَمْ لَبِثْتُمْ فِى ٱلْأَرْضِ عَدَدَ سِنِينَ ﴿١١٢﴾

113. «አንድ ቀንን ወይም ከፊል ቀንን ቆየን፡፡ ቆጣሪዎቹንም ጠይቅ» ይላሉ፡፡

قَالُوا۟ لَبِثْنَا يَوْمًا أَوْ بَعْضَ يَوْمٍ فَسْـَٔلِ ٱلْعَآدِّينَ ﴿١١٣﴾

114. «እናንተ (የቆያችሁትን መጠን) የምታውቁ ብትኾኑ ኖሮ (በእሳት ውስጥ በምትቆዩት አንፃር) ጥቂትን ጊዜ እንጂ አልቆያችሁም» ይላቸዋል፡፡

قَـٰلَ إِن لَّبِثْتُمْ إِلَّا قَلِيلًا ۖ لَّوْ أَنَّكُمْ كُنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿١١٤﴾

115. «የፈጠርናችሁ ለከንቱ መኾኑን እናንተም ወደኛ የማትመለሱ መኾናችሁን ጠረጠራችሁን» (ለከንቱ የፈጠርናችሁ መሰላችሁን)

أَفَحَسِبْتُمْ أَنَّمَا خَلَقْنَـٰكُمْ عَبَثًا وَأَنَّكُمْ إِلَيْنَا لَا تُرْجَعُونَ ﴿١١٥﴾

116. የእውነቱም ንጉስ አላህ ከፍተኛነት ተገባው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ የሚያምረው ዐርሽ ጌታ ነው፡፡

فَتَعَـٰلَى ٱللَّهُ ٱلْمَلِكُ ٱلْحَقُّ ۖ لَآ إِلَـٰهَ إِلَّا هُوَ رَبُّ ٱلْعَرْشِ ٱلْكَرِيمِ ﴿١١٦﴾

117. ከአላህም ጋር ሌላን አምላክ ለእርሱ በእርሱ ማስረጃ የሌለውን የሚገዛ ሰው ምርመራው እጌታው ዘንድ ብቻ ነው፡፡ እነሆ ከሓዲዎች አይድኑም፡፡

وَمَن يَدۡعُ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ لَا بُرۡهَٰنَ لَهُۥ بِهِۦ فَإِنَّمَا حِسَابُهُۥ عِندَ رَبِّهِۦٓۚ إِنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلۡكَٰفِرُونَ ﴿١١٧﴾

118. በልም «ጌታዬ ሆይ ማር፤ እዘንም፡፡ አንተም ከአዛኞች ሁሉ በላጭ ነህ፡፡»

وَقُل رَّبِّ ٱغۡفِرۡ وَٱرۡحَمۡ وَأَنتَ خَيۡرُ ٱلرَّٰحِمِينَ ﴿١١٨﴾

# ሱረቱ አል ኑር

# سورة النّور

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. (ይህች) ያወረድናትና የደነገግናት ምዕራፍ ናት፡፡ በእርሷም ውስጥ ትገሰፁ ዘንድ ግልጾችን አንቀጾች አውርደናል፡፡

سُورَةٌ أَنزَلۡنَٰهَا وَفَرَضۡنَٰهَا وَأَنزَلۡنَا فِيهَآ ءَايَٰتِۭ بَيِّنَٰتٖ لَّعَلَّكُمۡ تَذَكَّرُونَ ﴿١﴾

2. ዝሙተኛይቱና ዝሙተኛው ከሁለቱ እያንዳንዳቸውን (ያላገቡ እንደኾኑ) መቶ ግርፋትን ግረፉዋቸው፤ በእነርሱም በአላህ ፍርድ ርኅራኄ አትያዛችሁ፡፡ በአላህና በመጨረሻው ቀን የምታምኑ እንደኾናችሁ (አትራሩ)፡፡ ቅጣታቸውንም ከምእምናን ጭፍሮች ይገኙበት፡፡

ٱلزَّانِيَةُ وَٱلزَّانِي فَٱجۡلِدُواْ كُلَّ وَٰحِدٖ مِّنۡهُمَا مِاْئَةَ جَلۡدَةٖۖ وَلَا تَأۡخُذۡكُم بِهِمَا رَأۡفَةٞ فِي دِينِ ٱللَّهِ إِن كُنتُمۡ تُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِۖ وَلۡيَشۡهَدۡ عَذَابَهُمَا طَآئِفَةٞ مِّنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٢﴾

3. ዝሙተኛው ዝሙተኛይቱን ወይም አጋሪይቱን እንጂ አያገባም፡፡ ዝሙተኛይቱንም ዝሙተኛ ወይም አጋሪ እንጂ አያገባትም፡፡ ይህም በምእምናን ላይ ተከልክሏል፡ ፡

ٱلزَّانِي لَا يَنكِحُ إِلَّا زَانِيَةً أَوۡ مُشۡرِكَةٗ وَٱلزَّانِيَةُ لَا يَنكِحُهَآ إِلَّا زَانٍ أَوۡ مُشۡرِكٞۚ وَحُرِّمَ ذَٰلِكَ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٣﴾

4. እነዚያም ጥብቆችን ሴቶች (በዝሙት) የሚሰድቡ ከዚያም አራትን ምስክሮች ያላመጡ ሰማኒያን ግርፋት ግረፏቸው፡፡ ከእነርሱም ምስክርነትን ሁልጊዜ አትቀበሉ እነዚያም እነሱ አመጸኞች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَرۡمُونَ ٱلۡمُحۡصَنَٰتِ ثُمَّ لَمۡ يَأۡتُواْ بِأَرۡبَعَةِ شُهَدَآءَ فَٱجۡلِدُوهُمۡ ثَمَٰنِينَ جَلۡدَةٗ وَلَا تَقۡبَلُواْ لَهُمۡ شَهَٰدَةً أَبَدٗاۚ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ﴿٤﴾

5. እነዚያ ከዚህ በኋላ የተጸጸቱና ሥራቸውን ያሳመሩ ሲቀሩ፡፡ አላህ በጣም መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ تَابُواْ مِنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَ وَأَصۡلَحُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿٥﴾

6. እነዚያም ሚስቶቻቸውን (በዝሙት) የሚሰድቡ ለእነሱም ከነፍሶቻቸው በስተቀር ምስክሮች የሌሏቸው የኾኑ የአንዳቸው ምስክርነት እርሱ ከውነተኞች ለመኾኑ በአላህ ስም አራት ጊዜ ምሎ መመስከር ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَرۡمُونَ أَزۡوَٰجَهُمۡ وَلَمۡ يَكُن لَّهُمۡ شُهَدَآءُ إِلَّآ أَنفُسُهُمۡ فَشَهَٰدَةُ أَحَدِهِمۡ أَرۡبَعُ شَهَٰدَٰتِۭ بِٱللَّهِ إِنَّهُۥ لَمِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿٦﴾

7. አምስተኛይቱም ከውሸታሞች ቢኾን በእርሱ ላይ የአላህ እርግማን ይኑርበት (ብሎ መመስከር) ነው፡፡

وَٱلۡخَٰمِسَةُ أَنَّ لَعۡنَتَ ٱللَّهِ عَلَيۡهِ إِن كَانَ مِنَ ٱلۡكَٰذِبِينَ ٧

8. እርሱም ከውሸታሞች ነው ብላ አራት ጊዜ መመስከሮችን በአላህ ስም መመስከርዋ ከእርስዋ ላይ ቅጣትን ይገፈትርላታል፡፡

وَيَدۡرَؤُاْ عَنۡهَا ٱلۡعَذَابَ أَن تَشۡهَدَ أَرۡبَعَ شَهَٰدَٰتِۭ بِٱللَّهِ إِنَّهُۥ لَمِنَ ٱلۡكَٰذِبِينَ ٨

9. አምስተኛይቱም እርሱ ከውነተኞች ቢኾን በእርስዋ ላይ የአላህ ቁጣ ይኑርባት (ብላ መመስከርዋ) ነው፡፡

وَٱلۡخَٰمِسَةَ أَنَّ غَضَبَ ٱللَّهِ عَلَيۡهَآ إِن كَانَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ٩

10. በእናንተም ላይ የአላህ ችሮታና እዝነቱ ባልነበረ አላህም ጸጸትን ተቀባይ ጥበበኛ ባልኾነ ኖሮ (ውሸታሙን ይገልጸው ነበር)፡፡

وَلَوۡلَا فَضۡلُ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَرَحۡمَتُهُۥ وَأَنَّ ٱللَّهَ تَوَّابٌ حَكِيمٌ ١٠

11. እነዚያ መጥፎን ውሸት ያመጡ ከናንተው የኾኑ ጭፍሮች ናቸው፡፡ ለእናንተ ክፉ ነገር ነው ብላችሁ አታስቡት፡፡ በእውነቱ እርሱ ለእናንተ መልካም ነገር ነው፡፡ ከእነርሱ (ከጭፍሮቹ) ለያንዳንዱ ሰው ከኀጢአት የሠራው ሥራ ዋጋ አለው፡፡ ያም ከእነሱ ትልቁን ኀጢአት የተሸከመው ለእርሱ ከባድ ቅጣት አለው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ جَآءُو بِٱلۡإِفۡكِ عُصۡبَةٌ مِّنكُمۡۚ لَا تَحۡسَبُوهُ شَرًّا لَّكُمۖ بَلۡ هُوَ خَيۡرٌ لَّكُمۡۚ لِكُلِّ ٱمۡرِيٕٖ مِّنۡهُم مَّا ٱكۡتَسَبَ مِنَ ٱلۡإِثۡمِۚ وَٱلَّذِي تَوَلَّىٰ كِبۡرَهُۥ مِنۡهُمۡ لَهُۥ عَذَابٌ عَظِيمٞ ١١

12. (ውሸቱን) በሰማችሁት ጊዜ ምእምናንና ምእምናት በነፍሶቻቸው ለምን ደግን ነገር አልጠረጠሩም ለምንስ ይህ ግልጽ ውሸት ነው አላሉም

لَّوۡلَآ إِذۡ سَمِعۡتُمُوهُ ظَنَّ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتُ بِأَنفُسِهِمۡ خَيۡرٗا وَقَالُواْ هَٰذَآ إِفۡكٞ مُّبِينٞ ١٢

13. በእርሱ ላይ ለምን አራትን ምስክሮች አላመጡም ምስክሮቹንም ካላመጡ እነዚያ አላህ ዘንድ ውሸታሞቹ እነሱ ናቸው፡፡

لَّوۡلَا جَآءُو عَلَيۡهِ بِأَرۡبَعَةِ شُهَدَآءَۚ فَإِذۡ لَمۡ يَأۡتُواْ بِٱلشُّهَدَآءِ فَأُوْلَٰٓئِكَ عِندَ ٱللَّهِ هُمُ ٱلۡكَٰذِبُونَ ١٣

14. በቅርቢቱም በመጨረሻይቱም ዓለም በእናንተ ላይ የአላህ ችሮታና እዝነቱ ባልነበረ ኖሮ በውስጡ በገባችሁበት ወሬ ምክንያት ታላቅ ቅጣት በእርግጥ በደረሰባችሁ ነበር፡፡

وَلَوۡلَا فَضۡلُ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَرَحۡمَتُهُۥ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ لَمَسَّكُمۡ فِي مَآ أَفَضۡتُمۡ فِيهِ عَذَابٌ عَظِيمٌ ١٤

15. በምላሶቻችሁ በምትቀበባሉት ጊዜ ለእናንተም በእርሱ ዕውቀት በሌላችሁ ነገር በአፎቻችሁ በተናገራችሁና እርሱ አላህ ዘንድ ከባድ ኀጢአት ኾኖ ሳለ ቀላል አድርጋችሁ ባሰባችሁት ጊዜ (ከባድ ቅጣት በነካችሁ ነበር)፡፡

إِذۡ تَلَقَّوۡنَهُۥ بِأَلۡسِنَتِكُمۡ وَتَقُولُونَ بِأَفۡوَاهِكُم مَّا لَيۡسَ لَكُم بِهِۦ عِلۡمٞ وَتَحۡسَبُونَهُۥ هَيِّنٗا وَهُوَ عِندَ ٱللَّهِ عَظِيمٞ ١٥

16. በሰማችሁትም ጊዜ በዚህ ልንናገር ለእኛ አይገባንም፡፡ ጥራት ይገባህ፡፡ ይህ ከባድ ቅጥፈት ነው፤ አትሉም ነበርን

وَلَوۡلَآ إِذۡ سَمِعۡتُمُوهُ قُلۡتُم مَّا يَكُونُ لَنَآ أَن نَّتَكَلَّمَ بِهَٰذَا سُبۡحَٰنَكَ هَٰذَا بُهۡتَٰنٌ عَظِيمٞ ١٦

17. ምእመናን እንደኾናችሁ ወደ ብጤው በፍፁም እንዳትመለሱ አላህ ይገስጻችኋል፡፡

يَعِظُكُمُ ٱللَّهُ أَن تَعُودُواْ لِمِثۡلِهِۦٓ أَبَدًا إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ١٧

18. ለእናንተም አላህ አንቀጾችን ይገልጽላችኋል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَيُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمُ ٱلۡأٓيَٰتِۚ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ١٨

19. እነዚያ በእነዚያ ባመኑት ሰዎች ውስጥ መጥፎ ወሬ እንድትስፋፋ የሚወዱ ለእነሱ በቅርቢቱም በመጨረሻይቱም ዓለም አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡ አላህም ያውቃል እናንተ ግን አታውቁም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُحِبُّونَ أَن تَشِيعَ ٱلۡفَٰحِشَةُ فِي ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ وَأَنتُمۡ لَا تَعۡلَمُونَ ١٩

20. በእናንተም ላይ የአላህ ችሮታውና እዝነቱ ባልነበረ አላህም ሩኅሩኅና አዛኝ ባልኾነ ኖሮ (ቶሎ ባጠፋችሁ ነበር)፡፡

وَلَوۡلَا فَضۡلُ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَرَحۡمَتُهُۥ وَأَنَّ ٱللَّهَ رَءُوفٞ رَّحِيمٞ ٢٠

21. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! የሰይጣንን እርምጃዎች አትከተሉ፡፡ የሰይጣንንም እርምጃዎች የሚከተል ሰው (ኀጢአትን ተሸከመ)፡፡ እርሱ በመጥፎና በሚጠላ ነገር ያዛልና፡፡ በእናንተም ላይ የአላህ ችሮታና እዝነቱ ባልነበረ ኖሮ ከናንተ አንድም ፈጽሞ ባልጠራ ነበር፡፡ ግን አላህ የሚሻውን ሰው ያጠራል፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

۞يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّبِعُواْ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيۡطَٰنِۚ وَمَن يَتَّبِعۡ خُطُوَٰتِ ٱلشَّيۡطَٰنِ فَإِنَّهُۥ يَأۡمُرُ بِٱلۡفَحۡشَآءِ وَٱلۡمُنكَرِۚ وَلَوۡلَا فَضۡلُ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ وَرَحۡمَتُهُۥ مَا زَكَىٰ مِنكُم مِّنۡ أَحَدٍ أَبَدٗا وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يُزَكِّي مَن يَشَآءُۗ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ٢١

22. ከእናንተም የችሮታና የክብረት ባለቤቶች የኾኑት ለቅርብ ዘመዶችና ለድኾች በአላህም መንገድ ለተሰደዱ ሰዎች ላይሰጡ አይማሉ፡፡ ይቅርታም ያድርጉ፡፡ (ጥፋተኞቹን) ይለፉም፡፡ አላህ ለእናንተ ሊምር አትወዱምን አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلَا يَأۡتَلِ أُوْلُواْ ٱلۡفَضۡلِ مِنكُمۡ وَٱلسَّعَةِ أَن يُؤۡتُوٓاْ أُوْلِي ٱلۡقُرۡبَىٰ وَٱلۡمَسَٰكِينَ وَٱلۡمُهَٰجِرِينَ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِۖ وَلۡيَعۡفُواْ وَلۡيَصۡفَحُوٓاْۗ أَلَا تُحِبُّونَ أَن يَغۡفِرَ ٱللَّهُ لَكُمۡۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ٢٢

23. እነዚያ ጥብቆቹን ከዝሙት ዘንጊዎቹን ምእምናት የሚሰድቡ፤ በቅርቢቱም በመጨረሻይቱም ዓለም ተረገሙ፡፡ ለእነርሱም ታላቅ ቅጣት አላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَرۡمُونَ ٱلۡمُحۡصَنَٰتِ ٱلۡغَٰفِلَٰتِ ٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ لُعِنُواْ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ وَلَهُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٞ ٢٣

24. በእነሱ ላይ ምላሶቻቸው፣ እጆቻቸውና እግሮቻቸውም ይሠሩት በነበሩት ነገር በሚመሰክሩባቸው ቀን (ከባድ ቅጣት አላቸው)፡፡

يَوۡمَ تَشۡهَدُ عَلَيۡهِمۡ أَلۡسِنَتُهُمۡ وَأَيۡدِيهِمۡ وَأَرۡجُلُهُم بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٢٤

25. በዚያ ቀን አላህ እውነተኛ ዋጋቸውን ይሞላላቸዋል፡፡ አላህም እርሱ መኖሩ የተረጋገጠ (ሁሉን ነገር) ገላጭ መኾኑን ያውቃሉ፡፡

يَوۡمَئِذٖ يُوَفِّيهِمُ ٱللَّهُ دِينَهُمُ ٱلۡحَقَّ وَيَعۡلَمُونَ أَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡحَقُّ ٱلۡمُبِينُ ٢٥

26. መጥፎዎቹ ሴቶች ለመጥፎዎች ወንዶች መጥፎዎቹ ወንዶችም ለመጥፎዎቹ ሴቶች የተገቡ ናቸው፡፡ ጥሩዎቹ ሴቶችም ለጥሩዎቹ ወንዶች ጥሩዎቹ ወንዶችም ለጥሩዎቹ ሴቶች የሚገቡ ናቸው፡፡ እነዚያ (መጥፎዎቹ) ከሚሉት ነገር ንጹሕ የተደረጉ ናቸው፡፡ ለእነርሱ ምህረትና መልካም ሲሳይ አላቸው፡፡

ٱلْخَبِيثَٰتُ لِلْخَبِيثِينَ وَٱلْخَبِيثُونَ لِلْخَبِيثَٰتِ ۖ وَٱلطَّيِّبَٰتُ لِلطَّيِّبِينَ وَٱلطَّيِّبُونَ لِلطَّيِّبَٰتِ ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ مُبَرَّءُونَ مِمَّا يَقُولُونَ ۖ لَهُم مَّغْفِرَةٌ وَرِزْقٌ كَرِيمٌ ﴿٢٦﴾

27. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እስከምታስፈቅዱና በባለቤቶቿ ላይ ሰላምታን እስከምታቀርቡ ድረስ ከቤቶቻችሁ ሌላ የኾኑን ቤቶች አትግቡ፡፡ ይህ ለእናንተ መልካም ነው፡፡ እናንተ ትገነዘቡ ዘንድ (በዚህ ታዘዛችሁ)፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ لَا تَدْخُلُوا۟ بُيُوتًا غَيْرَ بُيُوتِكُمْ حَتَّىٰ تَسْتَأْنِسُوا۟ وَتُسَلِّمُوا۟ عَلَىٰٓ أَهْلِهَا ۚ ذَٰلِكُمْ خَيْرٌ لَّكُمْ لَعَلَّكُمْ تَذَكَّرُونَ ﴿٢٧﴾

28. በውስጧም አንድንም ሰው ባታገኙ ለእናንተ እስከሚፈቀድላችሁ ድረስ አትግቧት፡፡ ለእናንተ ተመለሱ ብትባሉም ተመለሱ፡፡ እርሱ ለእናንተ የተሻለ ነው፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

فَإِن لَّمْ تَجِدُوا۟ فِيهَآ أَحَدًا فَلَا تَدْخُلُوهَا حَتَّىٰ يُؤْذَنَ لَكُمْ ۖ وَإِن قِيلَ لَكُمُ ٱرْجِعُوا۟ فَٱرْجِعُوا۟ ۖ هُوَ أَزْكَىٰ لَكُمْ ۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ عَلِيمٌ ﴿٢٨﴾

29. መኖሪያ ያልኾኑን ቤቶች በውስጣቸው ለእናንተ ጥቅም ያላችሁን (ሳታስፈቅዱ) ብትገቡ በእናንተ ላይ ኀጢአት የለባችሁም፡፡ አላህም የምትገልጹትንና የምትደብቁትን ሁሉ ያውቃል፡፡

لَّيْسَ عَلَيْكُمْ جُنَاحٌ أَن تَدْخُلُوا۟ بُيُوتًا غَيْرَ مَسْكُونَةٍ فِيهَا مَتَٰعٌ لَّكُمْ ۚ وَٱللَّهُ يَعْلَمُ مَا تُبْدُونَ وَمَا تَكْتُمُونَ ﴿٢٩﴾

30. ለምእመናን ንገራቸው፡- ዓይኖቻቸውን (ያልተፈቀደን ከማየት) ይከልክሉ፤ ብልቶቻቸውንም ይጠብቁ፤ ይህ ለነሱ የተሻለ ነው፤ አላህ በሚሠሩት ሁሉ ውስጥ ዐዋቂ ነው፡፡

قُل لِّلْمُؤْمِنِينَ يَغُضُّوا۟ مِنْ أَبْصَٰرِهِمْ وَيَحْفَظُوا۟ فُرُوجَهُمْ ۚ ذَٰلِكَ أَزْكَىٰ لَهُمْ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرٌۢ بِمَا يَصْنَعُونَ ﴿٣٠﴾

31. ለምእምናትም ንገራቸው፡- ዓይኖቻቸውን ይከልክሉ፡፡ ብልቶቻቸውንም ይጠብቁ፡፡ ጌጣቸውንም ከእርሷ ግልጽ ከኾነው በስተቀር አይግለጡ፡፡ ጉፍታዎቻቸውንም በአንገትጌዎቻቸው ላይ ያጣፉ፡፡ (የውስጥ) ጌጣቸውንም ለባሎቻቸው ወይም ለአባቶቻቸው ወይም ለባሎቻቸው አባቶች ወይም ለወንዶች ልጆቻቸው ወይም ለባሎቻቸው ወንዶች ልጆች ወይም ለወንድሞቻቸው ወይም ለወንድሞቻቸው ወንዶች ልጆች ወይም ለእህቶቻቸው ወንዶች ልጆች ወይም ለሴቶቻቸው ወይም እጆቻቸው ለያዙት (ባሪያ) ወይም ከወንዶች ለሴት ጉዳይ የሌላቸው ለኾኑ ተከታዮች ወይም ለነዚያ በሴቶች ሐፍረተ ገላ ላይ ላላወቁ ሕፃናት ካልኾነ በስተቀር አይግለጹ፡፡ ከጌጣቸውም የሚሸፍኑት ይታወቅ ዘንድ በእግሮቻቸው አይምቱ፡፡ ምእመናኖች ሆይ! ትድኑ ዘንድ ሁላችሁም ወደ አላህ (በመመለስ) ተጸጸቱ፡፡

وَقُل لِّلْمُؤْمِنَٰتِ يَغْضُضْنَ مِنْ أَبْصَٰرِهِنَّ وَيَحْفَظْنَ فُرُوجَهُنَّ وَلَا يُبْدِينَ زِينَتَهُنَّ إِلَّا مَا ظَهَرَ مِنْهَا ۖ وَلْيَضْرِبْنَ بِخُمُرِهِنَّ عَلَىٰ جُيُوبِهِنَّ ۖ وَلَا يُبْدِينَ زِينَتَهُنَّ إِلَّا لِبُعُولَتِهِنَّ أَوْ ءَابَآئِهِنَّ أَوْ ءَابَآءِ بُعُولَتِهِنَّ أَوْ أَبْنَآئِهِنَّ أَوْ أَبْنَآءِ بُعُولَتِهِنَّ أَوْ إِخْوَٰنِهِنَّ أَوْ بَنِىٓ إِخْوَٰنِهِنَّ أَوْ بَنِىٓ أَخَوَٰتِهِنَّ أَوْ نِسَآئِهِنَّ أَوْ مَا مَلَكَتْ أَيْمَٰنُهُنَّ أَوِ ٱلتَّٰبِعِينَ غَيْرِ أُو۟لِى ٱلْإِرْبَةِ مِنَ ٱلرِّجَالِ أَوِ ٱلطِّفْلِ ٱلَّذِينَ لَمْ يَظْهَرُوا۟ عَلَىٰ عَوْرَٰتِ ٱلنِّسَآءِ ۖ وَلَا يَضْرِبْنَ بِأَرْجُلِهِنَّ لِيُعْلَمَ مَا يُخْفِينَ مِن زِينَتِهِنَّ ۚ وَتُوبُوٓا۟ إِلَى ٱللَّهِ جَمِيعًا أَيُّهَ ٱلْمُؤْمِنُونَ لَعَلَّكُمْ تُفْلِحُونَ ﴿٣١﴾

وَأَنكِحُواْ ٱلۡأَيَٰمَىٰ مِنكُمۡ وَٱلصَّٰلِحِينَ مِنۡ عِبَادِكُمۡ وَإِمَآئِكُمۡۚ إِن يَكُونُواْ فُقَرَآءَ يُغۡنِهِمُ ٱللَّهُ مِن فَضۡلِهِۦۗ وَٱللَّهُ وَٰسِعٌ عَلِيمٞ ٣٢

32. ከናንተም ትዳር የሌላቸውን አጋቡ፡፡ ከወንዶች ባሮቻችሁና ከሴቶች ባሮቻችሁም ለጋብቻ ብቁ የኾኑትን (አጋቡ)፡፡ ድኾች ቢኾኑ አላህ ከችሮታው ያከብራቸዋል፡፡ አላህም ስጦታው ሰፊ ዐዋቂ ነው፡፡

وَلۡيَسۡتَعۡفِفِ ٱلَّذِينَ لَا يَجِدُونَ نِكَاحًا حَتَّىٰ يُغۡنِيَهُمُ ٱللَّهُ مِن فَضۡلِهِۦۗ وَٱلَّذِينَ يَبۡتَغُونَ ٱلۡكِتَٰبَ مِمَّا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُكُمۡ فَكَاتِبُوهُمۡ إِنۡ عَلِمۡتُمۡ فِيهِمۡ خَيۡرٗاۖ وَءَاتُوهُم مِّن مَّالِ ٱللَّهِ ٱلَّذِيٓ ءَاتَىٰكُمۡۚ وَلَا تُكۡرِهُواْ فَتَيَٰتِكُمۡ عَلَى ٱلۡبِغَآءِ إِنۡ أَرَدۡنَ تَحَصُّنٗا لِّتَبۡتَغُواْ عَرَضَ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۚ وَمَن يُكۡرِههُّنَّ فَإِنَّ ٱللَّهَ مِنۢ بَعۡدِ إِكۡرَٰهِهِنَّ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٣٣

33. እነዚያም የማግቢያን ጣጣ የማያገኙ አላህ ከችሮታው እስከሚያከብራቸው ድረስ ይጠበቁ፡፡ እነዚያንም እጆቻችሁ ከጨበጧቸው አገልጋዮች (ገንዘብ ሰጥተው ነጻ ለመውጣት) መጻጻፍን የሚፈልጉትን ከእነሱ መልካምን ነገር ብታውቁ ተጻጻፉዋቸው፡፡ ከአላህም ገንዘብ ከዚያ ከሰጣችሁ ስጧቸው፡፡ ሴቶች ባሮቻችሁንም መጥጠበቅን ቢፈልጉ የቅርቢቱን ሕይወት ጥቅም ለመፈለግ ብላችሁ በዝሙት ላይ አታስገድዱዋቸው፡፡ የሚያስገድዳቸውም ሰው አላህ ከመገደዳቸው በኋላ (ለተገደዱት) መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلَقَدۡ أَنزَلۡنَآ إِلَيۡكُمۡ ءَايَٰتٖ مُّبَيِّنَٰتٖ وَمَثَلٗا مِّنَ ٱلَّذِينَ خَلَوۡاْ مِن قَبۡلِكُمۡ وَمَوۡعِظَةٗ لِّلۡمُتَّقِينَ ٣٤

34. ወደእናንተም አብራሪ የኾኑን አንቀጾች ከእነዚያ ከበፊታችሁ ካለፉትም (ምሳሌዎች ዓይነት) ምሳሌን ለጥንቁቆቹ መገሰጫንም በእርግጥ አወረድን፡፡

۞ٱللَّهُ نُورُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ مَثَلُ نُورِهِۦ كَمِشۡكَوٰةٖ فِيهَا مِصۡبَاحٌۖ ٱلۡمِصۡبَاحُ فِي زُجَاجَةٍۖ ٱلزُّجَاجَةُ كَأَنَّهَا كَوۡكَبٞ دُرِّيّٞ يُوقَدُ مِن شَجَرَةٖ مُّبَٰرَكَةٖ زَيۡتُونَةٖ لَّا شَرۡقِيَّةٖ وَلَا غَرۡبِيَّةٖ يَكَادُ زَيۡتُهَا يُضِيٓءُ وَلَوۡ لَمۡ تَمۡسَسۡهُ نَارٞۚ نُّورٌ عَلَىٰ نُورٖۚ يَهۡدِي ٱللَّهُ لِنُورِهِۦ مَن يَشَآءُۚ وَيَضۡرِبُ ٱللَّهُ ٱلۡأَمۡثَٰلَ لِلنَّاسِۗ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ٣٥

35. አላህ የሰማያትና የምድር አብሪ ነው፡፡ የብርሃኑ ምሳሌ በውስጧ መብራት እንዳለባት (ዝግ) መስኮት፣ መብራቱ በብርጭቆ ውስጥ የኾነ፣ ብርጭቆይቱ ፍፁም ሉላዊ ኮከብ የምትመስል፣ ምሥራቃዊው ምዕራባዊም ካልኾነች ከተባረከች የወይራ ዛፍ ዘይቷ እሳት ባይነካውም እንኳ ሊያበራ የሚቀርብ ከኾነች (ዘይት) የሚቃጠል እንደ ሆነ (መብራት) ነው፡፡ (ይህ) በብርሃን ላይ የኾነ ብርሃን ነው፡፡ አላህ ወደ ብርሃኑ የሚሻውን ሰው ይመራል፡፡ አላህም ለሰዎች ምሳሌዎችን ያቀርባል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

فِي بُيُوتٍ أَذِنَ ٱللَّهُ أَن تُرۡفَعَ وَيُذۡكَرَ فِيهَا ٱسۡمُهُۥ يُسَبِّحُ لَهُۥ فِيهَا بِٱلۡغُدُوِّ وَٱلۡأٓصَالِ ٣٦

36. አላህ እንድትከበርና ስሙ በውስጧ እንዲወሳ ባዘዘው ቤቶች ውስጥ (አወድሱት)፡፡ በውስጧ በጧትና በማታ ለእርሱ ያጠራሉ፡፡

رِجَالٞ لَّا تُلۡهِيهِمۡ تِجَٰرَةٞ وَلَا بَيۡعٌ عَن ذِكۡرِ ٱللَّهِ وَإِقَامِ ٱلصَّلَوٰةِ وَإِيتَآءِ ٱلزَّكَوٰةِ يَخَافُونَ يَوۡمٗا تَتَقَلَّبُ فِيهِ ٱلۡقُلُوبُ وَٱلۡأَبۡصَٰرُ ٣٧

37. አላህን ከማውሳትና ሶላትን ከመስገድ ዘካንም ከመስጠት ንግድም ሽያጭም የማያታልላቸው ልቦችና ዓይኖች በእርሱ የሚገላበጡበትን ቀን የሚፈሩ የኾኑ ሰዎች (ያጠሩታል)፡፡

38. አላህ የሠሩትን ሥራ መልካሙን ሊመነዳቸው ከችሮታውም ሊጨመርላቸው (ያጠሩታል)፡፡ አላህም ለሚሻው ሰው ያለ ግምት ይሰጣል፡፡

لِيَجۡزِيَهُمُ ٱللَّهُ أَحۡسَنَ مَا عَمِلُواْ وَيَزِيدَهُم مِّن فَضۡلِهِۦۗ وَٱللَّهُ يَرۡزُقُ مَن يَشَآءُ بِغَيۡرِ حِسَابٖ ٣٨

39. እነዚያም የካዱት ሰዎች ሥራዎቻቸው (መልካሞቹ) በበረሃ ሜዳ እንዳለ ሲራብዱ የጠማው ሰው ውሃ ነው ብሎ እንደሚያስበው በመጣውም ጊዜ ምንም ነገር ኾኖ እንደማያገኘው ነው፡፡ (ከሓዲው) አላህንም እሥራው ዘንድ ያገኘዋል፡፡ ምርመራውንም (ቅጣቱን) ይሞላለታል፡፡ አላህም ምርመራው ፈጣን ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَعۡمَٰلُهُمۡ كَسَرَابِۭ بِقِيعَةٖ يَحۡسَبُهُ ٱلظَّمۡـَٔانُ مَآءً حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَهُۥ لَمۡ يَجِدۡهُ شَيۡـٔٗا وَوَجَدَ ٱللَّهَ عِندَهُۥ فَوَفَّىٰهُ حِسَابَهُۥۗ وَٱللَّهُ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ٣٩

40. ወይም (መጥፎ ሥራዎቻቸውን) ከበላዩ ደመና ያለበት ማዕበል በሚሸፍነው ጥልቅ ባህር ውስጥ እንዳሉ ጨለማዎች ነው፡፡ (እነዚያ) ከፊላቸው ከከፊሉ በላይ ድርብርብ የኾኑ ጨለማዎች ናቸው፡፡ (በዚህች) የተሞከረ (ሰው) እጁን ባወጣ ጊዜ ሊያያት አይቀርብም፡ ፡ አላህም ለእርሱ ብርሃንን ያላደረገለት ሰው ለእርሱ ምንም ብርሃን የለውም፡፡

أَوۡ كَظُلُمَٰتٖ فِي بَحۡرٖ لُّجِّيّٖ يَغۡشَىٰهُ مَوۡجٞ مِّن فَوۡقِهِۦ مَوۡجٞ مِّن فَوۡقِهِۦ سَحَابٞۚ ظُلُمَٰتُۢ بَعۡضُهَا فَوۡقَ بَعۡضٍ إِذَآ أَخۡرَجَ يَدَهُۥ لَمۡ يَكَدۡ يَرَىٰهَاۗ وَمَن لَّمۡ يَجۡعَلِ ٱللَّهُ لَهُۥ نُورٗا فَمَا لَهُۥ مِن نُّورٍ ٤٠

41. አላህ በሰማያትና በምድር ያለ ሁሉ በራሪዎችም ክንፎቻቸውን (በአየር ላይ) ያንሳፈፉ ኾነው ለእርሱ የሚያጠሩ (የሚያወድሱ) መኾናቸውን አላወቅህምን ሁሉም ስግደቱንና ማጥራቱን በእርግጥ ዐወቀ፡፡ አላህም የሚሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ يُسَبِّحُ لَهُۥ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَٱلطَّيۡرُ صَٰٓفَّٰتٖۖ كُلّٞ قَدۡ عَلِمَ صَلَاتَهُۥ وَتَسۡبِيحَهُۥۗ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِمَا يَفۡعَلُونَ ٤١

42. የሰማያትና የምድርም ግዛት የአላህ ነው፡፡ መመለሻም ወደ አላህ ነው፡፡

وَلِلَّهِ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَإِلَى ٱللَّهِ ٱلۡمَصِيرُ ٤٢

43. አላህ ደመናን የሚነዳ መኾኑን አላየህምን ከዚያም ከፊሉን ከከፊሉ ያገናኛል፡፡ ከዚያም የተደራረበ ያደርገዋል፡፡ ዝናቡንም ከመካከሉ የሚወጣ ኾኖ ታየዋለህ፡፡ ከሰማይም (ከደመና) በውስጧ ካሉት ጋራዎች በረዶን ያወርዳል፡፡ በእርሱም የሚሻውን ሰው (በጉዳት) ይነካል፡፡ ከሚሻውም ሰው ላይ ይመልሰዋል፡ ፡ የብልጭታው ብርሃን ዓይኖችን ሊወስድ ይቀርባል፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ يُزۡجِي سَحَابٗا ثُمَّ يُؤَلِّفُ بَيۡنَهُۥ ثُمَّ يَجۡعَلُهُۥ رُكَامٗا فَتَرَى ٱلۡوَدۡقَ يَخۡرُجُ مِنۡ خِلَٰلِهِۦ وَيُنَزِّلُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مِن جِبَالٖ فِيهَا مِنۢ بَرَدٖ فَيُصِيبُ بِهِۦ مَن يَشَآءُ وَيَصۡرِفُهُۥ عَن مَّن يَشَآءُۖ يَكَادُ سَنَا بَرۡقِهِۦ يَذۡهَبُ بِٱلۡأَبۡصَٰرِ ٤٣

44. አላህ ሌሊትንና ቀንን ያገላብጣል፡፡ በዚህም ለባለ ውስጥ ዓይኖች በእርግጥ ማስረጃ አልለበት፡፡

يُقَلِّبُ ٱللَّهُ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَعِبۡرَةٗ لِّأُوْلِي ٱلۡأَبۡصَٰرِ ٤٤

45. አላህም ተንቀሳቃሽን ሁሉ ከውሃ ፈጠረ፡፡ ከእነሱም በሆዱ ላይ የሚኼድ አልለ፡፡ ከእነሱም በሁለት እግሮች ላይ የሚኼድ አልለ፡፡ አላህ የሚሻውን ሁሉ ይፈጥራል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

وَٱللَّهُ خَلَقَ كُلَّ دَآبَّةٖ مِّن مَّآءٖۖ فَمِنۡهُم مَّن يَمۡشِي عَلَىٰ بَطۡنِهِۦ وَمِنۡهُم مَّن يَمۡشِي عَلَىٰ رِجۡلَيۡنِ وَمِنۡهُم مَّن يَمۡشِي عَلَىٰٓ أَرۡبَعٖۚ يَخۡلُقُ ٱللَّهُ مَا يَشَآءُۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٤٥

46. አብራሪን አንቀጾች በእርግጥ አወረድን፡፡ አላህም የሚሻውን ሰው ወደ ቀጥተኛ መንገድ ይመራዋል፡፡

لَّقَدۡ أَنزَلۡنَآ ءَايَٰتٖ مُّبَيِّنَٰتٖۚ وَٱللَّهُ يَهۡدِي مَن يَشَآءُ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ﴿٤٦﴾

47. በአላህና በመልክተኛውም አምነናል ታዘናልም ይላሉ፡፡ ከዚያም ከዚህ በኋላ ከእነሱ ከፊሉ ይሸሻል፡፡ እነዚያም ምእምናን አይደሉም፤

وَيَقُولُونَ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَبِٱلرَّسُولِ وَأَطَعۡنَا ثُمَّ يَتَوَلَّىٰ فَرِيقٞ مِّنۡهُم مِّنۢ بَعۡدِ ذَٰلِكَۚ وَمَآ أُوْلَٰٓئِكَ بِٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٤٧﴾

48. ወደ አላህና ወደ መልክተኛውም በመካከላቸው ሊፈርድ በተጠሩ ጊዜ ከእነሱ ከፊሉ ወዲያውኑ ይሸሻሉ፡
፡

وَإِذَا دُعُوٓاْ إِلَى ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ لِيَحۡكُمَ بَيۡنَهُمۡ إِذَا فَرِيقٞ مِّنۡهُم مُّعۡرِضُونَ ﴿٤٨﴾

49. እውነቱም (ሐቁ) ለእነሱ ቢኾን ወደርሱ ታዛዦች ኾነው ይመጣሉ፡፡

وَإِن يَكُن لَّهُمُ ٱلۡحَقُّ يَأۡتُوٓاْ إِلَيۡهِ مُذۡعِنِينَ ﴿٤٩﴾

50. በልቦቻቸው ውስጥ በሺታ አለን ወይስ (በነቢይነቱ) ተጠራጠሩን ወይስ አላህና መልክተኛው በእነሱ ላይ የሚበድሉ መኾንን ይፈራሉን ይልቁንም፤ እነዚያ እነሱ በዳዮቹ ናቸው፡፡

أَفِي قُلُوبِهِم مَّرَضٌ أَمِ ٱرۡتَابُوٓاْ أَمۡ يَخَافُونَ أَن يَحِيفَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمۡ وَرَسُولُهُۥۚ بَلۡ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ﴿٥٠﴾

51. የምእምናን ቃል የነበረው ወደ አላህና ወደ መልክተኛው በመካከላቸው ሊፈርድ በተጠሩ ጊዜ ሰማን፤ ታዘዝንም ማለት ብቻ ነው፡፡ እነዚህም እነሱ የፈለጉትን የሚያገኙ ናቸው፡፡

إِنَّمَا كَانَ قَوۡلَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ إِذَا دُعُوٓاْ إِلَى ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ لِيَحۡكُمَ بَيۡنَهُمۡ أَن يَقُولُواْ سَمِعۡنَا وَأَطَعۡنَاۚ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ﴿٥١﴾

52. አላህንና መልክተኛውን የሚታዘዝም ሰው፣ አላህንም የሚፈራና የሚጠነቀቀው ሰው፤ እነዚያ እነርሱ ፍለጎታቸውን የሚያገኙ ናቸው፡፡

وَمَن يُطِعِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَيَخۡشَ ٱللَّهَ وَيَتَّقۡهِ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَآئِزُونَ ﴿٥٢﴾

53. (ለዘመቻ) ብታዛቸውም በእርግጥ ሊወጡ የጠነከሩ መሓሎቻቸውን በአላህ ስም ይምላሉ፡፡ «አትማሉ፤ የታወቀች (የንፍቅና) መታዘዝ ናትና፡፡ አላህ በምትሠሩት ነገር ሁሉ ውስጥ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

۞وَأَقۡسَمُواْ بِٱللَّهِ جَهۡدَ أَيۡمَٰنِهِمۡ لَئِنۡ أَمَرۡتَهُمۡ لَيَخۡرُجُنَّۖ قُل لَّا تُقۡسِمُواْۖ طَاعَةٞ مَّعۡرُوفَةٌۚ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ﴿٥٣﴾

54. «አላህን ተገዙ፡፡ መልክተኛውንም ታዘዙ፤ ብትሸሹም (አትጎዱትም)፡፡ በእርሱ ላይ ያለበት የተገደደውን ማድረስ ብቻ ነው፡፡ በእናንተም ላይ ያለባችሁ የተገደዳችሁት (መታዘዝ) ብቻ ነው፡፡ ብትታዘዙትም ትምመራላችሁ፡፡ በመልእክተኛውም ላይ ግልጽ ማድረስ እንጂ ሌላ የለበትም» በላቸው፡፡

قُلۡ أَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُواْ ٱلرَّسُولَۖ فَإِن تَوَلَّوۡاْ فَإِنَّمَا عَلَيۡهِ مَا حُمِّلَ وَعَلَيۡكُم مَّا حُمِّلۡتُمۡۖ وَإِن تُطِيعُوهُ تَهۡتَدُواْۚ وَمَا عَلَى ٱلرَّسُولِ إِلَّا ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ﴿٥٤﴾

55. አላህ እነዚያን ከእናንተ ያመኑትንና መልካም ሥራዎችን የሠሩትን እነዚያን ከእነሱ በፊት የነበሩትን እንደተካ በምድር ላይ በእርግጥ ሊተካቸው፣ ለእነሱም ያንን የወደደላቸውን ሃይማኖታቸውን ሊያደላድልላቸው፣ ከፍርሃታቸውም በኋላ ጸጥታን ሊለውጥላቸው ተስፋን ቃል ሰጥቷቸዋል፡፡ በእኔ ምንንም የማያጋሩ ኾነው ይግገዙኛል፡፡ ከዚያም በኋላ የካደ ሰው እነዚያ እነርሱ አመጸኞች ናቸው፡፡

وَعَدَ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مِنكُمۡ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَيَسۡتَخۡلِفَنَّهُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ كَمَا ٱسۡتَخۡلَفَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ وَلَيُمَكِّنَنَّ لَهُمۡ دِينَهُمُ ٱلَّذِي ٱرۡتَضَىٰ لَهُمۡ وَلَيُبَدِّلَنَّهُم مِّنۢ بَعۡدِ خَوۡفِهِمۡ أَمۡنٗاۚ يَعۡبُدُونَنِي لَا يُشۡرِكُونَ بِي شَيۡـٔٗاۚ وَمَن كَفَرَ بَعۡدَ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ۝٥٥

56. ሶላትንም አስተካክላችሁ ስገዱ፡፡ ምጽዋትንም ስጡ፡፡ መልክተኛውንም ታዘዙ፡፡ ለእናንተ ሊታዘንላችሁ ይከጀላልና፡፡

وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُواْ ٱلزَّكَوٰةَ وَأَطِيعُواْ ٱلرَّسُولَ لَعَلَّكُمۡ تُرۡحَمُونَ ۝٥٦

57. እነዚያን የካዱትን በምድር ውስጥ የሚያቅቱ አድርገህ አታስብ፡፡ መኖሪያቸውም እሳት ናት፡፡ በእርግጥም የከፉች መመለሻ ናት፡፡

لَا تَحۡسَبَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مُعۡجِزِينَ فِي ٱلۡأَرۡضِۚ وَمَأۡوَىٰهُمُ ٱلنَّارُۖ وَلَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ۝٥٧

58. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እነዚያ እጆቻችሁ የጨበጧቸው (ባሮች) እነዚያም ከእናንተ ለአካላ መጠን ያልደረሱት ከጎህ ስግደት በፊት፣ በቀትርም ልብሶቻችሁን በምታወልቁ ጊዜ ከምሽት ስግደትም በኋላ ሦስት ጊዜያት (ለመግባት ሲፈልጉ) ያስፈቅዷችሁ፡፡ (እነዚህ) ለእናንተ የኾኑ ሦስት የሐፍረተ ገላ መገለጫ ጊዜያቶች ናቸውና፡፡ ከእነዚህ በኋላ በእናንተም በእነርሱም ላይ (ያለፈቃድ በመግባት) ኀጢአት የለም፡፡ በእናንተ ላይ (ለማገልገል) ዙዋሪዎች ናቸውና፡፡ ከፊላችሁ በከፊሉ ላይ ዙዋሪ ነው፡፡ እንደዚሁ አላህ ለእናንተ ሕግጋትን ይገልጽላችኋል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لِيَسۡتَـٔۡذِنكُمُ ٱلَّذِينَ مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُكُمۡ وَٱلَّذِينَ لَمۡ يَبۡلُغُواْ ٱلۡحُلُمَ مِنكُمۡ ثَلَٰثَ مَرَّٰتٖۚ مِّن قَبۡلِ صَلَوٰةِ ٱلۡفَجۡرِ وَحِينَ تَضَعُونَ ثِيَابَكُم مِّنَ ٱلظَّهِيرَةِ وَمِنۢ بَعۡدِ صَلَوٰةِ ٱلۡعِشَآءِۚ ثَلَٰثُ عَوۡرَٰتٖ لَّكُمۡۚ لَيۡسَ عَلَيۡكُمۡ وَلَا عَلَيۡهِمۡ جُنَاحُۢ بَعۡدَهُنَّۚ طَوَّٰفُونَ عَلَيۡكُم بَعۡضُكُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖۚ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمُ ٱلۡأٓيَٰتِۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٞ ۝٥٨

59. ከእናንተም ሕፃናቶቹ አቅመ አዳምን በደረሱ ጊዜ እነዚያ ከእነሱ በፊት የነበሩት (ታላላቆቹ) እንዳስፈቀዱ ያስፈቅዱ፡፡ እንደዚሁ አላህ ለእናንተ አንቀጾቹን ያብራራል፤ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَإِذَا بَلَغَ ٱلۡأَطۡفَٰلُ مِنكُمُ ٱلۡحُلُمَ فَلۡيَسۡتَـٔۡذِنُواْ كَمَا ٱسۡتَـٔۡذَنَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمۡ ءَايَٰتِهِۦۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٞ ۝٥٩

60. ከሴቶችም እነዚያ ጋብቻን የማይፈልጉት ተቀማጮች (ባልቴቶች)፤ በጌጥ የተገለፁ ሳይኾኑ የላይ ልብሶቻቸውን ቢጥሉ በእነሱ ላይ ኀጢአት የለባቸውም፡፡ ግን መጠበቃቸው ለእነርሱ የተሻለ ነው፡፡ አላህም ሰሚ ዐዋቂ ነው፡፡

وَٱلۡقَوَٰعِدُ مِنَ ٱلنِّسَآءِ ٱلَّٰتِي لَا يَرۡجُونَ نِكَاحٗا فَلَيۡسَ عَلَيۡهِنَّ جُنَاحٌ أَن يَضَعۡنَ ثِيَابَهُنَّ غَيۡرَ مُتَبَرِّجَٰتِۭ بِزِينَةٖۖ وَأَن يَسۡتَعۡفِفۡنَ خَيۡرٞ لَّهُنَّۗ وَٱللَّهُ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ۝٦٠

61. (ከሰዎች ጋር በመብላት) በዕውር ላይ ኀጢአት የለበትም፡፡ በአንካሳም ላይ ኀጢአት የለበትም፡፡ በበሽተኛም ላይ ኀጢአት የለበትም፡፡ በነፍሶቻችሁም ላይ ከቤቶቻችሁ ወይም ከአባቶቻችሁ ቤቶች ወይም ከእናቶቻችሁ ቤቶች ወይም ከወንድሞቻችሁ ቤቶች ወይም ከእኅቶቻችሁ ቤቶች ወይም ከአጎቶቻችሁ ቤቶች ወይም ከአክስቶቻችሁ ቤቶች ወይም ከየሹሞቻችሁ ቤቶች ወይም ከየሹሜዎቻችሁ ቤቶች ወይም መክፈቻዎቹን ከያዛችሁት ቤት ወይም ከወዳጃችሁ ቤት (ብትበሉ) ኀጢአት የለባችሁም፡፡ ተሰብስባችሁ ወይም ተለያይታችሁ ብትበሉ በእናንተ ላይ ኀጢአት የለባችሁም፡፡ ቤቶችንም በገባችሁ ጊዜ፣ ከአላህ ዘንድ የኾነችን የተባረከች መልካም ሰላምታ በነፍሶቻችሁ ላይ ሰላም በሉ፡፡ እንደዚሁ አላህ አንቀጾችን ለእናንተ ያብራራል፡፡ ልታውቁ ይከጀላልና፡፡

لَّيۡسَ عَلَى ٱلۡأَعۡمَىٰ حَرَجٞ وَلَا عَلَى ٱلۡأَعۡرَجِ حَرَجٞ وَلَا عَلَى ٱلۡمَرِيضِ حَرَجٞ وَلَا عَلَىٰٓ أَنفُسِكُمۡ أَن تَأۡكُلُواْ مِنۢ بُيُوتِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ ءَابَآئِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ أُمَّهَٰتِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ إِخۡوَٰنِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ أَخَوَٰتِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ أَعۡمَٰمِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ عَمَّٰتِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ أَخۡوَٰلِكُمۡ أَوۡ بُيُوتِ خَٰلَٰتِكُمۡ أَوۡ مَا مَلَكۡتُم مَّفَاتِحَهُۥٓ أَوۡ صَدِيقِكُمۡۚ لَيۡسَ عَلَيۡكُمۡ جُنَاحٌ أَن تَأۡكُلُواْ جَمِيعًا أَوۡ أَشۡتَاتٗاۚ فَإِذَا دَخَلۡتُم بُيُوتٗا فَسَلِّمُواْ عَلَىٰٓ أَنفُسِكُمۡ تَحِيَّةٗ مِّنۡ عِندِ ٱللَّهِ مُبَٰرَكَةٗ طَيِّبَةٗۚ كَذَٰلِكَ يُبَيِّنُ ٱللَّهُ لَكُمُ ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّكُمۡ تَعۡقِلُونَ ﴿٦١﴾

62. ምእመናን ማለት እነዚያ በአላህና በመልክተኛው ያመኑት፣ ከእርሱ ጋር በሚሰበሰብ ጉዳይ ላይ በኾኑ ጊዜ እስከሚያስፈቅዱ ድረስ የማይኼዱት ብቻ ናቸው፡፡ እነዚያ የሚያስፈቅዱህ እነርሱ እነዚያ በአላህና በመልክተኛው የሚያምኑት ናቸው፡፡ ለግል ጉዳያቸውም ፈቃድ በጠየቁህ ጊዜ ከእነሱ ለሻኸው ሰው ፍቀድለት፡፡ ለእነሱም አላህን ምሕረትን ለምንላቸው አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَإِذَا كَانُواْ مَعَهُۥ عَلَىٰٓ أَمۡرٖ جَامِعٖ لَّمۡ يَذۡهَبُواْ حَتَّىٰ يَسۡتَـٔۡذِنُوهُۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَسۡتَـٔۡذِنُونَكَ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ يُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦۚ فَإِذَا ٱسۡتَـٔۡذَنُوكَ لِبَعۡضِ شَأۡنِهِمۡ فَأۡذَن لِّمَن شِئۡتَ مِنۡهُمۡ وَٱسۡتَغۡفِرۡ لَهُمُ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ﴿٦٢﴾

63. በመካከላችሁ የመልክተኛውን ጥሪ ከፊላችሁ ከፊሉን እንደ መጥራት አታድርጉት፡፡ ከእናንተ ውስጥ እነዚያን እየተከለሉ በመስለክለክ የሚወጡትን አላህ በእርግጥ ያውቃቸዋል፡፡ እነዚያም ትዕዛዙን የሚጥሱ መከራ እንዳትደርስባቸው ወይም አሳማሚ ቅጣት እንዳያገኛቸው ይጠንቀቁ፡፡

لَّا تَجۡعَلُواْ دُعَآءَ ٱلرَّسُولِ بَيۡنَكُمۡ كَدُعَآءِ بَعۡضِكُم بَعۡضٗاۚ قَدۡ يَعۡلَمُ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ يَتَسَلَّلُونَ مِنكُمۡ لِوَاذٗاۚ فَلۡيَحۡذَرِ ٱلَّذِينَ يُخَالِفُونَ عَنۡ أَمۡرِهِۦٓ أَن تُصِيبَهُمۡ فِتۡنَةٌ أَوۡ يُصِيبَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٌ ﴿٦٣﴾

64. ንቁ! በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ብቻ ነው፡፡ እናንተ በእርሱ ላይ ያላችሁበትን ኹኔታ በእርግጥ ያውቃል፡፡ ወደእርሱ የሚመለሱበትን ቀንም (ያውቃል)፡፡ የሠሩትንም ሁሉ ይነግራቸዋል፡፡ አላህም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَآ إِنَّ لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ قَدۡ يَعۡلَمُ مَآ أَنتُمۡ عَلَيۡهِ وَيَوۡمَ يُرۡجَعُونَ إِلَيۡهِ فَيُنَبِّئُهُم بِمَا عَمِلُواْۗ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمُۢ ﴿٦٤﴾

# ሱረቱ አልፉርቃን

# سورة الفرقان

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

1. ያ ፉርቃንን በባሪያው ላይ ለዓለማት አስፈራሪ ይኾን ዘንድ ያወረደው (አምላክ) ክብርና ጥራት ተገባው፡፡

2. (እርሱ) ያ የሰማያትና የምድር ንግሥና የእርሱ ብቻ የኾነ፣ ልጅንም ያልያዘ፣ በንግሥናውም ተጋሪ የሌለው፣ ነገሩንም ሁሉ የፈጠረና በትክክልም ያዘጋጀው ነው፡፡

3. (ከሓዲዎች) ከእርሱም ሌላ ምንንም የማይፈጥሩን፣ እነርሱም የሚፈጠሩን፣ ለነፍሶቻቸውም ጉዳትን ለመከላከል ጥቅምንም ለማምጣት የማይችሉን ሞትንና ሕይወትንም መቀስቀስንም የማይችሉን፣ አማልክት ያዙ፡፡

4. እነዚያም የካዱት ይህ (ቁርኣን ሙሐመድ) የቀጠፈው በእርሱም ላይ ሌሎች ሕዝቦች ያገዙት የኾነ ውሸት እንጂ ሌላ አይደለም አሉ፡፡ በእርግጥም በደልንና እብለትን ሠሩ፡፡

5. አሉም «የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ተረቶች ናት፡፡ አስጻፋት፡፡ እርሷም በእርሱ ላይ ጧትና ማታ ትነበብለታለች፡፡»

6. «ያ በሰማያትና በምድር ውስጥ ያለን ምስጢር የሚያውቀው አወረደው፡፡ እርሱ መሓሪ አዛኝ ነውና» በላቸው፡፡

7. ለዚህም መልክተኛ ምግብን የሚበላ፣ በገበያዎችም የሚኼድ ሲኾን ምን (መልክተኛነት) አለው ከርሱ ጋር አስፈራሪ ይኾን ዘንድ ወደርሱ መልአክ (ገሃድ) አይወረድም ኖሯልን አሉ፡፡

8. «ወይም ወደእርሱ ድልብ አይጣልለትምን ወይም ከእርሷ የሚበላላት አትክልት ለእርሱ አትኖረውምን» (አሉ)፡፡ በዳዮቹም (ላመኑት) «የተደገመበትን ሰው እንጂ ሌላ አትከተሉም» አሉ፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

تَبَارَكَ ٱلَّذِي نَزَّلَ ٱلۡفُرۡقَانَ عَلَىٰ عَبۡدِهِۦ لِيَكُونَ لِلۡعَٰلَمِينَ نَذِيرًا ١

ٱلَّذِي لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَلَمۡ يَتَّخِذۡ وَلَدٗا وَلَمۡ يَكُن لَّهُۥ شَرِيكٞ فِي ٱلۡمُلۡكِ وَخَلَقَ كُلَّ شَيۡءٖ فَقَدَّرَهُۥ تَقۡدِيرٗا ٢

وَٱتَّخَذُواْ مِن دُونِهِۦٓ ءَالِهَةٗ لَّا يَخۡلُقُونَ شَيۡـٔٗا وَهُمۡ يُخۡلَقُونَ وَلَا يَمۡلِكُونَ لِأَنفُسِهِمۡ ضَرّٗا وَلَا نَفۡعٗا وَلَا يَمۡلِكُونَ مَوۡتٗا وَلَا حَيَوٰةٗ وَلَا نُشُورٗا ٣

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّآ إِفۡكٌ ٱفۡتَرَىٰهُ وَأَعَانَهُۥ عَلَيۡهِ قَوۡمٌ ءَاخَرُونَۖ فَقَدۡ جَآءُو ظُلۡمٗا وَزُورٗا ٤

وَقَالُوٓاْ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٱكۡتَتَبَهَا فَهِيَ تُمۡلَىٰ عَلَيۡهِ بُكۡرَةٗ وَأَصِيلٗا ٥

قُلۡ أَنزَلَهُ ٱلَّذِي يَعۡلَمُ ٱلسِّرَّ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ إِنَّهُۥ كَانَ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ٦

وَقَالُواْ مَالِ هَٰذَا ٱلرَّسُولِ يَأۡكُلُ ٱلطَّعَامَ وَيَمۡشِي فِي ٱلۡأَسۡوَاقِ لَوۡلَآ أُنزِلَ إِلَيۡهِ مَلَكٞ فَيَكُونَ مَعَهُۥ نَذِيرًا ٧

أَوۡ يُلۡقَىٰٓ إِلَيۡهِ كَنزٌ أَوۡ تَكُونُ لَهُۥ جَنَّةٞ يَأۡكُلُ مِنۡهَاۚ وَقَالَ ٱلظَّٰلِمُونَ إِن تَتَّبِعُونَ إِلَّا رَجُلٗا مَّسۡحُورًا ٨

9. ላንተ ምሳሌዎችን እንዴት እንዳደረጉልህና እንደተሳሳቱ ተመልከት፡፡ (ወደ እውነት ለመድረስ) መንገድንም አይችሉም፡፡

ٱنظُرۡ كَيۡفَ ضَرَبُواْ لَكَ ٱلۡأَمۡثَٰلَ فَضَلُّواْ فَلَا يَسۡتَطِيعُونَ سَبِيلٗا ٩

10. ያ ቢሻ ከዚህ (ካሉት) የተሻለን ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን አትክልቶች ላንተ የሚያደርግልህ ሕንጻ ቤቶችንም ላንተ የሚያደርግልህ ጌታ ችሮታው በዛ፡፡

تَبَارَكَ ٱلَّذِيٓ إِن شَآءَ جَعَلَ لَكَ خَيۡرٗا مِّن ذَٰلِكَ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ وَيَجۡعَل لَّكَ قُصُورَۢا ١٠

11. ይልቁንም በትንሣኤ አስተባበሉ፡፡ በትንሣኤ ላስተባበለም ሰው ሁሉ ነዳጅን እሳት አዘጋጅተናል፡፡

بَلۡ كَذَّبُواْ بِٱلسَّاعَةِۖ وَأَعۡتَدۡنَا لِمَن كَذَّبَ بِٱلسَّاعَةِ سَعِيرًا ١١

12. ከሩቅ ስፍራ ባየቻቸው ጊዜ ለእርሷ የቁጭት መገንፈልንና ማናፋትን ይሰማሉ፡፡

إِذَا رَأَتۡهُم مِّن مَّكَانِۭ بَعِيدٖ سَمِعُواْ لَهَا تَغَيُّظٗا وَزَفِيرٗا ١٢

13. እጅ ከፍንጅ የታሠሩ ኾነውም ከእርሷ በጠባብ ስፍራ በተጣሉ ጊዜ በዚያ ስፍራ ጥፋትን ይጠራሉ፤ (ዋ ጥፋታችን ይላሉ)፡፡

وَإِذَآ أُلۡقُواْ مِنۡهَا مَكَانٗا ضَيِّقٗا مُّقَرَّنِينَ دَعَوۡاْ هُنَالِكَ ثُبُورٗا ١٣

14. ፡-ዛሬ አንድን ጥፋት ብቻ አትጥሩ ብዙንም ጥፋት ጥሩ (ይባላሉ)፡፡

لَّا تَدۡعُواْ ٱلۡيَوۡمَ ثُبُورٗا وَٰحِدٗا وَٱدۡعُواْ ثُبُورٗا كَثِيرٗا ١٤

15. (እንዲህ) በላቸው «ይህ የተሻለ ነውን ወይስ ጥንቁቆቹ ተስፋ የተሰጧት የዘለዓለሚ ገነት» ለእነርሱ ምንዳና መመለሻ ኾነች፡፡

قُلۡ أَذَٰلِكَ خَيۡرٌ أَمۡ جَنَّةُ ٱلۡخُلۡدِ ٱلَّتِي وُعِدَ ٱلۡمُتَّقُونَۚ كَانَتۡ لَهُمۡ جَزَآءٗ وَمَصِيرٗا ١٥

16. ለእነሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ኾነው የሚፈልጉት ሁሉ አልላቸው፡፡ (ይህም) ተስፋ ከጌታህ ተለማኝ ተስፋ ነው፡፡

لَّهُمۡ فِيهَا مَا يَشَآءُونَ خَٰلِدِينَۚ كَانَ عَلَىٰ رَبِّكَ وَعۡدٗا مَّسۡـُٔولٗا ١٦

17. እነርሱንና ከአላህ ሌላ የሚግገዟቸውንም የሚሰበስብባቸውንና «እናንተ እነዚህን ባሮቼን አሳሳታችሁን ወይስ እነሱው መንገድን ሳቱ» የሚልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ يَحۡشُرُهُمۡ وَمَا يَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ فَيَقُولُ ءَأَنتُمۡ أَضۡلَلۡتُمۡ عِبَادِي هَٰٓؤُلَآءِ أَمۡ هُمۡ ضَلُّواْ ٱلسَّبِيلَ ١٧

18. «ጥራት ይገባህ፤ ካንተ ሌላ ረዳቶችን ልንይዝ ለእኛ ተገቢያችን አልነበረም፡፡ ግን እነርሱንም አባቶቻቸውንም መገንዘብን እስከተዉ ድረስ አጣቀምካቸው፡፡ ጠፊ ሕዝቦችም ኾኑ» ይላሉ፡፡

قَالُواْ سُبۡحَٰنَكَ مَا كَانَ يَنۢبَغِي لَنَآ أَن نَّتَّخِذَ مِن دُونِكَ مِنۡ أَوۡلِيَآءَ وَلَٰكِن مَّتَّعۡتَهُمۡ وَءَابَآءَهُمۡ حَتَّىٰ نَسُواْ ٱلذِّكۡرَ وَكَانُواْ قَوۡمَۢا بُورٗا ١٨

19. በምትሉትም (አማልክቶቻችሁ) አስዋሹዋችሁ፡፡ ቅጣቴን መገፍተርንም መርዳትንም አትችሉም፡፡ ከእናንተም የሚበድለውን ታላቅን ቅጣት እናቀምሰዋለን፤ (ይባላሉ)፡፡

فَقَدۡ كَذَّبُوكُم بِمَا تَقُولُونَ فَمَا تَسۡتَطِيعُونَ صَرۡفٗا وَلَا نَصۡرٗاۚ وَمَن يَظۡلِم مِّنكُمۡ نُذِقۡهُ عَذَابٗا كَبِيرٗا ١٩

20. ከአንተ በፊትም ከመልክተኞች እነሱ በእርግጥ ምግብን የሚበሉ በገበያዎችም የሚኼዱ ኾነው በስተቀር አልላክንም፡፡ ከፊላችሁንም ለከፊሉ ፈተና አድርገናል፡፡ ትታገሳላችሁን ጌታህም ተመልካች ነው፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا قَبۡلَكَ مِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ إِلَّآ إِنَّهُمۡ لَيَأۡكُلُونَ ٱلطَّعَامَ وَيَمۡشُونَ فِي ٱلۡأَسۡوَاقِۗ وَجَعَلۡنَا بَعۡضَكُمۡ لِبَعۡضٖ فِتۡنَةً أَتَصۡبِرُونَۗ وَكَانَ رَبُّكَ بَصِيرٗا ﴿٢٠﴾

21. እነዚያም መገናኘታችንን የማይፈሩት በእኛ ላይ ለምን መላእክት አልወረደም፡፡ ወይም ጌታችንን ለምን አናይም አሉ፡ በነፍሶቻቸው ውስጥ በእርግጥ ኮሩ፡፡ ታላቅንም አመጽ አመፁ፡፡

۞وَقَالَ ٱلَّذِينَ لَا يَرۡجُونَ لِقَآءَنَا لَوۡلَآ أُنزِلَ عَلَيۡنَا ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ أَوۡ نَرَىٰ رَبَّنَاۗ لَقَدِ ٱسۡتَكۡبَرُواْ فِيٓ أَنفُسِهِمۡ وَعَتَوۡ عُتُوّٗا كَبِيرٗا ﴿٢١﴾

22. መላእክትን በሚያዩበት ቀን በዚያ ጊዜ ለአመጸኞች ምስራች የላቸውም፡፡ «የተከለከለ ክልክልም አድርገን» ይላሉ፡፡

يَوۡمَ يَرَوۡنَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ لَا بُشۡرَىٰ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُجۡرِمِينَ وَيَقُولُونَ حِجۡرٗا مَّحۡجُورٗا ﴿٢٢﴾

23. ከሥራም ወደ ሠሩት እናስባለን፡፡ የተበተነ ትቢያም እናደርገዋለን፡፡

وَقَدِمۡنَآ إِلَىٰ مَا عَمِلُواْ مِنۡ عَمَلٖ فَجَعَلۡنَٰهُ هَبَآءٗ مَّنثُورًا ﴿٢٣﴾

24. የገነት ሰዎች በዚያ ቀን በመርጊያ የተሻሉ በማረፊያም በጣም ያማሩ ናቸው፡፡

أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِ يَوۡمَئِذٍ خَيۡرٞ مُّسۡتَقَرّٗا وَأَحۡسَنُ مَقِيلٗا ﴿٢٤﴾

25. ሰማይም በደመና የምትቀደድበትንና መላእክትም መወረድን የሚወርድበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ تَشَقَّقُ ٱلسَّمَآءُ بِٱلۡغَمَٰمِ وَنُزِّلَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ تَنزِيلًا ﴿٢٥﴾

26. እውነተኛው ንግሥና በዚያ ቀን ለአልራሕማን ብቻ ነው፡፡ በከሓዲዎችም ላይ አስቸጋሪ ቀን ነው፡፡

ٱلۡمُلۡكُ يَوۡمَئِذٍ ٱلۡحَقُّ لِلرَّحۡمَٰنِۚ وَكَانَ يَوۡمًا عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ عَسِيرٗا ﴿٢٦﴾

27. በዳይም «ከመልክተኛው ጋር ቀጥተኛን መንገድ ይገቼ በኾነ ዋ ምኞቴ!» እያለ (በጸጸት) ሁለት እጆቹን የሚነክስበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ يَعَضُّ ٱلظَّالِمُ عَلَىٰ يَدَيۡهِ يَقُولُ يَٰلَيۡتَنِي ٱتَّخَذۡتُ مَعَ ٱلرَّسُولِ سَبِيلٗا ﴿٢٧﴾

28. «ዋ ጥፋቴ! እገሌን ወዳጅ ባልያዝኩ ኖሮ እመኛለሁ፡፡

يَٰوَيۡلَتَىٰ لَيۡتَنِي لَمۡ أَتَّخِذۡ فُلَانًا خَلِيلٗا ﴿٢٨﴾

29. (የእምነት ቃልን) ከመጣልኝ በኋላ ከማስታወስ በእርግጥ አሳሳተኝ» (ይላል)፡፡ ሰይጣንም ለሰው አጋላጭ ነው፡፡

لَّقَدۡ أَضَلَّنِي عَنِ ٱلذِّكۡرِ بَعۡدَ إِذۡ جَآءَنِيۗ وَكَانَ ٱلشَّيۡطَٰنُ لِلۡإِنسَٰنِ خَذُولٗا ﴿٢٩﴾

30. መልክተኛውም «ጌታዬ ሆይ! ሕዝቦቼ ይህንን ቁርአን የተተወ ነገር አድርገው ያዙት» አለ፡፡

وَقَالَ ٱلرَّسُولُ يَٰرَبِّ إِنَّ قَوۡمِي ٱتَّخَذُواْ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانَ مَهۡجُورٗا ﴿٣٠﴾

31. እንደዚሁም ለነቢዩ ሁሉ ከአመጸኞች የኾነ ጠላትን አድርገናል፡፡ መሪና ረዳትም በጌታህ በቃ፡፡

وَكَذَٰلِكَ جَعَلۡنَا لِكُلِّ نَبِيٍّ عَدُوّٗا مِّنَ ٱلۡمُجۡرِمِينَۗ وَكَفَىٰ بِرَبِّكَ هَادِيٗا وَنَصِيرٗا ﴿٣١﴾

32. እነዚያ የካዱትም «ቁርአን በእርሱ ላይ ለምን በጠቅላላ አንድ ጊዜ አልተወረደም» አሉ፡፡ እንደዚሁ በእርሱ ልብህን ልናረጋ (ከፋፍለን አወረድነው)፡፡ ቀስ በቀስ መለያየትንም ለየነው፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوۡلَا نُزِّلَ عَلَيۡهِ ٱلۡقُرۡءَانُ جُمۡلَةٗ وَٰحِدَةٗۚ كَذَٰلِكَ لِنُثَبِّتَ بِهِۦ فُؤَادَكَۖ وَرَتَّلۡنَٰهُ تَرۡتِيلٗا ﴿٣٢﴾

33. በጥያቄም አይመጡብህም እውነተኛውን (መልስ) መልካምን ፍችም የምናመጣልህ ብንኾን እንጅ::

وَلَا يَأۡتُونَكَ بِمَثَلٍ إِلَّا جِئۡنَٰكَ بِٱلۡحَقِّ وَأَحۡسَنَ تَفۡسِيرًا ٣٣

34. እነዚያ በፊቶቻቸው ላይ (እየተጎተቱ) ወደ ገሀነም የሚሰበሰቡ ናቸው:: እነዚያ ስፍራቸው የከፋ መንገዳቸውም የጠመመ ናቸው::

ٱلَّذِينَ يُحۡشَرُونَ عَلَىٰ وُجُوهِهِمۡ إِلَىٰ جَهَنَّمَ أُوْلَٰٓئِكَ شَرّٞ مَّكَانٗا وَأَضَلُّ سَبِيلٗا ٣٤

35. በእርግጥም ለሙሳ መጽሐፍን ሰጠነው:: ከእርሱም ጋር ወንድሙን ሃሩንን ረዳት አደረግንለት::

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡكِتَٰبَ وَجَعَلۡنَا مَعَهُۥٓ أَخَاهُ هَٰرُونَ وَزِيرٗا ٣٥

36. «ወደእነዚያም በተዓምራቶቻችን ወደ አስተባበሉት ሕዝቦች ኺዱ» አልናቸው:: (አስዋሿቸውም) ማጥፋትንም አጠፋናቸው::

فَقُلۡنَا ٱذۡهَبَآ إِلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا فَدَمَّرۡنَٰهُمۡ تَدۡمِيرٗا ٣٦

37. የኑሕን ሰዎችም መልክተኞችን ባስተባበሉ ጊዜ አሰጠምናቸው:: ለሰዎችም መገሰጫ አደረግናለቸው:: ለበደለኞችም አሳማሚን ቅጣት አዘጋጅተናል::

وَقَوۡمَ نُوحٖ لَّمَّا كَذَّبُواْ ٱلرُّسُلَ أَغۡرَقۡنَٰهُمۡ وَجَعَلۡنَٰهُمۡ لِلنَّاسِ ءَايَةٗۖ وَأَعۡتَدۡنَا لِلظَّٰلِمِينَ عَذَابًا أَلِيمٗا ٣٧

38. ዓድንም ሰሙድንም የረስን ሰዎችም በዚህ መካከል የነበሩትንም ብዙን የክፍለ ዘመናት ሕዝቦች (አጠፋን)::

وَعَادٗا وَثَمُودَاْ وَأَصۡحَٰبَ ٱلرَّسِّ وَقُرُونَۢا بَيۡنَ ذَٰلِكَ كَثِيرٗا ٣٨

39. ሁሉንም (ገሠጽን) ለእነሱ ምሳሌዎችን ገለጽን:: ሁሉንም ማጥፋትን አጠፋናቸውም::

وَكُلّٗا ضَرَبۡنَا لَهُ ٱلۡأَمۡثَٰلَۖ وَكُلّٗا تَبَّرۡنَا تَتۡبِيرٗا ٣٩

40. በዚያችም ክፉ ዝናምን በተዘነመችው ከተማ ላይ (የመካ ከሐዲዎች) በእርግጥ መጥተዋል:: የሚያዩዋት አልነበሩምን በእውነቱ መቀስቀስን የማይፈሩ ነበሩ::

وَلَقَدۡ أَتَوۡاْ عَلَى ٱلۡقَرۡيَةِ ٱلَّتِيٓ أُمۡطِرَتۡ مَطَرَ ٱلسَّوۡءِۚ أَفَلَمۡ يَكُونُواْ يَرَوۡنَهَاۚ بَلۡ كَانُواْ لَا يَرۡجُونَ نُشُورٗا ٤٠

41. ባዩህም ጊዜ ያ አላህ መልእክተኛ አድርጎ የላከው ይህ ነውን እያሉ መሳለቂያ እንጂ ሌላ አያደርጉህም::

وَإِذَا رَأَوۡكَ إِن يَتَّخِذُونَكَ إِلَّا هُزُوًا أَهَٰذَا ٱلَّذِي بَعَثَ ٱللَّهُ رَسُولًا ٤١

42. «እነሆ በእርሷ ላይ መታገሳችን ባልነበረ ኖሮ ከአማልክቶቻችን ሊያሳስተን ቀርቦ ነበር» (ሲሉም ይሳለቃሉ):: ወደፊትም ቅጣቱን በሚያዩ ጊዜ መንገድን በጣም ተሰሳቹ ማን እንደኾነ በእርግጥ ያውቃሉ::

إِن كَادَ لَيُضِلُّنَا عَنۡ ءَالِهَتِنَا لَوۡلَآ أَن صَبَرۡنَا عَلَيۡهَاۚ وَسَوۡفَ يَعۡلَمُونَ حِينَ يَرَوۡنَ ٱلۡعَذَابَ مَنۡ أَضَلُّ سَبِيلًا ٤٢

43. ፍላጎቱን አምላኩ አድርጎ የያዘውን ሰው አየህን አንተ በእርሱ ላይ ጠባቂ ትኾናለህን

أَرَءَيۡتَ مَنِ ٱتَّخَذَ إِلَٰهَهُۥ هَوَىٰهُ أَفَأَنتَ تَكُونُ عَلَيۡهِ وَكِيلًا ٤٣

44. ይልቁንም አብዛኛዎቻቸው የሚሰሙ ወይም የሚያውቁ መኾናቸውን ታስባለህን እነርሱ እንደ እንስሳዎች እንጂ ሌላ አይደሉም:: ከቶውንም እነሱ ይልቅ መንገድን የተሳሳቱ ናቸው::

أَمۡ تَحۡسَبُ أَنَّ أَكۡثَرَهُمۡ يَسۡمَعُونَ أَوۡ يَعۡقِلُونَۚ إِنۡ هُمۡ إِلَّا كَٱلۡأَنۡعَٰمِ بَلۡ هُمۡ أَضَلُّ سَبِيلًا ٤٤

45. ወደ ጌታህ (ሥራ) ጥላን እንዴት እንደ ዘረጋ አላየህምን በሻም ኖሮ የረጋ ባደረገው ነበር:: ከዚያም ፀሐይን በእርሱ ላይ ምልክት አደረግን::

أَلَمۡ تَرَ إِلَىٰ رَبِّكَ كَيۡفَ مَدَّ ٱلظِّلَّ وَلَوۡ شَآءَ لَجَعَلَهُۥ سَاكِنٗا ثُمَّ جَعَلۡنَا ٱلشَّمۡسَ عَلَيۡهِ دَلِيلٗا ٤٥

46. ከዚያም ቀስ በቀስ ወደእኛ ሰብስብነው::

ثُمَّ قَبَضۡنَٰهُ إِلَيۡنَا قَبۡضٗا يَسِيرٗا ٤٦

47. እርሱም ያ ለእናንተ ሌሊትን ልብስ እንቅልፍንም ማረፊያ ያደረገ፤ ቀንንም መበተኛ ያደረገላችሁ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِى جَعَلَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ لِبَاسٗا وَٱلنَّوۡمَ سُبَاتٗا وَجَعَلَ ٱلنَّهَارَ نُشُورٗا ﴿٤٧﴾

48. እርሱም ያ ነፋሶችን አብሳሪዎች ሲኾኑ ከዝናሙ በስተፊት የላከ ነው፡፡ ከሰማይም አጥሪ ውሃን አወረድን፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِىٓ أَرۡسَلَ ٱلرِّيَٰحَ بُشۡرَۢا بَيۡنَ يَدَىۡ رَحۡمَتِهِۦۚ وَأَنزَلۡنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ طَهُورٗا ﴿٤٨﴾

49. በእርሱ የሞተችን አገር ሕያው ልናደርግበት ከፈጠርነውም ፍጡር እንስሳዎችንና ብዙ ሰዎችንም ልናጠጣው (አወረድነው)፡፡

لِّنُحۡـِۧىَ بِهِۦ بَلۡدَةٗ مَّيۡتٗا وَنُسۡقِيَهُۥ مِمَّا خَلَقۡنَآ أَنۡعَٰمٗا وَأَنَاسِىَّ كَثِيرٗا ﴿٤٩﴾

50. (ጸጋችንን) ይገነዘቡም ዘንድ በመካከላቸው ከፋፈልነው፡፡ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች ክህደትን እንጂ እንቢ አሉ፡፡

وَلَقَدۡ صَرَّفۡنَٰهُ بَيۡنَهُمۡ لِيَذَّكَّرُواْ فَأَبَىٰٓ أَكۡثَرُ ٱلنَّاسِ إِلَّا كُفُورٗا ﴿٥٠﴾

51. በሻንም ኖሮ በየከተማይቱ አስፈራሪን በላክን ነበር፡፡

وَلَوۡ شِئۡنَا لَبَعَثۡنَا فِى كُلِّ قَرۡيَةٖ نَّذِيرٗا ﴿٥١﴾

52. ከሓዲዎችንም አትታዘዛቸው፡፡ በእርሱም (በቁርአን) ታላቅን ትግል ታገላቸው፡፡

فَلَا تُطِعِ ٱلۡكَٰفِرِينَ وَجَٰهِدۡهُم بِهِۦ جِهَادٗا كَبِيرٗا ﴿٥٢﴾

53. እርሱም ያ ሁለቱን ባሕሮች አጎራብቶ የለቀቀ ነው፡፡ ይህ ጥምን የሚቆርጥ ጣፋጭ ነው፡፡ ይህም የሚመረግግ ጨው ነው፡፡ በመካከላቸውም (ከመቀላቀል) መለያንና የተከለለን ክልል ያደረገ ነው፡፡

۞وَهُوَ ٱلَّذِى مَرَجَ ٱلۡبَحۡرَيۡنِ هَٰذَا عَذۡبٞ فُرَاتٞ وَهَٰذَا مِلۡحٌ أُجَاجٞ وَجَعَلَ بَيۡنَهُمَا بَرۡزَخٗا وَحِجۡرٗا مَّحۡجُورٗا ﴿٥٣﴾

54. እርሱም ያ ከውሃ ሰውን የፈጠረ፣ የዝምድናና የአማችም ባለቤት ያደረገው ነው፡፡ ጌታህም ቻይ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِى خَلَقَ مِنَ ٱلۡمَآءِ بَشَرٗا فَجَعَلَهُۥ نَسَبٗا وَصِهۡرٗاۗ وَكَانَ رَبُّكَ قَدِيرٗا ﴿٥٤﴾

55. ከአላህም ሌላ የማይጠቅማቸውንና የማይጎዳቸውን ይግገዛሉ፤ ከሓዲም በጌታው ላይ (በማመጽ ለሰይጣን) ረዳት ነው፡፡

وَيَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَا لَا يَنفَعُهُمۡ وَلَا يَضُرُّهُمۡۗ وَكَانَ ٱلۡكَافِرُ عَلَىٰ رَبِّهِۦ ظَهِيرٗا ﴿٥٥﴾

56. አብሳሪና አስፈራሪም አድርገን እንጂ አልላክንህም፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَٰكَ إِلَّا مُبَشِّرٗا وَنَذِيرٗا ﴿٥٦﴾

57. «በእርሱ ላይ ዋጋን በፍጹም አልጠይቃችሁም፡፡ ግን ወደ ጌታው (መልካም) መንገድን ለመያዝ የሻ ሰው (ይሥራ)» በላቸው፡፡

قُلۡ مَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍ إِلَّا مَن شَآءَ أَن يَتَّخِذَ إِلَىٰ رَبِّهِۦ سَبِيلٗا ﴿٥٧﴾

58. በዚያም በማይሞተው ሕያው አምላክ ላይ ተመካ፡፡ ከማመስገንም ጋር አጥራው፡፡ በባሮቹ ኀጢአቶችም ውስጠ ዐዋቂ በእርሱ በቃ፡፡

وَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱلۡحَىِّ ٱلَّذِى لَا يَمُوتُ وَسَبِّحۡ بِحَمۡدِهِۦۚ وَكَفَىٰ بِهِۦ بِذُنُوبِ عِبَادِهِۦ خَبِيرًا ﴿٥٨﴾

59. ያ ሰማያትና ምድርን በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ በስድስት ቀኖች ውስጥ የፈጠረ፣ ከዚያም በዐርሹ ላይ (ሥልጣኑ) የተደላደለ አልረሕማን ነው፡፡ ከእርሱም ዐዋቂን ጠይቅ፡፡

ٱلَّذِى خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَا فِى سِتَّةِ أَيَّامٖ ثُمَّ ٱسۡتَوَىٰ عَلَى ٱلۡعَرۡشِۖ ٱلرَّحۡمَٰنُ فَسۡـَٔلۡ بِهِۦ خَبِيرٗا ﴿٥٩﴾

60. ለእነርሱም ለአልረሕማን ስገዱ በተባሉ ጊዜ አልረሕማን ማነው ለምታዘዝን (እና ለማናውቀው) እንሰግዳለን ይላሉ፡፡ (ይህ) መራቅንም ጨመራቸው፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمُ ٱسۡجُدُواْ لِلرَّحۡمَٰنِ قَالُواْ وَمَا ٱلرَّحۡمَٰنُ أَنَسۡجُدُ لِمَا تَأۡمُرُنَا وَزَادَهُمۡ نُفُورٗا۩ ﴿٦٠﴾

61. ያ በሰማይ ቡሩጆችን ያደረገና በእርሷም አንጸባራቂን (ፀሐይ) አብሪ ጨረቃንም ያደረገ ጌታ ክብሩ በጣም ላቀ፡፡

تَبَارَكَ ٱلَّذِى جَعَلَ فِى ٱلسَّمَآءِ بُرُوجًا وَجَعَلَ فِيهَا سِرَٰجًا وَقَمَرًا مُّنِيرًا ﴿٦١﴾

62. እርሱም ያ (ያመለጠውን ሥራ) ማስታወስን ለሚፈልግ ወይም ማመስገንን ለሚፈልግ ሰው ሌሊትንና ቀንን ተተካኪ ያደረገ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِى جَعَلَ ٱلَّيْلَ وَٱلنَّهَارَ خِلْفَةً لِّمَنْ أَرَادَ أَن يَذَّكَّرَ أَوْ أَرَادَ شُكُورًا ﴿٦٢﴾

63. የአልረሕማንም ባሮች እነዚያ በምድር ላይ በዝግታ የሚኼዱት፣ ባለጌዎችም (በክፉ) ባነጋገሩዋቸው ጊዜ ሰላም የሚሉት ናቸው፡፡

وَعِبَادُ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلَّذِينَ يَمْشُونَ عَلَى ٱلْأَرْضِ هَوْنًا وَإِذَا خَاطَبَهُمُ ٱلْجَٰهِلُونَ قَالُوا۟ سَلَٰمًا ﴿٦٣﴾

64. እነዚያም ለጌታቸው በግንባራቸው ተደፊዎችና ቋሚዎች ኾነው የሚያድሩት ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَبِيتُونَ لِرَبِّهِمْ سُجَّدًا وَقِيَٰمًا ﴿٦٤﴾

65. እነዚያም «ጌታችን ሆይ! የገሀነምን ቅጣት ከእኛ ላይ መልስልን ቅጣቷ የማይለቅ ነውና» የሚሉት ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَقُولُونَ رَبَّنَا ٱصْرِفْ عَنَّا عَذَابَ جَهَنَّمَ ۖ إِنَّ عَذَابَهَا كَانَ غَرَامًا ﴿٦٥﴾

66. እርሷ መርጊያና መቀመጫ በመኾን ከፋች! (ይላሉ)፡፡

إِنَّهَا سَآءَتْ مُسْتَقَرًّا وَمُقَامًا ﴿٦٦﴾

67. እነዚያም በለገሱ ጊዜ የማያባክኑ የማይቆጥቡትም ናቸው፡፡ በዚህም መካከል (ልግስናቸው) ትክክለኛ የኾነ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ إِذَآ أَنفَقُوا۟ لَمْ يُسْرِفُوا۟ وَلَمْ يَقْتُرُوا۟ وَكَانَ بَيْنَ ذَٰلِكَ قَوَامًا ﴿٦٧﴾

68. እነዚያም ከአላህ ጋር ሌላን አምላክ የማይገዙት፣ ያችንም አላህ እርም ያደረጋትን ነፍስ ያለ ሕግ የማይገድሉት፣ የማያመነዝሩትም ናቸው፡፡ ይህንንም የሚሠራ ሰው ቅጣትን ያገኛል፡፡

وَٱلَّذِينَ لَا يَدْعُونَ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ وَلَا يَقْتُلُونَ ٱلنَّفْسَ ٱلَّتِى حَرَّمَ ٱللَّهُ إِلَّا بِٱلْحَقِّ وَلَا يَزْنُونَ ۚ وَمَن يَفْعَلْ ذَٰلِكَ يَلْقَ أَثَامًا ﴿٦٨﴾

69. በትንሣኤ ቀን ቅጣቱ ለእርሱ ይደራረብበል፡፡ በእርሱም ውስጥ የተዋረደ ኾኖ ይኖራል፡፡

يُضَٰعَفْ لَهُ ٱلْعَذَابُ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ وَيَخْلُدْ فِيهِۦ مُهَانًا ﴿٦٩﴾

70. ተጸጽቶ የተመለሰና ያመነ መልካምንም ሥራ የሠራ ሰው ብቻ ሲቀር፡፡ እነዚያም አላህ መጥፎ ሥራዎቻቸውን በመልካም ሥራዎች ይለውጣል፡፡ አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

إِلَّا مَن تَابَ وَءَامَنَ وَعَمِلَ عَمَلًا صَٰلِحًا فَأُو۟لَٰٓئِكَ يُبَدِّلُ ٱللَّهُ سَيِّـَٔاتِهِمْ حَسَنَٰتٍ ۗ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورًا رَّحِيمًا ﴿٧٠﴾

71. ተጸጽቶ የተመለሰም ሰው መልካምንም የሠራ እርሱ የተወደደን መመለስ ወደ አላህ ይመለሳል፡፡

وَمَن تَابَ وَعَمِلَ صَٰلِحًا فَإِنَّهُۥ يَتُوبُ إِلَى ٱللَّهِ مَتَابًا ﴿٧١﴾

72. እነዚያም እብለትን የማይመሰክሩ፤ በውድቅ ቃልም (ተናጋሪ አጠገብ) ባለፉ ጊዜ የከበሩ ኾነው የሚያልፉት ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ لَا يَشْهَدُونَ ٱلزُّورَ وَإِذَا مَرُّوا۟ بِٱللَّغْوِ مَرُّوا۟ كِرَامًا ﴿٧٢﴾

73. እነዚያም በጌታቸው አንቀጾች በተገሰጹ ጊዜ (የተረዱ ተቀባዮች ኾነው እንጂ) ደንቆሮዎችና ዕውሮች ኾነው በእርሷ ላይ የማይደፉት ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِّرُوا۟ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمْ لَمْ يَخِرُّوا۟ عَلَيْهَا صُمًّا وَعُمْيَانًا ﴿٧٣﴾

74. እነዚያም «ጌታችን ሆይ! ከሚስቶቻችንና ከዘሮቻችን ለዓይኖች መርጊያን ለእኛ ስጠን፡፡ አላህን ለሚፈሩትም መሪ አድርገን» የሚሉት ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَقُولُونَ رَبَّنَا هَبْ لَنَا مِنْ أَزْوَٰجِنَا وَذُرِّيَّٰتِنَا قُرَّةَ أَعْيُنٍ وَٱجْعَلْنَا لِلْمُتَّقِينَ إِمَامًا ﴿٧٤﴾

75. እነዚያ በመታገሳቸው የገነትን ሰገነቶች ይምመነዳሉ፡፡ በእርሷም ውስጥ ውዳሴንና ሰላምታን ይሰሰጣሉ፡፡

أُوْلَـٰٓئِكَ يُجْزَوْنَ ٱلْغُرْفَةَ بِمَا صَبَرُواْ وَيُلَقَّوْنَ فِيهَا تَحِيَّةً وَسَلَـٰمًا ٧٥

76. በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ኾነው (ይሰሰጣሉ)፡፡ መርጊያና መኖሪያይቱ አማረች፡፡

خَـٰلِدِينَ فِيهَا ۚ حَسُنَتْ مُسْتَقَرًّا وَمُقَامًا ٧٦

77. «ጸሎታችሁ ባልነበረ ኖሮ ጌታዬ እናንተን ከምንም አይቆጥራችሁም ነበር፡፡ በእርግጥም አስተባበላችሁ፤ ወደ ፊትም (ቅጣቱ) ያዣችሁ ይኾናል» በላቸው፡፡

قُلْ مَا يَعْبَؤُاْ بِكُمْ رَبِّى لَوْلَا دُعَآؤُكُمْ ۖ فَقَدْ كَذَّبْتُمْ فَسَوْفَ يَكُونُ لِزَامًۢا ٧٧

# ሱረቱ አል አሹዐራዕ

# سورة الشعراء

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَـٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ጠ.ሰ.መ. (ጧ ሲን ሚም)፡፡

طسٓمٓ ١

2. ይህች ግልጽ ከኾነው መጽሐፍ አንቀጾች ናት፡፡

تِلْكَ ءَايَـٰتُ ٱلْكِتَـٰبِ ٱلْمُبِينِ ٢

3. አማኞች ባለመኾናቸው፤ (በቁጭት) ነፍስህን ገዳይ መኾን ይፈራልሃል፡፡

لَعَلَّكَ بَـٰخِعٌ نَّفْسَكَ أَلَّا يَكُونُواْ مُؤْمِنِينَ ٣

4. ብንሻ በእነሱ ላይ ከሰማይ ተዓምረን እናወርድና አንገቶቻቸው (መሪዎቻቸው) ለእርሷ ተዋራጆች ይኾናሉ፡፡

إِن نَّشَأْ نُنَزِّلْ عَلَيْهِم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ ءَايَةً فَظَلَّتْ أَعْنَـٰقُهُمْ لَهَا خَـٰضِعِينَ ٤

5. ከአልረሕማንም ዘንድ አዲስ የተወረደ ቁርኣን አይመጣላቸውም፤ ከእርሱ የሚሸሹ ቢኾኑ እንጂ፡፡

وَمَا يَأْتِيهِم مِّن ذِكْرٍ مِّنَ ٱلرَّحْمَـٰنِ مُحْدَثٍ إِلَّا كَانُواْ عَنْهُ مُعْرِضِينَ ٥

6. በእርግጥም አስተባበሉ፡፡ የዚያም በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩት ወሬዎች (ፍጻሜ) ይመጣባቸዋል፡፡

فَقَدْ كَذَّبُواْ فَسَيَأْتِيهِمْ أَنۢبَـٰٓؤُاْ مَا كَانُواْ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ٦

7. ወደ ምድርም በውስጧ ከመልካም (በቃይ) ጎሳ ሁሉ ብዙን እንዳበቀልን አላዩምን፡፡

أَوَلَمْ يَرَوْاْ إِلَى ٱلْأَرْضِ كَمْ أَنۢبَتْنَا فِيهَا مِن كُلِّ زَوْجٍ كَرِيمٍ ٧

8. በዚህ አስደናቂ ምልክት አልለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም አማኞች አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَـَٔايَةً ۖ وَمَا كَانَ أَكْثَرُهُم مُّؤْمِنِينَ ٨

9. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊ አዛኝ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٩﴾

10. ጌታህም ሙሳን «ወደ በደለኞቹ ሕዝቦች ኺድ» በማለት በጠራው ጊዜ (አስታውስ)፡፡

وَإِذْ نَادَىٰ رَبُّكَ مُوسَىٰٓ أَنِ ٱئْتِ ٱلْقَوْمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٠﴾

11. «ወደ ፈርዖን ሕዝቦች (ኺድ) አላህን አይፈሩምን» (አለው)፡፡

قَوْمَ فِرْعَوْنَ ۚ أَلَا يَتَّقُونَ ﴿١١﴾

12. (ሙሳም) አለ «ጌታዬ ሆይ! እኔ ሊያስተባብሉኝ እፈራለሁ፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّىٓ أَخَافُ أَن يُكَذِّبُونِ ﴿١٢﴾

13. «ልቤም ይጠብባል፡፡ ምላሴም አይፈታም፡፡ ስለዚህ ወደ ሃሩን ላክ፡፡

وَيَضِيقُ صَدْرِى وَلَا يَنطَلِقُ لِسَانِى فَأَرْسِلْ إِلَىٰ هَٰرُونَ ﴿١٣﴾

14. «ለእነርሱም በእኔ ላይ (የደም) ወንጀል አልለ፡፡ ስለዚህ እንዳይገድሉኝ እፈራለሁ፡፡»

وَلَهُمْ عَلَىَّ ذَنۢبٌ فَأَخَافُ أَن يَقْتُلُونِ ﴿١٤﴾

15. (አላህ) አለ «ተው! (አይነኩህም)፡፡ በተዓምራቶቻችንም ኺዱ፡፡ እኛ ከእናንተ ጋር ሰሚዎች ነንና፡፡

قَالَ كَلَّا ۖ فَٱذْهَبَا بِـَٔايَٰتِنَآ ۖ إِنَّا مَعَكُم مُّسْتَمِعُونَ ﴿١٥﴾

16. «ወደ ፈርዖንም ኺዱ፡፡ በሉትም፡- እኛ የዓለማት ጌታ መልክተኞች ነን፡፡

فَأْتِيَا فِرْعَوْنَ فَقُولَآ إِنَّا رَسُولُ رَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿١٦﴾

17. «የእስራኤልን ልጆች ከእኛ ጋር ልቀቅ፡፡»

أَنْ أَرْسِلْ مَعَنَا بَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ ﴿١٧﴾

18. (ፈርዖንም) አለ «ልጅ ኾነህ በእኛ ውስጥ አላሳደግንህምን በእኛ ውስጥም ከዕድሜህ ብዙ ዓመታትን አልተቀመጥክምን

قَالَ أَلَمْ نُرَبِّكَ فِينَا وَلِيدًا وَلَبِثْتَ فِينَا مِنْ عُمُرِكَ سِنِينَ ﴿١٨﴾

19. «ያችንም የሠራሃትን ሥራህን አልሠራህምን አንተም ከውለታ ቢሶቹ ነህ» (አለ)፡፡

وَفَعَلْتَ فَعْلَتَكَ ٱلَّتِى فَعَلْتَ وَأَنتَ مِنَ ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿١٩﴾

20. (ሙሳም) አለ «ያን ጊዜ እኔም ከተሳሳቱት ኾኜ ሠራኋት፡፡

قَالَ فَعَلْتُهَآ إِذًا وَأَنَا۠ مِنَ ٱلضَّآلِّينَ ﴿٢٠﴾

21. «በፈራኋችሁም ጊዜ ከእንናተ ሸሸሁ፡፡ ጌታየም ለእኔ ጥበብን ሰጠኝ፡፡ ከመልክተኞቹም አደረገኝ፡፡

فَفَرَرْتُ مِنكُمْ لَمَّا خِفْتُكُمْ فَوَهَبَ لِى رَبِّى حُكْمًا وَجَعَلَنِى مِنَ ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿٢١﴾

22. «ይህችም የእስራኤልን ልጆች ባሪያ በማድረግህ በእኔ ላይ የምትመጻደቅባት ጸጋ ነት፡፡»

وَتِلْكَ نِعْمَةٌ تَمُنُّهَا عَلَىَّ أَنْ عَبَّدتَّ بَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ ﴿٢٢﴾

23. ፈርዖን አለ «(ላከኝ የምትለው) የዓለማትም ጌታ ምንድነው»

قَالَ فِرْعَوْنُ وَمَا رَبُّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٢٣﴾

24. (ሙሳ) «የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ጌታ ነው፡፡ የምታረጋግጡ ብትኾኑ (ነገሩ ይህ ነው)፤» አለው፡፡

قَالَ رَبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ وَمَا بَيْنَهُمَآ ۖ إِن كُنتُم مُّوقِنِينَ ﴿٢٤﴾

25. (ፈርዖንም) በዙሪያው ላሉት ሰዎች «አትሰሙምን» አለ፡፡

قَالَ لِمَنْ حَوْلَهُۥٓ أَلَا تَسْتَمِعُونَ ﴿٢٥﴾

26. (ሙሳ) «ጌታችሁና የመጀመሪያዎቹ አባቶቻችሁም ጌታ ነው» አለው፡፡

قَالَ رَبُّكُمۡ وَرَبُّ ءَابَآئِكُمُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٢٦

27. (ፈርዖን)«ያ ወደእናንተ የተላከው መልክተኛችሁ በእርግጥ ዕብድ ነው» አለ፡፡

قَالَ إِنَّ رَسُولَكُمُ ٱلَّذِيٓ أُرۡسِلَ إِلَيۡكُمۡ لَمَجۡنُونٞ ٢٧

28. (ሙሳ) «የምሥራቅና የምዕራብ በመካከላቸውም ያለው ነገር ሁሉ ጌታ ነው፡፡ ታውቁ እንደኾናችሁ (እመኑበት)» አለው፡፡

قَالَ رَبُّ ٱلۡمَشۡرِقِ وَٱلۡمَغۡرِبِ وَمَا بَيۡنَهُمَآۖ إِن كُنتُمۡ تَعۡقِلُونَ ٢٨

29. (ፈርዖን) «ከእኔ ሌላ አምላክን ብትይዝ በውነቱ ከእስረኞቹ አደርግሃለሁ» አለ፡፡

قَالَ لَئِنِ ٱتَّخَذۡتَ إِلَٰهًا غَيۡرِي لَأَجۡعَلَنَّكَ مِنَ ٱلۡمَسۡجُونِينَ ٢٩

30. (ሙሳ) «በግልጽ አስረጅ ብመጣህም እንኳ» አለው፡፡

قَالَ أَوَلَوۡ جِئۡتُكَ بِشَيۡءٖ مُّبِينٖ ٣٠

31. «እንግዲያውስ ከእውነተኞች እንደኾንክ (አስረጁን) አምጣው» አለ፡፡

قَالَ فَأۡتِ بِهِۦٓ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ٣١

32. በትሩንም ጣለ፡፡ እርሷም ወዲያውኑ ግልጽ እባብ ኾነች፡፡

فَأَلۡقَىٰ عَصَاهُ فَإِذَا هِيَ ثُعۡبَانٞ مُّبِينٞ ٣٢

33. እጁንም አወጣ፡፡ ወዲያውም እርሷ ለተመልካቾች (የምታበራ) ነጭ ኾነች፡፡

وَنَزَعَ يَدَهُۥ فَإِذَا هِيَ بَيۡضَآءُ لِلنَّٰظِرِينَ ٣٣

34. (ፈርዖን) በዙሪያው ላሉት መማክርት «ይህ በእርግጥ ዐዋቂ ድግምተኛ ነው» አለ፡፡

قَالَ لِلۡمَلَإِ حَوۡلَهُۥٓ إِنَّ هَٰذَا لَسَٰحِرٌ عَلِيمٞ ٣٤

35. «ከምድራችሁ በድግምቱ ሊያወጣችሁ ይፈልጋልና ምንን ታዛላችሁ» (አላቸው)፡፡

يُرِيدُ أَن يُخۡرِجَكُم مِّنۡ أَرۡضِكُم بِسِحۡرِهِۦ فَمَاذَا تَأۡمُرُونَ ٣٥

36. አሉት «እርሱን ወንድሙንም አቆይና በየከተሞቹ ሰብሳቢዎችን ላክ፡፡

قَالُوٓاْ أَرۡجِهۡ وَأَخَاهُ وَٱبۡعَثۡ فِي ٱلۡمَدَآئِنِ حَٰشِرِينَ ٣٦

37. «በጣም ዐዋቂ ድግምተኞችን ሁሉ ያመጡልሃልና፡ ፡»

يَأۡتُوكَ بِكُلِّ سَحَّارٍ عَلِيمٖ ٣٧

38. ድግምተኞቹም በታወቀ ቀን ቀጠሮ ተሰበሰቡ፡፡

فَجُمِعَ ٱلسَّحَرَةُ لِمِيقَٰتِ يَوۡمٖ مَّعۡلُومٖ ٣٨

39. ለሰዎቹም «እናንተ ተሰብስባችኋልን» ተባለ፡፡

وَقِيلَ لِلنَّاسِ هَلۡ أَنتُم مُّجۡتَمِعُونَ ٣٩

40. «ድግምተኞቹን እነሱ አሸናፊዎች ቢኾኑ እንከተል ዘንድ» (ተባለ)፡፡

لَعَلَّنَا نَتَّبِعُ ٱلسَّحَرَةَ إِن كَانُواْ هُمُ ٱلۡغَٰلِبِينَ ٤٠

41. «ድግምተኞቹም በመጡ ጊዜ ለፈርዖን እኛ አሸናፊዎች ብንሆን ለእኛ በእርግጥ ዋጋ አለን» አሉት፡፡

فَلَمَّا جَآءَ ٱلسَّحَرَةُ قَالُواْ لِفِرۡعَوۡنَ أَئِنَّ لَنَا لَأَجۡرًا إِن كُنَّا نَحۡنُ ٱلۡغَٰلِبِينَ ٤١

42. «አዎን፤ እናንተም ያን ጊዜ ከባለሟሎቹ ትኾናላችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ نَعَمۡ وَإِنَّكُمۡ إِذٗا لَّمِنَ ٱلۡمُقَرَّبِينَ ٤٢

43. ሙሳ «ለእነርሱ እናንተ የምትጥሉትን ጣሉ» አላቸው፡፡

قَالَ لَهُم مُّوسَىٰٓ أَلۡقُواْ مَآ أَنتُم مُّلۡقُونَ ﴿٤٣﴾

44. ገመዶቻቸውንና በትሮቻቸውንም ጣሉ፡፡ «በፈርዖንም ክብር ይኹንብን፡፡ እኛ በእርግጥ አሸናፊዎቹ እኛ ነን» አሉ፡፡

فَأَلۡقَوۡاْ حِبَالَهُمۡ وَعِصِيَّهُمۡ وَقَالُواْ بِعِزَّةِ فِرۡعَوۡنَ إِنَّا لَنَحۡنُ ٱلۡغَٰلِبُونَ ﴿٤٤﴾

45. ሙሳም በትሩን ጣለ፡፡ ወዲያውም እርሷ የሚያስመስሉትን ሁሉ ትውጣለች፡፡

فَأَلۡقَىٰ مُوسَىٰ عَصَاهُ فَإِذَا هِيَ تَلۡقَفُ مَا يَأۡفِكُونَ ﴿٤٥﴾

46. ድግምተኞቹም ሰጋጆች ኾነው ወደቁ፡፡

فَأُلۡقِيَ ٱلسَّحَرَةُ سَٰجِدِينَ ﴿٤٦﴾

47. (እነሱም) አሉ «በዓለማት ጌታ አመንን፡፡

قَالُوٓاْ ءَامَنَّا بِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٤٧﴾

48. «በሙሳና በሃሩን ጌታ፡፡»

رَبِّ مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ﴿٤٨﴾

49. (ፈርዖንም) «ለእናንተ ሳልፈቅድላችሁ በፊት ለእርሱ አመናችሁን እርሱ ያ ድግምትን ያስተማራችሁ ታላቃችሁ ነው፡፡ ወደፊትም (የሚያገኛችሁን) በእርግጥ ታውቃላችሁ፡፡ እጆቻችሁንና እግሮቻችሁን (ቀኝና ግራን) በማናጋት እቆረርጣለሁ፡፡ ሁላችሁንም እሰቅላችኋለሁም» አለ፡፡

قَالَ ءَامَنتُمۡ لَهُۥ قَبۡلَ أَنۡ ءَاذَنَ لَكُمۡۖ إِنَّهُۥ لَكَبِيرُكُمُ ٱلَّذِي عَلَّمَكُمُ ٱلسِّحۡرَ فَلَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَۚ لَأُقَطِّعَنَّ أَيۡدِيَكُمۡ وَأَرۡجُلَكُم مِّنۡ خِلَٰفٖ وَلَأُصَلِّبَنَّكُمۡ أَجۡمَعِينَ ﴿٤٩﴾

50. (እነርሱም) አሉ «ጉዳት የለብንም፡፡ እኛ ወደ ጌታችን ተመላሾች ነን፡፡

قَالُواْ لَا ضَيۡرَۖ إِنَّآ إِلَىٰ رَبِّنَا مُنقَلِبُونَ ﴿٥٠﴾

51. «እኛ የምእምናን መጀመሪያ በመኾናችን ጌታችን ኀጢአቶቻችንን ለእኛ ሊምር እንከጅላለን፡፡»

إِنَّا نَطۡمَعُ أَن يَغۡفِرَ لَنَا رَبُّنَا خَطَٰيَٰنَآ أَن كُنَّآ أَوَّلَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٥١﴾

52. ወደ ሙሳም «ባሮቼን ይዘህ ሌሊት ኺድ፡፡ እናንተ የሚከተሉዋችሁ ናችሁና» ስንል ላክን፡፡

۞وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰٓ أَنۡ أَسۡرِ بِعِبَادِيٓ إِنَّكُم مُّتَّبَعُونَ ﴿٥٢﴾

53. ፈርዖንም በየከተሞቹ ሰብሳቢዎችን (እንዲህ ሲል) ላከ፡፡

فَأَرۡسَلَ فِرۡعَوۡنُ فِي ٱلۡمَدَآئِنِ حَٰشِرِينَ ﴿٥٣﴾

54. «እነዚህ ጥቂቶች ጭፈሮች ናቸው፡፡

إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ لَشِرۡذِمَةٞ قَلِيلُونَ ﴿٥٤﴾

55. «እነርሱም ለእኛ አስቆጪዎች ናቸው፡፡

وَإِنَّهُمۡ لَنَا لَغَآئِظُونَ ﴿٥٥﴾

56. «እኛም ብዙዎች ጥንቁቆች ነን፤» (አለ)፡፡

وَإِنَّا لَجَمِيعٌ حَٰذِرُونَ ﴿٥٦﴾

57. አወጣናቸውም፡፡ ከአትክልቶችና ከምንጮች፡፡

فَأَخۡرَجۡنَٰهُم مِّن جَنَّٰتٖ وَعُيُونٖ ﴿٥٧﴾

58. ከድልቦችም ከመልካም መቀመጫዎችም፡፡

وَكُنُوزٖ وَمَقَامٖ كَرِيمٖ ٥٨

59. እንደዚሁ ለእስራኤል ልጆች አወረስናትም፡፡

كَذَٰلِكَۖ وَأَوۡرَثۡنَٰهَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٥٩

60. ፀሐይዋ ስትወጣም ተከተሉዋቸው፡፡

فَأَتۡبَعُوهُم مُّشۡرِقِينَ ٦٠

61. ሁለቱ ጭፍሮችም በተያዩ ጊዜ የሙሳ ጓዶች «እኛ(የፈርዖን ሰዎች) የሚደርሱብን ነን» አሉ፡፡

فَلَمَّا تَرَٰٓءَا ٱلۡجَمۡعَانِ قَالَ أَصۡحَٰبُ مُوسَىٰٓ إِنَّا لَمُدۡرَكُونَ ٦١

62. (ሙሳ) «ተዉዉ! ጌታዬ ከእኔ ጋር ነው፡፡ በእርግጥ ይመራኛል» አለ፡፡

قَالَ كَلَّآۖ إِنَّ مَعِيَ رَبِّي سَيَهۡدِينِ ٦٢

63. ወደ ሙሳም «ባሕሩን በበትርህ ምታው» ስንል ላክንበት፡፡ (መታውና) ተከፈለም፡፡ ክፍሉም ሁሉ እንደ ታላቅ ጋራ ኾነ፡፡

فَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰ مُوسَىٰٓ أَنِ ٱضۡرِب بِّعَصَاكَ ٱلۡبَحۡرَۖ فَٱنفَلَقَ فَكَانَ كُلُّ فِرۡقٖ كَٱلطَّوۡدِ ٱلۡعَظِيمِ ٦٣

64. እዚያም ዘንድ ሌሎችን አቀረብን፡፡

وَأَزۡلَفۡنَا ثَمَّ ٱلۡأٓخَرِينَ ٦٤

65. ሙሳንም ከእርሱ ገር ያሉትንም ሰዎች ሁሉንም አዳን፡፡

وَأَنجَيۡنَا مُوسَىٰ وَمَن مَّعَهُۥٓ أَجۡمَعِينَ ٦٥

66. ከዚያም ሌሎቹን አሰጠምን፡፡

ثُمَّ أَغۡرَقۡنَا ٱلۡأٓخَرِينَ ٦٦

67. በዚህ ውስጥ ታላቅ ታምር አለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም አማኞች አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ٦٧

68. ጌታህም እርሱ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ٦٨

69. በእነሱም (በሕዝቦችህ) ላይ የኢብራሂምን ወሬ አንብብላቸው፡፡

وَٱتۡلُ عَلَيۡهِمۡ نَبَأَ إِبۡرَٰهِيمَ ٦٩

70. ለአባቱና ለሕዝቦቹ «ምንን ትግገዛላችሁ» ባለ ጊዜ፡፡

إِذۡ قَالَ لِأَبِيهِ وَقَوۡمِهِۦ مَا تَعۡبُدُونَ ٧٠

71. «ጣዖታትን እንገዛለን፤ እርሷንም በመገዛት ላይ እንቆያለን» አሉ፡፡

قَالُواْ نَعۡبُدُ أَصۡنَامٗا فَنَظَلُّ لَهَا عَٰكِفِينَ ٧١

72. (እርሱም) አለ «በጠራችኋቸው ጊዜ ይሰሟችኋልን

قَالَ هَلۡ يَسۡمَعُونَكُمۡ إِذۡ تَدۡعُونَ ٧٢

73. «ወይስ ይጠቅሟችኋልን ወይስ ይጎዱችኋልን»

أَوۡ يَنفَعُونَكُمۡ أَوۡ يَضُرُّونَ ٧٣

74. «የለም! አባቶቻችን እንደዚሁ ሲሠሩ አገኘን» አሉት፡፡

قَالُواْ بَلۡ وَجَدۡنَآ ءَابَآءَنَا كَذَٰلِكَ يَفۡعَلُونَ ٧٤

قَالَ أَفَرَءَيۡتُم مَّا كُنتُمۡ تَعۡبُدُونَ ٧٥

75. «ትግገዙት የነበራችሁትን አስተዋላችሁን

أَنتُمۡ وَءَابَآؤُكُمُ ٱلۡأَقۡدَمُونَ ٧٦

76. «እናንተም የቀድሞዎቹ አባቶቻችሁም (የተግገዛችሁትን)፡፡»

فَإِنَّهُمۡ عَدُوّٞ لِّيٓ إِلَّا رَبَّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٧٧

77. «እነሱም (ጣዖቶቹ) ለእኔ ጠላቶች ናቸው፡፡ ግን የዓለማት ጌታ ሲቀር (እርሱ ወዳጄ ነው)፡፡

ٱلَّذِي خَلَقَنِي فَهُوَ يَهۡدِينِ ٧٨

78. «(እርሱ) ያ የፈጠረኝ ነው፡፡ እርሱም ይመራኛል፡፡

وَٱلَّذِي هُوَ يُطۡعِمُنِي وَيَسۡقِينِ ٧٩

79. «ያም እርሱ የሚያበላኝና የሚያጠጣኝ ነው፡፡

وَإِذَا مَرِضۡتُ فَهُوَ يَشۡفِينِ ٨٠

80. «በታመምኩም ጊዜ እርሱ ያሽረኛል፡፡

وَٱلَّذِي يُمِيتُنِي ثُمَّ يُحۡيِينِ ٨١

81. «ያም የሚገድለኝ ከዚያም ሕያው የሚያደርገኝ ነው፡፡

وَٱلَّذِيٓ أَطۡمَعُ أَن يَغۡفِرَ لِي خَطِيٓـَٔتِي يَوۡمَ ٱلدِّينِ ٨٢

82. ያም በፍርዱ ቀን ኀጢአቴን ለእኔ ሊምር የምከጅለው ነው፡፡

رَبِّ هَبۡ لِي حُكۡمٗا وَأَلۡحِقۡنِي بِٱلصَّٰلِحِينَ ٨٣

83. ጌታዬ ሆይ! ዕውቀትን ስጠኝ! በደጋጎቹም ሰዎች አስጠጋኝ፡፡

وَٱجۡعَل لِّي لِسَانَ صِدۡقٖ فِي ٱلۡأٓخِرِينَ ٨٤

84. በኋለኞቹም ሕዝቦች ውስጥ ለእኔ መልካም ዝናን አድርግልኝ፡፡

وَٱجۡعَلۡنِي مِن وَرَثَةِ جَنَّةِ ٱلنَّعِيمِ ٨٥

85. የጸጋይቱን ገነት ከሚወርሱትም አድርገኝ፡፡

وَٱغۡفِرۡ لِأَبِيٓ إِنَّهُۥ كَانَ مِنَ ٱلضَّآلِّينَ ٨٦

86. ለአባቴም ማር፡፡ እርሱ ከተሳሳቱት ነበረና፡፡

وَلَا تُخۡزِنِي يَوۡمَ يُبۡعَثُونَ ٨٧

87. በሚቀሰቀሱበት ቀንም አታዋርደኝ፡፡

يَوۡمَ لَا يَنفَعُ مَالٞ وَلَا بَنُونَ ٨٨

88. ገንዘብም ልጆችም በማይጠቅሙበት ቀን፡፡

إِلَّا مَنۡ أَتَى ٱللَّهَ بِقَلۡبٖ سَلِيمٖ ٨٩

89. ወደ አላህ በንጹህ ልብ የመጣ ሰው ቢኾን እንጅ፡፡ »

وَأُزۡلِفَتِ ٱلۡجَنَّةُ لِلۡمُتَّقِينَ ٩٠

90. ገነትም ለፈሪዎች በምትቀረብበት (ቀን)፡፡

وَبُرِّزَتِ ٱلۡجَحِيمُ لِلۡغَاوِينَ ٩١

91. ገሀነምም ለጠመሞች በምትገለጽበት (ቀን)፡፡

وَقِيلَ لَهُمۡ أَيۡنَ مَا كُنتُمۡ تَعۡبُدُونَ ٩٢

92. ለእነሱም በሚባል ቀን «ትግገዟቸው የነበራችሁት የት ናቸው»

93. «ከአላህ ሌላ ሲኾኑ ይረዱዋችኋልን ወይስ (ለራሳቸው) ይርረዳሉን»

مِن دُونِ ٱللَّهِ هَلۡ يَنصُرُونَكُمۡ أَوۡ يَنتَصِرُونَ ۝٩٣

94. በውስጧም እነሱና ጠማሞቹ በፊቶቻቸው ተጥለው ይንከባለላሉ፡፡

فَكُبۡكِبُواْ فِيهَا هُمۡ وَٱلۡغَاوُۥنَ ۝٩٤

95. የሰይጣንም ሰራዊቶች መላውም (ይጣላሉ)፡፡

وَجُنُودُ إِبۡلِيسَ أَجۡمَعُونَ ۝٩٥

96. እነርሱም በእርሷ ውስጥ የሚከራከሩ ኾነው ይላሉ፡-

قَالُواْ وَهُمۡ فِيهَا يَخۡتَصِمُونَ ۝٩٦

97. በአላህ እንምላለን፤ እኛ በግልጽ መሳሳት ውስጥ ነበርን፡፡

تَٱللَّهِ إِن كُنَّا لَفِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ۝٩٧

98. (ጣዖቶቹን) በዓለማት ጌታ ባስተካከልናችሁ ጊዜ፡፡

إِذۡ نُسَوِّيكُم بِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ۝٩٨

99. አመጸኞቹም እንጅ ሌላ አላሳሳተንም፡፡

وَمَآ أَضَلَّنَآ إِلَّا ٱلۡمُجۡرِمُونَ ۝٩٩

100. ከአማላጆችም ለእኛ ምንም የለንም፡፡

فَمَا لَنَا مِن شَٰفِعِينَ ۝١٠٠

101. አዛኝ ወዳጂም (የለንም)፡፡

وَلَا صَدِيقٍ حَمِيمٖ ۝١٠١

102. ለእኛም አንዲት ጊዜ መመለስ በኖረችንና ከአማኞቹ በኾን እንመኛለን (ይላሉ)፡፡

فَلَوۡ أَنَّ لَنَا كَرَّةٗ فَنَكُونَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ۝١٠٢

103. በዚህ ውስጥ አስደናቂ ግሳጼ አለለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም አማኞች አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ۝١٠٣

104. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ۝١٠٤

105. የኑሕ ሕዝቦች መልክተኞችን አስተባበሉ፡፡

كَذَّبَتۡ قَوۡمُ نُوحٍ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ۝١٠٥

106. ወንድማቸው ኑሕ ለእነሱ ባላቸው ጊዜ «አትጠነቀቁምን

إِذۡ قَالَ لَهُمۡ أَخُوهُمۡ نُوحٌ أَلَا تَتَّقُونَ ۝١٠٦

107. «እኔ ለእናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝ፡፡

إِنِّي لَكُمۡ رَسُولٌ أَمِينٞ ۝١٠٧

108. «አላህንም ፍሩ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ۝١٠٨

109. «በእርሱም ላይ ምንም ዋጋ አልጠይቃችሁም፡፡ ዋጋዬ በዓለማት ጌታ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡

وَمَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ۝١٠٩

110. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡»

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ﴿١١٠﴾

111. (እነርሱም) «ወራዶቹ የተከተሉህ ኾነህ ለአንተ እናምናለን» አሉት፡፡

۞قَالُوٓاْ أَنُؤۡمِنُ لَكَ وَٱتَّبَعَكَ ٱلۡأَرۡذَلُونَ ﴿١١١﴾

112. (እርሱም) አላቸው «ይሠሩት በነበሩት ነገር ምን ዕውቀት አለኝ፡፡

قَالَ وَمَا عِلۡمِي بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ﴿١١٢﴾

113. «ምርመራቸው በጌታዬ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡ ብታውቁ ኖሮ (ይህንን ትርረዱ ነበር)፡፡

إِنۡ حِسَابُهُمۡ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّيۖ لَوۡ تَشۡعُرُونَ ﴿١١٣﴾

114. «እኔም አማኞችን አባራሪ አይደለሁም፡፡

وَمَآ أَنَا۠ بِطَارِدِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿١١٤﴾

115. «እኔ ግልጽ አስፈራሪ እንጅ ሌላ አይደለሁም፡፡»

إِنۡ أَنَا۠ إِلَّا نَذِيرٞ مُّبِينٞ ﴿١١٥﴾

116. «ኑሕ ሆይ! (ከምትለው) ባትከለከል በእርግጥ ከሚወገሩት ትኾናለህ» አሉት፡፡

قَالُواْ لَئِن لَّمۡ تَنتَهِ يَٰنُوحُ لَتَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمَرۡجُومِينَ ﴿١١٦﴾

117. (እርሱም) አለ «ጌታዬ ሆይ! ሕዝቦቼ አስተባበሉኝ፡፡

قَالَ رَبِّ إِنَّ قَوۡمِي كَذَّبُونِ ﴿١١٧﴾

118. «በእኔና በእነርሱም መካከል (ተገቢ) ፍርድን ፍረድ፡፡ አድነኝም፡፡ ከእኔ ጋር ያሉትንም ምእምናን፡፡»

فَٱفۡتَحۡ بَيۡنِي وَبَيۡنَهُمۡ فَتۡحٗا وَنَجِّنِي وَمَن مَّعِيَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿١١٨﴾

119. እርሱንም ከእርሱ ጋር ያለውንም ሁሉ በተመላው መርከብ ውስጥ አዳን፡፡

فَأَنجَيۡنَٰهُ وَمَن مَّعَهُۥ فِي ٱلۡفُلۡكِ ٱلۡمَشۡحُونِ ﴿١١٩﴾

120. ከዚያም በኋላ ቀሪዎቹን አሰጠምን፡፡

ثُمَّ أَغۡرَقۡنَا بَعۡدُ ٱلۡبَاقِينَ ﴿١٢٠﴾

121. በዚህ ውስጥ ታላቅ ግሳጼ አለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም አማኞች አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ﴿١٢١﴾

122. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ﴿١٢٢﴾

123. ዓድ መልክተኞችን አስተባበለች፡፡

كَذَّبَتۡ عَادٌ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ﴿١٢٣﴾

124. ወንድማቸው ሁድ ለነርሱ ባላቸው ጊዜ «አትጠነቀቁምን

إِذۡ قَالَ لَهُمۡ أَخُوهُمۡ هُودٌ أَلَا تَتَّقُونَ ﴿١٢٤﴾

125. «እኔ ለናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝ፡፡

إِنِّي لَكُمۡ رَسُولٌ أَمِينٞ ﴿١٢٥﴾

126. «አላህንም ፍሩ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ﴿١٢٦﴾

127. «በእርሱም ላይ ምንም ዋጋ አለምናችሁም፡፡ ዋጋዬ በዓለማት ጌታ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡

وَمَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿١٢٧﴾

128. «የምትጫወቱ ኾናችሁ በከፍተኛ ስፍራ ሁሉ ላይ ምልክትን ትገነባላችሁን

أَتَبۡنُونَ بِكُلِّ رِيعٍ ءَايَةٗ تَعۡبَثُونَ ١٢٨

129. «የውሃ ማጠራቀሚያዎችንና ሕንፃዎችንም ዘላለም መኖርን የምትከጅሉ ኾናችሁ ትሠራላችሁን

وَتَتَّخِذُونَ مَصَانِعَ لَعَلَّكُمۡ تَخۡلُدُونَ ١٢٩

130. «በቀጣችሁም ጊዜ ጨካኞች ኾናችሁ ትቀጣላችሁን

وَإِذَا بَطَشۡتُم بَطَشۡتُمۡ جَبَّارِينَ ١٣٠

131. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ١٣١

132. «ያንንም በምታውቁት (ጸጋ) ያጣቀማችሁን ፍሩ፡፡

وَٱتَّقُواْ ٱلَّذِيٓ أَمَدَّكُم بِمَا تَعۡلَمُونَ ١٣٢

133. «በእንስሳዎችና በልጆች ያጣቀማችሁን፡፡

أَمَدَّكُم بِأَنۡعَٰمٖ وَبَنِينَ ١٣٣

134. «በአትክልቶችና በምንጮችም፡፡

وَجَنَّٰتٖ وَعُيُونٍ ١٣٤

135. «እኔ በእናንተ ላይ የታላቅን ቀን ቅጣት እፈራለሁና፡፡»

إِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ عَذَابَ يَوۡمٍ عَظِيمٖ ١٣٥

136. (እነርሱም) አሉ «ብትገሰጽም ወይም ከገሳጮቹ ባትኾንም በእኛ ላይ እኩል ነው፤ (ያለንበትን አንለቅም)፡፡

قَالُواْ سَوَآءٌ عَلَيۡنَآ أَوَعَظۡتَ أَمۡ لَمۡ تَكُن مِّنَ ٱلۡوَٰعِظِينَ ١٣٦

137. «ይህ የፊተኞቹ ሰዎች ፀባይ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا خُلُقُ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٣٧

138. «እኛም የምንቀቀጣ አይደለንም» (አሉ)፡፡

وَمَا نَحۡنُ بِمُعَذَّبِينَ ١٣٨

139. አስተባበሉትም፡፡ አጠፋናቸውም፡፡ በዚህም ውስጥ እርግጠኛ ግሳጼ አለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም ምእመናን አልነበሩም፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَأَهۡلَكۡنَٰهُمۡۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ١٣٩

140. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ١٤٠

141. ሰሙድ መልክተኞችን አስተባበለች፡፡

كَذَّبَتۡ ثَمُودُ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٤١

142. ወንድማቸው ሷሊህ ለእነርሱ ባላቸው ጊዜ «አትጠነቀቁምን

إِذۡ قَالَ لَهُمۡ أَخُوهُمۡ صَٰلِحٌ أَلَا تَتَّقُونَ ١٤٢

143. «እኔ ለእናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝ፡፡

إِنِّي لَكُمۡ رَسُولٌ أَمِينٞ ١٤٣

144. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ١٤٤

145. «በእርሱም ላይ ምንም ዋጋ አልለምናችሁም፡፡ ዋጋዬ በዓለማት ጌታ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡

وَمَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٤٥

146. «በዚያ እዚህ ባለው (ጸጋ) ውስጥ የረካችሁ ኾናችሁ ትተዋላችሁን

أَتُتۡرَكُونَ فِي مَا هَٰهُنَآ ءَامِنِينَ ١٤٦

147. «በአትክልቶችና በምንጮች ውስጥ፡፡

فِي جَنَّٰتٖ وَعُيُونٖ ١٤٧

148. «በአዝመራዎችም ፍሬዋ የበሰለ በኾነች ዘንባባም፤ (ውስጥ ትተዋላችሁን)

وَزُرُوعٖ وَنَخۡلٖ طَلۡعُهَا هَضِيمٞ ١٤٨

149. «ብልሆች ኾናችሁ ከጋራዎች ቤቶችንም ትጠርባላችሁ፡፡

وَتَنۡحِتُونَ مِنَ ٱلۡجِبَالِ بُيُوتٗا فَٰرِهِينَ ١٤٩

150. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ١٥٠

151. «የወሰን አላፊዎችንም ትዕዛዝ አትከተሉ፡፡

وَلَا تُطِيعُوٓاْ أَمۡرَ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ١٥١

152. «የእነዚያን በምድር ላይ የሚያጠፉትንና የማያበጁትን፡፡»

ٱلَّذِينَ يُفۡسِدُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا يُصۡلِحُونَ ١٥٢

153. (እነሱም) አሉ «አንተ በብዙ ከተደገመባቸው ሰዎች ብቻ ነህ፡፡

قَالُوٓاْ إِنَّمَآ أَنتَ مِنَ ٱلۡمُسَحَّرِينَ ١٥٣

154. «አንተ ብጤያችን ሰው እንጅ ሌላ አይደለህም፡፡ ከእውነተኞቹም እንደኾንክ ተዓምርን አምጣ፡፡»

مَآ أَنتَ إِلَّا بَشَرٞ مِّثۡلُنَا فَأۡتِ بِـَٔايَةٍ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ١٥٤

155. (እርሱም) አለ «ይህች ግመል ናት፡፡ ለእርሷ የመጠጥ ፋንታ አላት፡፡ ለእናንተም የታወቀ ቀን ፋንታ አላችሁ፡፡

قَالَ هَٰذِهِۦ نَاقَةٞ لَّهَا شِرۡبٞ وَلَكُمۡ شِرۡبُ يَوۡمٖ مَّعۡلُومٖ ١٥٥

156. «በክፉም አትንኳት፡፡ የታላቅ ቀን ቅጣት ይይዛችኋልና፡፡»

وَلَا تَمَسُّوهَا بِسُوٓءٖ فَيَأۡخُذَكُمۡ عَذَابُ يَوۡمٍ عَظِيمٖ ١٥٦

157. ወጓትም፡፡ ወዲያውም ተጸጻቾች ኾነው አነጉ፡፡

فَعَقَرُوهَا فَأَصۡبَحُواْ نَٰدِمِينَ ١٥٧

158. ቅጣቱም ያዛቸው፡፡ በዚህም ውስጥ ግሳጼ አልለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም ምእመናን አልነበሩም፡፡

فَأَخَذَهُمُ ٱلۡعَذَابُۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ١٥٨

159. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ١٥٩

160. የሉጥ ሕዝቦች መልክተኞችን አስተባባሉ፡፡

كَذَّبَتۡ قَوۡمُ لُوطٍ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٦٠

161. ወንድማቸው ሉጥ ለእነርሱ ባለ ጊዜ «አትጠነቀቁምን

إِذۡ قَالَ لَهُمۡ أَخُوهُمۡ لُوطٌ أَلَا تَتَّقُونَ ١٦١

162. «እኔ ለእናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝ፡፡

إِنِّي لَكُمۡ رَسُولٌ أَمِينٞ ١٦٢

163. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ١٦٣

164. «በእርሱም ላይ ምንም ዋጋ አልለምናችሁም፡፡ ዋጋዬ በዓለማት ጌታ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡

وَمَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٦٤

165. «ከዓለማት ሰዎች ወንዶችን ትመጣላችሁን

أَتَأۡتُونَ ٱلذُّكۡرَانَ مِنَ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٦٥

166. «ከሚስቶቻችሁም ጌታችሁ ለናንተ የፈጠረላችሁን ትተዋላችሁን በእውነቱ እናንተ ወሰን አላፊዎች ሕዝቦ ናችሁ፡፡»

وَتَذَرُونَ مَا خَلَقَ لَكُمۡ رَبُّكُم مِّنۡ أَزۡوَٰجِكُمۚ بَلۡ أَنتُمۡ قَوۡمٌ عَادُونَ ١٦٦

167. (እነርሱም) አሉ «ሉጥ ሆይ! ባትከለከል በእርግጥ (ከአገር) ከሚወጡት ትኾናለህ፡፡»

قَالُواْ لَئِن لَّمۡ تَنتَهِ يَٰلُوطُ لَتَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُخۡرَجِينَ ١٦٧

168. (እርሱም) አለ «እኔ ሥራችሁን ከሚጠሉት ሰዎች ነኝ፡፡

قَالَ إِنِّي لِعَمَلِكُم مِّنَ ٱلۡقَالِينَ ١٦٨

169. «ጌታዬ ሆይ! እኔንም ቤተሰቦቼንም ከሚሠሩት ሥራ (ቅጣት) አድነን፡፡»

رَبِّ نَجِّنِي وَأَهۡلِي مِمَّا يَعۡمَلُونَ ١٦٩

170. እርሱንም ቤተሰቦቹንም በጠቅላላ አዳንናቸው፡፡

فَنَجَّيۡنَٰهُ وَأَهۡلَهُۥٓ أَجۡمَعِينَ ١٧٠

171. በቀሪዎቹ ውስጥ የኾነች አሮጊት ብቻ ስትቀር (እርሷ ጠፋች)፡፡

إِلَّا عَجُوزٗا فِي ٱلۡغَٰبِرِينَ ١٧١

172. ከዚያም ሌሎቹን አጠፋን፡፡

ثُمَّ دَمَّرۡنَا ٱلۡأٓخَرِينَ ١٧٢

173. በእነሱም ላይ (የድንጋይን) ዝናምን አዘነምንባቸው፡፡ የተስፈራሪዎቹም ዝናም (ምንኛ) ከፋ፡፡

وَأَمۡطَرۡنَا عَلَيۡهِم مَّطَرٗاۖ فَسَآءَ مَطَرُ ٱلۡمُنذَرِينَ ١٧٣

174. በዚህ ውስጥ አስደናቂ ተዓምር አልለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም ምእመናን አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ١٧٤

175. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ١٧٥

176. የአይከት ሰዎች መልክተኞችን አስተባበሉ፤

كَذَّبَ أَصۡحَٰبُ لۡـَٔيۡكَةِ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٧٦

177. ሹዐይብ ለእነርሱ ባላቸው ጊዜ «አትጠነቀቁምን

إِذۡ قَالَ لَهُمۡ شُعَيۡبٌ أَلَا تَتَّقُونَ ١٧٧

178. «እኔ ለእናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝ፡፡

إِنِّي لَكُمۡ رَسُولٌ أَمِينٞ ١٧٨

179. «አላህንም ፍሩ፤ ታዘዙኝም፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ﴿١٧٩﴾

180. «በርሱም ላይ ምንም ዋጋ አልጠይቃችሁም፡፡ ዋጋዬ በዓለማት ጌታ ላይ እንጅ በሌላ ላይ አይደለም፡፡

وَمَآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ أَجۡرٍۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَىٰ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿١٨٠﴾

181. «ስፍርን ሙሉ፡፡ ከአጉዳዮቹም አትኹኑ፡፡

۞أَوۡفُواْ ٱلۡكَيۡلَ وَلَا تَكُونُواْ مِنَ ٱلۡمُخۡسِرِينَ ﴿١٨١﴾

182. «በትክክለኛ ሚዛንም መዝኑ፡፡

وَزِنُواْ بِٱلۡقِسۡطَاسِ ٱلۡمُسۡتَقِيمِ ﴿١٨٢﴾

183. «ሰዎችንም ነገሮቻቸውን አታጉድሉባቸው፡፡ በምድርም ላይ አጥፊዎች ኾናችሁ አታበላሹ፡፡

وَلَا تَبۡخَسُواْ ٱلنَّاسَ أَشۡيَآءَهُمۡ وَلَا تَعۡثَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُفۡسِدِينَ ﴿١٨٣﴾

184. «ያንንም የፈጠራችሁን የቀድሞዎቹንም ፍጡሮች (የፈጠረውን) ፍሩ፡፡»

وَٱتَّقُواْ ٱلَّذِي خَلَقَكُمۡ وَٱلۡجِبِلَّةَ ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿١٨٤﴾

185. አሉ «አንተ በብዛት ከተደገመባቸው ሰዎች ነህ፡፡

قَالُوٓاْ إِنَّمَآ أَنتَ مِنَ ٱلۡمُسَحَّرِينَ ﴿١٨٥﴾

186. «አንተም ብጤያችን ሰው እንጅ ሌላ አይደለህም፡ ፡ እነሆ ከውሸታሞች ነህ ብለን እንጠረጥርሃለን፡፡

وَمَآ أَنتَ إِلَّا بَشَرٞ مِّثۡلُنَا وَإِن نَّظُنُّكَ لَمِنَ ٱلۡكَٰذِبِينَ ﴿١٨٦﴾

187. «ከእውነተኞቹም እንደኾንክ በእኛ ላይ ከሰማይ ቁራጭን ጣልብን፡፡»

فَأَسۡقِطۡ عَلَيۡنَا كِسَفٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿١٨٧﴾

188. «ጌታዬ የምትሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፤» አላቸው፡፡

قَالَ رَبِّيٓ أَعۡلَمُ بِمَا تَعۡمَلُونَ ﴿١٨٨﴾

189. አስተባበሉትም፡፡ የጥላይቷ ቀን ቅጣትም ያዛቸው፡፡ እርሱ የከባድ ቀን ቅጣት ነበርና፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَأَخَذَهُمۡ عَذَابُ يَوۡمِ ٱلظُّلَّةِۚ إِنَّهُۥ كَانَ عَذَابَ يَوۡمٍ عَظِيمٍ ﴿١٨٩﴾

190. በዚህ ውስጥ አስደናቂ ተዓምር አልለበት፡፡ አብዛኞቻቸውም ምእምናን አልነበሩም፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗۖ وَمَا كَانَ أَكۡثَرُهُم مُّؤۡمِنِينَ ﴿١٩٠﴾

191. ጌታህም እርሱ በእርግጥ አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ﴿١٩١﴾

192. እርሱም (ቁርኣን) በእርግጥ ከዓለማት ጌታ የተወረደ ነው፡፡

وَإِنَّهُۥ لَتَنزِيلُ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿١٩٢﴾

193. እርሱን ታማኙ መንፈስ (ጂብሪል) አወረደው፤

نَزَلَ بِهِ ٱلرُّوحُ ٱلۡأَمِينُ ﴿١٩٣﴾

194. ከአስፈራሪዎቹ (ነቢያት) ትኾን ዘንድ በልብህ ላይ (አወረደው)፡፡

عَلَىٰ قَلۡبِكَ لِتَكُونَ مِنَ ٱلۡمُنذِرِينَ ﴿١٩٤﴾

195. ግልጽ በኾነ ዐረብኛ ቋንቋ፡፡

بِلِسَانٍ عَرَبِيّٖ مُّبِينٖ ﴿١٩٥﴾

196. እርሱም (ቁርኣን) በቀድሞዎቹ መጻሐፍት ውስጥ (የተወሳ ነው)፡፡

وَإِنَّهُۥ لَفِي زُبُرِ ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿١٩٦﴾

197. የእስራኤል ልጆች ሊቃውንት የሚያውቁት መኾኑ ለእነርሱ (ለመካ ከሓዲዎች) ምልክት አይኾናቸውምን

أَوَلَمۡ يَكُن لَّهُمۡ ءَايَةً أَن يَعۡلَمَهُۥ عُلَمَٰٓؤُاْ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ﴿١٩٧﴾

198. ከአዕጀሞች ባንዱ ላይ ባወረድነውም ኖሮ፤

وَلَوۡ نَزَّلۡنَٰهُ عَلَىٰ بَعۡضِ ٱلۡأَعۡجَمِينَ ﴿١٩٨﴾

199. በእነርሱ ላይ ባነበበውም በእርሱ አማኞች አይኾኑም ነበር፡፡

فَقَرَأَهُۥ عَلَيۡهِم مَّا كَانُواْ بِهِۦ مُؤۡمِنِينَ ﴿١٩٩﴾

200. እንደዚሁ (ማስተባበልን) በተንኮለኞች ልቦች ውስጥ አስገባነው፡፡

كَذَٰلِكَ سَلَكۡنَٰهُ فِي قُلُوبِ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ﴿٢٠٠﴾

201. አሳማሚ ቅጣትን እስከሚያዩ ድረስ በእርሱ አያምኑም፡፡

لَا يُؤۡمِنُونَ بِهِۦ حَتَّىٰ يَرَوُاْ ٱلۡعَذَابَ ٱلۡأَلِيمَ ﴿٢٠١﴾

202. እነርሱ የማያውቁ ሲኾኑ (ቅጣቱ) ድንገት እስከሚመጣባቸውም ድረስ (አያምኑም)፡፡

فَيَأۡتِيَهُم بَغۡتَةً وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ﴿٢٠٢﴾

203. (በመጣባቸው ጊዜ) «እኛ የምንቆይ ነን» እስከሚሉም (አያምኑም)፡፡

فَيَقُولُواْ هَلۡ نَحۡنُ مُنظَرُونَ ﴿٢٠٣﴾

204. በቅጣታችን ያቻኩላሉን

أَفَبِعَذَابِنَا يَسۡتَعۡجِلُونَ ﴿٢٠٤﴾

205. አየህን ብዙ ዓመታትን ብናጣቅማቸው፤

أَفَرَءَيۡتَ إِن مَّتَّعۡنَٰهُمۡ سِنِينَ ﴿٢٠٥﴾

206. ከዚያም ያ ይስፈራሩበት የነበሩት ቢመጣባቸው፤

ثُمَّ جَآءَهُم مَّا كَانُواْ يُوعَدُونَ ﴿٢٠٦﴾

207. ይጣቀሙበት የነበሩት ሁሉ ከእነሱ ምንም አያብቃቃቸውም፡፡

مَآ أَغۡنَىٰ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يُمَتَّعُونَ ﴿٢٠٧﴾

208. አንዲትንም ከተማ ለእርሷ አስፈራሪዎች ያሏት (እና ያስተባበለች) ኾና እንጅ አላጠፋንም፡፡

وَمَآ أَهۡلَكۡنَا مِن قَرۡيَةٍ إِلَّا لَهَا مُنذِرُونَ ﴿٢٠٨﴾

209. (ይህች) ግሳፄ ናት፡፡ በዳዮችም አልነበርንም፡፡

ذِكۡرَىٰ وَمَا كُنَّا ظَٰلِمِينَ ﴿٢٠٩﴾

210. ሰይጣናትም እርሱን (ቁርኣንን) አላወረዱትም፡፡

وَمَا تَنَزَّلَتۡ بِهِ ٱلشَّيَٰطِينُ ﴿٢١٠﴾

211. ለእነርሱም አይገባቸውም፤ አይችሉምም፡፡

وَمَا يَنۢبَغِي لَهُمۡ وَمَا يَسۡتَطِيعُونَ ﴿٢١١﴾

212. እነርሱ (የመላእክትን ንግግር) ከመስማት ተከለከሉ ናቸው፡፡

إِنَّهُمْ عَنِ ٱلسَّمْعِ لَمَعْزُولُونَ ﴿٢١٢﴾

213. ከአላህም ጋር ሌላን አምላክ አትግገዛ፤ ከሚቀጡት ትኾናለህና፡፡

فَلَا تَدْعُ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ فَتَكُونَ مِنَ ٱلْمُعَذَّبِينَ ﴿٢١٣﴾

214. ቅርቦች ዘመዶችህንም አስጠንቅቅ፡፡

وَأَنذِرْ عَشِيرَتَكَ ٱلْأَقْرَبِينَ ﴿٢١٤﴾

215. ከምእምናንም ለተከተሉህ ሰዎች ክንፍህን ዝቅ አድርግ፤ (ልዝብ ኹን)፡፡

وَٱخْفِضْ جَنَاحَكَ لِمَنِ ٱتَّبَعَكَ مِنَ ٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿٢١٥﴾

216. «እንቢ» ቢሉህም «እኔ ከምትሠሩት ንጹሕ ነኝ» በላቸው፡፡

فَإِنْ عَصَوْكَ فَقُلْ إِنِّى بَرِىٓءٌ مِّمَّا تَعْمَلُونَ ﴿٢١٦﴾

217. አሸናፊ አዛኝ በኾነው (ጌታህ) ላይም ተጠጋ፡፡

وَتَوَكَّلْ عَلَى ٱلْعَزِيزِ ٱلرَّحِيمِ ﴿٢١٧﴾

218. በዚያ ለሶላት በምትቆም ጊዜ በሚያይህ፡፡

ٱلَّذِى يَرَىٰكَ حِينَ تَقُومُ ﴿٢١٨﴾

219. በሰጋጆች ውስጥ መዘዋወርህንም (በሚያየው ጌታህ ላይ ተጠጋ)፡፡

وَتَقَلُّبَكَ فِى ٱلسَّٰجِدِينَ ﴿٢١٩﴾

220. እነሆ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና፡፡

إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلْعَلِيمُ ﴿٢٢٠﴾

221. ሰይጣናት በማን ላይ እንደሚወርዱ ልንገራችሁን

هَلْ أُنَبِّئُكُمْ عَلَىٰ مَن تَنَزَّلُ ٱلشَّيَٰطِينُ ﴿٢٢١﴾

222. በውሸታም ኀጢአተኛ ሁሉ ላይ ይወርዳሉ፡፡

تَنَزَّلُ عَلَىٰ كُلِّ أَفَّاكٍ أَثِيمٍ ﴿٢٢٢﴾

223. የሰሙትን (ወደ ጠንቋዮች) ይጥላሉ፡፡ አብዛኞቻቸውም ውሸታሞች ናቸው፡፡

يُلْقُونَ ٱلسَّمْعَ وَأَكْثَرُهُمْ كَٰذِبُونَ ﴿٢٢٣﴾

224. ባለ ቅኔዎችንም ጠማማዎቹ ይከተሉዋቸዋል፡፡

وَٱلشُّعَرَآءُ يَتَّبِعُهُمُ ٱلْغَاوُۥنَ ﴿٢٢٤﴾

225. እነርሱ በ(ንግግር) ሸለቆ ሁሉ የሚዋልሉ መኾናቸውን አታይምን

أَلَمْ تَرَ أَنَّهُمْ فِى كُلِّ وَادٍ يَهِيمُونَ ﴿٢٢٥﴾

226. እነሱም የማይሠሩትን ነገር የሚናገሩ መኾናቸውን (አታይምን)፤

وَأَنَّهُمْ يَقُولُونَ مَا لَا يَفْعَلُونَ ﴿٢٢٦﴾

227. እነዚያ ያመኑና መልካም ሥራዎችን የሠሩ አላህንም በብዛት ያወሱ ከተበደሉም በኋላ (በቅኔ) የተከላከሉ ሲቀሩ፤ (እነርሱ አይወቀሱም)፡፡ እነዚያም የበደሉ (ከሞቱ በኋላ) እንዴት ያለን መመለስ እንደሚመለሱ በእርግጥ ያውቃሉ፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَعَمِلُوا۟ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَذَكَرُوا۟ ٱللَّهَ كَثِيرًا وَٱنتَصَرُوا۟ مِنۢ بَعْدِ مَا ظُلِمُوا۟ ۗ وَسَيَعْلَمُ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓا۟ أَىَّ مُنقَلَبٍ يَنقَلِبُونَ ﴿٢٢٧﴾

# ሱረቱ አል ነምል

# سورة النمل

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ጠ.ሰ (ጣ ሲን) ይህቺ ከቁርኣኑና ከገላጩ መጽሐፍ አንቀጾች ናት፡፡

طسٓۚ تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱلۡقُرۡءَانِ وَكِتَابٖ مُّبِينٍ ١

2. ለምእምናን መሪና ብስራት ናት፡፡

هُدٗى وَبُشۡرَىٰ لِلۡمُؤۡمِنِينَ ٢

3. ለእነዚያ ሶላትን ለሚሰግዱት ዘካንም ለሚሰጡት እነሱም በመጨረሻይቱ ሕይወት እነሱ የሚያረጋግጡ ለኾኑት፡፡

ٱلَّذِينَ يُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَيُؤۡتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَهُم بِٱلۡأٓخِرَةِ هُمۡ يُوقِنُونَ ٣

4. እነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት ለእነሱ (ከፉ) ሥራዎቻቸውን ሸለምንላቸው፡፡ ስለዚህ እነርሱ ይዋልላሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ زَيَّنَّا لَهُمۡ أَعۡمَٰلَهُمۡ فَهُمۡ يَعۡمَهُونَ ٤

5. እነርሱ እነዚያ ከፉ ቅጣት ለእነርሱ ያላቸው ናቸው፡፡ እነርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም እነርሱ በጣም ከሳሪዎቹ ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ لَهُمۡ سُوٓءُ ٱلۡعَذَابِ وَهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ هُمُ ٱلۡأَخۡسَرُونَ ٥

6. አንተም ቁርኣንን ጥበበኛና ዐዋቂ ከኾነው (ጌታህ) ዘንድ በእርግጥ ትስሰጣለህ፡፡

وَإِنَّكَ لَتُلَقَّى ٱلۡقُرۡءَانَ مِن لَّدُنۡ حَكِيمٍ عَلِيمٍ ٦

7. ሙሳ ለቤተሰቦቹ «እኔ እሳትን አየሁ፡፡ ከእርሷ ወሬን አመጣላችኋለሁ፡፡ ወይም ትሞቁ ዘንድ የተለኮሰ ችቦን አመጣላችኋለሁ» ባለ ጊዜ (የኾነውን አውሳላቸው)፡፡

إِذۡ قَالَ مُوسَىٰ لِأَهۡلِهِۦٓ إِنِّيٓ ءَانَسۡتُ نَارٗا سَـَٔاتِيكُم مِّنۡهَا بِخَبَرٍ أَوۡ ءَاتِيكُم بِشِهَابٖ قَبَسٖ لَّعَلَّكُمۡ تَصۡطَلُونَ ٧

8. በመጣትም ጊዜ እንዲህ በማለት ተጠራ፤ «በእሳቲቱ ያለው ሰውና በዙሪያዋ ያሉም ሁሉ ተባረኩ፡፡ የዐለማትም ጌታ አላህ ጥራት ይገባው፡፡»

فَلَمَّا جَآءَهَا نُودِيَ أَنۢ بُورِكَ مَن فِي ٱلنَّارِ وَمَنۡ حَوۡلَهَا وَسُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٨

9. «ሙሳ ሆይ! እነሆ እኔ አሸናፊው ጥበበኛው አላህ ነኝ፡፡

يَٰمُوسَىٰٓ إِنَّهُۥٓ أَنَا ٱللَّهُ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٩

10. «በትርህንም ጣል» (ተባለ ጣለም)፡፡ እርሷ እንደ ትንሽ እባብ በፍጥነት ስትስለከለክ ባያትም ጊዜ፤ ወደ ኋላ ዞሮ ሸሸ፡፡ አልተመለሰምም፡፡ «ሙሳ ሆይ! አትፈራ፤ እኔ መልክተኞቹ እኔ ዘንድ አይፈሩምና፡፡

وَأَلۡقِ عَصَاكَۚ فَلَمَّا رَءَاهَا تَهۡتَزُّ كَأَنَّهَا جَآنّٞ وَلَّىٰ مُدۡبِرٗا وَلَمۡ يُعَقِّبۡۚ يَٰمُوسَىٰ لَا تَخَفۡ إِنِّي لَا يَخَافُ لَدَيَّ ٱلۡمُرۡسَلُونَ ١٠

11. «ግን የበደለ ሰው ከዚያም ከመጥፎ ሥራው በኋላ መልካምን የለወጠ እኔ መሓሪ አዛኝ ነኝ፡፡

إِلَّا مَن ظَلَمَ ثُمَّ بَدَّلَ حُسْنًۢا بَعْدَ سُوٓءٍ فَإِنِّى غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١١﴾

12. «እጅህንም በአንገትጌህ ውስጥ አግባ፡፡ ያለነውር (ያለ ለምጽ) ነጭ ኾና ትወጣለችና፡፡ በዘጠኝ ተዓምራት ወደ ፈርዖንና ወደ ሕዝቦቹ (ኺድ)፡፡ እነርሱ አመጸኞች ሕዝቦች ናቸውና፡፡

وَأَدْخِلْ يَدَكَ فِى جَيْبِكَ تَخْرُجْ بَيْضَآءَ مِنْ غَيْرِ سُوٓءٍ ۖ فِى تِسْعِ ءَايَٰتٍ إِلَىٰ فِرْعَوْنَ وَقَوْمِهِۦٓ ۚ إِنَّهُمْ كَانُوا۟ قَوْمًا فَٰسِقِينَ ﴿١٢﴾

13. ተዓምራታችንም ግልጽ ኾና በመጣቻቸው ጊዜ «ይህ ግልጽ ድግምት ነው» አሉ፡፡

فَلَمَّا جَآءَتْهُمْ ءَايَٰتُنَا مُبْصِرَةً قَالُوا۟ هَٰذَا سِحْرٌ مُّبِينٌ ﴿١٣﴾

14. ነፍሶቻቸውም ያረጋገጧት ሲኾኑ ለበደልና ለኩራት በእርሷ ካዱ፡፡ የአመጸኞችም ፍጻሜ እንዴት እንደ ነበረ ተመልከት፡፡

وَجَحَدُوا۟ بِهَا وَٱسْتَيْقَنَتْهَآ أَنفُسُهُمْ ظُلْمًا وَعُلُوًّا ۚ فَٱنظُرْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلْمُفْسِدِينَ ﴿١٤﴾

15. ለዳውድና ለሱለይማንም ዕውቀትን በእርግጥ ሰጠናቸው፡፡ አሉም፡- «ምስጋና ለአላህ ለእዚያ ከምእምናን ባሮቹ በብዙዎቹ ላይ ላበለጠን ይገባው፡፡»

وَلَقَدْ ءَاتَيْنَا دَاوُۥدَ وَسُلَيْمَٰنَ عِلْمًا ۖ وَقَالَا ٱلْحَمْدُ لِلَّهِ ٱلَّذِى فَضَّلَنَا عَلَىٰ كَثِيرٍ مِّنْ عِبَادِهِ ٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿١٥﴾

16. ሱለይማንም ዳውድን ወረሰ፡፡ አለም «ሰዎች ሆይ! የበራሪን ንግግር (የወፍን ቋንቋ) ተስተማርን፡፡ ከነገሩም ሁሉ ተሰጠን፡፡ ይህ እርሱ በእርግጥ ግልጽ የኾነ ችሮታ ነው፡፡»

وَوَرِثَ سُلَيْمَٰنُ دَاوُۥدَ ۖ وَقَالَ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ عُلِّمْنَا مَنطِقَ ٱلطَّيْرِ وَأُوتِينَا مِن كُلِّ شَىْءٍ ۖ إِنَّ هَٰذَا لَهُوَ ٱلْفَضْلُ ٱلْمُبِينُ ﴿١٦﴾

17. ለሱለይማንም ሰራዊቶቹ ከጋኔን፣ ከሰውም፣ ከበራሪም የኾኑት ተሰበሰቡ፡፡ እነሱም ይከመከማሉ፡፡

وَحُشِرَ لِسُلَيْمَٰنَ جُنُودُهُۥ مِنَ ٱلْجِنِّ وَٱلْإِنسِ وَٱلطَّيْرِ فَهُمْ يُوزَعُونَ ﴿١٧﴾

18. በጉንዳንም ሸለቆ በመጡ ጊዜ አንዲት ጉንዳን «እናንተ ጉንዳኖች ሆይ! ወደ መኖሪያዎቻችሁ

حَتَّىٰٓ إِذَآ أَتَوْا۟ عَلَىٰ وَادِ ٱلنَّمْلِ قَالَتْ نَمْلَةٌ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّمْلُ ٱدْخُلُوا۟ مَسَٰكِنَكُمْ لَا يَحْطِمَنَّكُمْ سُلَيْمَٰنُ وَجُنُودُهُۥ وَهُمْ لَا يَشْعُرُونَ ﴿١٨﴾

19. ከንግግርዋም እየሳቀ ጥርሱን ፈገግ አደረገ፡፡ «ጌታዬ ሆይ! ያቺን በእኔና በወላጆቼ ላይ የለገስካትን ጸጋህን እንዳመሰግን የምትወደውንም በጎ ሥራ እንድሠራ ምራኝ፡፡ በችሮታህም በመልካሞቹ ባሮችህ ውስጥ አግባኝ» አለ፡፡

فَتَبَسَّمَ ضَاحِكًا مِّن قَوْلِهَا وَقَالَ رَبِّ أَوْزِعْنِىٓ أَنْ أَشْكُرَ نِعْمَتَكَ ٱلَّتِىٓ أَنْعَمْتَ عَلَىَّ وَعَلَىٰ وَٰلِدَىَّ وَأَنْ أَعْمَلَ صَٰلِحًا تَرْضَىٰهُ وَأَدْخِلْنِى بِرَحْمَتِكَ فِى عِبَادِكَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿١٩﴾

20. በራሪዎቹንም ተመለከተ፤ አለም «ሁድሁድን ለምን አላየውም! በእውነቱ ከራቁት ነበርን፡፡

وَتَفَقَّدَ ٱلطَّيْرَ فَقَالَ مَا لِىَ لَآ أَرَى ٱلْهُدْهُدَ أَمْ كَانَ مِنَ ٱلْغَآئِبِينَ ﴿٢٠﴾

21. «ብርቱን ቅጣት በእርግጥ እቀጣዋለሁ፡፡ ወይም በእርግጥ ዐርደዋለሁ፤ ወይም ግልጽ በኾነ አስረጅ ይመጣኛል» (አለ)

لَأُعَذِّبَنَّهُۥ عَذَابًا شَدِيدًا أَوْ لَأَا۟ذْبَحَنَّهُۥٓ أَوْ لَيَأْتِيَنِّى بِسُلْطَٰنٍ مُّبِينٍ ﴿٢١﴾

22. (ወፉ) ዕሩቅ ያልኾነንም ጊዜ ቆዬ፡፡ አለም «ያላወቅከውን ነገር አወቅኩ፡፡ ከሰበእም እርግጠኛን ወሬ አመጣሁልህ፡፡

فَمَكَثَ غَيْرَ بَعِيدٍ فَقَالَ أَحَطتُ بِمَا لَمْ تُحِطْ بِهِۦ وَجِئْتُكَ مِن سَبَإِۭ بِنَبَإٍ يَقِينٍ ﴿٢٢﴾

23. «እኔ የምትገዛቸው የኾኑችን ሴት ከነገሩም ሁሉ የተሰጠችኝ አገኘሁ፡፡ ለእርሷም ታላቅ ዙፋን አልላት፡፡

إِنِّى وَجَدتُّ ٱمْرَأَةً تَمْلِكُهُمْ وَأُوتِيَتْ مِن كُلِّ شَىْءٍ وَلَهَا عَرْشٌ عَظِيمٌ ﴿٢٣﴾

24. «እርስዋንም ሕዝቦችዋንም ከአላህ ሌላ ለፀሐይ ሲሰግዱ አገኘኋቸው፡፡ ሰይጣንም ለእነሱ ሥራዎቻቸውን ሸልሞላቸዋል፡፡ ከእውነተኛውም መንገድ አግዷቸዋል፡፡ ስለዚህ እነሱ (ወደ እውነት) አይምመሩም፡፡»

وَجَدتُّهَا وَقَوْمَهَا يَسْجُدُونَ لِلشَّمْسِ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَزَيَّنَ لَهُمُ ٱلشَّيْطَٰنُ أَعْمَٰلَهُمْ فَصَدَّهُمْ عَنِ ٱلسَّبِيلِ فَهُمْ لَا يَهْتَدُونَ ﴿٢٤﴾

25. ለዚያ በሰማያትና በምድር የተደበቀውን ለሚያወጣው፣ የምትሸሽጉትንና የምትገ ልጹትንም ሁሉ ለሚያውቀው አላህ እንዳይሰግዱ (ሰይጣን አግዷቸዋል)፡፡

أَلَّا يَسْجُدُوا۟ لِلَّهِ ٱلَّذِى يُخْرِجُ ٱلْخَبْءَ فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ وَيَعْلَمُ مَا تُخْفُونَ وَمَا تُعْلِنُونَ ﴿٢٥﴾

26. አላህ ከርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ የታላቁ ዐርሽ (ዙፋን) ጌታ ነው፡፡

ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ رَبُّ ٱلْعَرْشِ ٱلْعَظِيمِ ۩ ﴿٢٦﴾

27. (ሱለይማንም) አለ «እውነት እንደ ተናገርክ ወይም ከውሸታሞቹ እንደ ኾንክ ወደፊት እናያለን፡፡

۞ قَالَ سَنَنظُرُ أَصَدَقْتَ أَمْ كُنتَ مِنَ ٱلْكَٰذِبِينَ ﴿٢٧﴾

28. «ይህንን ደብዳቤዬን ይዘህ ኺድ፡፡ ወደእነርሱም ጣለው፡፡ ከዚያም ከእነሱ ዘወር በል፡፡ ምን እንደሚመልሱም ተመልከት፡፡»

ٱذْهَب بِّكِتَٰبِى هَٰذَا فَأَلْقِهْ إِلَيْهِمْ ثُمَّ تَوَلَّ عَنْهُمْ فَٱنظُرْ مَاذَا يَرْجِعُونَ ﴿٢٨﴾

29. (እርሷም በደረሳት ጊዜ) አለች «እናንተ መማክርቶች ሆይ! እኔ ክብር ያለው ጽሑፍ ወደኔ ተጣለ፡፡

قَالَتْ يَٰٓأَيُّهَا ٱلْمَلَؤُا۟ إِنِّىٓ أُلْقِىَ إِلَىَّ كِتَٰبٌ كَرِيمٌ ﴿٢٩﴾

30. «እርሱ ከሱለይማን ነው፡፡ እርሱም በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩኅ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

إِنَّهُۥ مِن سُلَيْمَٰنَ وَإِنَّهُۥ ﴿٣٠﴾

31. «በእኔ ላይ አትኩሩ፡፡ ታዛዦችም ኾናችሁ ወደኔ ኑ፤ (የሚል ነው)፡፡

أَلَّا تَعْلُوا۟ عَلَىَّ وَأْتُونِى مُسْلِمِينَ ﴿٣١﴾

32. «እናንተ መማክርቶች ሆይ! በነገሬ (የሚበጀውን) ንገሩኝ፡፡ እስከምትገኙልኝ ድረስ አንድንም ነገር ቆራጭ አይደለሁምና» አለች፡፡

قَالَتْ يَٰٓأَيُّهَا ٱلْمَلَؤُا۟ أَفْتُونِى فِىٓ أَمْرِى مَا كُنتُ قَاطِعَةً أَمْرًا حَتَّىٰ تَشْهَدُونِ ﴿٣٢﴾

33. «እኛ የኀይል ባለቤቶች የብርቱ ጦርም ባለቤቶች ነን፡፡ ግን ትዕዛዙ ወደ አንቺ ነው፡፡ ምን እንደምታዢም አስተውዪ፤» አሏት፡፡

قَالُوا۟ نَحْنُ أُو۟لُوا۟ قُوَّةٍ وَأُو۟لُوا۟ بَأْسٍ شَدِيدٍ وَٱلْأَمْرُ إِلَيْكِ فَٱنظُرِى مَاذَا تَأْمُرِينَ ﴿٣٣﴾

34. (እርሷም) አለች «ንጉሦች ከተማን (በኀይል) በገቡባት ጊዜ ያበላሹዋታል፡፡ የተከበሩ ሰዎችዋንም ወራዶች ያደርጋሉ፡፡ እንደዚሁም (እነዚህ) ይሠራሉ፡፡

قَالَتْ إِنَّ ٱلْمُلُوكَ إِذَا دَخَلُوا۟ قَرْيَةً أَفْسَدُوهَا وَجَعَلُوٓا۟ أَعِزَّةَ أَهْلِهَآ أَذِلَّةً ۖ وَكَذَٰلِكَ يَفْعَلُونَ ﴿٣٤﴾

35. «እኔም ወደእነርሱ ገጸ በረከትን የምልክና መልክተኞቹ በምን እንደሚመለሱ የምጠባበቅ ነኝ፡፡»

وَإِنِّي مُرۡسِلَةٌ إِلَيۡهِم بِهَدِيَّةٖ فَنَاظِرَةُۢ بِمَ يَرۡجِعُ ٱلۡمُرۡسَلُونَ ٣٥

36. (መልክተኛው) ሱለይማንንም በመጣው ጊዜ አለ «በገንዘብ ትረዱኛላችሁን አላህም የሰጠኝ ከሰጣችሁ የበለጠ ነው፡፡ ይልቁንም እናንተ በገጸ በረከታችሁ ትደሰታላችሁ፡፡»

فَلَمَّا جَآءَ سُلَيۡمَٰنَ قَالَ أَتُمِدُّونَنِ بِمَالٖ فَمَآ ءَاتَىٰنِۦَ ٱللَّهُ خَيۡرٞ مِّمَّآ ءَاتَىٰكُمۚ بَلۡ أَنتُم بِهَدِيَّتِكُمۡ تَفۡرَحُونَ ٣٦

37. «ወደእነሱ ተመለስ፡፡ ለእነርሱም በእርሷ ችሎታ በሌላቸው ሰራዊት እንመጣባቸዋለን፡፡ ከእርሷም እነርሱ የተዋረዱ ኾነው በእርግጥ እናወጣቸዋለን» (አለ)፡፡

ٱرۡجِعۡ إِلَيۡهِمۡ فَلَنَأۡتِيَنَّهُم بِجُنُودٖ لَّا قِبَلَ لَهُم بِهَا وَلَنُخۡرِجَنَّهُم مِّنۡهَآ أَذِلَّةٗ وَهُمۡ صَٰغِرُونَ ٣٧

38. «እናንተ መኳንንቶች ሆይ! ሙስሊሞች ኾነው ሳይመጡኝ በፊት ዙፋንዋን የሚያመጣልኝ ማንኛችሁ ነው» አለ፡፡

قَالَ يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡمَلَؤُاْ أَيُّكُمۡ يَأۡتِينِي بِعَرۡشِهَا قَبۡلَ أَن يَأۡتُونِي مُسۡلِمِينَ ٣٨

39. ከጋኔን ኀይለኛው «ከችሎትህ ከመነሳትህ በፊት እኔ እርሱን አመጣልሃለሁ፡፡ እኔም በእርሱ ላይ ብርቱ ታማኝ ነኝ» አለ፡፡

قَالَ عِفۡرِيتٞ مِّنَ ٱلۡجِنِّ أَنَا۠ ءَاتِيكَ بِهِۦ قَبۡلَ أَن تَقُومَ مِن مَّقَامِكَۖ وَإِنِّي عَلَيۡهِ لَقَوِيٌّ أَمِينٞ ٣٩

40. ያ እርሱ ዘንድ ከመጽሐፉ ዕውቀት ያለው ሰው (የተገለጸው) «ዓይንህ ወደ አንተ ከመመለሱ በፊት እኔ እርሱን አመጣልሃለሁ» አለ፤ (እንደዚሁም አደረገ)፡፡ እርሱ ዘንድ ረግቶ ባየውም ጊዜ «ይህ ከጌታዬ ችሮታ ነው፡፡ የማመሰግን ወይም የምክድ መኾኔን ሊሞክረኝ (ቸረልኝ)፡፡ ያመሰገነም ሰው የሚያመሰግነው ለራሱ ነው፡፡ የካደም ሰው ጌታዬ ከእርሱ ተብቃቂ ቸር ነው» አለ፡፡

قَالَ ٱلَّذِي عِندَهُۥ عِلۡمٞ مِّنَ ٱلۡكِتَٰبِ أَنَا۠ ءَاتِيكَ بِهِۦ قَبۡلَ أَن يَرۡتَدَّ إِلَيۡكَ طَرۡفُكَۚ فَلَمَّا رَءَاهُ مُسۡتَقِرًّا عِندَهُۥ قَالَ هَٰذَا مِن فَضۡلِ رَبِّي لِيَبۡلُوَنِيٓ ءَأَشۡكُرُ أَمۡ أَكۡفُرُۖ وَمَن شَكَرَ فَإِنَّمَا يَشۡكُرُ لِنَفۡسِهِۦۖ وَمَن كَفَرَ فَإِنَّ رَبِّي غَنِيّٞ كَرِيمٞ ٤٠

41. «ዙፋንዋን ለእርሷ አሳስቱ፡፡ ታውቀው እንደኾነ ወይም ከእነዚያ ከማያወቁት ትኾን እንደሆነ፤ እናያለን፤ » አላቸው፡፡

قَالَ نَكِّرُواْ لَهَا عَرۡشَهَا نَنظُرۡ أَتَهۡتَدِيٓ أَمۡ تَكُونُ مِنَ ٱلَّذِينَ لَا يَهۡتَدُونَ ٤١

42. በመጣች ጊዜ፡- «ዙፋንሽ እንደዚህ ነውን» ተባለች፡፡ «እርሱ ልክ እርሱ ነው መሰለኝ» አለች፡፡ (ሱለይማን) «ከእርሷ በፊትም ዕውቀትን ተሰጠን ሙስሊሞችም ነበርን፤» (አለ)፡፡

فَلَمَّا جَآءَتۡ قِيلَ أَهَٰكَذَا عَرۡشُكِۖ قَالَتۡ كَأَنَّهُۥ هُوَۚ وَأُوتِينَا ٱلۡعِلۡمَ مِن قَبۡلِهَا وَكُنَّا مُسۡلِمِينَ ٤٢

43. ከአላህ ሌላ ትግገዛው የነበረችውንም ከለከላት፡፡ እርሷ ከከሓዲዎች ሕዝቦች ነበረችና፡፡

وَصَدَّهَا مَا كَانَت تَّعۡبُدُ مِن دُونِ ٱللَّهِۖ إِنَّهَا كَانَتۡ مِن قَوۡمٖ كَٰفِرِينَ ٤٣

44. ሕንጻውን ግቢ ተባለች፡፡ ባየቺውም ጊዜ ባሕር ነው ብላ ጠረጠረችው፡፡ ከባቶችዋም ገለጠች፡፡ «እርሱ ከመስተዋት የተለሰለሰ ሕንጻ ነው» አላት፡፡ «ጌታዬ ሆይ! እኔ ነፍሴን በደልኩ፡፡ ከሱለይማንም ጋር ሆኜ ለዓለማት ጌታ ለአላህ ታዘዝኩ» አለች፡፡

قِيلَ لَهَا ٱدْخُلِى ٱلصَّرْحَ ۖ فَلَمَّا رَأَتْهُ حَسِبَتْهُ لُجَّةً وَكَشَفَتْ عَن سَاقَيْهَا ۚ قَالَ إِنَّهُۥ صَرْحٌ مُّمَرَّدٌ مِّن قَوَارِيرَ ۗ قَالَتْ رَبِّ إِنِّى ظَلَمْتُ نَفْسِى وَأَسْلَمْتُ مَعَ سُلَيْمَٰنَ لِلَّهِ رَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٤٤﴾

45. ወደ ሰሙድም ወንድማቸውን ሷሊሕን አላህን ተገዙ በማለት በእርግጥ ላክነው፡፡ ወዲያውም እነሱ የሚነታረኩ ሁለት ጭፍሮች ኾኑ፡፡

وَلَقَدْ أَرْسَلْنَآ إِلَىٰ ثَمُودَ أَخَاهُمْ صَٰلِحًا أَنِ ٱعْبُدُوا۟ ٱللَّهَ فَإِذَا هُمْ فَرِيقَانِ يَخْتَصِمُونَ ﴿٤٥﴾

46. «ሕዝቦቼ ሆይ! ከመልካሙ በፊት በክፉው (ቅጣትን አምጣብን በማለት) ለምን ታስቸኩላላችሁ ይታዘንላችሁ ዘንድ አላህን ምሕረትን አትለምኑምን» አላቸው፡፡

قَالَ يَٰقَوْمِ لِمَ تَسْتَعْجِلُونَ بِٱلسَّيِّئَةِ قَبْلَ ٱلْحَسَنَةِ ۖ لَوْلَا تَسْتَغْفِرُونَ ٱللَّهَ لَعَلَّكُمْ تُرْحَمُونَ ﴿٤٦﴾

47. «ባንተና ከአንተም ጋር ባሉት ሰዎች ምክንያት ገደቢሶች ኾን» አሉት፡፡ «ገደቢስነታችሁ አላህ ዘንድ ነው፤ ይልቁንም እናንተ የምትፈተኑ ሕዝቦች ናችሁ» አላቸው፡፡

قَالُوا۟ ٱطَّيَّرْنَا بِكَ وَبِمَن مَّعَكَ ۚ قَالَ طَٰٓئِرُكُمْ عِندَ ٱللَّهِ ۖ بَلْ أَنتُمْ قَوْمٌ تُفْتَنُونَ ﴿٤٧﴾

48. በከተማይቱም ውስጥ በምድር ውስጥ የሚያበላሹና የማያሳምሩ ዘጠኝ ሰዎች ነበሩ፡፡

وَكَانَ فِى ٱلْمَدِينَةِ تِسْعَةُ رَهْطٍ يُفْسِدُونَ فِى ٱلْأَرْضِ وَلَا يُصْلِحُونَ ﴿٤٨﴾

49. «እርሱንና ቤተሰቦቹን ሌሊት ልንገድል ከዚያም ለዘመዱ የቤተሰቦቹን ጥፋት (መገደላቸውን) አላየንም፤ እኛም እውነተኞች ነን ልንል በአላህ ተማማሉ» አሉ፡፡

قَالُوا۟ تَقَاسَمُوا۟ بِٱللَّهِ لَنُبَيِّتَنَّهُۥ وَأَهْلَهُۥ ثُمَّ لَنَقُولَنَّ لِوَلِيِّهِۦ مَا شَهِدْنَا مَهْلِكَ أَهْلِهِۦ وَإِنَّا لَصَٰدِقُونَ ﴿٤٩﴾

50. ተንኮልንም መከሩ፡፡ እነርሱም የማያወቁ ሲኾኑ በተንኮላቸው አጠፋናቸው፡፡

وَمَكَرُوا۟ مَكْرًا وَمَكَرْنَا مَكْرًا وَهُمْ لَا يَشْعُرُونَ ﴿٥٠﴾

51. የተንኮላቸውም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ እኛ እነርሱንም ሕዝቦቻቸውንም በሙሉ እንዴት እንዳጠፋናቸው ተመልከት፡፡

فَٱنظُرْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ مَكْرِهِمْ أَنَّا دَمَّرْنَٰهُمْ وَقَوْمَهُمْ أَجْمَعِينَ ﴿٥١﴾

52. እኚህም በበደላቸው ምክንያት ባዶዎች ሲሆኑ ቤቶቻቸው ናቸው፡፡ በዚህም ውስጥ ለሚያወቁ ሕዝቦች አስደናቂ ተዓምር አለበት፡፡

فَتِلْكَ بُيُوتُهُمْ خَاوِيَةًۢ بِمَا ظَلَمُوٓا۟ ۗ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَةً لِّقَوْمٍ يَعْلَمُونَ ﴿٥٢﴾

53. እነዚያንም ያመኑትንና ከክሕደት ይጠነቀቁ የነበሩትን አዳን፡፡

وَأَنجَيْنَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَكَانُوا۟ يَتَّقُونَ ﴿٥٣﴾

54. ሉጥንም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፤ «እናንተ የምታዩ ስትኾኑ ፀያፍን ነገር ትሠራላችሁን

وَلُوطًا إِذْ قَالَ لِقَوْمِهِۦٓ أَتَأْتُونَ ٱلْفَٰحِشَةَ وَأَنتُمْ تُبْصِرُونَ ﴿٥٤﴾

55. «እናንተ ከሴቶች አልፋችሁ ወንዶችን ለመከጀል ትመጣላችሁን በእውነቱ እናንተ የምትሳሳቱ ሕዝቦች ናችሁ፡፡»

أَئِنَّكُمْ لَتَأْتُونَ ٱلرِّجَالَ شَهْوَةً مِّن دُونِ ٱلنِّسَآءِ ۚ بَلْ أَنتُمْ قَوْمٌ تَجْهَلُونَ ﴿٥٥﴾

56. የሕዝቦቹም መልስ የሉጥን ቤተሰቦች «ከከተማችሁ አውጡ፡፡ እነርሱ የሚጥራሩ ሰዎች ናቸውና» ማለት እንጅ ሌላ አልነበረም፡፡

۞فَمَا كَانَ جَوَابَ قَوۡمِهِۦٓ إِلَّآ أَن قَالُوٓاْ أَخۡرِجُوٓاْ ءَالَ لُوطٖ مِّن قَرۡيَتِكُمۡۖ إِنَّهُمۡ أُنَاسٞ يَتَطَهَّرُونَ ٥٦

57. እርሱንና ቤተሰቦቹንም አዳን፡፡ ሚስቱ፤ ብቻ ስትቀር፡፡ (በጥፋቱ ውስጥ) ከቀሪዎቹ አደረግናት፡፡

فَأَنجَيۡنَٰهُ وَأَهۡلَهُۥٓ إِلَّا ٱمۡرَأَتَهُۥ قَدَّرۡنَٰهَا مِنَ ٱلۡغَٰبِرِينَ ٥٧

58. በእነርሱም ላይ (የድንጋይ) ዝናብን አዘነብንባቸው፡፡ የተስፈራሪዎቹም ዝናብ ከፉ፡፡

وَأَمۡطَرۡنَا عَلَيۡهِم مَّطَرٗاۖ فَسَآءَ مَطَرُ ٱلۡمُنذَرِينَ ٥٨

59. (ሙሐመድ ሆይ) በል «ምስጋና ለአላህ ይገባው፡፡ በእነዚያም በመረጣቸው ባሮቹ ላይ ሰላም ይውረድ፡፡ አላህ በላጭ ነውን ወይስ ያ የሚያጋሩት (ጣዖት)፡፡

قُلِ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ وَسَلَٰمٌ عَلَىٰ عِبَادِهِ ٱلَّذِينَ ٱصۡطَفَىٰٓۗ ءَآللَّهُ خَيۡرٌ أَمَّا يُشۡرِكُونَ ٥٩

60. ወይም ያ ሰማያትንና ምድርን የፈጠረና ከሰማይም ለእናንተ ውሃን ያወረደው (ይበልጣል ወይስ የሚያጋሩት) በእርሱም ባለውበት የኾኑትን የታጠሩ አትክልቶችን ዛፍዋን ልታበቅሉ ለናንተ ችሎታ ያልነበራችሁን አበቀልን፡፡ ከአላህ ጋር ሌላ አምላክ አለን (የለም)፡፡ ግን እነርሱ (ከእውነት) የሚያዘነብሉ ሕዝቦች ናቸው፡፡

أَمَّنۡ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَأَنزَلَ لَكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَنۢبَتۡنَا بِهِۦ حَدَآئِقَ ذَاتَ بَهۡجَةٖ مَّا كَانَ لَكُمۡ أَن تُنۢبِتُواْ شَجَرَهَآۗ أَءِلَٰهٞ مَّعَ ٱللَّهِۚ بَلۡ هُمۡ قَوۡمٞ يَعۡدِلُونَ ٦٠

61. ወይም ያ ምድርን መርጊያ ያደረገና በመካከሏም ወንዞችን ያደረገ፣ ለእርሷም ጋራዎችን ያደረገ፣ በሁለቱ ባሕሮችም (በጣፋጩና በጨው ባሕር) መካከል ግርዶን ያደረገ (ይበልጣልን ወይስ የሚያጋሩት) ከአላህ ጋር ሌላ አምላክ አለን ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

أَمَّن جَعَلَ ٱلۡأَرۡضَ قَرَارٗا وَجَعَلَ خِلَٰلَهَآ أَنۡهَٰرٗا وَجَعَلَ لَهَا رَوَٰسِيَ وَجَعَلَ بَيۡنَ ٱلۡبَحۡرَيۡنِ حَاجِزًاۗ أَءِلَٰهٞ مَّعَ ٱللَّهِۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٦١

62. ወይም ያ ችግረኛን በለመነው ጊዜ የሚቀበል፣ መከራንም የሚያስወግድ፣ በምድርም ላይ ምትኮች የሚያደረጋችሁ፤ (ይበልጣልን ወይስ የሚያጋሩት) ከአላህ ጋር ሌላ አምላክ አለን ጥቂትንም አትገሠጹም፡፡

أَمَّن يُجِيبُ ٱلۡمُضۡطَرَّ إِذَا دَعَاهُ وَيَكۡشِفُ ٱلسُّوٓءَ وَيَجۡعَلُكُمۡ خُلَفَآءَ ٱلۡأَرۡضِۗ أَءِلَٰهٞ مَّعَ ٱللَّهِۚ قَلِيلٗا مَّا تَذَكَّرُونَ ٦٢

63. ወይም ያ በየብስና በባሕር ጨለማዎች ውስጥ የሚመራችሁ ነፋሶችንም ከዝናሙ በፊት አብሳሪ ኾነው የሚልክ (ይበልጣልን ወይስ የሚያጋሩት) ከአላህ ጋር ሌላ አምላክ አለን አላህ (በእርሱ) ከሚያጋሩዋቸው ሁሉ ላቀ፡፡

أَمَّن يَهۡدِيكُمۡ فِي ظُلُمَٰتِ ٱلۡبَرِّ وَٱلۡبَحۡرِ وَمَن يُرۡسِلُ ٱلرِّيَٰحَ بُشۡرَۢا بَيۡنَ يَدَيۡ رَحۡمَتِهِۦٓۗ أَءِلَٰهٞ مَّعَ ٱللَّهِۚ تَعَٰلَى ٱللَّهُ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ٦٣

64. ወይም ያ መፍጠርን የሚጀምር ከዚያም የሚመልሰው ከሰማይና ከምድርም ሲሳይን የሚሰጣችሁ አምላክ (ይበልጣልን ወይስ የሚያጋሩት) ከአላህ ጋር ሌላ አምላክ አለን «እውነተኞች እንደኾናችሁ፤ አስረጃችሁን አምጡ» በላቸው፡፡

أَمَّن يَبۡدَؤُاْ ٱلۡخَلۡقَ ثُمَّ يُعِيدُهُۥ وَمَن يَرۡزُقُكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِۗ أَءِلَٰهٞ مَّعَ ٱللَّهِۚ قُلۡ هَاتُواْ بُرۡهَٰنَكُمۡ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٦٤

قُل لَّا يَعۡلَمُ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ ٱلۡغَيۡبَ إِلَّا ٱللَّهُۚ وَمَا يَشۡعُرُونَ أَيَّانَ يُبۡعَثُونَ ﴿٦٥﴾

65. «በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ ሩቅን ምስጢር አያውቅም፡፡ ግን አላህ (ያውቀዋል)፡፡ መቼ እንደሚቀሰቀሱም አያውቁም» በላቸው፡፡

بَلِ ٱدَّٰرَكَ عِلۡمُهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِۚ بَلۡ هُمۡ فِي شَكّٖ مِّنۡهَاۖ بَلۡ هُم مِّنۡهَا عَمُونَ ﴿٦٦﴾

66. በእውነት የመጨረሻይቱን ዓለም (ኹኔታ) ማወቃቸው ተሟላን አይደለም እነርሱ ከእርሷ በመጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡ በእውነትም እነርሱ ከእርሷ ዕውሮች ናቸው፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَءِذَا كُنَّا تُرَٰبٗا وَءَابَآؤُنَآ أَئِنَّا لَمُخۡرَجُونَ ﴿٦٧﴾

67. እነዚያም የካዱት አሉ «እኛም አባቶቻችንም ዐፈር በኾን ጊዜ እኛ (ከመቃብር) የምንወጣ ነን

لَقَدۡ وُعِدۡنَا هَٰذَا نَحۡنُ وَءَابَآؤُنَا مِن قَبۡلُ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّآ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿٦٨﴾

68. «ይህንን እኛም ከፊት የነበሩት አባቶቻችንም በእርግጥ ተቀጥረንበታል፡፡ ይህ የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ተረቶች እንጅ ሌላ አይደለም» (አሉ)፡፡

قُلۡ سِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَٱنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ﴿٦٩﴾

69. «በምድር ላይ ኺዱ፡፡ የአመጸኞችም መጨረሻ እንዴት እንደ ነበረ ተመልከቱ» በላቸው፡፡

وَلَا تَحۡزَنۡ عَلَيۡهِمۡ وَلَا تَكُن فِي ضَيۡقٖ مِّمَّا يَمۡكُرُونَ ﴿٧٠﴾

70. በእነሱም ላይ አትዘን፡፡ ከሚመክሩብህም ነገር በጭንቀት ውስጥ አትኹን፡፡

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلۡوَعۡدُ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ﴿٧١﴾

71. «እውነተኞችም እንደ ኾናችሁ ይህ ቀጠሮ መቼ ነው» ይላሉ፡፡

قُلۡ عَسَىٰٓ أَن يَكُونَ رَدِفَ لَكُم بَعۡضُ ٱلَّذِي تَسۡتَعۡجِلُونَ ﴿٧٢﴾

72. «የዚያ የምትቻኮሉበት ከፊሉ ለእናንተ የቀረበ መኾኑ ተረጋግጧል» በላቸው፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَذُو فَضۡلٍ عَلَى ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَشۡكُرُونَ ﴿٧٣﴾

73. ጌታህም በሰዎች ላይ በእርግጥ የችሮታ ባለቤት ነው፡፡ ግን አብዛኛዎቻቸው አያመሰግኑም፡፡

وَإِنَّ رَبَّكَ لَيَعۡلَمُ مَا تُكِنُّ صُدُورُهُمۡ وَمَا يُعۡلِنُونَ ﴿٧٤﴾

74. ጌታህም ልቦቻቸው የሚደብቁትንና የሚገልጹትን ያውቃል፡፡

وَمَا مِنۡ غَآئِبَةٖ فِي ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِ إِلَّا فِي كِتَٰبٖ مُّبِينٍ ﴿٧٥﴾

75. በሰማይና በምድር ውስጥ ምንም የተደበቀ ነገር የለም ገላጭ በኾነው መጽሐፍ ውስጥ ያለ ቢኾን እንጅ፡
፡

إِنَّ هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانَ يَقُصُّ عَلَىٰ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ أَكۡثَرَ ٱلَّذِي هُمۡ فِيهِ يَخۡتَلِفُونَ ﴿٧٦﴾

76. ይህ ቁርኣን በእስራኤል ልጆች ላይ የእነዚያን እነርሱ በእርሱ የሚለያዩበትን አብዛኛውን ይነግራል፡፡

وَإِنَّهُۥ لَهُدٗى وَرَحۡمَةٞ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٧٧﴾

77. እርሱም ለምእምናን መምሪያና እዝነት ነው፡፡

إِنَّ رَبَّكَ يَقۡضِي بَيۡنَهُم بِحُكۡمِهِۦۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿٧٨﴾

78. ጌታህ በመካከላቸው በትክክል ፍርዱ ይፈርዳል፡፡ እርሱም አሸናፊው ዐዋቂው ነው፡፡

79. በአላህም ላይ ተጠጋ፡፡ አንተ ግልጽ በኾነው እውነት ላይ ነህና፡፡

فَتَوَكَّلْ عَلَى ٱللَّهِ ۖ إِنَّكَ عَلَى ٱلْحَقِّ ٱلْمُبِينِ ٧٩

80. አንተ ሙታንን አታሰማም፡፡ ደንቆሮዎችንም የሚተው ኾነው በዞሩ ጊዜ ጥሪን አታሰማም፡፡

إِنَّكَ لَا تُسْمِعُ ٱلْمَوْتَىٰ وَلَا تُسْمِعُ ٱلصُّمَّ ٱلدُّعَآءَ إِذَا وَلَّوْا۟ مُدْبِرِينَ ٨٠

81. አንተም (ልበ) ዕውሮችን ከጥመታቸው አቅኚ አይደለህም፡፡ በአንቀጾቻችን የሚያምኑትን በስተቀር አታሰማም፡፡ እነርሱ ፍጹም ታዛዦች ናቸውና፡፡

وَمَآ أَنتَ بِهَٰدِى ٱلْعُمْىِ عَن ضَلَٰلَتِهِمْ ۖ إِن تُسْمِعُ إِلَّا مَن يُؤْمِنُ بِـَٔايَٰتِنَا فَهُم مُّسْلِمُونَ ٨١

82. በእነርሱም ላይ (የቅጣት) ቃሉ በተረጋገጠ ጊዜ ሰዎቹ በአንቀጾቻችን የማያረጋግጡ እንደነበሩ የምትነግራቸውን እንስሳ ለእነርሱ ከምድር እናወጣለን፡ ፡

۞ وَإِذَا وَقَعَ ٱلْقَوْلُ عَلَيْهِمْ أَخْرَجْنَا لَهُمْ دَآبَّةً مِّنَ ٱلْأَرْضِ تُكَلِّمُهُمْ أَنَّ ٱلنَّاسَ كَانُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَا لَا يُوقِنُونَ ٨٢

83. ከሕዝቦቹም ሁሉ ባንቀፆቻችን የሚያስተባብሉትን ጭፍሮች የምንሰበስብበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ እነሱም ይከመከማሉ፡፡

وَيَوْمَ نَحْشُرُ مِن كُلِّ أُمَّةٍ فَوْجًا مِّمَّن يُكَذِّبُ بِـَٔايَٰتِنَا فَهُمْ يُوزَعُونَ ٨٣

84. በመጡም ጊዜ (አላህ) ይላቸዋል «በአንቀጾቼ እርሷን በማወቅ ያላዳረሳችሁ ስትሆኑ አስተባበላችሁን ወይስ ምንን ትሠሩ ነበራችሁ»

حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءُو قَالَ أَكَذَّبْتُم بِـَٔايَٰتِى وَلَمْ تُحِيطُوا۟ بِهَا عِلْمًا أَمَّاذَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ٨٤

85. በመበደላቸውም በእነርሱ ላይ ቃሉ ይፈጸምባቸዋል፡፡ እነርሱም አይናገሩም፡፡

وَوَقَعَ ٱلْقَوْلُ عَلَيْهِم بِمَا ظَلَمُوا۟ فَهُمْ لَا يَنطِقُونَ ٨٥

86. እኛ ሌሊትን በእርሱ ውስጥ እንዲያርፉበት ቀንንም የሚያሳይ እንዳደረግን አያዩምን ለሚያምኑ ሕዝቦች በዚህ ውስጥ ተዓምራቶች አሉበት፡፡

أَلَمْ يَرَوْا۟ أَنَّا جَعَلْنَا ٱلَّيْلَ لِيَسْكُنُوا۟ فِيهِ وَٱلنَّهَارَ مُبْصِرًا ۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَٰتٍ لِّقَوْمٍ يُؤْمِنُونَ ٨٦

87. በቀንዱም በሚነፋ ቀን በሰማያት ውስጥ ያሉትና በምድርም ውስጥ ያሉት ሁሉ አላህ የሻው ነገር ብቻ ሲቀር በሚደነግጡ ጊዜ (የሚኾነውን አስታውስ)፡፡ ሁሉም የተናነሱ ኾነውም ወደርሱ ይመጣሉ፡፡

وَيَوْمَ يُنفَخُ فِى ٱلصُّورِ فَفَزِعَ مَن فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَن فِى ٱلْأَرْضِ إِلَّا مَن شَآءَ ٱللَّهُ ۚ وَكُلٌّ أَتَوْهُ دَٰخِرِينَ ٨٧

88. ጋራዎችንም እርሷ እንደ ደመና አስተላለፍ የምታልፍ ስትኾን የቆመች ናት ብለህ የምታስባት ሆና ታያታለህ፡፡ የዚያን ነገሩን ሁሉ ያጠነከረውን የአላህን ጥበብ (ተመልከት)፡፡ እርሱ በምትሠሩት ሁሉ ውስጥ ዐዋቂ ነው፡፡

وَتَرَى ٱلْجِبَالَ تَحْسَبُهَا جَامِدَةً وَهِىَ تَمُرُّ مَرَّ ٱلسَّحَابِ ۚ صُنْعَ ٱللَّهِ ٱلَّذِىٓ أَتْقَنَ كُلَّ شَىْءٍ ۚ إِنَّهُۥ خَبِيرٌۢ بِمَا تَفْعَلُونَ ٨٨

89. በመልካም ሥራ የመጣ ሰው ለእርሱ ከእርስዋ የበለጠ ምንዳ አልለው፡፡ እነርሱም በዚያ ቀን ከድንጋጤ ጸጥተኞች ናቸው፡፡

مَن جَآءَ بِٱلْحَسَنَةِ فَلَهُۥ خَيْرٌ مِّنْهَا وَهُم مِّن فَزَعٍ يَوْمَئِذٍ ءَامِنُونَ ٨٩

90. በመጥፎም የመጡ ሰዎች ፊቶቻቸው በእሳት ውስጥ ይደፋሉ፡፡ «ትሠሩት የነበራችሁትን እንጅ አትመነዱም» (ይባላሉ)፡፡

وَمَن جَآءَ بِٱلسَّيِّئَةِ فَكُبَّتْ وُجُوهُهُمْ فِى ٱلنَّارِ هَلْ تُجْزَوْنَ إِلَّا مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ٩٠

91. የታዘዝኩት የዚህችን አገር ጌታ ያንን ክልል ያደረጋትን እንድግገዛ ብቻ ነው:: ነገሩንም ሁሉ የእርሱ ነው:: ከሙስሊሞችም እንድኾን ታዝዣለሁ (በላቸው)::

إِنَّمَآ أُمِرۡتُ أَنۡ أَعۡبُدَ رَبَّ هَٰذِهِ ٱلۡبَلۡدَةِ ٱلَّذِي حَرَّمَهَا وَلَهُۥ كُلُّ شَيۡءٖۖ وَأُمِرۡتُ أَنۡ أَكُونَ مِنَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ٩١

92. ቁርአንንም እንዳነብ (ታዝዣለሁ):: የተመራም ሰው የሚመራው ለእራሱ ብቻ ነው:: የተሳሳተም ሰው «እኔ ከአስጠንቃቂዎች ነኝ እንጅ ሌላ አይደለሁም» በለው::

وَأَنۡ أَتۡلُوَاْ ٱلۡقُرۡءَانَۖ فَمَنِ ٱهۡتَدَىٰ فَإِنَّمَا يَهۡتَدِي لِنَفۡسِهِۦۖ وَمَن ضَلَّ فَقُلۡ إِنَّمَآ أَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُنذِرِينَ ٩٢

93. ምስጋናም ለአላህ ነው:: ተዓምራቶቹን ወደፊት ያሳያችኋል:: «ታውቋትምአላችሁ» በላቸው:: ጌታህም ከምትሠሩት ሁሉ ዘንጊ አይደለም::

وَقُلِ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ سَيُرِيكُمۡ ءَايَٰتِهِۦ فَتَعۡرِفُونَهَاۚ وَمَا رَبُّكَ بِغَٰفِلٍ عَمَّا تَعۡمَلُونَ ٩٣

# ሱረቱ አል ቀሶስ

# سورة القصص

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ጠ.ሰ.መ (ጣ ሲን ሚም)::

طسٓمٓ ١

2. ይህቺ ገላጭ ከሆነው መጽሐፍ አንቀጾች ናት::

تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱلۡكِتَٰبِ ٱلۡمُبِينِ ٢

3. ከሙሳና ከፈርዖን ዜና እውነተኞች ስንኾን ለሚያምኑ ሕዝቦች ባንተ ላይ እናነባለን::

نَتۡلُواْ عَلَيۡكَ مِن نَّبَإِ مُوسَىٰ وَفِرۡعَوۡنَ بِٱلۡحَقِّ لِقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ٣

4. ፈርዖን በምድር ላይ ተንበጣረረ:: ነዋሪዎቿንም የተከፋፈሉ ጓዶች አደረጋቸው:: ከእነርሱ ጭፍሮችን ያዳከማል:: ወንዶች ልጆቻቸውን በብዛት ያርዳል:: ሴቶቻቸውንም ይተዋል፤ እርሱ ከሚያበላሹት ሰዎች ነበርና::

إِنَّ فِرۡعَوۡنَ عَلَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَجَعَلَ أَهۡلَهَا شِيَعٗا يَسۡتَضۡعِفُ طَآئِفَةٗ مِّنۡهُمۡ يُذَبِّحُ أَبۡنَآءَهُمۡ وَيَسۡتَحۡيِۦ نِسَآءَهُمۡۚ إِنَّهُۥ كَانَ مِنَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ٤

5. በእነዚያም በምድር ውስጥ በተጨቆኑ ላይ ልንለግስ፣ መሪዎችም ልናደርጋቸው ወራሾችም ልናደርጋቸው እንሻለን::

وَنُرِيدُ أَن نَّمُنَّ عَلَى ٱلَّذِينَ ٱسۡتُضۡعِفُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَنَجۡعَلَهُمۡ أَئِمَّةٗ وَنَجۡعَلَهُمُ ٱلۡوَٰرِثِينَ ٥

6. ለእነርሱም በምድር ላይ ልናስመች ፈርዖንንና ሃማንንም ሰራዊቶቻቸውንም ከእነሱ ይፈሩት የነበሩትን ነገር ልናሳያቸው (እንሻለን)፡፡

وَنُمَكِّنَ لَهُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَنُرِيَ فِرۡعَوۡنَ وَهَٰمَٰنَ وَجُنُودَهُمَا مِنۡهُم مَّا كَانُواْ يَحۡذَرُونَ ٦

7. ወደ ሙሳም እናት «አጥቢው፣ በርሱም ላይ በፈራሽ ጊዜ በባሕሩ ውስጥ ጣይው አትፈሪም፣ አትዘኝም፣ እኛ ወዳንቺ መላሾቹና ከመልክተኞቹም አድራጊዎቹ ነንና» ማለትን አመለከትን፡፡

وَأَوۡحَيۡنَآ إِلَىٰٓ أُمِّ مُوسَىٰٓ أَنۡ أَرۡضِعِيهِۖ فَإِذَا خِفۡتِ عَلَيۡهِ فَأَلۡقِيهِ فِي ٱلۡيَمِّ وَلَا تَخَافِي وَلَا تَحۡزَنِيٓۖ إِنَّا رَآدُّوهُ إِلَيۡكِ وَجَاعِلُوهُ مِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ٧

8. የፈርዖን ቤተሰቦችም (መጨረሻው) ለእነርሱ ጠላት ሐዘንም ይሆን ዘንድ አነሱት፡፡ ፈርዖንና ሃማንም ሰራዊቶቻቸውም ሀጢአተኞች ነበሩ፡፡

فَٱلۡتَقَطَهُۥٓ ءَالُ فِرۡعَوۡنَ لِيَكُونَ لَهُمۡ عَدُوّٗا وَحَزَنًاۗ إِنَّ فِرۡعَوۡنَ وَهَٰمَٰنَ وَجُنُودَهُمَا كَانُواْ خَٰطِـِٔينَ ٨

9. የፈርዖንም ሚስት «ለእኔ የዓይኔ መርጊያ ነው፡፡ ለአንተም፡፡ አትግደሉት፡፡ ሊጠቅመን ወይም ልጅ አድርገን ልንይዘው ይከጀላልና» አለች፡፡ እነርሱም (ፍጻሜውን) የማያውቁ ሆነው (አነሱት)፡፡

وَقَالَتِ ٱمۡرَأَتُ فِرۡعَوۡنَ قُرَّتُ عَيۡنٖ لِّي وَلَكَۖ لَا تَقۡتُلُوهُ عَسَىٰٓ أَن يَنفَعَنَآ أَوۡ نَتَّخِذَهُۥ وَلَدٗا وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ٩

10. የሙሳም እናት ልብ ባዶ ሆነ፡፡ ከምእምናን ትሆን ዘንድ በልቧ ላይ ባላጠነከርን ኖሮ ልትገልጸው ቀርባ ነበር፡፡

وَأَصۡبَحَ فُؤَادُ أُمِّ مُوسَىٰ فَٰرِغًاۖ إِن كَادَتۡ لَتُبۡدِي بِهِۦ لَوۡلَآ أَن رَّبَطۡنَا عَلَىٰ قَلۡبِهَا لِتَكُونَ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٠

11. ለእኅቱም ተከታተይው አለቻት፡፡ እርሱንም እነሱ የማያውቁ ሲሆኑ በሩቅ ሆና አየችው፡፡

وَقَالَتۡ لِأُخۡتِهِۦ قُصِّيهِۖ فَبَصُرَتۡ بِهِۦ عَن جُنُبٖ وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ١١

12. (ወደናቱ ከመመለሱ) በፊትም አጥቢዎችን (መጥባትን) በእርሱ ላይ እርም አደረግን፡፡ (እኅቱ) «ለእናንተ የሚያሳድጉላችሁን እነርሱም ለእርሱ ቅን አገልጋዮች የሆኑን ቤተሰቦች ላመልክታችሁን» አለችም፡፡

۞وَحَرَّمۡنَا عَلَيۡهِ ٱلۡمَرَاضِعَ مِن قَبۡلُ فَقَالَتۡ هَلۡ أَدُلُّكُمۡ عَلَىٰٓ أَهۡلِ بَيۡتٖ يَكۡفُلُونَهُۥ لَكُمۡ وَهُمۡ لَهُۥ نَٰصِحُونَ ١٢

13. ወደእናቱም ዓይንዋ እንድትረጋ፣ እንዳታዝንም፣ የአላህም የተስፋ ቃል እርግጥ መሆኑን እንድታውቅ መለስነው፡፡ ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

فَرَدَدۡنَٰهُ إِلَىٰٓ أُمِّهِۦ كَيۡ تَقَرَّ عَيۡنُهَا وَلَا تَحۡزَنَ وَلِتَعۡلَمَ أَنَّ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٞ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ١٣

14. ብርታቱንም በደረሰና በተስተካከለ ጊዜ ጥበብንና ዕውቀትን ሰጠነው፡፡ እንዲሁም መልካም ሠሪዎችን እንመነዳለን፡፡

وَلَمَّا بَلَغَ أَشُدَّهُۥ وَٱسۡتَوَىٰٓ ءَاتَيۡنَٰهُ حُكۡمٗا وَعِلۡمٗاۚ وَكَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٤

15. ከተማይቱንም ሰዎቿ በዝንጋቴ ጊዜ ላይ ሆነው ሳሉ ገባ፡፡ በእርሷም ውስጥ የሚጋደሉን ሁለት ሰዎችን አገኘ፡፡ ይህ ከወገኑ ነው፤ ይህም ከጠላቱ ነው፡፡ ያም ከወገኑ የሆነው ሰው በዚያ ከጠላቱ በሆነው ሰው ላይ እርዳታን ጠየቀው፡፡ ሙሳም በጡጫ መታው፡፡ ገደለውም፡፡ ይህ ከሰይጣን ሥራ ነው፡፡ እርሱ ግልጽ አሳሳች ጠላት ነውና አለ፡፡

وَدَخَلَ ٱلۡمَدِينَةَ عَلَىٰ حِينِ غَفۡلَةٖ مِّنۡ أَهۡلِهَا فَوَجَدَ فِيهَا رَجُلَيۡنِ يَقۡتَتِلَانِ هَٰذَا مِن شِيعَتِهِۦ وَهَٰذَا مِنۡ عَدُوِّهِۦۖ فَٱسۡتَغَٰثَهُ ٱلَّذِي مِن شِيعَتِهِۦ عَلَى ٱلَّذِي مِنۡ عَدُوِّهِۦ فَوَكَزَهُۥ مُوسَىٰ فَقَضَىٰ عَلَيۡهِۖ قَالَ هَٰذَا مِنۡ عَمَلِ ٱلشَّيۡطَٰنِۖ إِنَّهُۥ عَدُوّٞ مُّضِلّٞ مُّبِينٞ ﴿١٥﴾

16. «ጌታዬ ሆይ! እኔ ነፍሴን በደልኩ፡፡ ለእኔም ማር አለ፡፡» ለእርሱም ምሕረት አደረገለት እርሱ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّي ظَلَمۡتُ نَفۡسِي فَٱغۡفِرۡ لِي فَغَفَرَ لَهُۥٓۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿١٦﴾

17. «ጌታዬ ሆይ! በእኔ ላይ በመለገስህ ይሁንብኝ (ከስህተቴ እጸጸታለሁ)፤ ለአመጸኞችም ፈጽሞ ረዳት አልሆንም አለ፡፡

قَالَ رَبِّ بِمَآ أَنۡعَمۡتَ عَلَيَّ فَلَنۡ أَكُونَ ظَهِيرٗا لِّلۡمُجۡرِمِينَ ﴿١٧﴾

18. በከተማይቱም ውስጥ ፈሪ የሚጠባበቅ ሆኖ አደረ፡ ፡ በድንገትም ያ ትላንት እርዳታን የጠየቀው ሰው በጩኸት እርዳታን ይጠይቀዋል፡፡ ሙሳ ለርሱ «አንተ በእርግጥ ግልጽ ጠማማ ነህ» አለው፡፡

فَأَصۡبَحَ فِي ٱلۡمَدِينَةِ خَآئِفٗا يَتَرَقَّبُ فَإِذَا ٱلَّذِي ٱسۡتَنصَرَهُۥ بِٱلۡأَمۡسِ يَسۡتَصۡرِخُهُۥۚ قَالَ لَهُۥ مُوسَىٰٓ إِنَّكَ لَغَوِيّٞ مُّبِينٞ ﴿١٨﴾

19. (ሙሳ) ያንን እርሱ ለሁለቱም ጠላት የሆነውን ሰው በኃይል ሊይዘው በፈለገም ጊዜ «ሙሳ ሆይ! በትላንትናው ቀን ነፍስን እንደ ገደልክ ልትገድለኝ ትፈልጋለህን በምድር ለይ ጨካኝ መሆንን እንጅ ሌላ አትፈልግም፡፡ ከመልካም ሠሪዎችም መሆንን አትፈልግም» አለው፡፡

فَلَمَّآ أَنۡ أَرَادَ أَن يَبۡطِشَ بِٱلَّذِي هُوَ عَدُوّٞ لَّهُمَا قَالَ يَٰمُوسَىٰٓ أَتُرِيدُ أَن تَقۡتُلَنِي كَمَا قَتَلۡتَ نَفۡسَۢا بِٱلۡأَمۡسِۖ إِن تُرِيدُ إِلَّآ أَن تَكُونَ جَبَّارٗا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا تُرِيدُ أَن تَكُونَ مِنَ ٱلۡمُصۡلِحِينَ ﴿١٩﴾

20. ከከተማይቱም ዳርቻ አንድ ሰው እየሮጠ መጣ፡፡ «ሙሳ ሆይ! ሹማምንቶቹ ሊገድሉህ ባንተ ይመካከራሉና ውጣ፡፡ እኔ ላንተ ከመካሪዎች ነኝና» አለው፡፡

وَجَآءَ رَجُلٞ مِّنۡ أَقۡصَا ٱلۡمَدِينَةِ يَسۡعَىٰ قَالَ يَٰمُوسَىٰٓ إِنَّ ٱلۡمَلَأَ يَأۡتَمِرُونَ بِكَ لِيَقۡتُلُوكَ فَٱخۡرُجۡ إِنِّي لَكَ مِنَ ٱلنَّٰصِحِينَ ﴿٢٠﴾

21. የፈራና የሚጠባበቅ ሆኖም ከእርሷ ወጣ፡፡ «ጌታዬ ሆይ! ከበደለኞቹ ሕዝቦች አድነኝ» አለ፡፡

فَخَرَجَ مِنۡهَا خَآئِفٗا يَتَرَقَّبُۖ قَالَ رَبِّ نَجِّنِي مِنَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٢١﴾

22. ወደ መድየን አቅጣጫ ፊቱን ባዞረ ጊዜም «ጌታዬ ቀጥተኛውን መንገድ ሊመራኝ እከጅላለሁ» አለ፡፡

وَلَمَّا تَوَجَّهَ تِلۡقَآءَ مَدۡيَنَ قَالَ عَسَىٰ رَبِّيٓ أَن يَهۡدِيَنِي سَوَآءَ ٱلسَّبِيلِ ﴿٢٢﴾

23. ወደ መድየንም ውሃ በመጣ ጊዜ በእርሱ ላይ ከሰዎች ጭፍሮችን (መንጋዎቻቸውን) የሚያጠጡ ሆነው አገኘ፡፡ ከእነርሱ በታችም (ከውሃው መንጎቻቸውን) የሚከለክሉን ሁለት ሴቶች አገኘ፡፡ «ነገራችሁ ምንድን ነው» አላቸው፡፡ «እረኞቹ ሁሉ (መንጋዎቻቸውን) እስከሚመልሱ አናጠጣም፡፡ አባታችንም ትልቅ ሽማግሌ ነው» አሉት፡፡

وَلَمَّا وَرَدَ مَآءَ مَدۡيَنَ وَجَدَ عَلَيۡهِ أُمَّةً مِّنَ ٱلنَّاسِ يَسۡقُونَ وَوَجَدَ مِن دُونِهِمُ ٱمۡرَأَتَيۡنِ تَذُودَانِۖ قَالَ مَا خَطۡبُكُمَاۖ قَالَتَا لَا نَسۡقِي حَتَّىٰ يُصۡدِرَ ٱلرِّعَآءُۖ وَأَبُونَا شَيۡخٞ كَبِيرٞ ﴿٢٣﴾

24. ለሁለቱም አጠጣላቸው፡፡ ከዚያም ወደ ጥላው ዘወር አለ፡፡ «ጌታዬ ሆይ! እኔ ከመልካም ነገር ወደኔ ለምታወርደው ፈላጊ ነኝ» አለ፡፡

فَسَقَىٰ لَهُمَا ثُمَّ تَوَلَّىٰٓ إِلَى ٱلظِّلِّ فَقَالَ رَبِّ إِنِّي لِمَآ أَنزَلۡتَ إِلَيَّ مِنۡ خَيۡرٖ فَقِيرٞ ﴿٢٤﴾

25. ከሁለቱ አንደኛይቱም ከሐፍረት ጋር የምትኼድ ሆና መጣችው፡፡ «አባቴ ለእኛ ያጠጣህልንን ዋጋ ሊሰጥህ ይጠራሃል» አለችው፡፡ ወደእርሱ በመጣና ወሬውን በእርሱ ላይ በተረከለትም ጊዜ «አትፍራ ከበደለኞቹ ሕዝቦች ድነሃል» አለው፡፡

فَجَآءَتۡهُ إِحۡدَىٰهُمَا تَمۡشِي عَلَى ٱسۡتِحۡيَآءٖ قَالَتۡ إِنَّ أَبِي يَدۡعُوكَ لِيَجۡزِيَكَ أَجۡرَ مَا سَقَيۡتَ لَنَاۚ فَلَمَّا جَآءَهُۥ وَقَصَّ عَلَيۡهِ ٱلۡقَصَصَ قَالَ لَا تَخَفۡۖ نَجَوۡتَ مِنَ ٱلۡقَوۡمِ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٢٥﴾

26. ከሁለቱ አንደኛይቱም «አባቴ ሆይ ቅጠረው፡፡ ከቀጠርከው ሰው ሁሉ በላጩ ብርቱው ታማኙ ነውና» አለችው፡፡

قَالَتۡ إِحۡدَىٰهُمَا يَٰٓأَبَتِ ٱسۡتَـٔۡجِرۡهُۖ إِنَّ خَيۡرَ مَنِ ٱسۡتَـٔۡجَرۡتَ ٱلۡقَوِيُّ ٱلۡأَمِينُ ﴿٢٦﴾

27. «ስምንትን ዓመታት ልታገለግለኝ እኔ ከእነዚህ ሁለት ሴቶች ልጆቼ አንዷቱን ላጋባህ እሻለሁ፡፡ ዐስርን ብትሞላም ከአንተ ነው፡፡ ባንተ ላይ ማስቸገርንም አልሻም፡፡ አላህ የሻ እንደ ኾነ ከመልካሞቹ ሰዎች ኾኜ ታገኘኛለህ» አለው፡፡

قَالَ إِنِّيٓ أُرِيدُ أَنۡ أُنكِحَكَ إِحۡدَى ٱبۡنَتَيَّ هَٰتَيۡنِ عَلَىٰٓ أَن تَأۡجُرَنِي ثَمَٰنِيَ حِجَجٖۖ فَإِنۡ أَتۡمَمۡتَ عَشۡرٗا فَمِنۡ عِندِكَۖ وَمَآ أُرِيدُ أَنۡ أَشُقَّ عَلَيۡكَۚ سَتَجِدُنِيٓ إِن شَآءَ ٱللَّهُ مِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿٢٧﴾

28. (ሙሳም) «ይህ (ውለታ) በእኔና ባንተ መካከል (ረጊ) ነው፡፡ ከሁለቱ ጊዜያቶች ማንኛውንም ብፈጽም በእኔ ላይ ወሰን ማለፍ የለም፡፡ አላህም በምንለነው ላይ ምስክር» ነው አለ፡፡

قَالَ ذَٰلِكَ بَيۡنِي وَبَيۡنَكَۖ أَيَّمَا ٱلۡأَجَلَيۡنِ قَضَيۡتُ فَلَا عُدۡوَٰنَ عَلَيَّۖ وَٱللَّهُ عَلَىٰ مَا نَقُولُ وَكِيلٞ ﴿٢٨﴾

29. ሙሳም ጊዜውን በጨረሰና ከቤተሰቦቹ ጋር በኼደ ጊዜ ከጡር ተራራ ጎን እሳትን አየ፡፡ ለቤተሰቡ (እዚህ) «ቆዩ፡፡ እኔ እሳትን አየሁ፡፡ ከእርሷ ወሬን ወይም ትሞቁ ዘንድ ከእሳት ትንታግን አመጣላችኋለሁ» አለ፡፡

۞فَلَمَّا قَضَىٰ مُوسَى ٱلۡأَجَلَ وَسَارَ بِأَهۡلِهِۦٓ ءَانَسَ مِن جَانِبِ ٱلطُّورِ نَارٗاۖ قَالَ لِأَهۡلِهِ ٱمۡكُثُوٓاْ إِنِّيٓ ءَانَسۡتُ نَارٗا لَّعَلِّيٓ ءَاتِيكُم مِّنۡهَا بِخَبَرٍ أَوۡ جَذۡوَةٖ مِّنَ ٱلنَّارِ لَعَلَّكُمۡ تَصۡطَلُونَ ﴿٢٩﴾

30. በመጣትም ጊዜ ከሸለቆው ቀኝ ዳርቻ ከዛፊቱ በኩል በተባረከችው ስፍራ ውስጥ «ሙሳ ሆይ! እኔ የዓለማት ጌታ አላህ እኔ ነኝ» በማለት ተጠራ፡፡

فَلَمَّآ أَتَىٰهَا نُودِيَ مِن شَٰطِيِٕ ٱلۡوَادِ ٱلۡأَيۡمَنِ فِي ٱلۡبُقۡعَةِ ٱلۡمُبَٰرَكَةِ مِنَ ٱلشَّجَرَةِ أَن يَٰمُوسَىٰٓ إِنِّيٓ أَنَا ٱللَّهُ رَبُّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٣٠

31. «በትርህንም ጣል» (ተባለ)፡፡ እንደ ትንሽ እባብ ስትስለከለክ ባያትም ጊዜ ወደ ኋላ ዞሮ ሸሸ፤ አልተመለሰምም፡፡ «ሙሳ ሆይ! ተመለስ አትፍራም፤ አንተ ከጥብቆቹ ነህና» (ተባለም)፡፡

وَأَنۡ أَلۡقِ عَصَاكَۚ فَلَمَّا رَءَاهَا تَهۡتَزُّ كَأَنَّهَا جَآنّٞ وَلَّىٰ مُدۡبِرٗا وَلَمۡ يُعَقِّبۡۚ يَٰمُوسَىٰٓ أَقۡبِلۡ وَلَا تَخَفۡۖ إِنَّكَ مِنَ ٱلۡأٓمِنِينَ ٣١

32. «እጅህን በአንገትጌህ ውስጥ አግባ፡፡ ያለ ነውር ነጭ ሆና ትወጣለችና፡፡ ክንፍህንም ከፍርሃት (ለመዳን) ወዳንተ አጣብቅ፡፡ እነዚህም ከጌታህ የሆኑ ወደ ፈርዖንና ወደ መኳንንቶቹ የሚደርሱ ሁለት አስረጅዎች ናቸው፡፡ እነርሱ አመጸኞች ሕዝቦች ነበሩና፡፡»

ٱسۡلُكۡ يَدَكَ فِي جَيۡبِكَ تَخۡرُجۡ بَيۡضَآءَ مِنۡ غَيۡرِ سُوٓءٖ وَٱضۡمُمۡ إِلَيۡكَ جَنَاحَكَ مِنَ ٱلرَّهۡبِۖ فَذَٰنِكَ بُرۡهَٰنَانِ مِن رَّبِّكَ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَمَلَإِيْهِۦٓۚ إِنَّهُمۡ كَانُواْ قَوۡمٗا فَٰسِقِينَ ٣٢

33. (ሙሳ) አለ «ጌታዬ ሆይ! እኔ ከእነርሱ ነፍስን ገድያለሁ፡፡ ስለዚህ እንዳይገድሉኝ እፈራለሁ፡፡

قَالَ رَبِّ إِنِّي قَتَلۡتُ مِنۡهُمۡ نَفۡسٗا فَأَخَافُ أَن يَقۡتُلُونِ ٣٣

34. «ወንድሜም ሃሩን እርሱ ምላሱ ከእኔ የተባ ነው፡፡ እውነተኛነቴንም የሚያረጋግጥልኝ ረዳት ኾኖ ከእኔ ጋር ላከው፡፡ እኔ ሊያስተባብሉኝ እፈራለሁና፡፡»

وَأَخِي هَٰرُونُ هُوَ أَفۡصَحُ مِنِّي لِسَانٗا فَأَرۡسِلۡهُ مَعِيَ رِدۡءٗا يُصَدِّقُنِيٓۖ إِنِّيٓ أَخَافُ أَن يُكَذِّبُونِ ٣٤

35. (አላህም) «ጡንቻህን በወንድምህ በእርግጥ እናበረታለን፡፡ ለሁለታችሁም ስልጣንን እናደርጋለን፡፡ ወደእናንተም (በመጥፎ) አይደርሱም፡፡ በተዓምራቶቻችን (ኺዱ)፡፡ እናንተና የተከተላችሁም ሁሉ አሸናፊዎች ናችሁ» አላቸው፡፡

قَالَ سَنَشُدُّ عَضُدَكَ بِأَخِيكَ وَنَجۡعَلُ لَكُمَا سُلۡطَٰنٗا فَلَا يَصِلُونَ إِلَيۡكُمَا بِـَٔايَٰتِنَآۚ أَنتُمَا وَمَنِ ٱتَّبَعَكُمَا ٱلۡغَٰلِبُونَ ٣٥

36. ሙሳም በታምራቶቻችን ግልጽ ኾነው በመጣባቸው ጊዜ «ይህ የተቀጠፈ ድግምት እንጅ ሌላ አይደለም፡፡ ይህንንም በመጀመሪያዎቹ አባቶቻችን ውስጥ አልሰማንም» አሉ፡፡

فَلَمَّا جَآءَهُم مُّوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَا بَيِّنَٰتٖ قَالُواْ مَا هَٰذَآ إِلَّا سِحۡرٞ مُّفۡتَرٗى وَمَا سَمِعۡنَا بِهَٰذَا فِيٓ ءَابَآئِنَا ٱلۡأَوَّلِينَ ٣٦

37. ሙሳም «ጌታዬ ከእርሱ ዘንድ በቀጥታው መንገድ የመጣውን ሰው ምስጉኒቱም አገር ለእርሱ የምትኾንለትን ሰው ዐዋቂ ነው፡፡ እነሆ በደለኞቹ አይድኑም» አለ፡፡

وَقَالَ مُوسَىٰ رَبِّيٓ أَعۡلَمُ بِمَن جَآءَ بِٱلۡهُدَىٰ مِنۡ عِندِهِۦ وَمَن تَكُونُ لَهُۥ عَٰقِبَةُ ٱلدَّارِۚ إِنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٣٧

38. ፈርዖንም «እናንተ ጭፍሮች ሆይ! ከእኔ ሌላ ለእናንተ አምላክን ምንም አላወቅሁም፡፡ ሃማንም ሆይ! ጭቃን ለእኔ አቃጥልልኝ፤ (ጡብ ሥራልኝ)፡፡ ለእኔም ከፍተኛ ሕንጻን ሥራልኝ፡፡ ወደ ሙሳ አምላክ ልወጣ እከጅላለሁና፡፡ እኔም ከውሸታሞቹ መኾኑን እጠረጥረዋለሁ» አለ፡፡

وَقَالَ فِرۡعَوۡنُ يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡمَلَأُ مَا عَلِمۡتُ لَكُم مِّنۡ إِلَٰهٍ غَيۡرِي فَأَوۡقِدۡ لِي يَٰهَٰمَٰنُ عَلَى ٱلطِّينِ فَٱجۡعَل لِّي صَرۡحٗا لَّعَلِّيٓ أَطَّلِعُ إِلَىٰٓ إِلَٰهِ مُوسَىٰ وَإِنِّي لَأَظُنُّهُۥ مِنَ ٱلۡكَٰذِبِينَ ٣٨

39. እርሱም ሰራዊቶቹም በምድር ላይ ያለ አግባብ ኮሩ፡፡ እነርሱም ወደእኛ የማይመለሱ መኾናቸውን ጠረጠሩ፡፡

وَٱسْتَكْبَرَ هُوَ وَجُنُودُهُۥ فِى ٱلْأَرْضِ بِغَيْرِ ٱلْحَقِّ وَظَنُّوٓا۟ أَنَّهُمْ إِلَيْنَا لَا يُرْجَعُونَ ﴿٣٩﴾

40. እርሱንም ሰራዊቱንም በጥብቅ ያዝናቸው፡፡ በባሕርም ውስጥ ጣልናቸው፡፡ የበደለኞች መጨረሻም፤ እንዴት እንደ ነበረ ተመልከት፡፡

فَأَخَذْنَٰهُ وَجُنُودَهُۥ فَنَبَذْنَٰهُمْ فِى ٱلْيَمِّ ۖ فَٱنظُرْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٤٠﴾

41. ወደ እሳት የሚጠሩ መሪዎችም አደረግናቸው፡፡ በትንሣኤም ቀን አይርረዱም፡፡

وَجَعَلْنَٰهُمْ أَئِمَّةً يَدْعُونَ إِلَى ٱلنَّارِ ۖ وَيَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ لَا يُنصَرُونَ ﴿٤١﴾

42. በይህችም በቅርቢቱም ዓለም ውስጥ እርግማንን አስከተልናቸው፡፡ በትንሣኤም ቀን እነሱ ከሚባረሩት ናቸው፡፡

وَأَتْبَعْنَٰهُمْ فِى هَٰذِهِ ٱلدُّنْيَا لَعْنَةً ۖ وَيَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ هُم مِّنَ ٱلْمَقْبُوحِينَ ﴿٤٢﴾

43. የፊተኞቹን የክፍለ ዘመናት ሕዝቦችም ከአጠፋን በኋላ ለሰዎች የልብ ብርሃን መሪም እዝነትም ሲኾን ይገሰጹ ዘንድ ለሙሳ መጽሐፉን በእርግጥ ሰጠነው፡፡

وَلَقَدْ ءَاتَيْنَا مُوسَى ٱلْكِتَٰبَ مِنۢ بَعْدِ مَآ أَهْلَكْنَا ٱلْقُرُونَ ٱلْأُولَىٰ بَصَآئِرَ لِلنَّاسِ وَهُدًى وَرَحْمَةً لَّعَلَّهُمْ يَتَذَكَّرُونَ ﴿٤٣﴾

44. ወደ ሙሳም ትዕዛዝን ባወረድንለት ጊዜ (ከተራራው) በምዕራባዊው ጎን አልነበርክም ከተጣዱትም አልነበርክም፡፡

وَمَا كُنتَ بِجَانِبِ ٱلْغَرْبِىِّ إِذْ قَضَيْنَآ إِلَىٰ مُوسَى ٱلْأَمْرَ وَمَا كُنتَ مِنَ ٱلشَّٰهِدِينَ ﴿٤٤﴾

45. ግን እኛ (ከእርሱ በኋላ) የክፍለ ዘመናትን ሰዎች አስገኘን፡፡ በእነሱም ላይ ዕድሜዎች ተራዘሙ፡፡ በመድየንም ሰዎች ውስጥ ተቀማጭ በእነሱ ላይ አንቀጾቻችን የምታነብ አልነበርክም፡፡ ግን እኛ ላኪዎችህ ኾንን፡፡

وَلَٰكِنَّآ أَنشَأْنَا قُرُونًا فَتَطَاوَلَ عَلَيْهِمُ ٱلْعُمُرُ ۚ وَمَا كُنتَ ثَاوِيًا فِىٓ أَهْلِ مَدْيَنَ تَتْلُوا۟ عَلَيْهِمْ ءَايَٰتِنَا وَلَٰكِنَّا كُنَّا مُرْسِلِينَ ﴿٤٥﴾

46. በጠራነውም ጊዜ በጡር ጎን አልነበርክም፡፡ ግን ከአንተ በፊት ምንም አስፈራሪ ያልመጣቸውን ሕዝቦች ታስፈራራ ዘንድ ከጌታህ በኾነ ችሮታ (ላክንህ) ሊገሰጹ ይከጀላልና፡፡

وَمَا كُنتَ بِجَانِبِ ٱلطُّورِ إِذْ نَادَيْنَا وَلَٰكِن رَّحْمَةً مِّن رَّبِّكَ لِتُنذِرَ قَوْمًا مَّآ أَتَىٰهُم مِّن نَّذِيرٍ مِّن قَبْلِكَ لَعَلَّهُمْ يَتَذَكَّرُونَ ﴿٤٦﴾

47. እጆቻቸውም ባሳለፉት ምክንያት መከራ የምትነካቸውና «ጌታችን ሆይ! አንቀጾችህን እንድንከተል ከምእምናንም እንድንኾን ወደኛ መልክተኛን አትልክም ኖሯልን» የሚሉ ባልኾኑ ኖሮ (አንልክም ነበር)፡፡

وَلَوْلَآ أَن تُصِيبَهُم مُّصِيبَةٌۢ بِمَا قَدَّمَتْ أَيْدِيهِمْ فَيَقُولُوا۟ رَبَّنَا لَوْلَآ أَرْسَلْتَ إِلَيْنَا رَسُولًا فَنَتَّبِعَ ءَايَٰتِكَ وَنَكُونَ مِنَ ٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿٤٧﴾

48. እውነቱም ከእኛ ዘንድ በመጣላቸው ጊዜ «ለሙሳ የተሰጠው ብጤ አይስሰጠውም ኖሯልን» አሉ፡፡ «ከዚህ በፊት ሙሳ በተሰጠው አልካዱምን የተረዳዱ ሁለት ድግምቶች ናቸው» አሉ፡፡ «እኛ በሁሉም ከሓዲዎች ነንም» አሉ፡፡

فَلَمَّا جَآءَهُمُ ٱلْحَقُّ مِنْ عِندِنَا قَالُوا۟ لَوْلَآ أُوتِىَ مِثْلَ مَآ أُوتِىَ مُوسَىٰٓ ۚ أَوَلَمْ يَكْفُرُوا۟ بِمَآ أُوتِىَ مُوسَىٰ مِن قَبْلُ ۖ قَالُوا۟ سِحْرَانِ تَظَٰهَرَا وَقَالُوٓا۟ إِنَّا بِكُلٍّ كَٰفِرُونَ ﴿٤٨﴾

49. «ከአላህ ዘንድ የኾነን መጽሐፍ እርሱ ከሁለቱም ይበልጥ ቅን የኾነን አምጡ፡፡ እውነተኞች እንደ ኾናችሁ (ብታመጡት) እከተለዋለሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ فَأۡتُواْ بِكِتَٰبٖ مِّنۡ عِندِ ٱللَّهِ هُوَ أَهۡدَىٰ مِنۡهُمَآ أَتَّبِعۡهُ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٤٩

50. እሺ ባይሉህም፣ የሚከተሉት፣ ዝንባሌዎቻቸውን ብቻ መኾኑን ዕወቅ፡፡ ከአላህም የኾነ መመሪያ ሳይኖረው ዝንባሌውን ከተከተለ ሰው ይበልጥ የጠመመ አንድም የለም፡፡ አላህ በደለኞች ሕዝቦችን አይመራምና፡፡

فَإِن لَّمۡ يَسۡتَجِيبُواْ لَكَ فَٱعۡلَمۡ أَنَّمَا يَتَّبِعُونَ أَهۡوَآءَهُمۡۚ وَمَنۡ أَضَلُّ مِمَّنِ ٱتَّبَعَ هَوَىٰهُ بِغَيۡرِ هُدٗى مِّنَ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٥٠

51. ይገሰጹም ዘንድ ቃልን (ቁርኣንን በያይነቱ) ለእነርሱ በእርግጥ አስከታተልን፡፡

۞وَلَقَدۡ وَصَّلۡنَا لَهُمُ ٱلۡقَوۡلَ لَعَلَّهُمۡ يَتَذَكَّرُونَ ٥١

52. እነዚያ ከእርሱ በፊት መጽሐፍን የሰጠናቸው እነርሱ በእርሱ ያምናሉ፡፡

ٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ مِن قَبۡلِهِۦ هُم بِهِۦ يُؤۡمِنُونَ ٥٢

53. በእነሱ ላይ በሚነበብላቸውም ጊዜ «በእርሱ አምነናል፡፡ እርሱ ከጌታችን የኾነ እውነት ነው፡፡ እኛ ከርሱ በፊት ሙስሊሞች ነበርን» ይላሉ፡፡

وَإِذَا يُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ قَالُوٓاْ ءَامَنَّا بِهِۦٓ إِنَّهُ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّنَآ إِنَّا كُنَّا مِن قَبۡلِهِۦ مُسۡلِمِينَ ٥٣

54. እነዚያ በመታገሳቸው ዋጋቸውን ሁለት ጊዜ ይሰሰጣሉ፡፡ ክፋውንም ነገር በበጎ ምግባር ይገፈትራሉ፡፡ ከሰጠናቸውም ሲሳይ ይለግሳሉ፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ يُؤۡتَوۡنَ أَجۡرَهُم مَّرَّتَيۡنِ بِمَا صَبَرُواْ وَيَدۡرَءُونَ بِٱلۡحَسَنَةِ ٱلسَّيِّئَةَ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ٥٤

55. ውድቅንም ቃል በሰሙ ጊዜ ከእርሱ ይርቃሉ፡፡ «ለእኛ ሥራዎቻችን አሉን፡፡ ለናንተም ሥራዎቻችሁ አሏችሁ፡፡ ሰላም በእናንተ ላይ (ይኹን) ባለጌዎችን አንፈልግም» ይላሉ፡፡

وَإِذَا سَمِعُواْ ٱللَّغۡوَ أَعۡرَضُواْ عَنۡهُ وَقَالُواْ لَنَآ أَعۡمَٰلُنَا وَلَكُمۡ أَعۡمَٰلُكُمۡ سَلَٰمٌ عَلَيۡكُمۡ لَا نَبۡتَغِي ٱلۡجَٰهِلِينَ ٥٥

56. አንተ የወደድከውን ሰው ፈጽሞ አታቀናም፡፡ ግን አላህ የሚሻውን ሰው ያቀናል እርሱም ቅኖቹን ዐዋቂ ነው፡፡

إِنَّكَ لَا تَهۡدِي مَنۡ أَحۡبَبۡتَ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يَهۡدِي مَن يَشَآءُۚ وَهُوَ أَعۡلَمُ بِٱلۡمُهۡتَدِينَ ٥٦

57. «ከአንተ ጋር ቅንን መንገድ ብንከተል ከምድራችን እንባረራለን» አሉም፡፡ ከእኛ ዘንድ (የተሰጠ) ሲሳይ ሲሆን የነገሩ ሁሉ ፍሬዎች ወደእርሱ የሚነዱበትን ጸጥተኛ ክልል (መካን) ለእነሱ አላስመቸናቸውምን ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

وَقَالُوٓاْ إِن نَّتَّبِعِ ٱلۡهُدَىٰ مَعَكَ نُتَخَطَّفۡ مِنۡ أَرۡضِنَآۚ أَوَ لَمۡ نُمَكِّن لَّهُمۡ حَرَمًا ءَامِنٗا يُجۡبَىٰٓ إِلَيۡهِ ثَمَرَٰتُ كُلِّ شَيۡءٖ رِّزۡقٗا مِّن لَّدُنَّا وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٥٧

58. ከከተማም ኑሮዋን (ምቾቷን) የካደችን (ከተማ) ያጠፋናት ብዙ ናት፡፡ እነዚህም ከእነሱ በኋላ ጥቂት ጊዜ እንጅ ያልተኖረባቸው ሲኾኑ መኖሪያዎቻቸው ናቸው፡፡ እኛም (ከእነርሱ) ወራሾች ነበርን፡፡

وَكَمۡ أَهۡلَكۡنَا مِن قَرۡيَةِۭ بَطِرَتۡ مَعِيشَتَهَاۖ فَتِلۡكَ مَسَٰكِنُهُمۡ لَمۡ تُسۡكَن مِّنۢ بَعۡدِهِمۡ إِلَّا قَلِيلٗاۖ وَكُنَّا نَحۡنُ ٱلۡوَٰرِثِينَ ٥٨

59. ጌታህም ከተሞችን በዋናዋ (ከተማ) ውስጥ አንቀጾቻችንን በእነሱ ላይ የሚያነብ መልክተኛን እስከሚልክ ድረስ አጥፊ አልነበረም፡፡ ከተሞችንም ባለቤቶቿ በዳዮች ሆነው እንጅ አጥፊዎች አልነበርንም፡ ፡

وَمَا كَانَ رَبُّكَ مُهۡلِكَ ٱلۡقُرَىٰ حَتَّىٰ يَبۡعَثَ فِيٓ أُمِّهَا رَسُولٗا يَتۡلُواْ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتِنَاۚ وَمَا كُنَّا مُهۡلِكِي ٱلۡقُرَىٰٓ إِلَّا وَأَهۡلُهَا ظَٰلِمُونَ ٥٩

60. ከማንኛውም ነገር የተሰጣችሁት፤ የቅርቢቱ ሕይወት ጥቅምና ጌጧ ነው፡፡ አላህ ዘንድ ያለውም (ምንዳ) በጣም በላጭና ዘውታሪ ነው አታውቁምን

وَمَآ أُوتِيتُم مِّن شَيۡءٖ فَمَتَٰعُ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَزِينَتُهَاۚ وَمَا عِندَ ٱللَّهِ خَيۡرٞ وَأَبۡقَىٰٓۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ٦٠

61. መልካምን ተስፋ ቃል የገባንለትና እርሱም አግኚው የሆነ ሰው የቅርቢቱን ሕይወት ጥቅም እንዳስመቸነውና ከዚያም እርሱ በትንሣኤ ቀን (ለእሳት) ከሚቀረቡት እንደ ኾነው ሰው ነውን

أَفَمَن وَعَدۡنَٰهُ وَعۡدًا حَسَنٗا فَهُوَ لَٰقِيهِ كَمَن مَّتَّعۡنَٰهُ مَتَٰعَ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا ثُمَّ هُوَ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ مِنَ ٱلۡمُحۡضَرِينَ ٦١

62. (አላህ) የሚጠራባቸውንና እነዚያ ተጋሪዎቼ ትሏቸው የነበራችሁት የት ናቸው የሚልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ يُنَادِيهِمۡ فَيَقُولُ أَيۡنَ شُرَكَآءِيَ ٱلَّذِينَ كُنتُمۡ تَزۡعُمُونَ ٦٢

63. እነዚያ በእነርሱ ላይ ቃሉ የተረጋገጠባቸው ይላሉ «ጌታችን ሆይ! እነዚህ እነዚያ ያጠመምናቸው ናቸው፡፡ እንደጠመምን አጠመምናቸው፡፡ (ከእነሱ) ወዳንተ ተጥራራን፡፡ እኛን ይግገዙ አልነበሩም፡፡

قَالَ ٱلَّذِينَ حَقَّ عَلَيۡهِمُ ٱلۡقَوۡلُ رَبَّنَا هَٰٓؤُلَآءِ ٱلَّذِينَ أَغۡوَيۡنَآ أَغۡوَيۡنَٰهُمۡ كَمَا غَوَيۡنَاۖ تَبَرَّأۡنَآ إِلَيۡكَۖ مَا كَانُوٓاْ إِيَّانَا يَعۡبُدُونَ ٦٣

64. «(ለአላህ) የምታጋሯቸውንም ጥሩ» ይባላሉ፤ ይጠሯቸዋልም፡፡ ግን ለእነርሱ አይመልሱላቸውም፡፡ ቅጣቱንም ያያሉ፡፡ እነርሱ ይመሩ በነበሩ ኖሮ (አያዩትም ነበር)፡፡

وَقِيلَ ٱدۡعُواْ شُرَكَآءَكُمۡ فَدَعَوۡهُمۡ فَلَمۡ يَسۡتَجِيبُواْ لَهُمۡ وَرَأَوُاْ ٱلۡعَذَابَۚ لَوۡ أَنَّهُمۡ كَانُواْ يَهۡتَدُونَ ٦٤

65. «የሚጠራባቸውንና ለመልክተኞቹም ምንን መለሳችሁ» የሚልበትን ቀን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ يُنَادِيهِمۡ فَيَقُولُ مَاذَآ أَجَبۡتُمُ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ٦٥

66. በዚያም ቀን ወሬዎቹ ሁሉ በእነርሱ ላይ ይሰውሩባቸዋል፡፡ እነርሱም አይጠያየቁም፡፡

فَعَمِيَتۡ عَلَيۡهِمُ ٱلۡأَنۢبَآءُ يَوۡمَئِذٖ فَهُمۡ لَا يَتَسَآءَلُونَ ٦٦

67. የተጸጸተና ያመነ ሰውማ መልካምንም የሠራ ከሚድኑት ሊኾን ይከጀላል፡፡

فَأَمَّا مَن تَابَ وَءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَعَسَىٰٓ أَن يَكُونَ مِنَ ٱلۡمُفۡلِحِينَ ٦٧

68. ጌታህም የሚሻውን ይፈጥራል፤ ይመርጣልም፡፡ ለእነርሱ (ለሰዎቹ) ምርጫ የላቸውም፡፡ አላህ ከማይገባው ሁሉ ጠራ፡፡ ከሚያጋሯቸውም ላቀ፡፡

وَرَبُّكَ يَخۡلُقُ مَا يَشَآءُ وَيَخۡتَارُۗ مَا كَانَ لَهُمُ ٱلۡخِيَرَةُۚ سُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ٦٨

69. ጌታህም ልቦቻቸው የሚደብቁትንና የሚገልጹትን ሁሉ ያውቃል፡፡

وَرَبُّكَ يَعۡلَمُ مَا تُكِنُّ صُدُورُهُمۡ وَمَا يُعۡلِنُونَ ٦٩

70. እርሱም አላህ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ ምስጋና በመጀመሪያይቱም በመጨረሻይቱም ዓለም ለእርሱ ብቻ ነው፡፡ ፍርዱም የእርሱ ብቻ ነው፡፡ ወደእርሱም ትመለሳላችሁ፡፡

وَهُوَ ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ لَهُ ٱلۡحَمۡدُ فِي ٱلۡأُولَىٰ وَٱلۡأٓخِرَةِۖ وَلَهُ ٱلۡحُكۡمُ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٧٠

71. አያችሁን (ንገሩኝ) «አላህ በእናንተ ላይ ሌሊትን እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ ዘውታሪ ቢያደርገው ከአላህ ሌላ ብርሃንን የሚያመጣላችሁ አምላክ ማነው አትሰሙምን» በላቸው፡፡

قُلۡ أَرَءَيۡتُمۡ إِن جَعَلَ ٱللَّهُ عَلَيۡكُمُ ٱلَّيۡلَ سَرۡمَدًا إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ مَنۡ إِلَٰهٌ غَيۡرُ ٱللَّهِ يَأۡتِيكُم بِضِيَآءٍۚ أَفَلَا تَسۡمَعُونَ ٧١

72. አያችሁን «አላህ በእናንተ ላይ ቀንን እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስ ዘውታሪ ቢያደርገው ከአላህ ሌላ በውስጡ የምታርፉበትን ሌሊት የሚያመጣላችሁ አምላክ ማን ነው (ንገሩኝ) አታስተውሉምን» በላቸው፡፡

قُلۡ أَرَءَيۡتُمۡ إِن جَعَلَ ٱللَّهُ عَلَيۡكُمُ ٱلنَّهَارَ سَرۡمَدًا إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ مَنۡ إِلَٰهٌ غَيۡرُ ٱللَّهِ يَأۡتِيكُم بِلَيۡلٖ تَسۡكُنُونَ فِيهِۚ أَفَلَا تُبۡصِرُونَ ٧٢

73. ከችሮታውም ለእናንተ ሌሊትንና ቀንን በውስጡ ልታርፉበት፣ ከትሩፋቱም ልትፈልጉበት፣ አመስገኞችም ልትኾኑ አደረገላችሁ፡፡

وَمِن رَّحۡمَتِهِۦ جَعَلَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَ لِتَسۡكُنُواْ فِيهِ وَلِتَبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِهِۦ وَلَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ٧٣

74. የሚጠራባቸውንም ቀንና «እነዚያ ተጋሪዎቼ ትሏቸው የነበራችሁት የት ናቸው» የሚልበትን (አስታውስ)፡፡

وَيَوۡمَ يُنَادِيهِمۡ فَيَقُولُ أَيۡنَ شُرَكَآءِيَ ٱلَّذِينَ كُنتُمۡ تَزۡعُمُونَ ٧٤

75. ከሕዝቦችም ሁሉ መስካሪን እናወጣለን፡፡ (ያን ጊዜ) እውነተኛውም አምላክነት ለአላህ ብቻ መኾኑን ያውቃሉ፡፡ ይቀጣጥፉት የነበሩትም ከእነርሱ ይጠፉቻቸዋል፡፡

وَنَزَعۡنَا مِن كُلِّ أُمَّةٖ شَهِيدٗا فَقُلۡنَا هَاتُواْ بُرۡهَٰنَكُمۡ فَعَلِمُوٓاْ أَنَّ ٱلۡحَقَّ لِلَّهِ وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ٧٥

76. ቃሩን ከሙሳ ነገዶች ነበር፡፡ በእነርሱም ላይ አመጸ፡፡ ከድልቦችም ያንን መከፈቻዎቹ ብቻ የኃይል ባለቤቶች የኾኑ ጭፍሮችን (ሸክሙ) የሚከብድን ሰጠነው፡፡ ወገኖቹ ለእርሱ አትኩራ፤ አላህ ኩራተኞችን አይወድምና ባሉት ጊዜ (አስታውስ)፡፡

۞إِنَّ قَٰرُونَ كَانَ مِن قَوۡمِ مُوسَىٰ فَبَغَىٰ عَلَيۡهِمۡۖ وَءَاتَيۡنَٰهُ مِنَ ٱلۡكُنُوزِ مَآ إِنَّ مَفَاتِحَهُۥ لَتَنُوٓأُ بِٱلۡعُصۡبَةِ أُوْلِي ٱلۡقُوَّةِ إِذۡ قَالَ لَهُۥ قَوۡمُهُۥ لَا تَفۡرَحۡۖ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلۡفَرِحِينَ ٧٦

77. «አላህም በሰጠህ ሀብት የመጨረሻይቱን አገር ፈልግ፡፡ ከቅርቢቱም ዓለም ፋንታህን አትርሳ፡፡ አላህም ወደ አንተ መልካምን እንዳደረገልህ (ለሰዎች) መልካምን አድርግ፡፡ በምድርም ውስጥ ማጥፋትን አትፈልግ፡፡ አላህ አጥፊዎችን አይወድምና» (አሉት)፡፡

وَٱبۡتَغِ فِيمَآ ءَاتَىٰكَ ٱللَّهُ ٱلدَّارَ ٱلۡأٓخِرَةَۖ وَلَا تَنسَ نَصِيبَكَ مِنَ ٱلدُّنۡيَاۖ وَأَحۡسِن كَمَآ أَحۡسَنَ ٱللَّهُ إِلَيۡكَۖ وَلَا تَبۡغِ ٱلۡفَسَادَ فِي ٱلۡأَرۡضِۖ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ٧٧

78. (ሀብቱን) «የተሰጠሁት እኔ ዘንድ ባለው እውቀት ብቻ ነው አለ፡፡ አላህ ከእርሱ በፊት ከክፍለ ዘመናት ሰዎች በኀይል ከእርሱ ይበልጥ የበረቱትን (ሀብትን) በመሰብሰብም ይበልጥ የበዙትን በእርግጥ ያጠፋ መኾኑን አያውቅምን አመጸኞችም ከኀጢአቶቻቸው (ምሕረት የሚከተለውን ጥያቄ) አይጠየቁም፡፡

قَالَ إِنَّمَآ أُوتِيتُهُۥ عَلَىٰ عِلۡمٍ عِندِيٓۚ أَوَلَمۡ يَعۡلَمۡ أَنَّ ٱللَّهَ قَدۡ أَهۡلَكَ مِن قَبۡلِهِۦ مِنَ ٱلۡقُرُونِ مَنۡ هُوَ أَشَدُّ مِنۡهُ قُوَّةٗ وَأَكۡثَرُ جَمۡعٗاۚ وَلَا يُسۡـَٔلُ عَن ذُنُوبِهِمُ ٱلۡمُجۡرِمُونَ ٧٨

79. በሕዝቦቹም ላይ በጌጡ ውስጥ ኾኖ ወጣ፡፡ እነዚያ ቅርቢቱን ሕይወት የሚፈልጉት «ወይ ምኞታችን! ቃሩን የተሰጠው ብጤ ምነው ለእኛ በኖረን፤ እርሱ የታላቅ ዕድል ባለቤት ነውና» አሉ፡፡

فَخَرَجَ عَلَىٰ قَوۡمِهِۦ فِي زِينَتِهِۦۖ قَالَ ٱلَّذِينَ يُرِيدُونَ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا يَٰلَيۡتَ لَنَا مِثۡلَ مَآ أُوتِيَ قَٰرُونُ إِنَّهُۥ لَذُو حَظٍّ عَظِيمٖ ٧٩

80. እነዚያም ዕውቀትን የተሰጡት «ወዮላችሁ! የአላህ ምንዳ ለአመነ ሰው መልካምንም ለሠራ በላጭ ነው፡፡ ታጋሾችም እንጅ ሌላው አያገኛትም» አሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡعِلۡمَ وَيۡلَكُمۡ ثَوَابُ ٱللَّهِ خَيۡرٞ لِّمَنۡ ءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحٗاۚ وَلَا يُلَقَّىٰهَآ إِلَّا ٱلصَّٰبِرُونَ ٨٠

81. በእርሱም በቤቱም ምድርን ደረባን፡፡ ለእርሱም ከአላህ ሌላ የሚረዱት ጭፍሮች ምንም አልነበሩትም፡፡ ከሚርረዱትም አልነበረም፡፡

فَخَسَفۡنَا بِهِۦ وَبِدَارِهِ ٱلۡأَرۡضَ فَمَا كَانَ لَهُۥ مِن فِئَةٖ يَنصُرُونَهُۥ مِن دُونِ ٱللَّهِ وَمَا كَانَ مِنَ ٱلۡمُنتَصِرِينَ ٨١

82. እነዚያም በትላንትናው ቀን ስፍራውን ይመኙ የነበሩት «ወይ ጉድ! ለካ አላህ ከባሮቹ ለሚሻው ሰው ሲሳይን ያሰፋል፤ ያጠባልም፡፡ አላህ በእኛ ላይ (በእምነት) ባልለገሰልን ኖሮ ምድርን በእኛ ላይ በገለበጠብን ነበር፡፡ ወይ ጉድ! ከሓዲዎች አይድኑም» የሚሉ ኾነው አነጉ፡፡

وَأَصۡبَحَ ٱلَّذِينَ تَمَنَّوۡاْ مَكَانَهُۥ بِٱلۡأَمۡسِ يَقُولُونَ وَيۡكَأَنَّ ٱللَّهَ يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦ وَيَقۡدِرُۖ لَوۡلَآ أَن مَّنَّ ٱللَّهُ عَلَيۡنَا لَخَسَفَ بِنَاۖ وَيۡكَأَنَّهُۥ لَا يُفۡلِحُ ٱلۡكَٰفِرُونَ ٨٢

83. ይህች የመጨረሻይቱ አገር ለእነዚያ በምድር ውስጥ ኩራትንና ማመፅን ለማይፈልጉት እናደርጋታለን፡፡ ምስጉኒቱም መጨረሻ ለጥንቁቆቹ ናት፡፡

تِلۡكَ ٱلدَّارُ ٱلۡأٓخِرَةُ نَجۡعَلُهَا لِلَّذِينَ لَا يُرِيدُونَ عُلُوّٗا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فَسَادٗاۚ وَٱلۡعَٰقِبَةُ لِلۡمُتَّقِينَ ٨٣

84. በደግ ሥራ የመጣ ሰው ለእርሱ ከእርሷ በላጭ ምንዳ አልለው፡፡ በክፉም ሥራ የመጡ ሰዎች እነዚህ መጥፎዎችን የሠሩ ይሠሩት የነበሩትን እንጅ አይመነዱም፡፡

مَن جَآءَ بِٱلۡحَسَنَةِ فَلَهُۥ خَيۡرٞ مِّنۡهَاۖ وَمَن جَآءَ بِٱلسَّيِّئَةِ فَلَا يُجۡزَى ٱلَّذِينَ عَمِلُواْ ٱلسَّيِّـَٔاتِ إِلَّا مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٨٤

85. ያ ቁርኣንን የተከፋፈለ ኾኖ ባንተ ላይ ያወረደው (አምላክ) ወደ መመለሻ (ወደመካ) በእርግጥ መላሽህ ነው፡፡ «ጌታዬ በቅን መንገድ የመጣውን ሰውና እርሱም በግልጽ ስሕተት ውስጥ የኾነውን ሰው ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِي فَرَضَ عَلَيۡكَ ٱلۡقُرۡءَانَ لَرَآدُّكَ إِلَىٰ مَعَادٖۚ قُل رَّبِّيٓ أَعۡلَمُ مَن جَآءَ بِٱلۡهُدَىٰ وَمَنۡ هُوَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ٨٥

86. መጽሐፉ ወዳንተ መወረዱን ተስፋ የምታደርግ አልነበርክም፡፡ ግን ከጌታህ ችሮታ (ተወረደልህ)፡፡ ለከሓዲዎችም በፍጹም ረዳት አትኹን፡፡

وَمَا كُنتَ تَرۡجُوٓاْ أَن يُلۡقَىٰٓ إِلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبُ إِلَّا رَحۡمَةٗ مِّن رَّبِّكَۖ فَلَا تَكُونَنَّ ظَهِيرٗا لِّلۡكَٰفِرِينَ ٨٦

87. ከአላህም አንቀጾች ወዳንተ ከተወረዱ ጊዜ በኋላ አያግዱህ፡፡ ወደ ጌታህም (ሰዎችን) ጥራ፡፡ ከአጋሪዎቹም አትኹን፤

وَلَا يَصُدُّنَّكَ عَنۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ بَعۡدَ إِذۡ أُنزِلَتۡ إِلَيۡكَۖ وَٱدۡعُ إِلَىٰ رَبِّكَۖ وَلَا تَكُونَنَّ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٨٧

88. ከአላህም ጋር ሌላን አምላክ አትግገዛ፡፡ ከእርሱ በቀር አምላክ የለም፡፡ ነገሩ ሁሉ ከአላህ በቀር ጠፊ ነው፡፡ ፍርዱ የርሱ፤ ብቻ ነው፡፡ ወደእርሱም ትመለሳላችሁ፡፡

وَلَا تَدۡعُ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَۘ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۚ كُلُّ شَيۡءٍ هَالِكٌ إِلَّا وَجۡهَهُۥۚ لَهُ ٱلۡحُكۡمُ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٨٨

# ሱረቱ አል ዓንከቡት

# سورة العنكبوت

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ለ.መ (አሊፍ ላም ሚም)

الٓمٓ ١

2. ሰዎቹ አምነናል በማለታቸው ብቻ እነሱ ሳይፈተኑ የሚተው መኾናቸውን ጠረጠሩን

أَحَسِبَ ٱلنَّاسُ أَن يُتۡرَكُوٓاْ أَن يَقُولُوٓاْ ءَامَنَّا وَهُمۡ لَا يُفۡتَنُونَ ٢

3. እነዚያንም ከእነሱ በፊት የነበሩትን በእርግጥ ፈትነናል፡፡ እነዚያንም እውነት የተናገሩትን አላህ በእርግጥ ያውቃል፡፡ ውሸታሞቹንም ያውቃል፡፡

وَلَقَدۡ فَتَنَّا ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۖ فَلَيَعۡلَمَنَّ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ صَدَقُواْ وَلَيَعۡلَمَنَّ ٱلۡكَٰذِبِينَ ٣

4. ይልቁንም እነዚያ መጥፎዎችን ሥራዎች የሚሠሩት ሊያመልጡን ይጠረጥራሉን ያ የሚፈርዱት (ፍርድ) ከፋ፡፡

أَمۡ حَسِبَ ٱلَّذِينَ يَعۡمَلُونَ ٱلسَّيِّـَٔاتِ أَن يَسۡبِقُونَاۚ سَآءَ مَا يَحۡكُمُونَ ٤

5. የአላህን መገናኘት ተስፋ የሚያደርግ ሰው (ይዘጋጅ)፡፡ የአላህ ቀጠሮ በእርግጥ መጪ ነውና፡፡ እርሱም ሰሚው ዐዋቂው ነው፡፡

مَن كَانَ يَرۡجُواْ لِقَآءَ ٱللَّهِ فَإِنَّ أَجَلَ ٱللَّهِ لَأٓتٖۚ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٥

6. የታገለ ሰውም የሚታገለው ለነፍሱ ነው፡፡ አላህ ከዓለማት በእርግጥ ተብቃቂ ነውና፡፡

وَمَن جَٰهَدَ فَإِنَّمَا يُجَٰهِدُ لِنَفۡسِهِۦٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَغَنِيٌّ عَنِ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٦

7. እነዚያም ያመኑ፤ መልካሞችንም የሠሩ መጥፎዎቹን ሥራዎቻቸውን ከእነሱ ላይ እናብስላቸዋለን፡፡ በዚያም ይሠሩት በነበሩት መልካም ሥራ በእርግጥ እንመነዳቸዋለን፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَنُكَفِّرَنَّ عَنۡهُمۡ سَيِّـَٔاتِهِمۡ وَلَنَجۡزِيَنَّهُمۡ أَحۡسَنَ ٱلَّذِي كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٧

8. ሰውንም በወላጆቹ መልካም አድራጎትን አዘዝነው፡፡ ላንተም በእርሱ ዕውቀት የሌለህን (ጣዖት) በእኔ እንድታጋራ ቢታገሉህ አትታዘዛቸው፡፡ መመለሻችሁ ወደኔ ነው፡፡ ትሠሩት የነበራችሁትንም ሁሉ እነግራችኋለሁ፡፡

وَوَصَّيۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ بِوَٰلِدَيۡهِ حُسۡنٗاۖ وَإِن جَٰهَدَاكَ لِتُشۡرِكَ بِي مَا لَيۡسَ لَكَ بِهِۦ عِلۡمٞ فَلَا تُطِعۡهُمَآۚ إِلَيَّ مَرۡجِعُكُمۡ فَأُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٨

9. እነዚያንም ያመኑ፤ መልካም ሥራዎችንም የሠሩ በደጋጎቹ ውስጥ በእርግጥ እናገባቸዋለን፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَنُدۡخِلَنَّهُمۡ فِي ٱلصَّٰلِحِينَ ٩

10. ከሰዎችም በአላህ አመንን የሚል ሰው አልለ፡፡ በአላህም (በማመኑ) በተሰቃየ ጊዜ የሰዎችን ማሰቃየት እንደ አላህ ቅጣት ያደርጋል፡፡ ከጌታህም እርዳታ ቢመጣ እኛ በእርግጥ ከእናንተ ጋር ነበርን ይላሉ፡፡ አላህ በዓለማት ሕዝብ ልቦች ውስጥ ያለውን ሁሉ ዐዋቂ አይደለምን

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَقُولُ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ فَإِذَآ أُوذِىَ فِى ٱللَّهِ جَعَلَ فِتْنَةَ ٱلنَّاسِ كَعَذَابِ ٱللَّهِ ۖ وَلَئِن جَآءَ نَصْرٌ مِّن رَّبِّكَ لَيَقُولُنَّ إِنَّا كُنَّا مَعَكُمْ ۚ أَوَلَيْسَ ٱللَّهُ بِأَعْلَمَ بِمَا فِى صُدُورِ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿١٠﴾

11. አላህም እነዚያን ያመኑትን በእርግጥ ያውቃል፡፡ መናፍቆቹንም ያውቃል፡፡

وَلَيَعْلَمَنَّ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَلَيَعْلَمَنَّ ٱلْمُنَٰفِقِينَ ﴿١١﴾

12. እነዚያም የካዱት ሰዎች ለእነዚያ ላመኑት «መንገዳችንን ተከተሉ፤ ኀጢአቶቻችሁንም እንሸከማለን» አሉ፡፡ እነርሱም ከኀጢአቶቻቸው ምንንም ተሸካሚዎች አይደሉም፡፡ እነርሱ በእርግጥ ውሸታሞች ናቸው፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ لِلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ٱتَّبِعُوا۟ سَبِيلَنَا وَلْنَحْمِلْ خَطَٰيَٰكُمْ وَمَا هُم بِحَٰمِلِينَ مِنْ خَطَٰيَٰهُم مِّن شَىْءٍ ۖ إِنَّهُمْ لَكَٰذِبُونَ ﴿١٢﴾

13. ሸክሞቻቸውንና ከሸክሞቻቸው ጋር (ሌሎች) ሸክሞችንም በእርግጥ ይሸከማሉ፡፡ በትንሣኤም ቀን ይቀጥፉት ከነበሩት በእርግጥ ይጠየቃሉ፡፡

وَلَيَحْمِلُنَّ أَثْقَالَهُمْ وَأَثْقَالًا مَّعَ أَثْقَالِهِمْ ۖ وَلَيُسْـَٔلُنَّ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ عَمَّا كَانُوا۟ يَفْتَرُونَ ﴿١٣﴾

14. ኑሕንም ወደ ሕዝቦቹ በእርግጥ ላክነው፡፡ በውስጣቸውም ሺህ ዓመትን አምሳ ዓመት ሲቀር ተቀመጠ፡፡ እነርሱ በዳዮች ኾነውም የውሃው ማጥለቅለቅ ያዛቸው፡፡

وَلَقَدْ أَرْسَلْنَا نُوحًا إِلَىٰ قَوْمِهِۦ فَلَبِثَ فِيهِمْ أَلْفَ سَنَةٍ إِلَّا خَمْسِينَ عَامًا فَأَخَذَهُمُ ٱلطُّوفَانُ وَهُمْ ظَٰلِمُونَ ﴿١٤﴾

15. ኑሕንና የመርከቢቱንም ጓዶች አዳናቸው፡፡ እርሷንም ለዓለማት ተዓምር አደረግናት፡፡

فَأَنجَيْنَٰهُ وَأَصْحَٰبَ ٱلسَّفِينَةِ وَجَعَلْنَٰهَآ ءَايَةً لِّلْعَٰلَمِينَ ﴿١٥﴾

16. ኢብራሂምንም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «አላህን ተገዙ ፍሩትም፡፡ ይህ የምታውቁ ብትሆኑ ለእናንተ በላጭ ነው፡፡

وَإِبْرَٰهِيمَ إِذْ قَالَ لِقَوْمِهِ ٱعْبُدُوا۟ ٱللَّهَ وَٱتَّقُوهُ ۖ ذَٰلِكُمْ خَيْرٌ لَّكُمْ إِن كُنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿١٦﴾

17. «ከአላህ ሌላ የምትገዙዙት ጣዖታትን ብቻ ነው፡፡ ውሸትንም ትቀጣጥፉላችሁ፡፡ እነዚያ ከአላህ ሌላ የምትግገዙዋቸው ለእናንተ ሲሳይን ሊሰጧችሁ አይችሉም፡፡ ስለዚህ ሲሳይን ከአላህ ዘንድ ብቻ ፈልጉ፡፡ ተገዙትም፡፡ ለእርሱም አመስግኑ፡፡ ወደእርሱ ትመለሳላችሁ፡፡

إِنَّمَا تَعْبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَوْثَٰنًا وَتَخْلُقُونَ إِفْكًا ۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ تَعْبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ لَا يَمْلِكُونَ لَكُمْ رِزْقًا فَٱبْتَغُوا۟ عِندَ ٱللَّهِ ٱلرِّزْقَ وَٱعْبُدُوهُ وَٱشْكُرُوا۟ لَهُۥٓ ۖ إِلَيْهِ تُرْجَعُونَ ﴿١٧﴾

18. «ብታስተባብሉም ከፊታችሁ የነበሩት ሕዝቦች በእርግጥ አስተባብለዋል፡፡ በመልክተኛውም ላይ ግልጽ ማድረስ እንጂ ሌላ የለበትም፡፡»

وَإِن تُكَذِّبُوا۟ فَقَدْ كَذَّبَ أُمَمٌ مِّن قَبْلِكُمْ ۖ وَمَا عَلَى ٱلرَّسُولِ إِلَّا ٱلْبَلَٰغُ ٱلْمُبِينُ ﴿١٨﴾

19. አላህ መፍጠርን እንዴት እንደሚጀምር ከዚያም እንዴት እንደሚመልሰው አይመለከቱምን ይህ በአላህ ላይ ቀላል ነው፡፡

أَوَلَمْ يَرَوْا۟ كَيْفَ يُبْدِئُ ٱللَّهُ ٱلْخَلْقَ ثُمَّ يُعِيدُهُۥٓ ۚ إِنَّ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٌ ﴿١٩﴾

20. «፡--በምድር ላይ ኺዱ፤ መፍጠርንም እንዴት እንደ ጀመረ ተመልከቱ፡፡ ከዚያም፤ አላህ የመጨረሻይቱን መነሳት ያስነሳል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና» በላቸው፡፡

قُلۡ سِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَٱنظُرُواْ كَيۡفَ بَدَأَ ٱلۡخَلۡقَۚ ثُمَّ ٱللَّهُ يُنشِئُ ٱلنَّشۡأَةَ ٱلۡأٓخِرَةَۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٢٠

21. የሚሻውን ሰው ይቀጣል፡፡ የሚሻውንም ሰው ያዝንለታል፡፡ ወደእርሱም ትመለሳላችሁ፡፡

يُعَذِّبُ مَن يَشَآءُ وَيَرۡحَمُ مَن يَشَآءُۖ وَإِلَيۡهِ تُقۡلَبُونَ ٢١

22. እናንተም በምድርም ኾነ በሰማይ የምታቅቱ አይደላችሁም፡፡ ከአላህም ሌላ ረዳትም ተከላካይም ምንም የላችሁም፡፡

وَمَآ أَنتُم بِمُعۡجِزِينَ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فِي ٱلسَّمَآءِۖ وَمَا لَكُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ مِن وَلِيّٖ وَلَا نَصِيرٖ ٢٢

23. እነዚያም በአላህ አንቀጾችና በመገናኘቱ የካዱ እነዚያ ከእዝነቴ ተስፋን ቆረጡ፡፡ እነዚያም ለእነሱ አሳማሚ ቅጣት አላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَلِقَآئِهِۦٓ أُوْلَٰٓئِكَ يَئِسُواْ مِن رَّحۡمَتِي وَأُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٢٣

24. የሕዝቦቹም መልስ፡- «ግደሉት፤ ወይም አቃጥሉት» ማለት እንጂ ሌላ አልነበረም፡፡ ከእሳቲቱም አላህ አዳነው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያምኑ ሕዝቦች ተዓምራቶች አሉበት፡፡

فَمَا كَانَ جَوَابَ قَوۡمِهِۦٓ إِلَّآ أَن قَالُواْ ٱقۡتُلُوهُ أَوۡ حَرِّقُوهُ فَأَنجَىٰهُ ٱللَّهُ مِنَ ٱلنَّارِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يُؤۡمِنُونَ ٢٤

25. (ኢብራሂም) አለም «ከአላህ ሌላ ጣዖታትን (አማልክት) የያዛችሁት በቅርቢቱ ሕይወት በመካከላችሁ ለመዋደድ ብቻ ነው፡፡ ከዚያም በትንሣኤ ቀን ከፊላችሁ በከፊሉ ይክዳል፡፡ ከፊላችሁም ከፊሉን ይረግማል፡፡ መኖሪያችሁም እሳት ናት፡፡ ለእናንተም ከረዳቶች ምንም የላችሁም፡፡»

وَقَالَ إِنَّمَا ٱتَّخَذۡتُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ أَوۡثَٰنٗا مَّوَدَّةَ بَيۡنِكُمۡ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ ثُمَّ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ يَكۡفُرُ بَعۡضُكُم بِبَعۡضٖ وَيَلۡعَنُ بَعۡضُكُم بَعۡضٗا وَمَأۡوَىٰكُمُ ٱلنَّارُ وَمَا لَكُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٢٥

26. ሉጥም ለእርሱ አመነ፤ (ኢብራሂም) «እኔ ወደ ጌታዬ ተሰዳጅ ነኝ፡፡ እነሆ እርሱ አሸናፊው ጥበበኛው ነውና» አለም፡፡

۞فَـَٔامَنَ لَهُۥ لُوطٞۘ وَقَالَ إِنِّي مُهَاجِرٌ إِلَىٰ رَبِّيٓۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٢٦

27. ለእርሱም ኢስሐቅንና ያዕቆብን ሰጠነው፡፡ በዘሩም ውስጥ ነብይነትንና መጽሐፍን አደረግን፡፡ ምንዳውንም በቅርቢቱ ዓለም ሰጠነው፡፡ እርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም ከደጋጎቹ ነው፡፡

وَوَهَبۡنَا لَهُۥٓ إِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ وَجَعَلۡنَا فِي ذُرِّيَّتِهِ ٱلنُّبُوَّةَ وَٱلۡكِتَٰبَ وَءَاتَيۡنَٰهُ أَجۡرَهُۥ فِي ٱلدُّنۡيَاۖ وَإِنَّهُۥ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ لَمِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ٢٧

28. ሉጥንም ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ) «እናንተ ጠያፍን ስራ ትሠራላችሁን በእርሷ ከዓለማት አንድም አልቀደማችሁም፡፡

وَلُوطًا إِذۡ قَالَ لِقَوۡمِهِۦٓ إِنَّكُمۡ لَتَأۡتُونَ ٱلۡفَٰحِشَةَ مَا سَبَقَكُم بِهَا مِنۡ أَحَدٖ مِّنَ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٢٨

أَئِنَّكُمۡ لَتَأۡتُونَ ٱلرِّجَالَ وَتَقۡطَعُونَ ٱلسَّبِيلَ وَتَأۡتُونَ فِي نَادِيكُمُ ٱلۡمُنكَرَۖ فَمَا كَانَ جَوَابَ قَوۡمِهِۦٓ إِلَّآ أَن قَالُواْ ٱئۡتِنَا بِعَذَابِ ٱللَّهِ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿٢٩﴾

29. «እናንተ በእርግጥ ወንዶችን ትመጣላችሁን መንገድንም ትቆርጣላችሁን በሸንጓችሁም የሚነወርን ነገር ትሠራላችሁን» (አላቸው)፡፡ የሕዝቦቹም መልስ «ከእውነተኞቹ እንደ ሆንክ የአላህን ቅጣት አምጣብን» ማለት እንጂ ሌላ አልነበረም፡፡

قَالَ رَبِّ ٱنصُرۡنِي عَلَى ٱلۡقَوۡمِ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ﴿٣٠﴾

30. «ጌታዬ ሆይ! በአመጸኞች ሕዝቦች ላይ እርዳኝ» አለ፡፡

وَلَمَّا جَآءَتۡ رُسُلُنَآ إِبۡرَٰهِيمَ بِٱلۡبُشۡرَىٰ قَالُوٓاْ إِنَّا مُهۡلِكُوٓاْ أَهۡلِ هَٰذِهِ ٱلۡقَرۡيَةِۖ إِنَّ أَهۡلَهَا كَانُواْ ظَٰلِمِينَ ﴿٣١﴾

31. መልክተኞቻችንም ኢብራሂምን በብስራት በመጡት ጊዜ «እኛ የዚህችን ከተማ ሰዎች አጥፊዎች ነን፡፡ ሰዎቿ በዳዮች ነበሩና» አሉት፡፡

قَالَ إِنَّ فِيهَا لُوطٗاۚ قَالُواْ نَحۡنُ أَعۡلَمُ بِمَن فِيهَاۖ لَنُنَجِّيَنَّهُۥ وَأَهۡلَهُۥٓ إِلَّا ٱمۡرَأَتَهُۥ كَانَتۡ مِنَ ٱلۡغَٰبِرِينَ ﴿٣٢﴾

32. «በእርሷ ውስጥ ሉጥ አለ እኮ» አላቸው፡፡ «እኛ በውስጧ ያለውን ይበልጥ ዐዋቂ ነን፡፡ (እርሱን) በእርግጥ እናድነዋለን፡፡ ቤተሰቦቹንም ጭምር፡፡ ሚስቱ ብቻ ስትቀር፡፡ እርሷ በጥፋቱ ውስጥ ከሚቀሩት ናት» አሉት፡፡

وَلَمَّآ أَن جَآءَتۡ رُسُلُنَا لُوطٗا سِيٓءَ بِهِمۡ وَضَاقَ بِهِمۡ ذَرۡعٗاۖ وَقَالُواْ لَا تَخَفۡ وَلَا تَحۡزَنۡ إِنَّا مُنَجُّوكَ وَأَهۡلَكَ إِلَّا ٱمۡرَأَتَكَ كَانَتۡ مِنَ ٱلۡغَٰبِرِينَ ﴿٣٣﴾

33. መልክተኞቻችንም ሉጥን በመጡት ጊዜ በእነሱ ምክንያት አዘነ፡፡ በእነርሱም ልቡ ተጨነቀ፡፡ «አትፍራ፤ አትዘንም፡፡ እኛ አዳኞችህ ነን፡፡ ቤተሰቦችህንም፤ ሚስትህ ብቻ ስትቀር፡፡ እርሷ በጥፋቱ ውስጥ ከቀሪዎቹ ናት» አሉትም፡፡

إِنَّا مُنزِلُونَ عَلَىٰٓ أَهۡلِ هَٰذِهِ ٱلۡقَرۡيَةِ رِجۡزٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ بِمَا كَانُواْ يَفۡسُقُونَ ﴿٣٤﴾

34. «እኛ በዚህች ከተማ ሰዎች ላይ ያምጹ በነበሩት ምክንያት ከሰማይ ቅጣትን አውራጆች ነን፡፡»

وَلَقَد تَّرَكۡنَا مِنۡهَآ ءَايَةَۢ بَيِّنَةٗ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ﴿٣٥﴾

35. በእርግጥም ለሚያስቡ ሰዎች ከእርሷ ግልጽ ምልክትን ተውን (አስቀረን)፡፡

وَإِلَىٰ مَدۡيَنَ أَخَاهُمۡ شُعَيۡبٗا فَقَالَ يَٰقَوۡمِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ وَٱرۡجُواْ ٱلۡيَوۡمَ ٱلۡأٓخِرَ وَلَا تَعۡثَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ مُفۡسِدِينَ ﴿٣٦﴾

36. ወደ መድየንም ወንድማቸውን ሹዐይብን (ላክን)፡፡ «ሕዝቦቼ ሆይ! አላህን ተገዙ፣ የመጨረሻውንም ቀን ፍሩ፣ በምድርም ውስጥ የምታጠፉ ሆናችሁ አታበላሹ አላቸውም፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلرَّجۡفَةُ فَأَصۡبَحُواْ فِي دَارِهِمۡ جَٰثِمِينَ ﴿٣٧﴾

37. አስተባባሉትም፡፡ የምድር መንቀጥቀጥ ያዘቻቸው፡፡ በሃገራቸውም ውስጥ ተንከፍርረው አነጉ፡፡

وَعَادٗا وَثَمُودَاْ وَقَد تَّبَيَّنَ لَكُم مِّن مَّسَٰكِنِهِمۡۖ وَزَيَّنَ لَهُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُ أَعۡمَٰلَهُمۡ فَصَدَّهُمۡ عَنِ ٱلسَّبِيلِ وَكَانُواْ مُسۡتَبۡصِرِينَ ﴿٣٨﴾

38. ዓድንና ሰሙድንም (አጠፋን)፡፡ ከመኖሪያዎቻቸውም (ፍርስራሾች በኩል መጥፋታቸው) ለእናንተ በእውነት ተገለጠላችሁ፡፡ ሰይጣንም ሥራዎቻቸውን ለእነርሱ ሸለመላቸው፡፡ ከመንገድም አገዳቸው፡፡ የማስተዋልም ባለቤቶች ነበሩ፤ (ግን አላስተዋሉም)፡፡

39. ቃሩንንም ፈርዖንንም ሃማንንም (አጠፋን)፡፡ ሙሳም በተዓምራቶች በእርግጥ መጣባቸው፡፡ በምድርም ላይ ኮሩ፡፡ አምላጪዎችም አልነበሩም፡፡

وَقَٰرُونَ وَفِرۡعَوۡنَ وَهَٰمَٰنَۖ وَلَقَدۡ جَآءَهُم مُّوسَىٰ بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَٱسۡتَكۡبَرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا كَانُواْ سَٰبِقِينَ ٣٩

40. ሁሉንም በኀጢአቱ ያዝነው፡፡ ከእነሱም ውስጥ ጠጠርን ያዘለ ነፋስን የላክንበት አልለ፡፡ ከእነሱም ውስጥ ጩኸት የያዘችው አልለ፡፡ ከእነርሱም ውስጥ በእርሱ ምድርን የደረባንበት አልለ፡፡ ከእነሱም ውስጥ ያሰጠምንው አልለ፡፡ አላህም የሚበድላቸው አልነበረም፡፡ ግን ነፍሶቻቸውን የሚበድሉ ነበሩ፡፡

فَكُلًّا أَخَذۡنَا بِذَنۢبِهِۦۖ فَمِنۡهُم مَّنۡ أَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِ حَاصِبٗا وَمِنۡهُم مَّنۡ أَخَذَتۡهُ ٱلصَّيۡحَةُ وَمِنۡهُم مَّنۡ خَسَفۡنَا بِهِ ٱلۡأَرۡضَ وَمِنۡهُم مَّنۡ أَغۡرَقۡنَاۚ وَمَا كَانَ ٱللَّهُ لِيَظۡلِمَهُمۡ وَلَٰكِن كَانُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ يَظۡلِمُونَ ٤٠

41. የእነዚያ ከአላህ ሌላ ረዳቶችን (ጣዖታትን) የያዙ ሰዎች ምሳሌ ቤትን እንደ ሠራች ሸረሪት ብጤ ነው፡፡ ከቤቶችም ሁሉ በጣም ደካማው የሸረሪት ቤት ነው፡፡ ቢያውቁ ኖሮ (አማልክት አድርገው አይግገዟቸውም ነበር)፡፡

مَثَلُ ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَوۡلِيَآءَ كَمَثَلِ ٱلۡعَنكَبُوتِ ٱتَّخَذَتۡ بَيۡتٗاۖ وَإِنَّ أَوۡهَنَ ٱلۡبُيُوتِ لَبَيۡتُ ٱلۡعَنكَبُوتِۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٤١

42. አላህ ያንን ከእርሱ ሌላ የሚግገዙትን ማንኛውንም ያውቃል፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ مَا يَدۡعُونَ مِن دُونِهِۦ مِن شَيۡءٖۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٤٢

43. እነዚህንም ምሳሌዎች ለሰዎች እንገልጻቸዋለን፡፡ ከሊቃውንቶቹም በስተቀር ሌሎቹ አያውቋትም፡፡

وَتِلۡكَ ٱلۡأَمۡثَٰلُ نَضۡرِبُهَا لِلنَّاسِۖ وَمَا يَعۡقِلُهَآ إِلَّا ٱلۡعَٰلِمُونَ ٤٣

44. «አላህ ሰማያትንና ምድርን እውነተኛ ሆኖ ፈጠረ፡፡ » በዚህ ውስጥ ለምእምናን ተዓምር አለበት፡፡

خَلَقَ ٱللَّهُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ بِٱلۡحَقِّۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ ٤٤

45. ከመጽሐፍ ወደ አንተ የተወረደውን አንብብ፡፡ ሶላትንም ደንቡን ጠብቀህ ስገድ፡፡ ሶላት ከመጥፎና ከሚጠላ ነገር ሁሉ ትከለክላለችና፡፡ አላህንም ማውሳት ከሁሉ ነገር በላጭ ነው፤ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ያውቃል፡፡

ٱتۡلُ مَآ أُوحِيَ إِلَيۡكَ مِنَ ٱلۡكِتَٰبِ وَأَقِمِ ٱلصَّلَوٰةَۖ إِنَّ ٱلصَّلَوٰةَ تَنۡهَىٰ عَنِ ٱلۡفَحۡشَآءِ وَٱلۡمُنكَرِۗ وَلَذِكۡرُ ٱللَّهِ أَكۡبَرُۗ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ مَا تَصۡنَعُونَ ٤٥

46. የመጽሐፉን ባለቤቶችም በዚያች እርሷ መልካም በኾነችው ክርክር እንጂ አትከራከሩ፡፡ ከእነርሱ እነዚያን የበደሉትን ሲቀር፡፡ በሉም «በዚያ ወደኛ በተወረደው ወደናንተም በተወረደው አመንን፡፡ አምላካችንም አምላካችሁም አንድ ነው፡፡ እኛም ለእርሱ ታዛዦች ነን፡ ፡»

۞وَلَا تُجَٰدِلُوٓاْ أَهۡلَ ٱلۡكِتَٰبِ إِلَّا بِٱلَّتِي هِيَ أَحۡسَنُ إِلَّا ٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنۡهُمۡۖ وَقُولُوٓاْ ءَامَنَّا بِٱلَّذِيٓ أُنزِلَ إِلَيۡنَا وَأُنزِلَ إِلَيۡكُمۡ وَإِلَٰهُنَا وَإِلَٰهُكُمۡ وَٰحِدٞ وَنَحۡنُ لَهُۥ مُسۡلِمُونَ ٤٦

47. እንደዚሁም ወዳንተ መጽሐፍን አወረድን፡፡ እነዚያም መጽሐፍን የሰጠናቸው፤ በእርሱ ያምናሉ፡፡ ከእነዚህም (ከመካ ሰዎች) በእርሱ የሚያምኑ አልሉ፡፡ በተዓምራቶቻችንም ከሓዲዎቹ እንጂ ማንም አይክድም፡፡

وَكَذَٰلِكَ أَنزَلۡنَآ إِلَيۡكَ ٱلۡكِتَٰبَۚ فَٱلَّذِينَ ءَاتَيۡنَٰهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ يُؤۡمِنُونَ بِهِۦۖ وَمِنۡ هَٰٓؤُلَآءِ مَن يُؤۡمِنُ بِهِۦۚ وَمَا يَجۡحَدُ بِـَٔايَٰتِنَآ إِلَّا ٱلۡكَٰفِرُونَ ٤٧

48. ከእርሱ በፊትም መጽሐፍን የምታነብ በቀኝህም የምትጽፈው አልነበርክም፡፡ ያን ጊዜ አጥፊዎቹ በእርግጥ በተጠራጠሩ ነበር፡፡

وَمَا كُنتَ تَتْلُواْ مِن قَبْلِهِۦ مِن كِتَٰبٍ وَلَا تَخُطُّهُۥ بِيَمِينِكَۖ إِذًا لَّٱرْتَابَ ٱلْمُبْطِلُونَ ٤٨

49. አይደለም እርሱ (ቁርኣን) በእነዚያ ዕውቀትን በተሰጡት ሰዎች ልቦች ውስጥ (የጠለቀ) ግልጾች አንቀጾች ነው፡፡ በአንቀጾቻችንም በዳዮቹ እንጂ ሌላው አይክድም፡፡

بَلْ هُوَ ءَايَٰتُۢ بَيِّنَٰتٌ فِى صُدُورِ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلْعِلْمَۚ وَمَا يَجْحَدُ بِـَٔايَٰتِنَآ إِلَّا ٱلظَّٰلِمُونَ ٤٩

50. «በእርሱ ላይም ከጌታህ ዘንድ ተዓምራቶች ለምን አልተወረዱም» አሉ፡፡ «ተዓምራቶች አላህ ዘንድ ብቻ ናቸው፡፡ እኔም ግልጽ አስፈራሪ ብቻ ነኝ» በላቸው፡፡

وَقَالُواْ لَوْلَآ أُنزِلَ عَلَيْهِ ءَايَٰتٌ مِّن رَّبِّهِۦۖ قُلْ إِنَّمَا ٱلْءَايَٰتُ عِندَ ٱللَّهِ وَإِنَّمَآ أَنَا۠ نَذِيرٌ مُّبِينٌ ٥٠

51. እኛ መጽሐፉን በእነሱ ላይ የሚነበብ ኾኖ ባንተ ላይ ማውረዳችን አይበቃቸውምን በዚህ ውስጥ ለሚያምኑ ሕዝቦች ችሮታና ግሳጼ አለበት፡፡

أَوَلَمْ يَكْفِهِمْ أَنَّآ أَنزَلْنَا عَلَيْكَ ٱلْكِتَٰبَ يُتْلَىٰ عَلَيْهِمْۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَرَحْمَةً وَذِكْرَىٰ لِقَوْمٍ يُؤْمِنُونَ ٥١

52. «በእኔና በእናንተ መካከል መስካሪ በአላህ በቃ፡፡ በሰማያትና በምድርም ያለውን ሁሉ ያውቃል» በላቸው፡፡ እነዚያም በብላሽ ነገር ያመኑ በአላህም የካዱ እነዚያ እነሱ ከሳሪዎች ናቸው፡፡

قُلْ كَفَىٰ بِٱللَّهِ بَيْنِى وَبَيْنَكُمْ شَهِيدًاۖ يَعْلَمُ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِۗ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱلْبَٰطِلِ وَكَفَرُواْ بِٱللَّهِ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلْخَٰسِرُونَ ٥٢

53. በቅጣትም ያስቸኩሉሃል፡፡ የተወሰነም ጊዜ ባልነበረ ኖሮ ቅጣቱ በመጣባቸው ነበር፡፡ እነርሱ የማያውቁ ሲኾኑም በድንገት በእርግጥ ይመጣባቸዋል፡
፡

وَيَسْتَعْجِلُونَكَ بِٱلْعَذَابِ وَلَوْلَآ أَجَلٌ مُّسَمًّى لَّجَآءَهُمُ ٱلْعَذَابُۚ وَلَيَأْتِيَنَّهُم بَغْتَةً وَهُمْ لَا يَشْعُرُونَ ٥٣

54. በቅጣት ያስቸኩሉሃል፡፡ ገሀነምም ከሓዲዎችን በእርግጥ ከባቢ ናት፡፡

يَسْتَعْجِلُونَكَ بِٱلْعَذَابِ وَإِنَّ جَهَنَّمَ لَمُحِيطَةٌۢ بِٱلْكَٰفِرِينَ ٥٤

55. ቅጣቱ ከበላያቸው፣ ከእግሮቻቸውም ሥር በሚሸፍናቸው ቀን ትሠሩት የነበራችሁትን ቅመሱ በሚላቸውም (ቀን ትከበባቸዋለች)፡፡

يَوْمَ يَغْشَىٰهُمُ ٱلْعَذَابُ مِن فَوْقِهِمْ وَمِن تَحْتِ أَرْجُلِهِمْ وَيَقُولُ ذُوقُواْ مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ٥٥

56. እናንተ ያመናችሁ ባሮቼ ሆይ! ምድሬ በእርግጥ ሰፊ ናት፤ (ብትቸገሩ ተሰደዱ)፡፡ እኔንም ብቻ ተገዙኝ፡፡

يَٰعِبَادِىَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِنَّ أَرْضِى وَٰسِعَةٌ فَإِيَّٰىَ فَٱعْبُدُونِ ٥٦

57. ነፍስ ሁሉ ሞትን ቀማሽ ናት፡፡ ከዚያም ወደኛ ትመለሳላችሁ፡፡

كُلُّ نَفْسٍ ذَآئِقَةُ ٱلْمَوْتِۖ ثُمَّ إِلَيْنَا تُرْجَعُونَ ٥٧

58. እነዚያም ያመኑና መልካም ሥራዎችን የሠሩ ከገነት በሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ሰገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ በእርግጥ እናሰፍራቸዋለን፡፡ የሠራተኞች ምንዳ ምንኛ አማረ!

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَنُبَوِّئَنَّهُم مِّنَ ٱلْجَنَّةِ غُرَفًا تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَاۚ نِعْمَ أَجْرُ ٱلْعَٰمِلِينَ ٥٨

59. (እነሱ) እነዚያ የታገሱ በጌታቸውም ላይ የሚመኩ ናቸው::

ٱلَّذِينَ صَبَرُواْ وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٥٩

60. ከተንቀሳቃሽም ምግቧን ለመሸከም የማትችለው ብዙ ናት:: አላህ ይመግባታል:: እናንተንም (ይመግባል):: እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና::

وَكَأَيِّن مِّن دَآبَّةٍ لَّا تَحۡمِلُ رِزۡقَهَا ٱللَّهُ يَرۡزُقُهَا وَإِيَّاكُمۡۚ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٦٠

61. ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ ፀሐይንና ጨረቃንም የገራ ማን እንደኾነ ብትጠይቃቸው «በእርግጥ አላህ ነው» ይሉሃል:: ታድያ እንዴት ይመለሳሉ::

وَلَئِن سَأَلۡتَهُم مَّنۡ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَسَخَّرَ ٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَ لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُۖ فَأَنَّىٰ يُؤۡفَكُونَ ٦١

62. አላህ ከባሮቹ ለሚሻው ሲሳይን ያሰፋል:: ለእርሱም ያጠብባል:: አላህ በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነውና::

ٱللَّهُ يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦ وَيَقۡدِرُ لَهُۥٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ٦٢

63. ከሰማይም ውሃን ያወረደና በእርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው ያደረጋት ማን እንደኾነ ብትጠይቃቸው «አላህ ነው» ይሉሃል:: «ምስጋና ለአላህ ነው» በላቸው:: ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም::

وَلَئِن سَأَلۡتَهُم مَّن نَّزَّلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَحۡيَا بِهِ ٱلۡأَرۡضَ مِنۢ بَعۡدِ مَوۡتِهَا لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُۚ قُلِ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡقِلُونَ ٦٣

64. ይህችም የቅርቢቱ ሕይወት መታለያና ጨዋታ እንጂ ሌላ አይደለችም:: የመጨረሻይቱም አገር እርሷ በእርግጥ የዘላለም ሕይወት አገር ናት:: የሚያውቁ ቢኾኑ ኖሮ፤ (ጠፊይቱን ሕይወት አይመርጡም ነበር)::

وَمَا هَٰذِهِ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَآ إِلَّا لَهۡوٞ وَلَعِبٞۚ وَإِنَّ ٱلدَّارَ ٱلۡأٓخِرَةَ لَهِيَ ٱلۡحَيَوَانُۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٦٤

65. በመርከቦች ውስጥ በተሳፈሩ ጊዜም አላህን መገዛትን ለእርሱ ብቻ ያጠሩ ኾነው ይጠሩታል:: ወደ የብስ (በማውጣት) ባዳናቸው ጊዜም ወዲያውኑ እነርሱ (ጣዖትን) ያጋራሉ::

فَإِذَا رَكِبُواْ فِي ٱلۡفُلۡكِ دَعَوُاْ ٱللَّهَ مُخۡلِصِينَ لَهُ ٱلدِّينَ فَلَمَّا نَجَّىٰهُمۡ إِلَى ٱلۡبَرِّ إِذَا هُمۡ يُشۡرِكُونَ ٦٥

66. በሰጠናቸው ጸጋ ሊክዱና ሊጠቃቀሙ (ያጋራሉ):: ወደፊትም (የሚጠብቃቸውን) ያውቃሉ::

لِيَكۡفُرُواْ بِمَآ ءَاتَيۡنَٰهُمۡ وَلِيَتَمَتَّعُواْۚ فَسَوۡفَ يَعۡلَمُونَ ٦٦

67. ሰዎቹ ከዙሪያቸው ሲነጠቁ እኛ (አገራቸውን ) ጸጥተኛ ክልል ማድረጋችንን አያዩምን በውድቅ ነገር ያምናሉን በአላህም ጸጋ ይክዳሉን

أَوَلَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّا جَعَلۡنَا حَرَمًا ءَامِنٗا وَيُتَخَطَّفُ ٱلنَّاسُ مِنۡ حَوۡلِهِمۡۚ أَفَبِٱلۡبَٰطِلِ يُؤۡمِنُونَ وَبِنِعۡمَةِ ٱللَّهِ يَكۡفُرُونَ ٦٧

68. በአላህ ላይም ውሸትን ከቀጣጠፈ ሰው ወይም እውነቱ በመጣለት ጊዜ ከአስዋሸ ይበልጥ በዳይ ማነው በገሀነም ውስጥ ለከሓዲዎች መኖሪያ የለምን

وَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّنِ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا أَوۡ كَذَّبَ بِٱلۡحَقِّ لَمَّا جَآءَهُۥٓۚ أَلَيۡسَ فِي جَهَنَّمَ مَثۡوٗى لِّلۡكَٰفِرِينَ ٦٨

69. እነዚያም በእኛ መንገድ የታገሉ መንገዳችንን በእርግጥ እንመራቸዋለን:: አላህም በእርግጥ ከበጎ ሠሪዎች ጋር ነው::

وَٱلَّذِينَ جَٰهَدُواْ فِينَا لَنَهۡدِيَنَّهُمۡ سُبُلَنَاۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَمَعَ ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٦٩

# ሱረቱ አል ሩም

# سورة الروم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ለ.መ (አሊፍ ላም ሚም)::

الٓمٓ ١

2. ሩም ተሸነፈች::

غُلِبَتِ ٱلرُّومُ ٢

3. በጣም ቅርብ በሆነችው ምድር:: እነርሱም ከመሸነፋቸው በኋላ በእርግጥ ያሸንፋሉ::

فِيٓ أَدۡنَى ٱلۡأَرۡضِ وَهُم مِّنۢ بَعۡدِ غَلَبِهِمۡ سَيَغۡلِبُونَ ٣

4. በጥቂት ዓመታት ውስጥ (ያሸንፋሉ):: ትዕዛዙ በፊትም በኋላም የአላህ ነው:: በዚያ ቀንም ምእመናን ይደሰታሉ::

فِي بِضۡعِ سِنِينَۗ لِلَّهِ ٱلۡأَمۡرُ مِن قَبۡلُ وَمِنۢ بَعۡدُۚ وَيَوۡمَئِذٖ يَفۡرَحُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٤

5. በአላህ እርዳታ (ይደሰታሉ):: የሚሻውን ሰው ይረዳል፤ እርሱም አሸናፊው አዛኙ ነው::

بِنَصۡرِ ٱللَّهِۚ يَنصُرُ مَن يَشَآءُۖ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ٥

6. አላህ እርዳታን ቀጠረ:: አላህ ቀጠሮውን አያፈርስም:: ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያውቁም::

وَعۡدَ ٱللَّهِۖ لَا يُخۡلِفُ ٱللَّهُ وَعۡدَهُۥ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٦

7. ከቅርቢቱ ህይወት ግልጹን ብቻ ያውቃሉ:: እነርሱም ከኋለኛይቱ ዓለም እነርሱ ዘንጊዎች ናቸው::

يَعۡلَمُونَ ظَٰهِرٗا مِّنَ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَهُمۡ عَنِ ٱلۡأٓخِرَةِ هُمۡ غَٰفِلُونَ ٧

8. በነፍሶቻቸው (ሁኔታ) አያስተውሉምን? ሰማያትንና ምድርን በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ አላህ በእውነትና በተወሰነ ጊዜ እንጂ አልፈጠራቸውም:: ከሰዎቹም ብዙዎቹ በጌታቸው መገናኘት ከሓዲዎች ናቸው::

أَوَلَمۡ يَتَفَكَّرُواْ فِيٓ أَنفُسِهِمۗ مَّا خَلَقَ ٱللَّهُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَآ إِلَّا بِٱلۡحَقِّ وَأَجَلٖ مُّسَمّٗىۗ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِ بِلِقَآيِٕ رَبِّهِمۡ لَكَٰفِرُونَ ٨

9. በምድር ላይ አይኼዱምና የእነዚያን ከበፊታቸው የነበሩትን ሰዎች ፍጻሜ እንዴት እንደነበረ አይመለከቱምን? በኀይል ከእነርሱም ይበልጥ የጠነከሩ ነበሩ:: ምድርንም አረሱ:: (እነዚህ) ከአለሟትም የበዛ አለሟት:: መልዕክተ ኞቻቸውም በተዓምራቶች መጡባቸው፤ (አስተባበሉምና ጠፉ):: አላህም የሚበድላቸው አልነበረም፤ ግን ነፍሶቻቸውን ይበድሉ ነበሩ::

أَوَلَمۡ يَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَيَنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَانُوٓاْ أَشَدَّ مِنۡهُمۡ قُوَّةٗ وَأَثَارُواْ ٱلۡأَرۡضَ وَعَمَرُوهَآ أَكۡثَرَ مِمَّا عَمَرُوهَا وَجَآءَتۡهُمۡ رُسُلُهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِۖ فَمَا كَانَ ٱللَّهُ لِيَظۡلِمَهُمۡ وَلَٰكِن كَانُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ يَظۡلِمُونَ ٩

10. ከዚያም የእነዚያ ያጠፉት ሰዎች መጨረሻ በአላህ አንቀጾች በማስተባበላቸውና በእርሷ የሚሳለቁ በመኾናቸው ምክንያት መጥፎ ቅጣት ሆነች::

ثُمَّ كَانَ عَٰقِبَةَ ٱلَّذِينَ أَسَٰٓـُٔواْ ٱلسُّوٓأَىٰٓ أَن كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَكَانُواْ بِهَا يَسۡتَهۡزِءُونَ ١٠

11. አላህ መፍጠርን ይጀምራል:: ከዚያም ይመልሰዋል፤ ከዚያም ወደርሱ ትመለሳላችሁ::

ٱللَّهُ يَبۡدَؤُاْ ٱلۡخَلۡقَ ثُمَّ يُعِيدُهُۥ ثُمَّ إِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ١١

12. ሰዓቲቱም በምትቆምበት ቀን አመጸኞች ጭጭ ይላሉ፡፡

وَيَوۡمَ تَقُومُ ٱلسَّاعَةُ يُبۡلِسُ ٱلۡمُجۡرِمُونَ ١٢

13. ለእነርሱም ከሚያጋሩዋቸው (ጣዖታት) አማላጆች አይኖሯቸውም፤ በሚያጋሯቸውም (ጣዖታት) ከሓዲዎች ይኾናሉ፡፡

وَلَمۡ يَكُن لَّهُم مِّن شُرَكَآئِهِمۡ شُفَعَٰٓؤُاْ وَكَانُواْ بِشُرَكَآئِهِمۡ كَٰفِرِينَ ١٣

14. ሰዓቲቱ በምትቆምበት ቀንም በዚያ ቀን ይለያያሉ፡፡

وَيَوۡمَ تَقُومُ ٱلسَّاعَةُ يَوۡمَئِذٖ يَتَفَرَّقُونَ ١٤

15. እነዚያ ያመኑትና መልካሞችን ሥራዎች የሠሩትማ እነርሱ በገነት ጨፌ ውስጥ ይደሰታሉ፡፡

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فَهُمۡ فِي رَوۡضَةٖ يُحۡبَرُونَ ١٥

16. እነዚያም የካዱትማ በአንቀጾቻችንና በኋለኛይቱም ዓለም መገናኘት ያስተባበሉት እነዚያ በቅጣቱ ውስጥ የሚጣዱ ናቸው፡፡

وَأَمَّا ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا وَلِقَآيِٕ ٱلۡأٓخِرَةِ فَأُوْلَٰٓئِكَ فِي ٱلۡعَذَابِ مُحۡضَرُونَ ١٦

17. አላህንም በምታመሹ ጊዜ በምታነጉም ጊዜ አጥሩት፤ (ስገዱለት)፡፡

فَسُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ حِينَ تُمۡسُونَ وَحِينَ تُصۡبِحُونَ ١٧

18. ምስጋናም በሰማያትና በምድር ውስጥ ለርሱ ብቻ (የተገባው) ነው፡፡ በሰርክም፤ በቀትር ውስጥ በምትገቡም ጊዜ፤ (አጥሩት)፡፡

وَلَهُ ٱلۡحَمۡدُ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَعَشِيّٗا وَحِينَ تُظۡهِرُونَ ١٨

19. ሕያውን ከሙት ያወጣል፡፡ ሙታንም ከሕያው ያወጣል፡፡ ምድርንም ከሞተች በኋላ ህያው ያደርጋታል፡፡ እንደዚሁም (ከመቃብር) ትወጣላችሁ፡፡

يُخۡرِجُ ٱلۡحَيَّ مِنَ ٱلۡمَيِّتِ وَيُخۡرِجُ ٱلۡمَيِّتَ مِنَ ٱلۡحَيِّ وَيُحۡيِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَاۚ وَكَذَٰلِكَ تُخۡرَجُونَ ١٩

20. እናንተንም ከዐፈር መፍጠሩ ከዚያም እናንተ ወዲያውኑ የምትበታተኑ ሰዎች መኾናችሁ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦٓ أَنۡ خَلَقَكُم مِّن تُرَابٖ ثُمَّ إِذَآ أَنتُم بَشَرٞ تَنتَشِرُونَ ٢٠

21. ለእናንተም ከነፍሶቻችሁ (ከጎሶቻችሁ) ሚስቶችን ወደእነርሱ ትረኩ ዘንድ መፍጠሩ፣ በመካከላችሁም ፍቅርንና እዝነትን ማድረጉ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያስተውሉ ሕዝቦች ተዓምራቶች አሉ፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦٓ أَنۡ خَلَقَ لَكُم مِّنۡ أَنفُسِكُمۡ أَزۡوَٰجٗا لِّتَسۡكُنُوٓاْ إِلَيۡهَا وَجَعَلَ بَيۡنَكُم مَّوَدَّةٗ وَرَحۡمَةًۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَتَفَكَّرُونَ ٢١

22. ሰማያትንና ምድርንም መፍጠሩ፣ የቋንቋዎቻችሁና የመልኮቻችሁም መለያየት፣ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡ ፡ በዚህ ውስጥ ለዐዋቂዎች ተዓምራቶች አሉበት፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦ خَلۡقُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَٱخۡتِلَٰفُ أَلۡسِنَتِكُمۡ وَأَلۡوَٰنِكُمۡۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّلۡعَٰلِمِينَ ٢٢

23. በሌሊትና በቀንም መተኛታችሁ፣ ከችሮታውም መፈለጋችሁ ከምልክቶቹ ነው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚሰሙ ሕዝቦች ተዓምራቶች አሉበት፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦ مَنَامُكُم بِٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِ وَٱبۡتِغَآؤُكُم مِّن فَضۡلِهِۦٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَسۡمَعُونَ ٢٣

24. ብልጭታንም ፈሪዎችና ከጀዮች ስትሆኑ ለእናንተ ማሳየቱ፣ ከሰማይም ውሃን ማውረዱ፣ በእርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው ማድረጉ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያስቡ ሕዝቦች ተዓምራቶች አልሉበት፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦ يُرِيكُمُ ٱلۡبَرۡقَ خَوۡفٗا وَطَمَعٗا وَيُنَزِّلُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَيُحۡيِۦ بِهِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَآۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ٢٤

25. ሰማይና ምድርም (ያለምሰሶ) በትዕዛዙ መቆማቸው፣ ከዚያም (መልአኩ ለትንሣኤ) ከምድር ጥሪን በጠራችሁ ጊዜ እናንተ ወዲያውኑ የምትወጡ መሆናችሁ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦٓ أَن تَقُومَ ٱلسَّمَآءُ وَٱلۡأَرۡضُ بِأَمۡرِهِۦۚ ثُمَّ إِذَا دَعَاكُمۡ دَعۡوَةٗ مِّنَ ٱلۡأَرۡضِ إِذَآ أَنتُمۡ تَخۡرُجُونَ ٢٥

26. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የእርሱ ብቻ ነው፡ ፡ ሁሉም ለእርሱ ታዛዦች ናቸው፡፡

وَلَهُۥ مَن فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ كُلّٞ لَّهُۥ قَٰنِتُونَ ٢٦

27. እርሱም ያ መፍጠርን የሚጀምር ከዚያም የሚመልሰው ነው፡፡ እርሱም (መመለሱ) በእርሱ ላይ በጣም ገር ነው፡፡ ለእርሱም በሰማያትም በምድርም ከፍተኛ ባሕርይ (አንድነትና ለእርሱ ብጤ የሌለው መኾን) አልለው፡፡ እርሱም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي يَبۡدَؤُاْ ٱلۡخَلۡقَ ثُمَّ يُعِيدُهُۥ وَهُوَ أَهۡوَنُ عَلَيۡهِۚ وَلَهُ ٱلۡمَثَلُ ٱلۡأَعۡلَىٰ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٢٧

28. ለእናንተ ከነፍሶቻችሁ የሆነን ምሳሌ አደረገላችሁ፡ ፡ (እርሱም) እጆቻችሁ ከያዟቸው (ባሮች) ውስጥ በሰጠናችሁ ጸጋ ለእናንተ ተጋሪዎች አሏችሁን? ታዲያ እናንተና እነርሱ በእርሱ ትክክል ናችሁን? ነፍሶቻችሁን (ብጤዎቻችሁን) እንደምትፈሩ ትፈሯቸዋላችሁን? እንደዚሁ ለሚያስተውሉ ሕዝቦች፤ አንቀጾችን እንገልጻለን፡፡

ضَرَبَ لَكُم مَّثَلٗا مِّنۡ أَنفُسِكُمۡۖ هَل لَّكُم مِّن مَّا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُكُم مِّن شُرَكَآءَ فِي مَا رَزَقۡنَٰكُمۡ فَأَنتُمۡ فِيهِ سَوَآءٞ تَخَافُونَهُمۡ كَخِيفَتِكُمۡ أَنفُسَكُمۡۚ كَذَٰلِكَ نُفَصِّلُ ٱلۡأٓيَٰتِ لِقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ٢٨

29. ይልቁንም እነዚያ የበደሉ ሰዎች ያለ ዕውቀት ዝንባሌዎቻቸውን ተከተሉ፡፡ አላህም ያጠመመውን ሰው የሚያቀናው ማነው? ለእነርሱም ከረዳቶች ምንም የላቸውም፡፡

بَلِ ٱتَّبَعَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوٓاْ أَهۡوَآءَهُم بِغَيۡرِ عِلۡمٖۖ فَمَن يَهۡدِي مَنۡ أَضَلَّ ٱللَّهُۖ وَمَا لَهُم مِّن نَّٰصِرِينَ ٢٩

30. ወደ እውነት ተዘንባይ ኾነህም ፊትህን ለሃይማኖት ቀጥ አድርግ፡፡ የአላህን ፍጥረት ያችን አላህ ሰዎችን በእርስዋ ላይ የፈጠረባትን (ሃይማኖት ያዟት)፡፡ የአላህን ፍጥረት መለወጥ የለም፡፡ ይህ ቀጥተኛ ሃይማኖት ነው፡ ፡ ግን አብዛኛዎቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

فَأَقِمۡ وَجۡهَكَ لِلدِّينِ حَنِيفٗاۚ فِطۡرَتَ ٱللَّهِ ٱلَّتِي فَطَرَ ٱلنَّاسَ عَلَيۡهَاۚ لَا تَبۡدِيلَ لِخَلۡقِ ٱللَّهِۚ ذَٰلِكَ ٱلدِّينُ ٱلۡقَيِّمُ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٣٠

31. ወደእርሱ ተመላሾች ሆናችሁ (የአላህን ሃይማኖት ያዙ)፡፡ ፍሩትም፡፡ ሶላትንም አስተካክላችሁ ስገዱ፡፡ ከአጋሪዎቹም አትሁኑ፡፡

۞مُنِيبِينَ إِلَيۡهِ وَٱتَّقُوهُ وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَلَا تَكُونُواْ مِنَ ٱلۡمُشۡرِكِينَ ٣١

32. ከእነዚያ ሃይማኖታቸውን ከለያዩትና ክፍልፍሎችም ከሆኑት (አትሁኑ)፡፡ ሕዝብ ሁሉ እነሱ ዘንድ ባለው ነገር ተደሳቾች ናቸው፡፡

مِنَ ٱلَّذِينَ فَرَّقُواْ دِينَهُمۡ وَكَانُواْ شِيَعٗاۖ كُلُّ حِزۡبِۭ بِمَا لَدَيۡهِمۡ فَرِحُونَ ٣٢

33. ሰዎችንም ችግር ባገኛቸው ጊዜ ጌታቸውን ወደርሱ ተመላሾች ሆነው ይጠሩታል፡፡ ከዚያም ከእርሱ ችሮታን ባቀመሳቸው ጊዜ ከእነርሱ ከፊሎቹ ወዲያውኑ በጌታቸው (ጣዖትን) ያጋራሉ፡፡

34. በሰጠናቸው ጸጋ ሊክዱ (ያጋራሉ)፡፡ ተጣቀሙም፤ በእርግጥም (መጨረሻችሁን) ወደፊት ታውቃላችሁ፡፡

35. በእነርሱ ላይ አስረጅ አወረድን? ታዲያ እርሱ በዚያ በእርሱ ያጋሩ በነበሩት ነገር ይናገራልን;(የለም)፡፡

36. ሰዎችንም ችሮታን ባቀመስናቸው ገዜ በእርሷ ይደሰታሉ፡፡ እጆቻቸውም ባሳለፉት ምክንያት መከራ ብታገኛቸው ወዲያውኑ እነርሱ ተስፋ ይቆርጣሉ፡፡

37. አላህ ለሚሻው ሰው ሲሳይን የሚያሰፋ የሚያጠብም መሆኑን አያዩምን በዚህ ውስጥ ለሚያምኑ ሕዝቦች አስደናቂ ምልክቶች አሉሉበት፡፡

38. የዝምድናን ባለቤት ተገቢውን ስጠው፡፡ ለድኻም ለመንገደኛም (እርዳ)፡፡ ይህ ለእነዚያ የአላህን ፊት (ውዴታውን) ለሚሹ መልካም ነው፡፡ እነዚያም እነርሱ የፈለጉትን የሚያገኙ ናቸው፡፡

39. ከበረከትም በሰዎች ገንዘቦች ውስጥ ይጨመር ዘንድ የምትሰጡት አላህ ዘንድ አይጨምርም፡፡ ከምጽዋትም የአላህን ፊት የምትሹ ሆናችሁ የምትሰጡት እነዚያ (ሰጪዎች) አበርካቾች እነርሱ ናቸው፡፡

40. አላህ ያ የፈጠራችሁ፣ ከዚያም ሲሳይን የሰጣችሁ፣ ከዚያም የሚገድላችሁ ከዚያም ሕያው የሚያደርጋችሁ ነው፡፡ ከምታጋሯቸው (ጣዖታት) ውስጥ ከዚህ ነገር አንዳችን የሚሠራ አለን ለአላህ ጥራት ይገባው፡፡ (በእርሱ) ከሚያጋሩትም ሁሉ ላቀ፡፡

41. የሰዎች እጆች በሠሩት ኃጢአት ምክንያት የዚያን የሠሩትን ከፊሉን ያቀምሳቸው ዘንድ መከራው በየብስና በባሕር ተገለጠ፤ (ተሰራጨ)፡፡ እነርሱ ሊመለሱ ይከጀላልና፡፡

42. «በምድር ላይ ኺዱ የእነዚያንም በፊት የነበሩትን ሰዎች መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከቱ» በላቸው፡፡ አብዛኞቻቸው አጋሪዎች ነበሩ፡፡

43. ለርሱ መመለስ የሌለው ቀን (የትንሣኤ ቀን) ከአላህ ሳይመጣ በፊት ፊትህን ወደ ቀጥተኛው ሃይማኖት ቀጥ አድርግ፡፡ በዚያ ቀን (ወደ ገነትና ወደ እሳት) ይለያያሉ፡፡

وَإِذَا مَسَّ ٱلنَّاسَ ضُرٌّ دَعَوْاْ رَبَّهُم مُّنِيبِينَ إِلَيْهِ ثُمَّ إِذَآ أَذَاقَهُم مِّنْهُ رَحْمَةً إِذَا فَرِيقٌ مِّنْهُم بِرَبِّهِمْ يُشْرِكُونَ ٣٣

لِيَكْفُرُواْ بِمَآ ءَاتَيْنَٰهُمْۚ فَتَمَتَّعُواْ فَسَوْفَ تَعْلَمُونَ ٣٤

أَمْ أَنزَلْنَا عَلَيْهِمْ سُلْطَٰنًا فَهُوَ يَتَكَلَّمُ بِمَا كَانُواْ بِهِۦ يُشْرِكُونَ ٣٥

وَإِذَآ أَذَقْنَا ٱلنَّاسَ رَحْمَةً فَرِحُواْ بِهَاۖ وَإِن تُصِبْهُمْ سَيِّئَةٌۢ بِمَا قَدَّمَتْ أَيْدِيهِمْ إِذَا هُمْ يَقْنَطُونَ ٣٦

أَوَلَمْ يَرَوْاْ أَنَّ ٱللَّهَ يَبْسُطُ ٱلرِّزْقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقْدِرُۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٍ لِّقَوْمٍ يُؤْمِنُونَ ٣٧

فَـَٔاتِ ذَا ٱلْقُرْبَىٰ حَقَّهُۥ وَٱلْمِسْكِينَ وَٱبْنَ ٱلسَّبِيلِۚ ذَٰلِكَ خَيْرٌ لِّلَّذِينَ يُرِيدُونَ وَجْهَ ٱللَّهِۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُفْلِحُونَ ٣٨

وَمَآ ءَاتَيْتُم مِّن رِّبًا لِّيَرْبُوَاْ فِيٓ أَمْوَٰلِ ٱلنَّاسِ فَلَا يَرْبُواْ عِندَ ٱللَّهِۖ وَمَآ ءَاتَيْتُم مِّن زَكَوٰةٍ تُرِيدُونَ وَجْهَ ٱللَّهِ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُضْعِفُونَ ٣٩

ٱللَّهُ ٱلَّذِي خَلَقَكُمْ ثُمَّ رَزَقَكُمْ ثُمَّ يُمِيتُكُمْ ثُمَّ يُحْيِيكُمْۖ هَلْ مِن شُرَكَآئِكُم مَّن يَفْعَلُ مِن ذَٰلِكُم مِّن شَيْءٍۚ سُبْحَٰنَهُۥ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يُشْرِكُونَ ٤٠

ظَهَرَ ٱلْفَسَادُ فِي ٱلْبَرِّ وَٱلْبَحْرِ بِمَا كَسَبَتْ أَيْدِي ٱلنَّاسِ لِيُذِيقَهُم بَعْضَ ٱلَّذِي عَمِلُواْ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ ٤١

قُلْ سِيرُواْ فِي ٱلْأَرْضِ فَٱنظُرُواْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلُۚ كَانَ أَكْثَرُهُم مُّشْرِكِينَ ٤٢

فَأَقِمْ وَجْهَكَ لِلدِّينِ ٱلْقَيِّمِ مِن قَبْلِ أَن يَأْتِيَ يَوْمٌ لَّا مَرَدَّ لَهُۥ مِنَ ٱللَّهِۖ يَوْمَئِذٍ يَصَّدَّعُونَ ٤٣

44. የካደ ሰው ክህደቱ (ጠንቁ) በእርሱው ላይ ነው፡፡ መልካምም የሠሩ ለነፍሶቻቸው (ማረፊያዎችን) ያዘጋጃሉ፡፡

45. እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችንም የሠሩትን ከችሮታው ይመነዳ ዘንድ (ይለያያሉ)፡፡ እርሱ ከሓዲዎችን አይወድምና፡፡

46. ነፋሶችንም (በዝናብ) ልታበስራችሁ፣ ከችሮታውም (በእርሷ) ሊያቀምሳችሁ፣ መርከቦችም በትዕዛዙ እንዲንሻለሉ፣ ከችሮታውም እንድትፈልጉ፣ ታመሰግኑትም ዘንድ መላኩ ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡ ፡

47. ከአንተ በፊትም መልክተኞችን ወደየሕዝቦቻቸው በእርግጥ ላክን፡፡ በግልጽ ማስረጃዎችም መጡባቸው፡፡ ከእነዚያ ካመጹትም ተበቀልን፡፡ ምእመናቹንም መርዳት በእኛ ላይ ተገቢ ሆነ፡፡

48. አላህ ያ ነፋሶችን የሚልክ ነው፡፡ ደመናንም ይቀሰቅሳሉ፡፡ በሰማይ ላይም እንደሚሻ ይዘረጋዋል፡፡ ቁርጥራጮችም ያደርገዋል፡፡ ዝናቡንም ከደመናው መካከል ሲወጣ ታያለህ፡፡ በእርሱም ከባሮቹ የሚሻውን በለየ ጊዜ ወዲያውኑ እነሱ ይደሰታሉ፡፡

49. በእነርሱም ላይ ከመወረዱ በፊት ከእርሱ በፊት በእርግጥ ተስፋ ቆራጮች ነበሩ፡፡

50. ምድርንም ከሞተች በኋላ እንዴት ሕያው እንደሚያደርጋት ወደ አላህ ችሮታ ፈለጎች ተመልከት፡፡ ይህ (አድራጊ) ሙታንንም በእርግጥ ሕያው አድራጊ ነው፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

51. ነፋስንም (በአዝመራዎች ላይ) ብንልክና ገርጥቶ ቢያዩት ከእርሱ በኋላ በእርግጥ (ችሮታውን) የሚክዱ ይሆናሉ፡፡

52. አንተም ሙታንን አታሰማም፡፡ ደንቆሮዎችንም ዟሪዎች ሆነው በሸሹ ጊዜ ጥሪን አታሰማም፡፡

53. አንተ ዕውሮችንም ከጥመታቸው የምታቀና አይደለህም፡፡ በአንቀጾቻችን የሚያምኑትን ሰዎች እንጂ ሌላን አታሰማም፡፡ እነርሱም ታዛዦች ናቸው፡፡

54. አላህ ያ ከደካማ (ፍትወት ጠብታ) የፈጠራችሁ ነው፡፡ ከዚያም ከደካማነት በኋላ ኀይልን አደረገ፡፡ ከዚያም ከብርቱነት በኋላ ደካማነትንና ሽበትን አደረገ፡፡ የሚሻውን ይፈጥራል፡፡ እርሱም ዐዋቂው ቻዩ ነው፡፡

مَن كَفَرَ فَعَلَيۡهِ كُفۡرُهُۥۖ وَمَنۡ عَمِلَ صَٰلِحٗا فَلِأَنفُسِهِمۡ يَمۡهَدُونَ ﴿٤٤﴾

لِيَجۡزِيَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ مِن فَضۡلِهِۦٓۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلۡكَٰفِرِينَ ﴿٤٥﴾

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦٓ أَن يُرۡسِلَ ٱلرِّيَاحَ مُبَشِّرَٰتٖ وَلِيُذِيقَكُم مِّن رَّحۡمَتِهِۦ وَلِتَجۡرِيَ ٱلۡفُلۡكُ بِأَمۡرِهِۦ وَلِتَبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِهِۦ وَلَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ﴿٤٦﴾

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا مِن قَبۡلِكَ رُسُلًا إِلَىٰ قَوۡمِهِمۡ فَجَآءُوهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَٱنتَقَمۡنَا مِنَ ٱلَّذِينَ أَجۡرَمُواْۖ وَكَانَ حَقًّا عَلَيۡنَا نَصۡرُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ﴿٤٧﴾

ٱللَّهُ ٱلَّذِي يُرۡسِلُ ٱلرِّيَٰحَ فَتُثِيرُ سَحَابٗا فَيَبۡسُطُهُۥ فِي ٱلسَّمَآءِ كَيۡفَ يَشَآءُ وَيَجۡعَلُهُۥ كِسَفٗا فَتَرَى ٱلۡوَدۡقَ يَخۡرُجُ مِنۡ خِلَٰلِهِۦۖ فَإِذَآ أَصَابَ بِهِۦ مَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦٓ إِذَا هُمۡ يَسۡتَبۡشِرُونَ ﴿٤٨﴾

وَإِن كَانُواْ مِن قَبۡلِ أَن يُنَزَّلَ عَلَيۡهِم مِّن قَبۡلِهِۦ لَمُبۡلِسِينَ ﴿٤٩﴾

فَٱنظُرۡ إِلَىٰٓ ءَاثَٰرِ رَحۡمَتِ ٱللَّهِ كَيۡفَ يُحۡيِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَآۚ إِنَّ ذَٰلِكَ لَمُحۡيِ ٱلۡمَوۡتَىٰۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ﴿٥٠﴾

وَلَئِنۡ أَرۡسَلۡنَا رِيحٗا فَرَأَوۡهُ مُصۡفَرّٗا لَّظَلُّواْ مِنۢ بَعۡدِهِۦ يَكۡفُرُونَ ﴿٥١﴾

فَإِنَّكَ لَا تُسۡمِعُ ٱلۡمَوۡتَىٰ وَلَا تُسۡمِعُ ٱلصُّمَّ ٱلدُّعَآءَ إِذَا وَلَّوۡاْ مُدۡبِرِينَ ﴿٥٢﴾

وَمَآ أَنتَ بِهَٰدِ ٱلۡعُمۡيِ عَن ضَلَٰلَتِهِمۡۖ إِن تُسۡمِعُ إِلَّا مَن يُؤۡمِنُ بِـَٔايَٰتِنَا فَهُم مُّسۡلِمُونَ ﴿٥٣﴾

۞ٱللَّهُ ٱلَّذِي خَلَقَكُم مِّن ضَعۡفٖ ثُمَّ جَعَلَ مِنۢ بَعۡدِ ضَعۡفٖ قُوَّةٗ ثُمَّ جَعَلَ مِنۢ بَعۡدِ قُوَّةٖ ضَعۡفٗا وَشَيۡبَةٗۚ يَخۡلُقُ مَا يَشَآءُۚ وَهُوَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡقَدِيرُ ﴿٥٤﴾

55. ሰዓቲቱ በምትሆንበት ቀን ከሓዲዎች «ከአንዲት ሰዓት በስተቀር (በመቃብር) አልቆየንም» ብለው ይምላሉ፡፡ እንደዚሁ (ከእውነት) ይመለሱ ነበሩ፡፡

وَيَوْمَ تَقُومُ ٱلسَّاعَةُ يُقْسِمُ ٱلْمُجْرِمُونَ مَا لَبِثُوا۟ غَيْرَ سَاعَةٍ ۚ كَذَٰلِكَ كَانُوا۟ يُؤْفَكُونَ ﴿٥٥﴾

56. እነዚያንም ዕውቀትንና እምነትን የተሰጡት «በአላህ መጽሐፍ (ፍርድ) እስከ ትንሣኤ ቀን በእርግጥ ቆያችሁ፡፡ ይህም (የካዳችሁት) የትንሣኤ ቀን ነው፡፡ ግን እናንተ የማታውቁ ነበራችሁ» ይሏቸዋል፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ ٱلْعِلْمَ وَٱلْإِيمَـٰنَ لَقَدْ لَبِثْتُمْ فِى كِتَـٰبِ ٱللَّهِ إِلَىٰ يَوْمِ ٱلْبَعْثِ ۖ فَهَـٰذَا يَوْمُ ٱلْبَعْثِ وَلَـٰكِنَّكُمْ كُنتُمْ لَا تَعْلَمُونَ ﴿٥٦﴾

57. በዚያም ቀን እነዚያን የበደሉትን ማመካኘታቸው አይጠቅማቸውም፡፡ እነርሱም በወቀሳ አይታለፉም፡፡

فَيَوْمَئِذٍ لَّا يَنفَعُ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوا۟ مَعْذِرَتُهُمْ وَلَا هُمْ يُسْتَعْتَبُونَ ﴿٥٧﴾

58. በዚያም ቁርአን ውስጥ ከምሳሌ ሁሉ ለሰዎች በእርግጥ ገለጽን፡፡ በተዓምርም ብትመጣባቸው እነዚያ የካዱት ሰዎች «እናንተ አበላሺዎች እንጂ ሌላ አይደላችሁም» ይላሉ፡፡

وَلَقَدْ ضَرَبْنَا لِلنَّاسِ فِى هَـٰذَا ٱلْقُرْءَانِ مِن كُلِّ مَثَلٍ ۚ وَلَئِن جِئْتَهُم بِـَٔايَةٍ لَّيَقُولَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ إِنْ أَنتُمْ إِلَّا مُبْطِلُونَ ﴿٥٨﴾

59. እንደዚሁ አላህ በእነዚያ በማያውቁት ሰዎች ልቦች ላይ ያትማል፡፡

كَذَٰلِكَ يَطْبَعُ ٱللَّهُ عَلَىٰ قُلُوبِ ٱلَّذِينَ لَا يَعْلَمُونَ ﴿٥٩﴾

60. ስለዚህ ታገስ፡፡ የአላህ ቀጠሮ እውነት ነውና፡፡ እነዚያም በትንሣኤ የሚያረጋግጡት አያቅልሉህ፡፡

فَٱصْبِرْ إِنَّ وَعْدَ ٱللَّهِ حَقٌّ ۖ وَلَا يَسْتَخِفَّنَّكَ ٱلَّذِينَ لَا يُوقِنُونَ ﴿٦٠﴾

## ሱረቱ አል ሉቅማን

## سورة لقمان

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَـٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አ.ለ.መ. (አሊፍ ላም ሚም)፡፡

الٓمٓ ﴿١﴾

2. ይህች ጥበብ ከተመላው መጽሐፍ አንቀጾች ናት፡፡

تِلْكَ ءَايَـٰتُ ٱلْكِتَـٰبِ ٱلْحَكِيمِ ﴿٢﴾

3. ለበጎ አድራጊዎች መሪና እዝነት ስትኾን፡፡

هُدًى وَرَحْمَةً لِّلْمُحْسِنِينَ ﴿٣﴾

4. ለእነዚያ ሶላትን አስተካክለው ለሚያደርሱት፣ ዘካንም ለሚሰጡት፣ እነርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም እነርሱ የሚያረጋግጡ ለሆኑት፡፡

ٱلَّذِينَ يُقِيمُونَ ٱلصَّلَوٰةَ وَيُؤْتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَهُم بِٱلْـَٔاخِرَةِ هُمْ يُوقِنُونَ ﴿٤﴾

5. እነዚያ ከጌታቸው በሆነ ቅን መንገድ ላይ ናቸው፡፡ እነዚያም እነርሱ ምኞታቸውን ያገኙ ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ عَلَىٰ هُدٗى مِّن رَّبِّهِمۡۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ٥

6. ከሰዎችም ያለ ዕውቀት ሆኖ ከአላህ መንገድ ሊያሳስትና ማላገጫ አድርጎ ሊይዛት አታላይ ወሬን የሚገዛ አልለ፡፡ እነዚያ ለእነርሱ አዋራጅ ቅጣት አላቸው፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يَشۡتَرِي لَهۡوَ ٱلۡحَدِيثِ لِيُضِلَّ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ بِغَيۡرِ عِلۡمٖ وَيَتَّخِذَهَا هُزُوًاۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٞ مُّهِينٞ ٦

7. አንቀጾቻችንም በእርሱ ላይ በሚነበቡ ጊዜ እንዳልሰማትና በጆሮቹ ድንቁርና እንዳለበት የኩራ ሆኖ ይዞራል፡፡ በአሳማሚ ቅጣትም አብስረው፡፡

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِ ءَايَٰتُنَا وَلَّىٰ مُسۡتَكۡبِرٗا كَأَن لَّمۡ يَسۡمَعۡهَا كَأَنَّ فِيٓ أُذُنَيۡهِ وَقۡرٗاۖ فَبَشِّرۡهُ بِعَذَابٍ أَلِيمٍ ٧

8. እነዚያ ያመኑና መልካሞችንም የሠሩ ለእነርሱ የጸጋ ገነቶች አሏቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُمۡ جَنَّٰتُ ٱلنَّعِيمِ ٨

9. በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ሲሆኑ፤ አላህም እውነተኛን ተስፋ ቃል ገባላቸው፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَاۖ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٗاۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٩

10. ሰማያትን ያለምታዩዋት አዕማድ (ምሰሶዎች) ፈጠረ፡፡ በምድርም ውስጥ በእናንተ እንዳታረገርግ ተራራዎችን ጣለ፡፡ በእርሷም ላይ ከተንቀሳቃሽ ሁሉ በተነ፡፡ ከሰማይም ውሃን አወረድን፡፡ በእርሷም ውስጥ ከመልካም ዓይነት ሁሉ አበቀልን፡፡

خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ بِغَيۡرِ عَمَدٖ تَرَوۡنَهَاۖ وَأَلۡقَىٰ فِي ٱلۡأَرۡضِ رَوَٰسِيَ أَن تَمِيدَ بِكُمۡ وَبَثَّ فِيهَا مِن كُلِّ دَآبَّةٖۚ وَأَنزَلۡنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَأَنۢبَتۡنَا فِيهَا مِن كُلِّ زَوۡجٖ كَرِيمٍ ١٠

11. ይህ የአላህ ፍጡር ነው፡፡ እነዚያ ከእርሱ ሌላ ያሉት ምንን እንደፈጠሩ እስኪ አሳዩኝ፡፡ በእውነቱ በዳዮቹ በግልጽ ጥመት ውስጥ ናቸው፡፡

هَٰذَا خَلۡقُ ٱللَّهِ فَأَرُونِي مَاذَا خَلَقَ ٱلَّذِينَ مِن دُونِهِۦۚ بَلِ ٱلظَّٰلِمُونَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ١١

12. ለሉቅማንም ጥበብን በእርግጥ ሰጠነው፡፡ (አልነውም)፡- «አላህን አመስግን፡፡» ያመሰገነም ሰው የሚያመሰግነው ለራሱ ብቻ ነው፡፡ የካደም ሰው (በራሱ ላይ ነው)፡፡ አላህ ተብቃቂ ምስጉን ነውና፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا لُقۡمَٰنَ ٱلۡحِكۡمَةَ أَنِ ٱشۡكُرۡ لِلَّهِۚ وَمَن يَشۡكُرۡ فَإِنَّمَا يَشۡكُرُ لِنَفۡسِهِۦۖ وَمَن كَفَرَ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَنِيٌّ حَمِيدٞ ١٢

13. ሉቅማንም ለልጁ እርሱ የሚገሥጸው ሲኾን «ልጄ ሆይ! በአላህ (ጣዖትን) አታጋራ፡፡ ማጋራት ታላቅ በደል ነውና» ያለውን (አስታውስ)፡፡

وَإِذۡ قَالَ لُقۡمَٰنُ لِٱبۡنِهِۦ وَهُوَ يَعِظُهُۥ يَٰبُنَيَّ لَا تُشۡرِكۡ بِٱللَّهِۖ إِنَّ ٱلشِّرۡكَ لَظُلۡمٌ عَظِيمٞ ١٣

14. ሰውንም በወላጆቹ (በጎ እንዲያደርግ) በጥብቅ አዘዝነው፡፡ እናቱ ከድካም በላይ በሆነ ድካም አረገዘችው፡፡ ጡት መጣያውም በሁለት ዓመት ውስጥ ነው፡፡ ለእኔም ለወላጆችህም አመስግን በማለት (አዘዝነው)፡፡ መመለሻው ወደኔ ነው፡፡

وَوَصَّيۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ بِوَٰلِدَيۡهِ حَمَلَتۡهُ أُمُّهُۥ وَهۡنًا عَلَىٰ وَهۡنٖ وَفِصَٰلُهُۥ فِي عَامَيۡنِ أَنِ ٱشۡكُرۡ لِي وَلِوَٰلِدَيۡكَ إِلَيَّ ٱلۡمَصِيرُ ١٤

15. ለአንተ በእርሱ ዕውቀት የሌለህን ነገር በእኔ እንድታጋራ ቢታገሉህም አትታዘዛቸው፡፡ በቅርቢቱም ዓለም፤ በመልካም ሥራ ተወዳጃቸው፡፡ ወደእኔም የተመለሰን ሰው መንገድ ተከተል፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደእኔ ነው፡፡ ትሠሩት የነበራችሁትንም ሁሉ እነግራችኋለሁ፤ (አልነው)፡፡

وَإِن جَٰهَدَاكَ عَلَىٰٓ أَن تُشۡرِكَ بِي مَا لَيۡسَ لَكَ بِهِۦ عِلۡمٞ فَلَا تُطِعۡهُمَاۖ وَصَاحِبۡهُمَا فِي ٱلدُّنۡيَا مَعۡرُوفٗاۖ وَٱتَّبِعۡ سَبِيلَ مَنۡ أَنَابَ إِلَيَّۚ ثُمَّ إِلَيَّ مَرۡجِعُكُمۡ فَأُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ١٥

16. (ሉቅማንም አለ) «ልጄ ሆይ! እርሷ የሰናፍጭ ቅንጣት ክብደት ያህል ብትሆንና በቋጥኝ ውስጥ ወይም በሰማያት ውስጥ ወይም በምድር ውስጥ ብትሆን አላህ ያመጣታል፡፡ አላህ ሩኅሩኅ ውስጥ ዐዋቂ ነውና፡፡

يَٰبُنَيَّ إِنَّهَآ إِن تَكُ مِثۡقَالَ حَبَّةٖ مِّنۡ خَرۡدَلٖ فَتَكُن فِي صَخۡرَةٍ أَوۡ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ أَوۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ يَأۡتِ بِهَا ٱللَّهُۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَطِيفٌ خَبِيرٞ ١٦

17. «ልጄ ሆይ! ሶላትን አስተካክለህ ስገድ፡፡ በበጎ ነገርም እዘዝ፡፡ ከሚጠላም ሁሉ ከልክል፡፡ በሚያገኝህም መከራ ላይ ታገስ፡፡ ይህ በምር ከሚያዙ ነገሮች ነው፡፡

يَٰبُنَيَّ أَقِمِ ٱلصَّلَوٰةَ وَأۡمُرۡ بِٱلۡمَعۡرُوفِ وَٱنۡهَ عَنِ ٱلۡمُنكَرِ وَٱصۡبِرۡ عَلَىٰ مَآ أَصَابَكَۖ إِنَّ ذَٰلِكَ مِنۡ عَزۡمِ ٱلۡأُمُورِ ١٧

18. «ጉንጭህንም (በኩራት) ከሰዎች አታዙር፡፡ በምድርም ላይ ተንበጥርረህ አትሂድ፡፡ አላህ ተንበጥራሪን ጉረኛን ሁሉ አይወድምና፡፡

وَلَا تُصَعِّرۡ خَدَّكَ لِلنَّاسِ وَلَا تَمۡشِ فِي ٱلۡأَرۡضِ مَرَحًاۖ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يُحِبُّ كُلَّ مُخۡتَالٖ فَخُورٖ ١٨

19. «በአካኼድህም መካከለኛ ኹን፡፡ ከድምጽህም ዝቅ አድርግ፡፡ ከድምጾች ሁሉ አስከፊው የአህዮች ድምጽ ነውና፡፡»

وَٱقۡصِدۡ فِي مَشۡيِكَ وَٱغۡضُضۡ مِن صَوۡتِكَۚ إِنَّ أَنكَرَ ٱلۡأَصۡوَٰتِ لَصَوۡتُ ٱلۡحَمِيرِ ١٩

20. አላህ በሰማያት ያለውንና በምድርም ያለውን ሁሉ ለእናንተ ያገራላችሁ ጸጋዎቹንም ግልጽም ድብቅም ሲኾኑ የሞላላችሁ መኾኑን አታዩምን? ከሰዎችም ያለ ዕውቀትና ያለ መሪ፣ ያለግልጽ መጽሐፍም በአላህ የሚከራከር አልለ፡፡

أَلَمۡ تَرَوۡاْ أَنَّ ٱللَّهَ سَخَّرَ لَكُم مَّا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَأَسۡبَغَ عَلَيۡكُمۡ نِعَمَهُۥ ظَٰهِرَةٗ وَبَاطِنَةٗۗ وَمِنَ ٱلنَّاسِ مَن يُجَٰدِلُ فِي ٱللَّهِ بِغَيۡرِ عِلۡمٖ وَلَا هُدٗى وَلَا كِتَٰبٖ مُّنِيرٖ ٢٠

21. ለእነርሱም አላህ ያወረደውን ተከተሉ በተባሉ ጊዜ አይደለም በእርሱ ላይ አባቶቻችንን ያገኘንበትን እንከተላለን ይላሉ፡፡ ሰይጣን ወደ እሳት ቅጣት የሚጠራቸው ቢሆንም (ይከተሉዋቸዋልን?)

وَإِذَا قِيلَ لَهُمُ ٱتَّبِعُواْ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ قَالُواْ بَلۡ نَتَّبِعُ مَا وَجَدۡنَا عَلَيۡهِ ءَابَآءَنَآۚ أَوَلَوۡ كَانَ ٱلشَّيۡطَٰنُ يَدۡعُوهُمۡ إِلَىٰ عَذَابِ ٱلسَّعِيرِ ٢١

22. እርሱ መልካም ሠሪ ሆኖ ፊቱን ወደ አላህ የሚሰጥም ሰው ጠንካራን ገመድ በእርግጥ ጨበጠ፡፡ የነገሩም ሁሉ ፍጻሜ ወደ አላህ ነው፡፡

۞وَمَن يُسۡلِمۡ وَجۡهَهُۥٓ إِلَى ٱللَّهِ وَهُوَ مُحۡسِنٞ فَقَدِ ٱسۡتَمۡسَكَ بِٱلۡعُرۡوَةِ ٱلۡوُثۡقَىٰۗ وَإِلَى ٱللَّهِ عَٰقِبَةُ ٱلۡأُمُورِ ٢٢

23. የካደም ሰው ክህደቱ አያሳዝንህ፡፡ መመለሻቸው ወደኛ ነው፤ የሠሩትንም ሁሉ እንነግራቸዋለን፡፡ አላህ በልቦች ውስጥ ያለን ሁሉ ያውቃልና፡፡

وَمَن كَفَرَ فَلَا يَحۡزُنكَ كُفۡرُهُۥٓۚ إِلَيۡنَا مَرۡجِعُهُمۡ فَنُنَبِّئُهُم بِمَا عَمِلُوٓاْۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٢٣

24. ጥቂትን እናጣቅማቸዋለን፡፡ ከዚያም ወደ ብርቱ ቅጣት እናስገድዳቸዋለን፡፡

نُمَتِّعُهُمۡ قَلِيلٗا ثُمَّ نَضۡطَرُّهُمۡ إِلَىٰ عَذَابٍ غَلِيظٖ ٢٤

25. ሰማያትንና ምድርንም የፈጠረ ማን እንደሆነ ብትጠይቃቸው በእርግጥ አላህ ነው ይላሉ፡፡ ምስጋና ለአላህ ይገባው በላቸው፡፡ ይልቁንም አብዛኞዎቹ አያውቁም፡፡

وَلَئِن سَأَلۡتَهُم مَّنۡ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُۚ قُلِ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٢٥

26. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ አላህ እርሱ ተብቃቂ ምስጉን ነው፡፡

لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡغَنِيُّ ٱلۡحَمِيدُ ٢٦

27. ከዛፍም በምድር ያለው ሁሉ ብእሮች ቢሆኑ ኖሮ ባሕሩም ከእርሱ (ማለቅ) በኋላ ሰባት ባህሮች የሚጨመሩለት ሆኖ (ቀለም ቢሆንና ቢጻፍባቸው) የአላህ ቃላት ባላለቀች ነበር፡፡ አላህ አሸናፊ ጥበበኛ ነውና፡፡

وَلَوۡ أَنَّمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ مِن شَجَرَةٍ أَقۡلَٰمٞ وَٱلۡبَحۡرُ يَمُدُّهُۥ مِنۢ بَعۡدِهِۦ سَبۡعَةُ أَبۡحُرٖ مَّا نَفِدَتۡ كَلِمَٰتُ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ حَكِيمٞ ﴿٢٧﴾

28. እናንተን መፍጠርና እናንተን መቀስቀስ እንደ አንዷት ነፍስ እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ አላህ ሰሚ ተመልካች ነውና፡፡

مَّا خَلۡقُكُمۡ وَلَا بَعۡثُكُمۡ إِلَّا كَنَفۡسٖ وَٰحِدَةٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعُۢ بَصِيرٌ ﴿٢٨﴾

29. አላህ ሌሊትን በቀን ውስጥ የሚያስገባ፣ ቀንንም በሌሊት ውስጥ የሚያስገባ፣ ፀሐይንና ጨረቃንም የገራ መሆኑን አታይምን? ሁሉም እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ ይሮጣሉ፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ يُولِجُ ٱلَّيۡلَ فِي ٱلنَّهَارِ وَيُولِجُ ٱلنَّهَارَ فِي ٱلَّيۡلِ وَسَخَّرَ ٱلشَّمۡسَ وَٱلۡقَمَرَۖ كُلّٞ يَجۡرِيٓ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗى وَأَنَّ ٱللَّهَ بِمَا تَعۡمَلُونَ خَبِيرٞ ﴿٢٩﴾

30. ይህ አላህ እርሱ እውነት ከእርሱም ሌላ የሚግገዙት (ጣዖት) ውሸት በመሆኑና አላህም እርሱ የበላይ ታላቅ በመሆኑ ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡحَقُّ وَأَنَّ مَا يَدۡعُونَ مِن دُونِهِ ٱلۡبَٰطِلُ وَأَنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡعَلِيُّ ٱلۡكَبِيرُ ﴿٣٠﴾

31. ከአስደናቂ ምልክቶቹ ሊያሳያችሁ መርከቦች በአላህ ችሮታ በባህር ውስጥ የሚንሻለሉ መሆናቸውን አታይምን? በዚህ ውስጥ በጣም ታጋሽ አመስጋኝ ለሆኑ ሁሉ ተዓምራቶች አሉበት፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱلۡفُلۡكَ تَجۡرِي فِي ٱلۡبَحۡرِ بِنِعۡمَتِ ٱللَّهِ لِيُرِيَكُم مِّنۡ ءَايَٰتِهِۦٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّكُلِّ صَبَّارٖ شَكُورٖ ﴿٣١﴾

32. እንደ ጥላዎችም የሆነ ማዕበል በሸፈናቸው ጊዜ አላህን ሃይማኖትን ለእርሱ ብቻ ያጠሩ ሆነው ይጠሩታል፡፡ ወደ የብስም ባዳናቸው ጊዜ ከእነሱ ትክክለኛም አልለ፡፡ (ከእነርሱም የሚክድ አለ)፡፡ በአንቀጾቻችንም አታላይ ከዳተኛ ሁሉ እንጂ ሌላው አይክድም፡፡

وَإِذَا غَشِيَهُم مَّوۡجٞ كَٱلظُّلَلِ دَعَوُاْ ٱللَّهَ مُخۡلِصِينَ لَهُ ٱلدِّينَ فَلَمَّا نَجَّىٰهُمۡ إِلَى ٱلۡبَرِّ فَمِنۡهُم مُّقۡتَصِدٞۚ وَمَا يَجۡحَدُ بِـَٔايَٰتِنَآ إِلَّا كُلُّ خَتَّارٖ كَفُورٖ ﴿٣٢﴾

33. እናንተ ሰዎች ሆይ! ጌታችሁን ፍሩ፡፡ ወላጅም ከልጁ (በምንም) የማይጠቅምበትን፤ ተወላጅም እርሱ ወላጅን በምንም ጠቃሚ የማይሆንበትን ቀን ፍሩ፡፡ የአላህ ቀጠሮ እውነት ነውና፡፡ ቅርቢቱም ሕይወት አትሸንግላችሁ፡፡ በአላህም (መታገስ) አታላዩ (ሰይጣን) አያታልላችሁ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ٱتَّقُواْ رَبَّكُمۡ وَٱخۡشَوۡاْ يَوۡمٗا لَّا يَجۡزِي وَالِدٌ عَن وَلَدِهِۦ وَلَا مَوۡلُودٌ هُوَ جَازٍ عَن وَالِدِهِۦ شَيۡـًٔاۚ إِنَّ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٞۖ فَلَا تَغُرَّنَّكُمُ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا وَلَا يَغُرَّنَّكُم بِٱللَّهِ ٱلۡغَرُورُ ﴿٣٣﴾

34. አላህ የሰዓቲቱ ዕውቀት እርሱ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ ዝናብንም ያወርዳል፡፡ በማሕፀኖችም ውስጥ ያለን ሁሉ ያውቃል፡፡ ማንኛይቱ ነፍስም ነገ የምትሠራውን አታውቅም፡፡ ማንኛይቱ ነፍስም በየትኛው ምድር እንደምትሞት አታውቅም፡፡ አላህ ዐዋቂ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ عِندَهُۥ عِلۡمُ ٱلسَّاعَةِ وَيُنَزِّلُ ٱلۡغَيۡثَ وَيَعۡلَمُ مَا فِي ٱلۡأَرۡحَامِۖ وَمَا تَدۡرِي نَفۡسٞ مَّاذَا تَكۡسِبُ غَدٗاۖ وَمَا تَدۡرِي نَفۡسُۢ بِأَيِّ أَرۡضٖ تَمُوتُۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌ خَبِيرُۢ ﴿٣٤﴾

# ሱረቱ አል ሰጅዳህ

# سورة السجدة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

1. አ.ለ.መ (አሊፍ ላም ሚም)፡፡

2. የመጽሐፉ መወረድ ጥርጥር የለበትም፡፡ ከዓለማት ጌታ ነው፡፡

3. ይልቁንም «ቀጠፈው» ይላሉን? አይደለም፡፡ እርሱ ከጌታህ ዘንድ የሆነ እውነት ነው፡፡ በእርሱ ከአንተ በፊት ከአስፈራሪ (ነቢይ) ያልመጣባቸውን ሕዝቦች ልታስፈራራበት (ያወረደልህ ነው)፡፡ እነርሱ ሊምመሩ ይከጀላልና፡፡

4. አላህ ያ ሰማያትንና ምድርን በመካከላቸውም ያለውን ሁሉ በስድስት ቀኖች ውስጥ የፈጠረ ከዚያም በዐርሹ ላይ (ስልጣኑ) የተደላደለ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ ለእናንተ ረዳትም አማላጅም ምንም የላችሁም፤ አትገሰጹምን?

5. ነገሩን ሁሉ ከሰማይ ወደ ምድር ያዘጋጃል፡፡ ከዚያም ከምትቆጥሩት (ዘመን) ልኩ ሺህ ዓመት በሆነ ቀን ውስጥ ወደርሱ ይወጣል (ይመለሳል)፡፡

6. ይህ (ይህንን የሠራው) ሩቁንም ቅርቡንም ሁሉ ዐዋቂው አሸናፊው፣ አዛኙ (ጌታ) ነው፡፡

7. ያ የፈጠረውን ነገር ሁሉ ያሳመረው የሰውንም ፍጥረት ከጭቃ የጀመረው ነው፡፡

8. ከዚያም ዘሮቹን ከተንጣለለ፣ ከደካማ ውሃ ያደረገ ነው፡፡

9. ከዚያም (ቅርጹን) አስተካከለው፡፡ በእርሱ ውስጥም ከመንፈሱ ነፋበት፤ (ነፍስ ዘራበት)፡፡ ለእናንተም ጆሮዎችን፣ ዓይኖችንና ልቦችንም አደረገላችሁ፡፡ በጣም ጥቂትን ብቻ ታመሰግናላችሁ፡፡

10. «በምድርም ውስጥ (በስብሰን) በጠፋን ጊዜ እኛ በአዲስ መፈጠር ውስጥ እንሆናለን?» አሉ፡፡ በእውነቱ እነርሱ በጌታቸው መገናኘት ከሓዲዎች ናቸው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

الٓمٓ ﴿١﴾

تَنزِيلُ ٱلۡكِتَٰبِ لَا رَيۡبَ فِيهِ مِن رَّبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٢﴾

أَمۡ يَقُولُونَ ٱفۡتَرَىٰهُۚ بَلۡ هُوَ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّكَ لِتُنذِرَ قَوۡمٗا مَّآ أَتَىٰهُم مِّن نَّذِيرٖ مِّن قَبۡلِكَ لَعَلَّهُمۡ يَهۡتَدُونَ ﴿٣﴾

ٱللَّهُ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَا فِي سِتَّةِ أَيَّامٖ ثُمَّ ٱسۡتَوَىٰ عَلَى ٱلۡعَرۡشِۖ مَا لَكُم مِّن دُونِهِۦ مِن وَلِيّٖ وَلَا شَفِيعٍۚ أَفَلَا تَتَذَكَّرُونَ ﴿٤﴾

يُدَبِّرُ ٱلۡأَمۡرَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ إِلَى ٱلۡأَرۡضِ ثُمَّ يَعۡرُجُ إِلَيۡهِ فِي يَوۡمٖ كَانَ مِقۡدَارُهُۥٓ أَلۡفَ سَنَةٖ مِّمَّا تَعُدُّونَ ﴿٥﴾

ذَٰلِكَ عَٰلِمُ ٱلۡغَيۡبِ وَٱلشَّهَٰدَةِ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٦﴾

ٱلَّذِيٓ أَحۡسَنَ كُلَّ شَيۡءٍ خَلَقَهُۥۖ وَبَدَأَ خَلۡقَ ٱلۡإِنسَٰنِ مِن طِينٖ ﴿٧﴾

ثُمَّ جَعَلَ نَسۡلَهُۥ مِن سُلَٰلَةٖ مِّن مَّآءٖ مَّهِينٖ ﴿٨﴾

ثُمَّ سَوَّىٰهُ وَنَفَخَ فِيهِ مِن رُّوحِهِۦۖ وَجَعَلَ لَكُمُ ٱلسَّمۡعَ وَٱلۡأَبۡصَٰرَ وَٱلۡأَفۡـِٔدَةَۚ قَلِيلٗا مَّا تَشۡكُرُونَ ﴿٩﴾

وَقَالُوٓاْ أَءِذَا ضَلَلۡنَا فِي ٱلۡأَرۡضِ أَءِنَّا لَفِي خَلۡقٖ جَدِيدِۭۚ بَلۡ هُم بِلِقَآءِ رَبِّهِمۡ كَٰفِرُونَ ﴿١٠﴾

11. «በእናንተ የተወከለው መልአከ ሞት ይገድላችኋል፡፡ ከዚያም ወደ ጌታችሁ ትመለሳላችሁ» በላቸው፡፡

۞قُلۡ يَتَوَفَّىٰكُم مَّلَكُ ٱلۡمَوۡتِ ٱلَّذِي وُكِّلَ بِكُمۡ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّكُمۡ تُرۡجَعُونَ ١١

12. አመጸኞችም በጌታቸው ዘንድ ራሶቻቸውን ያቀረቀሩ ሆነው «ጌታችን ሆይ! አየን፣ ሰማንም፡፡ መልካምን እንሠራለንና (ወደ ምድረ ዓለም) መልሰን፡፡ እኛ አረጋጋጮች ነን፡፡» (የሚሉ ሲሆኑ) ብታይ ኖሮ (አስደንጋጭን ነገር ታይ ነበር)፡፡

وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذِ ٱلۡمُجۡرِمُونَ نَاكِسُواْ رُءُوسِهِمۡ عِندَ رَبِّهِمۡ رَبَّنَآ أَبۡصَرۡنَا وَسَمِعۡنَا فَٱرۡجِعۡنَا نَعۡمَلۡ صَٰلِحًا إِنَّا مُوقِنُونَ ١٢

13. በሻንም ኖሮ ነፍስን ሁሉ ቅንነቷን (እምነቷን) በሰጠናት ነበር፡፡ ግን ገሀነምን ከአጋንንትና ከሰዎች የተሰበሰቡ ሆነው በእርግጥ እሞላለሁ ማለት ቃሉ ከእኔ ተረጋግጧል፡፡

وَلَوۡ شِئۡنَا لَأٓتَيۡنَا كُلَّ نَفۡسٍ هُدَىٰهَا وَلَٰكِنۡ حَقَّ ٱلۡقَوۡلُ مِنِّي لَأَمۡلَأَنَّ جَهَنَّمَ مِنَ ٱلۡجِنَّةِ وَٱلنَّاسِ أَجۡمَعِينَ ١٣

14. ይህንንም ቀናችሁን መገናኘትን በመርሳታችሁ ምክንያት (ቅጣትን) ቅመሱ! እኛ ተውናችሁ፡፡ ትሠሩት በነበራችሁትም ጥፋት ዘውታሪን ቅጣት ቅመሱ (ይባላሉ)፡፡

فَذُوقُواْ بِمَا نَسِيتُمۡ لِقَآءَ يَوۡمِكُمۡ هَٰذَآ إِنَّا نَسِينَٰكُمۡۖ وَذُوقُواْ عَذَابَ ٱلۡخُلۡدِ بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ١٤

15. በአንቀጾቻችን የሚያምኑት እነዚያ በእርሷ በተገሰጹ ጊዜ ሰጋጆች ሆነው የሚወድቁትና እነርሱም የማይኮሩ ሆነው በጌታቸው ምስጋና (ተጎናጽፈው) የሚያወድሱት ብቻ ናቸው፡፡

إِنَّمَا يُؤۡمِنُ بِـَٔايَٰتِنَا ٱلَّذِينَ إِذَا ذُكِّرُواْ بِهَا خَرُّواْ سُجَّدٗا وَسَبَّحُواْ بِحَمۡدِ رَبِّهِمۡ وَهُمۡ لَا يَسۡتَكۡبِرُونَ۩ ١٥

16. ጌታቸውን ለመፍራትና ለመከጀል የሚጠሩት ሆነው ጎኖቻቸው ከመጋደሚያ ስፍራዎች ይራራቃሉ፡፡ ከሰጠናቸውም (ጸጋ) ይለግሳሉ፡፡

تَتَجَافَىٰ جُنُوبُهُمۡ عَنِ ٱلۡمَضَاجِعِ يَدۡعُونَ رَبَّهُمۡ خَوۡفٗا وَطَمَعٗا وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ١٦

17. ይሠሩትም በነበሩት ለመመንዳት ከዓይኖች መርጊያ ለእነርሱ የተደበቀላቸውን (ጸጋ) ማንኛይቱም ነፍስ አታውቅም፡፡

فَلَا تَعۡلَمُ نَفۡسٞ مَّآ أُخۡفِيَ لَهُم مِّن قُرَّةِ أَعۡيُنٖ جَزَآءَۢ بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٧

18. አማኝ የሆነ ሰው አመጸኛ እንደ ሆነ ሰው ነውን? አይስተካከሉም፡፡

أَفَمَن كَانَ مُؤۡمِنٗا كَمَن كَانَ فَاسِقٗاۚ لَّا يَسۡتَوُۥنَ ١٨

19. እነዚያ ያመኑና መልካሞችን የሰሩማ ለእነርሱ ይሠሩት በነበሩት ምክንያት መስተንግዶ ሲሆኑ መኖሪያ ገነቶች አሏቸው፡፡

أَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فَلَهُمۡ جَنَّٰتُ ٱلۡمَأۡوَىٰ نُزُلَۢا بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ١٩

20. እነዚያ ያመጹትማ፤ መኖሪያቸው እሳት ናት፡፡ ከእርሷ መውጣትን በፈለጉ ቁጥር በእርሷ ውስጥ ይመለሳሉ፡፡ ለእነርሱም «ያንን በእርሱ ታስተባብሉበት የነበራችሁትን የእሳት ቅጣት ቅመሱ» ይባላሉ፡፡

وَأَمَّا ٱلَّذِينَ فَسَقُواْ فَمَأۡوَىٰهُمُ ٱلنَّارُۖ كُلَّمَآ أَرَادُوٓاْ أَن يَخۡرُجُواْ مِنۡهَآ أُعِيدُواْ فِيهَا وَقِيلَ لَهُمۡ ذُوقُواْ عَذَابَ ٱلنَّارِ ٱلَّذِي كُنتُم بِهِۦ تُكَذِّبُونَ ٢٠

وَلَنُذِيقَنَّهُم مِّنَ ٱلْعَذَابِ ٱلْأَدْنَىٰ دُونَ ٱلْعَذَابِ ٱلْأَكْبَرِ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ ﴿٢١﴾

21. ይመለሱ ዘንድም ከትልቁ ቅጣት በፊት (በዚህ ዓለም) ከትንሹ ቅጣት በእርግጥ እናቀምሳቸዋለን፡፡

وَمَنْ أَظْلَمُ مِمَّن ذُكِّرَ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِۦ ثُمَّ أَعْرَضَ عَنْهَآ ۚ إِنَّا مِنَ ٱلْمُجْرِمِينَ مُنتَقِمُونَ ﴿٢٢﴾

22. በጌታውም አንቀጾች ከተገሰጸና ከዚያም ከተዋት ሰው ይበልጥ በደለኛ ማነው? (የለም)፤ እኛ ከተንኮለኞቹ ተበቃዮች ነን፡፡

وَلَقَدْ ءَاتَيْنَا مُوسَى ٱلْكِتَٰبَ فَلَا تَكُن فِى مِرْيَةٍ مِّن لِّقَآئِهِۦ ۖ وَجَعَلْنَٰهُ هُدًى لِّبَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ ﴿٢٣﴾

23. ሙሳንም መጽሐፍን በእርግጥ ሰጠነው፡፡ እርሱን ከመገናኘትህም በመጠራጠር ውስጥ አትሁን፡፡ ለእስራኤል ልጆችም መሪ አደረግነው፡፡

وَجَعَلْنَا مِنْهُمْ أَئِمَّةً يَهْدُونَ بِأَمْرِنَا لَمَّا صَبَرُوا۟ ۖ وَكَانُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَا يُوقِنُونَ ﴿٢٤﴾

24. በታገሱና በተዓምራቶቻችን የሚያረጋግጡ በሆኑም ጊዜ ከእነርሱ በትዕዛዛችን የሚመሩ መሪዎች አደረግን፡፡

إِنَّ رَبَّكَ هُوَ يَفْصِلُ بَيْنَهُمْ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ فِيمَا كَانُوا۟ فِيهِ يَخْتَلِفُونَ ﴿٢٥﴾

25. ጌታህ እርሱ በዚያ በእርሱ ይለያዩበት በነበሩት ነገር በትንሣኤ ቀን በመካከላቸው (በፍርድ) ይለያል፡፡

أَوَلَمْ يَهْدِ لَهُمْ كَمْ أَهْلَكْنَا مِن قَبْلِهِم مِّنَ ٱلْقُرُونِ يَمْشُونَ فِى مَسَٰكِنِهِمْ ۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَٰتٍ ۖ أَفَلَا يَسْمَعُونَ ﴿٢٦﴾

26. ከክፍለ ዘመናት ሰዎች ብዙዎችን ያጠፋን መሆናችን በመኖሪያዎቻቸው የሚሄዱ ሲሆኑ ለእነርሱ አልተገለፀላቸውምን? በዚህ ውስጥ ምልክቶች አሉት፤ አይሰሙምን?

أَوَلَمْ يَرَوْا۟ أَنَّا نَسُوقُ ٱلْمَآءَ إِلَى ٱلْأَرْضِ ٱلْجُرُزِ فَنُخْرِجُ بِهِۦ زَرْعًا تَأْكُلُ مِنْهُ أَنْعَٰمُهُمْ وَأَنفُسُهُمْ ۖ أَفَلَا يُبْصِرُونَ ﴿٢٧﴾

27. እኛ ውሃን ወደ ደረቅ ምድር የምንነዳ እንስሶቻቸውና ነፍሶቻቸው ከእርሱ የሚበሉለትንም አዝመራ በእርሱ የምናወጣ መኾናችንን አያዩምን? አይመለከቱምን?

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلْفَتْحُ إِن كُنتُمْ صَٰدِقِينَ ﴿٢٨﴾

28. «ከእውነተኞችም እንደሆናችሁ ይህ ፍርድ መቼ ነው?» ይላሉ፡፡

قُلْ يَوْمَ ٱلْفَتْحِ لَا يَنفَعُ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ إِيمَٰنُهُمْ وَلَا هُمْ يُنظَرُونَ ﴿٢٩﴾

29. «በፍርድ ቀን እነዚያን የካዱትን ሰዎች እምነታቸው አይጠቅማቸውም፡፡ እነርሱም ጊዜን አይሰጡም፤» በላቸው፡፡

فَأَعْرِضْ عَنْهُمْ وَٱنتَظِرْ إِنَّهُم مُّنتَظِرُونَ ﴿٣٠﴾

30. እነርሱንም ተዋቸው፡፡ ተጠባበቅም፤ እነርሱ ተጠባባቂዎች ናቸውና፡፡

# ሱረቱ አል አሕዛብ

# سورة الأحزاب

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

1. አንተ ነቢዩ ሆይ! አላህን ፍራ:: ከሓዲዎችንና መናፍቃንንም አትታዘዝ:: አላህ ዐዋቂ ጥበበኛ ነውና::

2. ከጌታህም ወደ አንተ የሚወረደውን ተከተል:: አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውሰጠ አዋቂ ነውና::

3. በአላህም ላይ ተመካ:: መመኪያም በአላህ በቃ::

4. አላህ ለአንድ ሰው በሆዱ ውስጥ ሁለትን ልቦች አላደረገም:: ሚስቶቻችሁንም እነዚያን ከእነርሱ እንደናቶቻችሁ ጀርባዎች ይሁኑብን የምትሏቸውን እናቶቻችሁ አላደረገም:: ልጅ በማድረግ የምታስጠጓቸውንም ልጆቻችሁ አላደረገም:: ይህ በአፎቻችሁ የምትሉት ነው:: አላህም እውነቱን ይናገራል:: እርሱም ትክክለኛውን መንገድ ይመራል::

5. ለአባቶቻቸው (በማስጠጋት) ጥሯቸው:: እርሱ አላህ ዘንድ ትክክለኛ ነው:: አባቶቻቸውንም ባታውቁ በሃይማኖት ወንድሞቻችሁና ዘመዶቻችሁ ናቸው:: በእርሱ በተሳሳታችሁበት ነገርም በእናንተ ላይ ኀጢአት የለባችሁም:: ግን ልቦቻችሁ ዐውቀው በሠሩት (ኀጢአት አለባችሁ):: አላህም መሓሪ አዛኝ ነው::

6. ነቢዩ በምእምናን ከነፍሶቻቸው ይበልጥ ተገቢ ነው:: ሚስቶቹም እናቶቻቸው ናቸው:: የዝምድና ባለቤቶችም ከፊላቸው በከፊሉ (ውርስ) በአላህ መጽሐፍ ውስጥ ከምእምናንና ከስደተኞቹ ይልቅ የተገባቸው ናቸው::ግን ወደ ወዳጆቻችሁ (በኑዛዜ) መልካምን ብትሰሩ (ይፈቀዳል):: ይህ በመጽሐፉ ውስጥ የተመዘገበ ነው::

7. ከነቢዮችም የጠበቀ ኪዳናቸውን ከአንተም፣ ከኑሕም፣ ከኢብራሒምም፣ ከሙሳም ከመርየም ልጅ ዒሳም በያዝን ጊዜ (አስታወስ):: ከእነርሱም የከበደን ቃል ኪዳን ያዝን::

8. (አላህ) እውነተኞችን ከውነታቸው ሊጠይቅ (ይህንን ሠራ):: ለከሓዲዎችም አሳማሚን ቅጣት አዘጋጀ::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ ٱتَّقِ ٱللَّهَ وَلَا تُطِعِ ٱلۡكَٰفِرِينَ وَٱلۡمُنَٰفِقِينَۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ عَلِيمًا حَكِيمٗا ١

وَٱتَّبِعۡ مَا يُوحَىٰٓ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِمَا تَعۡمَلُونَ خَبِيرٗا ٢

وَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِۚ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ وَكِيلٗا ٣

مَّا جَعَلَ ٱللَّهُ لِرَجُلٖ مِّن قَلۡبَيۡنِ فِي جَوۡفِهِۦۚ وَمَا جَعَلَ أَزۡوَٰجَكُمُ ٱلَّٰٓـِٔي تُظَٰهِرُونَ مِنۡهُنَّ أُمَّهَٰتِكُمۡۚ وَمَا جَعَلَ أَدۡعِيَآءَكُمۡ أَبۡنَآءَكُمۡۚ ذَٰلِكُمۡ قَوۡلُكُم بِأَفۡوَٰهِكُمۡۖ وَٱللَّهُ يَقُولُ ٱلۡحَقَّ وَهُوَ يَهۡدِي ٱلسَّبِيلَ ٤

ٱدۡعُوهُمۡ لِأٓبَآئِهِمۡ هُوَ أَقۡسَطُ عِندَ ٱللَّهِۚ فَإِن لَّمۡ تَعۡلَمُوٓاْ ءَابَآءَهُمۡ فَإِخۡوَٰنُكُمۡ فِي ٱلدِّينِ وَمَوَٰلِيكُمۡۚ وَلَيۡسَ عَلَيۡكُمۡ جُنَاحٞ فِيمَآ أَخۡطَأۡتُم بِهِۦ وَلَٰكِن مَّا تَعَمَّدَتۡ قُلُوبُكُمۡۚ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورٗا رَّحِيمًا ٥

ٱلنَّبِيُّ أَوۡلَىٰ بِٱلۡمُؤۡمِنِينَ مِنۡ أَنفُسِهِمۡۖ وَأَزۡوَٰجُهُۥٓ أُمَّهَٰتُهُمۡۗ وَأُوْلُواْ ٱلۡأَرۡحَامِ بَعۡضُهُمۡ أَوۡلَىٰ بِبَعۡضٖ فِي كِتَٰبِ ٱللَّهِ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُهَٰجِرِينَ إِلَّآ أَن تَفۡعَلُوٓاْ إِلَىٰٓ أَوۡلِيَآئِكُم مَّعۡرُوفٗاۚ كَانَ ذَٰلِكَ فِي ٱلۡكِتَٰبِ مَسۡطُورٗا ٦

وَإِذۡ أَخَذۡنَا مِنَ ٱلنَّبِيِّـۧنَ مِيثَٰقَهُمۡ وَمِنكَ وَمِن نُّوحٖ وَإِبۡرَٰهِيمَ وَمُوسَىٰ وَعِيسَى ٱبۡنِ مَرۡيَمَۖ وَأَخَذۡنَا مِنۡهُم مِّيثَٰقًا غَلِيظٗا ٧

لِّيَسۡـَٔلَ ٱلصَّٰدِقِينَ عَن صِدۡقِهِمۡۚ وَأَعَدَّ لِلۡكَٰفِرِينَ عَذَابًا أَلِيمٗا ٨

9. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ብዙ ሰራዊት በመጣችባችሁና በእነርሱ ላይ ነፋስንና ያላያችኋትን ሰራዊት በላክን ጊዜ በእናንተ ላይ (ያደረገላችሁን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَةَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡ إِذۡ جَآءَتۡكُمۡ جُنُودٞ فَأَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ رِيحٗا وَجُنُودٗا لَّمۡ تَرَوۡهَاۚ وَكَانَ ٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرًا ٩

10. ከበላያችሁም ከናንተ በታችም በመጡባችሁ ጊዜ፣ ዓይኖችም በቃበዙ፣ ልቦችም ላንቃዎች በደረሱና በአላህም ጥርጣሬዎችን በጠረጠራችሁ ጊዜ (ያደረገላችሁን አስታውሱ)፡፡

إِذۡ جَآءُوكُم مِّن فَوۡقِكُمۡ وَمِنۡ أَسۡفَلَ مِنكُمۡ وَإِذۡ زَاغَتِ ٱلۡأَبۡصَٰرُ وَبَلَغَتِ ٱلۡقُلُوبُ ٱلۡحَنَاجِرَ وَتَظُنُّونَ بِٱللَّهِ ٱلظُّنُونَا۠ ١٠

11. እዚያ ዘንድ ምእምናን ተሞከሩ፡፡ ብርቱን መንቀጥቀጥም ተንቀጠቀጡ፡፡

هُنَالِكَ ٱبۡتُلِيَ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ وَزُلۡزِلُواْ زِلۡزَالٗا شَدِيدٗا ١١

12. መናፍቆችና እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ በሽታ ያለባቸውም «አላህና መልክተኛው ማታለልን እንጂ ሌላን አልቀጠሩንም» በሚሉ ጊዜ (ያደረገላችሁን አስታውሱ)፡፡

وَإِذۡ يَقُولُ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ وَٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ مَّا وَعَدَنَا ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥٓ إِلَّا غُرُورٗا ١٢

13. ከእነርሱም የሆኑ ጭፍሮች «የየስሪብ ሰዎች ሆይ! ለእናንተ ስፍራ የላችሁምና ተመለሱ» ባሉ ጊዜ (አስታውሱ)፡፡ ከእነርሱም «ከፊሎቹ እርሷ ነውረኛ ሳትሆን ቤቶቻችን ነውረኛ ናቸው» የሚሉ ሆነው ነቢዩን (ከጦሩ ለመመለስ) ፈቃድን ይጠይቃሉ፡፡ መሸሽን እንጂ ሌላ አይፈልጉም፡፡

وَإِذۡ قَالَت طَّآئِفَةٞ مِّنۡهُمۡ يَٰٓأَهۡلَ يَثۡرِبَ لَا مُقَامَ لَكُمۡ فَٱرۡجِعُواْۚ وَيَسۡتَـٔۡذِنُ فَرِيقٞ مِّنۡهُمُ ٱلنَّبِيَّ يَقُولُونَ إِنَّ بُيُوتَنَا عَوۡرَةٞ وَمَا هِيَ بِعَوۡرَةٍۖ إِن يُرِيدُونَ إِلَّا فِرَارٗا ١٣

14. በእነርሱም ላይ (ቤቶቻቸው) ከየቀበሌዋ በተገባባት ከዚያም ከኢስላም መመለስን በተጠየቁ ኖሮ በሠሯት ነበር፡፡ በእርሷም ጥቂትን ጊዜ እንጂ አይቆዩም ነበር፡፡

وَلَوۡ دُخِلَتۡ عَلَيۡهِم مِّنۡ أَقۡطَارِهَا ثُمَّ سُئِلُواْ ٱلۡفِتۡنَةَ لَأٓتَوۡهَا وَمَا تَلَبَّثُواْ بِهَآ إِلَّا يَسِيرٗا ١٤

15. ጀርባዎችንም ላያዞሩ ከዚያ በፊት በእርግጥ አላህን ቃል ኪዳን የተጋቡ ነበሩ፡፡ የአላህም ቃል ኪዳን የሚጠየቁበት ነው፡፡

وَلَقَدۡ كَانُواْ عَٰهَدُواْ ٱللَّهَ مِن قَبۡلُ لَا يُوَلُّونَ ٱلۡأَدۡبَٰرَۚ وَكَانَ عَهۡدُ ٱللَّهِ مَسۡـُٔولٗا ١٥

16. ከሞት ወይም ከመገደል ብትሸሹ መሸሻችሁ ፈጽሞ አይጠቅማችሁም፡፡ ያን ጊዜም ጥቂትን እንጂ የምትጣቀሙ አትደረጉም በላቸው፡፡

قُل لَّن يَنفَعَكُمُ ٱلۡفِرَارُ إِن فَرَرۡتُم مِّنَ ٱلۡمَوۡتِ أَوِ ٱلۡقَتۡلِ وَإِذٗا لَّا تُمَتَّعُونَ إِلَّا قَلِيلٗا ١٦

17. «(አላህ) በእናንተ ክፉን ነገር ቢሻ ያ ከአላህ የሚጠብቃችሁ ማነው? ወይም ለእናንተ ችሮታን ቢሻ፤ (በክፉ የሚነካችሁ ማነው?)» በላቸው፤ ከአላህም ሌላ ለእነርሱ ወዳጅም ረዳትም አያገኙም፡፡

قُلۡ مَن ذَا ٱلَّذِي يَعۡصِمُكُم مِّنَ ٱللَّهِ إِنۡ أَرَادَ بِكُمۡ سُوٓءًا أَوۡ أَرَادَ بِكُمۡ رَحۡمَةٗۚ وَلَا يَجِدُونَ لَهُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ وَلِيّٗا وَلَا نَصِيرٗا ١٧

18. ከእናንተ ውስጥ የሚያሳንፉትን፣ ለወንድሞቻቸውም «ወደኛ ኑ» የሚሉትን፣ ውጊያንም ጥቂትን እንጂ የማይመጡትን በእርግጥ አላህ ያውቃቸዋል፡፡

۞قَدۡ يَعۡلَمُ ٱللَّهُ ٱلۡمُعَوِّقِينَ مِنكُمۡ وَٱلۡقَآئِلِينَ لِإِخۡوَٰنِهِمۡ هَلُمَّ إِلَيۡنَاۖ وَلَا يَأۡتُونَ ٱلۡبَأۡسَ إِلَّا قَلِيلًا ١٨

19. በእናንተ ላይ (እርዳታን) የነፈጉ ሆነው እንጅ (የማይመጡትን)፣ ሽብሩም በመጣ ጊዜ እንደዚያ ከሞት (መከራ) በርሱ ላይ የሚሸፍን ዐይጋ እንደወደቀበት ዓይኖቻቸው ወዲያና ወዲህ የምትዞር ኾና ወዳንተ ሲመለከቱ ታያቸዋለህ፡፡ ሽብሩም በኼደ ጊዜ በገንዘብ ላይ የሚሳሱ ኾነው በተቡ ምላሶች ይነድፏችኋል፡፡ እነዚያ አላመኑም፡፡ ስለዚህ አላህ ሥራዎቻቸውን አበላሸ፡፡ ይህም በአላህ ላይ ገርነው፡፡

أَشِحَّةً عَلَيۡكُمۡۖ فَإِذَا جَآءَ ٱلۡخَوۡفُ رَأَيۡتَهُمۡ يَنظُرُونَ إِلَيۡكَ تَدُورُ أَعۡيُنُهُمۡ كَٱلَّذِي يُغۡشَىٰ عَلَيۡهِ مِنَ ٱلۡمَوۡتِۖ فَإِذَا ذَهَبَ ٱلۡخَوۡفُ سَلَقُوكُم بِأَلۡسِنَةٍ حِدَادٍ أَشِحَّةً عَلَى ٱلۡخَيۡرِۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَمۡ يُؤۡمِنُواْ فَأَحۡبَطَ ٱللَّهُ أَعۡمَٰلَهُمۡۚ وَكَانَ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٗا ١٩

20. (መናፍቆች) አሕዛብን አልኼዱም ብለው ያስባሉ፡፡ አሕዛቦቹም ቢመጡ እነርሱ በዘላኖች ውስጥ በገጠር (የራቁ) ሊሆኑ ይመኛሉ፡፡ ከወሬዎቻችሁ ይጠይቃሉ፡፡ በእናንተ ውስጥ በነበሩም ኖሮ ጥቂትን እንጂ አይዋጉም ነበር፡

يَحۡسَبُونَ ٱلۡأَحۡزَابَ لَمۡ يَذۡهَبُواْۖ وَإِن يَأۡتِ ٱلۡأَحۡزَابُ يَوَدُّواْ لَوۡ أَنَّهُم بَادُونَ فِي ٱلۡأَعۡرَابِ يَسۡـَٔلُونَ عَنۡ أَنۢبَآئِكُمۡۖ وَلَوۡ كَانُواْ فِيكُم مَّا قَٰتَلُوٓاْ إِلَّا قَلِيلٗا ٢٠

21. ለእናንተ አላህንና የመጨረሻውን ቀን የሚከጅል ለሆነ ሰው፣ አላህንም በብዙ ለሚያወሳ በአላህ መልዕክተኛ መልካም መከተል አልላችሁ፡፡

لَّقَدۡ كَانَ لَكُمۡ فِي رَسُولِ ٱللَّهِ أُسۡوَةٌ حَسَنَةٞ لِّمَن كَانَ يَرۡجُواْ ٱللَّهَ وَٱلۡيَوۡمَ ٱلۡأٓخِرَ وَذَكَرَ ٱللَّهَ كَثِيرٗا ٢١

22. አማኞቹም አሕዛብን ባዩ ጊዜ «ይህ አላህና መልክተኛው የቀጠሩን ነው፡፡ አላህና መልክተኛውም እውነትን ተናገሩ» አሉ፡፡ (ይህ) እምነትንና መታዘዝንም እንጂ ሌላን አልጨመረላቸውም፡፡

وَلَمَّا رَءَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلۡأَحۡزَابَ قَالُواْ هَٰذَا مَا وَعَدَنَا ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥ وَصَدَقَ ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥۚ وَمَا زَادَهُمۡ إِلَّآ إِيمَٰنٗا وَتَسۡلِيمٗا ٢٢

23. ከአማኞቹ በእርሱ ላይ ለአላህ ቃል ኪዳን የገቡበትን በእውነት የፈጸሙ ወንዶች አሉ፡፡ ከነርሱም ስለቱን የፈጸመ (ለሃይማኖቱ የተገደለ) አለ፤ ከነርሱም ገና የሚጠባበቅ አለ፡፡ (የገቡበትን ቃል) መለወጥንም አልለወጡም፡፡

مِّنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ رِجَالٞ صَدَقُواْ مَا عَٰهَدُواْ ٱللَّهَ عَلَيۡهِۖ فَمِنۡهُم مَّن قَضَىٰ نَحۡبَهُۥ وَمِنۡهُم مَّن يَنتَظِرُۖ وَمَا بَدَّلُواْ تَبۡدِيلٗا ٢٣

24. አላህ እውነተኞችን በውነተኛነታቸው ሊመነዳ መናፍቃንንም ቢሻ ሊቀጣ ወይም (ቢመለሱ) በእነርሱ ላይ ጸጸታቸውን ሊቀበል (ይህን አደረገ)፡፡ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና፡፡

لِّيَجۡزِيَ ٱللَّهُ ٱلصَّٰدِقِينَ بِصِدۡقِهِمۡ وَيُعَذِّبَ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ إِن شَآءَ أَوۡ يَتُوبَ عَلَيۡهِمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ٢٤

25. እነዚያንም የካዱትን በቁጭታቸው የተመሉ መልካምን ነገር ያላገኙ ሆነው አላህ መለሳቸው፡፡ አማኞቹንም አላህ መጋደልን በቃቸው፡፡ አላህም ብርቱ አሸናፊ ነው፡፡

وَرَدَّ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِغَيۡظِهِمۡ لَمۡ يَنَالُواْ خَيۡرٗاۚ وَكَفَى ٱللَّهُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٱلۡقِتَالَۚ وَكَانَ ٱللَّهُ قَوِيًّا عَزِيزٗا ٢٥

26. እነዚያንም ከመጽሐፉ ባለቤቶች (አሕዛቦችን) የረዷቸውን (ቁረይዟን) ከምሽጎቻቸው አወረዳቸው፡፡ በልቦቻቸውም ውስጥ መባባትን ጣለባቸው፡፡ ከፊሉን ትገድላላችሁ፡፡ ከፊሉንም ትማርካላችሁ፡፡

وَأَنزَلَ ٱلَّذِينَ ظَٰهَرُوهُم مِّنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ مِن صَيَاصِيهِمۡ وَقَذَفَ فِي قُلُوبِهِمُ ٱلرُّعۡبَ فَرِيقٗا تَقۡتُلُونَ وَتَأۡسِرُونَ فَرِيقٗا ٢٦

27. ምድራቸውንም፣ ቤቶቻቸውንም፣ ገንዘቦቻቸውንም ገና ያልረገጣችኋትንም ምድር አወረሳችሁ፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَأَوۡرَثَكُمۡ أَرۡضَهُمۡ وَدِيَٰرَهُمۡ وَأَمۡوَٰلَهُمۡ وَأَرۡضٗا لَّمۡ تَطَـُٔوهَاۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٗا ﴿٢٧﴾

28. አንተ ነቢይ ሆይ! ለሚስቶችህ (እንዲህ) በላቸው «ቅርቢቱን ሕይወትና ጌጧን የምትፈልጉ እንደ ሆናችሁ ኑ፤ አጣቅማችኋለሁና፡፡ መልካምንም ማሰማራት (በመፍታት) አሰማራችኋለሁና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ قُل لِّأَزۡوَٰجِكَ إِن كُنتُنَّ تُرِدۡنَ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا وَزِينَتَهَا فَتَعَالَيۡنَ أُمَتِّعۡكُنَّ وَأُسَرِّحۡكُنَّ سَرَاحٗا جَمِيلٗا ﴿٢٨﴾

29. «አላህንና መልክተኛውን የመጨረሻይቱን አገርም የምትፈልጉ ብትሆኑም፤ እነሆ አላህ ከእናንተ ለመልካም ሠሪዎቹ ትልቅን ምንዳ አዘጋጅቷል፡፡»

وَإِن كُنتُنَّ تُرِدۡنَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَٱلدَّارَ ٱلۡأٓخِرَةَ فَإِنَّ ٱللَّهَ أَعَدَّ لِلۡمُحۡسِنَٰتِ مِنكُنَّ أَجۡرًا عَظِيمٗا ﴿٢٩﴾

30. የነቢዩ ሴቶች ሆይ! ከእናንተ ውስጥ ግልጽ የሆነን መጥፎ ሥራ የምትሠራ ለእርሷ ቅጣቱ ሁለት እጥፍ ሆኖ ይነባበርባታል፡፡ ይህም በአላህ ላይ ገር ነው፡፡

يَٰنِسَآءَ ٱلنَّبِيِّ مَن يَأۡتِ مِنكُنَّ بِفَٰحِشَةٖ مُّبَيِّنَةٖ يُضَٰعَفۡ لَهَا ٱلۡعَذَابُ ضِعۡفَيۡنِۚ وَكَانَ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٗا ﴿٣٠﴾

31. ከእናንተም ለአላህና ለመልክተኛው የምትታዘዝ መልካም ሥራንም የምትሠራ ምንዳዋን ሁለት ጊዜ እንሰጣታለን፡፡ ለእርሷም የከበረን ሲሳይ አዘጋጅተንላታል፡፡

۞وَمَن يَقۡنُتۡ مِنكُنَّ لِلَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَتَعۡمَلۡ صَٰلِحٗا نُّؤۡتِهَآ أَجۡرَهَا مَرَّتَيۡنِ وَأَعۡتَدۡنَا لَهَا رِزۡقٗا كَرِيمٗا ﴿٣١﴾

32. የነቢዩ ሴቶች ሆይ! ከሴቶች እንደማናቸው አይደላችሁም፡፡ አላህን ብትፈሩ (ትበልጣላችሁ)፡፡ ያ በልቡ ውስጥ በሽታ ያለበት እንዳይከጅል በንግግር አትለስልሱም፡፡ መልካምንም ንግግር ተናገሩ፡፡

يَٰنِسَآءَ ٱلنَّبِيِّ لَسۡتُنَّ كَأَحَدٖ مِّنَ ٱلنِّسَآءِ إِنِ ٱتَّقَيۡتُنَّۚ فَلَا تَخۡضَعۡنَ بِٱلۡقَوۡلِ فَيَطۡمَعَ ٱلَّذِي فِي قَلۡبِهِۦ مَرَضٞ وَقُلۡنَ قَوۡلٗا مَّعۡرُوفٗا ﴿٣٢﴾

33. በቤቶቻችሁም ውስጥ እርጉ፡፡ እንደ ፊተኛይቱ መሃይምነት ጊዜ መገለጥም በማጌጥ አትገለጡ፡፡ ሶላትንም በደንቡ ስገዱ፡፡ ዘካንም ስጡ፡፡ አላህንና መልክተኛውንም ታዘዙ፡፡ የነቢዩ ቤተሰቦች ሆይ! አላህ የሚሻው ከእናንተ ላይ እርክሰትን ሊያስወግድና ማጥራትንም ሊያጠራችሁ ብቻ ነው፡፡

وَقَرۡنَ فِي بُيُوتِكُنَّ وَلَا تَبَرَّجۡنَ تَبَرُّجَ ٱلۡجَٰهِلِيَّةِ ٱلۡأُولَىٰۖ وَأَقِمۡنَ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتِينَ ٱلزَّكَوٰةَ وَأَطِعۡنَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥٓۚ إِنَّمَا يُرِيدُ ٱللَّهُ لِيُذۡهِبَ عَنكُمُ ٱلرِّجۡسَ أَهۡلَ ٱلۡبَيۡتِ وَيُطَهِّرَكُمۡ تَطۡهِيرٗا ﴿٣٣﴾

34. ከአላህ አንቀጾችና ከጥበቡም በቤቶቻችሁ የሚነበበውን አስታውሱ፡፡ አላህ እዝነቱ ረቂቅ ውስጠ ዐዋቂ ነውና፡፡

وَٱذۡكُرۡنَ مَا يُتۡلَىٰ فِي بُيُوتِكُنَّ مِنۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ وَٱلۡحِكۡمَةِۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ لَطِيفًا خَبِيرًا ﴿٣٤﴾

35. ሙስሊሞች ወንዶችና ሙስሊሞች ሴቶች፣ ምእምናንና ምእምናትም፣ ታዛዦች ወንዶችና ታዛዦች ሴቶችም፣ እውነተኞች ወንዶችና እውነተኞች ሴቶችም፣ ታጋሾች ወንዶችና ታጋሾች ሴቶችም፣ አላህን ፈሪዎች ወንዶችና አላህን ፈሪዎች ሴቶችም፣ መጽዋቾች ወንዶችና መጽዋቾች ሴቶችም፣ ጿሚዎች ወንዶችና ጿሚዎች ሴቶችም፣ (ካልተፈቀደ ሥራ) ብልቶቻቸውን ጠባቂዎች ወንዶችና ጠባቂ ሴቶችም፣ አላህን በብዙ አውሺዎች ወንዶችና አውሺዎች ሴቶችም፣ አላህ ለእነርሱ ምሕረትንና ታላቅን ምንዳ አዘጋጅቶላቸዋል፡፡

إِنَّ ٱلْمُسْلِمِينَ وَٱلْمُسْلِمَٰتِ وَٱلْمُؤْمِنِينَ وَٱلْمُؤْمِنَٰتِ وَٱلْقَٰنِتِينَ وَٱلْقَٰنِتَٰتِ وَٱلصَّٰدِقِينَ وَٱلصَّٰدِقَٰتِ وَٱلصَّٰبِرِينَ وَٱلصَّٰبِرَٰتِ وَٱلْخَٰشِعِينَ وَٱلْخَٰشِعَٰتِ وَٱلْمُتَصَدِّقِينَ وَٱلْمُتَصَدِّقَٰتِ وَٱلصَّٰٓئِمِينَ وَٱلصَّٰٓئِمَٰتِ وَٱلْحَٰفِظِينَ فُرُوجَهُمْ وَٱلْحَٰفِظَٰتِ وَٱلذَّٰكِرِينَ ٱللَّهَ كَثِيرًا وَٱلذَّٰكِرَٰتِ أَعَدَّ ٱللَّهُ لَهُم مَّغْفِرَةً وَأَجْرًا عَظِيمًا ﴿٣٥﴾

36. አላህና መልክተኛውም ነገርን በፈረዱ ጊዜ ለምእምናንና ለምእምናት ከነገራቸው ለእነርሱ ምርጫ ሊኖራቸው አይገባም! የአላህንና የመልክተኛውንም ትእዛዝ የጣሰ ሰው ግልጽ የሆነን መሳሳት በእርግጥ ተሳሳተ፡፡

وَمَا كَانَ لِمُؤْمِنٍ وَلَا مُؤْمِنَةٍ إِذَا قَضَى ٱللَّهُ وَرَسُولُهُۥٓ أَمْرًا أَن يَكُونَ لَهُمُ ٱلْخِيَرَةُ مِنْ أَمْرِهِمْ ۗ وَمَن يَعْصِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ فَقَدْ ضَلَّ ضَلَٰلًا مُّبِينًا ﴿٣٦﴾

37. ለእዚያም አላህ በእርሱ ላይ ለለገሰለትና (አንተም ነጻ በማውጣት) በእርሱ ላይ ለለገስከለት ሰው (ለዘይድ) አላህ ገላጩ የሆነን ነገር በነፍስህ ውስጥ የምትደብቅና አላህ ልትፈራው ይልቅ የተገባው ሲሆን ሰዎችን የምትፈራ ሆነህ «ሚስትህን ባንተ ዘንድ ያዝ፤ (ከመፍታት) አላህንም ፍራ» በምትል ጊዜ (አስታውስ)፡ ፡ ዘይድም ከእርሷ ጉዳይን በፈጸመ ጊዜ በምእምናኖች ላይ ልጅ አድርገው ባስጠጉዋቸው (ሰዎች) ሚስቶች ከእነርሱ ጉዳይን በፈጸሙ ጊዜ (በማግባት) ችግር እንዳይኖርባቸው እርሷን አጋባንህ፡፡ የአላህም ትእዛዝ ተፈጻሚ ነው፡፡

وَإِذْ تَقُولُ لِلَّذِىٓ أَنْعَمَ ٱللَّهُ عَلَيْهِ وَأَنْعَمْتَ عَلَيْهِ أَمْسِكْ عَلَيْكَ زَوْجَكَ وَٱتَّقِ ٱللَّهَ وَتُخْفِى فِى نَفْسِكَ مَا ٱللَّهُ مُبْدِيهِ وَتَخْشَى ٱلنَّاسَ وَٱللَّهُ أَحَقُّ أَن تَخْشَىٰهُ ۖ فَلَمَّا قَضَىٰ زَيْدٌ مِّنْهَا وَطَرًا زَوَّجْنَٰكَهَا لِكَىْ لَا يَكُونَ عَلَى ٱلْمُؤْمِنِينَ حَرَجٌ فِىٓ أَزْوَٰجِ أَدْعِيَآئِهِمْ إِذَا قَضَوْا۟ مِنْهُنَّ وَطَرًا ۚ وَكَانَ أَمْرُ ٱللَّهِ مَفْعُولًا ﴿٣٧﴾

38. በነቢዩ ላይ አላህ ለእርሱ በፈረደው ነገር ምንም ችግር ሊኖርበት አይገባም፡፡ በእነዚያ ከዚያ በፊት ባለፉት (ነቢያት) አላህ ደነገገው፡፡ የአላህም ትእዛዝ የተፈረደ ፍርድ ነው፡፡

مَّا كَانَ عَلَى ٱلنَّبِىِّ مِنْ حَرَجٍ فِيمَا فَرَضَ ٱللَّهُ لَهُۥ ۖ سُنَّةَ ٱللَّهِ فِى ٱلَّذِينَ خَلَوْا۟ مِن قَبْلُ ۚ وَكَانَ أَمْرُ ٱللَّهِ قَدَرًا مَّقْدُورًا ﴿٣٨﴾

39. ለእነዚያ የአላህን መልእክቶች ለሚያደርሱና ለሚፈሩት ከአላህ በስተቀርም አንድንም ለማይፈሩት (ተደነገገ)፡፡ ተቆጣጣሪም በአላህ በቃ፡፡

ٱلَّذِينَ يُبَلِّغُونَ رِسَٰلَٰتِ ٱللَّهِ وَيَخْشَوْنَهُۥ وَلَا يَخْشَوْنَ أَحَدًا إِلَّا ٱللَّهَ ۗ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ حَسِيبًا ﴿٣٩﴾

40. ሙሐመድ ከወንዶቻችሁ የአንድም ሰው አባት አይደለም፡፡ ግን የአላህ መልክተኛና የነቢዮች መደምደሚያ ነው፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

مَّا كَانَ مُحَمَّدٌ أَبَآ أَحَدٍ مِّن رِّجَالِكُمْ وَلَٰكِن رَّسُولَ ٱللَّهِ وَخَاتَمَ ٱلنَّبِيِّۦنَ ۗ وَكَانَ ٱللَّهُ بِكُلِّ شَىْءٍ عَلِيمًا ﴿٤٠﴾

41. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ብዙ ማውሳትን አውሱት፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ٱذْكُرُوا۟ ٱللَّهَ ذِكْرًا كَثِيرًا ﴿٤١﴾

42. በቀኑ መጀመሪያና መጨረሻም አጥሩት፡፡

وَسَبِّحُوهُ بُكۡرَةٗ وَأَصِيلًا ٤٢

43. እርሱ ያ በእናንተ ላይ እዝነትን የሚያወርድ ነው፡፡ መላእክቶቹም (እንደዚሁ ምሕረትን የሚለምኑላችሁ ናቸው)፡፡ ከጨለማዎች ወደ ብርሃን ያወጣችሁ ዘንድ (ያዝንላችኋል)፡፡ ለአማኞችም በጣም አዛኝ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي يُصَلِّي عَلَيۡكُمۡ وَمَلَٰٓئِكَتُهُۥ لِيُخۡرِجَكُم مِّنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِۚ وَكَانَ بِٱلۡمُؤۡمِنِينَ رَحِيمٗا ٤٣

44. በሚገናኙት ቀን መከባበሪያቸው ሰላም መባባል ነው፡፡ ለእነርሱም የከበረን ምንዳ አዘጋጅቶላቸዋል፡፡

تَحِيَّتُهُمۡ يَوۡمَ يَلۡقَوۡنَهُۥ سَلَٰمٞۚ وَأَعَدَّ لَهُمۡ أَجۡرٗا كَرِيمٗا ٤٤

45. አንተ ነቢዩ ሆይ! እኛ መስካሪ፣ አብሳሪና አስፈራሪም አድርገን ላክንህ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ إِنَّآ أَرۡسَلۡنَٰكَ شَٰهِدٗا وَمُبَشِّرٗا وَنَذِيرٗا ٤٥

46. ወደ አላህም በፈቃዱ ጠሪ፣ አብሪ ብርሃንም (አድርገን ላክንህ)፡፡

وَدَاعِيًا إِلَى ٱللَّهِ بِإِذۡنِهِۦ وَسِرَاجٗا مُّنِيرٗا ٤٦

47. አማኞችንም ከአላህ ዘንድ ለእነርሱ ታላቅ ችሮታ ያላቸው መኾኑን አብስራቸው፡፡

وَبَشِّرِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ بِأَنَّ لَهُم مِّنَ ٱللَّهِ فَضۡلٗا كَبِيرٗا ٤٧

48. ከሓዲዎችንና መናፍቃንንም አትታዘዛቸው፡፡ ማስቃየታቸውንም (ለአላህ) ተው፡፡ በአላህም ላይ ተጠጋ፡፡ መጠጊያም በአላህ በቃ፡፡

وَلَا تُطِعِ ٱلۡكَٰفِرِينَ وَٱلۡمُنَٰفِقِينَ وَدَعۡ أَذَىٰهُمۡ وَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِۚ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ وَكِيلٗا ٤٨

49. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ምእምናትን ባገባችሁና ከዚያም ሳትነኩዋቸው በፊት በፈታችኋቸው ጊዜ ለእናንተ በእነርሱ ላይ የምትቆጥሩዋት ዒዳ ምንም የላችሁም፡፡ አጣቅሚቸውም፤ (ጉርሻ ስጧቸው)፡፡ መልካም ማሰናበትንም አሰናብቷቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا نَكَحۡتُمُ ٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ ثُمَّ طَلَّقۡتُمُوهُنَّ مِن قَبۡلِ أَن تَمَسُّوهُنَّ فَمَا لَكُمۡ عَلَيۡهِنَّ مِنۡ عِدَّةٖ تَعۡتَدُّونَهَاۖ فَمَتِّعُوهُنَّ وَسَرِّحُوهُنَّ سَرَاحٗا جَمِيلٗا ٤٩

50. አንተ ነቢዩ ሆይ! እኛ እነዚያን መህሮቻቸውን የሰጠሃቸውን ሚስቶችህን፣ አላህ ባንተ ላይ ከመለሰልህም እነዚያን እጅህ የጨበጠቻቸውን ምርኮኞች፣ እነዚያንም ከአንተ ጋር የተሰደዱትን የአጎትህን ሴቶች ልጆች፣ የአክስቶችህንም ሴቶች ልጆች፣ የየሹማህንም ሴቶች ልጆች፣ የየሹሜዎችህንም ሴቶች ልጆች (ማግባትን) ለአንተ ፈቅደንልሃል፡፡ የአመነችንም ሴት ነፍሷን (ራሷን) ለነቢዩ ብትሰጥ ነቢዩ ሊያገባት የፈለገ እንደ ኾነ ከምእምናን ሌላ ላንተ ብቻ የጠራች ስትኾን (ፈቀድንልህ)፡፡ በእነርሱ (በምእምናን) ላይ በሚስቶቻቸውና እጆቻቸው በጨበጧቸው (ባሮች ነገር) ግዴታ ያደረግንባቸውን በእርግጥ ዐውቀናል፡፡ ባንተ ላይ ችግር እንዳይኖር (ያለፉትን ፈቀድንልህ)፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ إِنَّآ أَحۡلَلۡنَا لَكَ أَزۡوَٰجَكَ ٱلَّٰتِيٓ ءَاتَيۡتَ أُجُورَهُنَّ وَمَا مَلَكَتۡ يَمِينُكَ مِمَّآ أَفَآءَ ٱللَّهُ عَلَيۡكَ وَبَنَاتِ عَمِّكَ وَبَنَاتِ عَمَّٰتِكَ وَبَنَاتِ خَالِكَ وَبَنَاتِ خَٰلَٰتِكَ ٱلَّٰتِي هَاجَرۡنَ مَعَكَ وَٱمۡرَأَةٗ مُّؤۡمِنَةً إِن وَهَبَتۡ نَفۡسَهَا لِلنَّبِيِّ إِنۡ أَرَادَ ٱلنَّبِيُّ أَن يَسۡتَنكِحَهَا خَالِصَةٗ لَّكَ مِن دُونِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۗ قَدۡ عَلِمۡنَا مَا فَرَضۡنَا عَلَيۡهِمۡ فِيٓ أَزۡوَٰجِهِمۡ وَمَا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُهُمۡ لِكَيۡلَا يَكُونَ عَلَيۡكَ حَرَجٞۗ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ٥٠

51. ከእነርሱ የምትሻትን ታቆያለህ፡፡ የምትሻውንም ወደ አንተ ታስጠጋለህ፡፡ (በመፍታት) ከአራቅሃትም የፈለግሃትን (በመመለስ ብታስጠጋ) በአንተ ላይ ኀጢአት የለብህም፡፡ ይህ ዓይኖቻቸው ወደ መርጋት፣ ወደ አለማዘናቸውም፣ ለሁሉም በሰጠሃቸው ነገር ወደ መውደዳቸውም በጣም የቀረበ ነው፡፡ አላህም በልቦቻችሁ ውስጥ ያለውን ሁሉ ያውቃል፡፡ አላህም ዐዋቂ ታጋሽ ነው፡፡

52. ከእነዚህ በኋላ እጅህ ከጨበጠቻቸው (ባሮች) በስተቀር ሴቶች ለአንተ አይፈቀዱልህም፡፡ ከሚስቶችም መልካቸው ቢደንቅህም እንኳ በእነርሱ ልታላውጥ (አይፈቀደልህም)፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ተጠባባቂ ነው፡፡

53. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! መድረሱን የማትጠባበቁ ስትኾኑ ወደ ምግብ ካልተፈቀደላችሁ በስተቀር የነቢዩን ቤቶች (በምንም ጊዜ) አትግቡ፡፡ ግን በተጠራችሁ ጊዜ ግቡ፡፡ በተመገባችሁም ጊዜ ወዲያውኑ ተበተኑ፡፡ ለወግ የምትጫወቱ ኾናችሁም (አትቆዩ)፡፡ ይህ ነቢዩን በእርግጥ ያስቸግራል፡፡ ከእናንተም ያፍራል፡፡ ግን አላህ ከእውነት አያፍርም፡፡ ዕቃንም (ለመዋስ) በጠየቃችኋቸው ጊዜ ከመጋረጃ ኋላ ኾናችሁ ጠይቋቸው፡፡ ይህ ለልቦቻችሁ፤ ለልቦቻቸውም የበለጠ ንጽሕና ነው፡፡ የአላህንም መልክተኛ ልታስቸግሩ ሚስቶቹንም ከእርሱ በኋላ ምንጊዜም ልታገቡ ለእናንተ አይገባችሁም፡፡ ይህ አላህ ዘንድ ከባድ (ኀጢአት) ነው፡፡

54. ማንኛውንም ነገር ብትገልጹ ወይም ብትደብቁት (በርሱ ይመነዳችኋል)፡፡ አላህ ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነውና፡፡

55. (የነቢዩ ሚስቶች) በአባቶቻቸው፣ በወንዶች ልጆቻቸውም፣ በወንድሞቻቸውም፣ ወንድሞቻቸው ወንዶች ልጆችም፣ በእኅቶቻቸው ወንዶች ልጆችም፣ (ምእምናት በኾኑት) በሴቶቻቸውም፣ እጆቻቸው በጨበጧቸውም ባሮች (አጠገብ በመገለጥ) በእነርሱ ላይ ኃጢአት የለባቸውም፡፡ (ሴቶች ሆይ! ታዘዙ) አላህንም ፍሩ፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ መስካሪ ነውና፡፡

56. አላህና መላእክቱ በነቢዩ ላይ የአክብሮት እዝነትን ያወርዳሉ፡፡ እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በእርሱ ላይ የአክብሮት እዝነትን አውርዱ፡፡ የማክበርንም ሰላምታ ሰላም በሉ፡፡

۞تُرۡجِي مَن تَشَآءُ مِنۡهُنَّ وَتُـٔۡوِيٓ إِلَيۡكَ مَن تَشَآءُۖ وَمَنِ ٱبۡتَغَيۡتَ مِمَّنۡ عَزَلۡتَ فَلَا جُنَاحَ عَلَيۡكَۚ ذَٰلِكَ أَدۡنَىٰٓ أَن تَقَرَّ أَعۡيُنُهُنَّ وَلَا يَحۡزَنَّ وَيَرۡضَيۡنَ بِمَآ ءَاتَيۡتَهُنَّ كُلُّهُنَّۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ مَا فِي قُلُوبِكُمۡۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلِيمًا حَلِيمٗا ﴿٥١﴾

لَّا يَحِلُّ لَكَ ٱلنِّسَآءُ مِنۢ بَعۡدُ وَلَآ أَن تَبَدَّلَ بِهِنَّ مِنۡ أَزۡوَٰجٖ وَلَوۡ أَعۡجَبَكَ حُسۡنُهُنَّ إِلَّا مَا مَلَكَتۡ يَمِينُكَۗ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ رَّقِيبٗا ﴿٥٢﴾

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَدۡخُلُواْ بُيُوتَ ٱلنَّبِيِّ إِلَّآ أَن يُؤۡذَنَ لَكُمۡ إِلَىٰ طَعَامٍ غَيۡرَ نَٰظِرِينَ إِنَىٰهُ وَلَٰكِنۡ إِذَا دُعِيتُمۡ فَٱدۡخُلُواْ فَإِذَا طَعِمۡتُمۡ فَٱنتَشِرُواْ وَلَا مُسۡتَـٔۡنِسِينَ لِحَدِيثٍۚ إِنَّ ذَٰلِكُمۡ كَانَ يُؤۡذِي ٱلنَّبِيَّ فَيَسۡتَحۡيِۦ مِنكُمۡۖ وَٱللَّهُ لَا يَسۡتَحۡيِۦ مِنَ ٱلۡحَقِّۚ وَإِذَا سَأَلۡتُمُوهُنَّ مَتَٰعٗا فَسۡـَٔلُوهُنَّ مِن وَرَآءِ حِجَابٖۚ ذَٰلِكُمۡ أَطۡهَرُ لِقُلُوبِكُمۡ وَقُلُوبِهِنَّۚ وَمَا كَانَ لَكُمۡ أَن تُؤۡذُواْ رَسُولَ ٱللَّهِ وَلَآ أَن تَنكِحُوٓاْ أَزۡوَٰجَهُۥ مِنۢ بَعۡدِهِۦٓ أَبَدًاۚ إِنَّ ذَٰلِكُمۡ كَانَ عِندَ ٱللَّهِ عَظِيمًا ﴿٥٣﴾

إِن تُبۡدُواْ شَيۡـًٔا أَوۡ تُخۡفُوهُ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٗا ﴿٥٤﴾

لَّا جُنَاحَ عَلَيۡهِنَّ فِيٓ ءَابَآئِهِنَّ وَلَآ أَبۡنَآئِهِنَّ وَلَآ إِخۡوَٰنِهِنَّ وَلَآ أَبۡنَآءِ إِخۡوَٰنِهِنَّ وَلَآ أَبۡنَآءِ أَخَوَٰتِهِنَّ وَلَا نِسَآئِهِنَّ وَلَا مَا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُهُنَّۗ وَٱتَّقِينَ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ شَهِيدًا ﴿٥٥﴾

إِنَّ ٱللَّهَ وَمَلَٰٓئِكَتَهُۥ يُصَلُّونَ عَلَى ٱلنَّبِيِّۚ يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ صَلُّواْ عَلَيۡهِ وَسَلِّمُواْ تَسۡلِيمًا ﴿٥٦﴾

57. እነዚያ አላህንና መልክተኛውን የሚያስከፉ በቅርቢቱ ዓለም በመጨረሻይቱም አላህ ረግሟቸዋል፡፡ ለእነርሱም አዋራጅን ቅጣት ደግሶላቸዋል፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُؤۡذُونَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ لَعَنَهُمُ ٱللَّهُ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِ وَأَعَدَّ لَهُمۡ عَذَابٗا مُّهِينٗا ٥٧

58. እነዚያንም ምእምናንንና ምእምናነትን ባልሰሩት ነገር (በመዝለፍ) የሚያሰቃዩ ዕብለትንና ግልጽ ኃጢአትን በእርግጥ ተሸከሙ፡፡

وَٱلَّذِينَ يُؤۡذُونَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ بِغَيۡرِ مَا ٱكۡتَسَبُواْ فَقَدِ ٱحۡتَمَلُواْ بُهۡتَٰنٗا وَإِثۡمٗا مُّبِينٗا ٥٨

59. አንተ ነቢዩ ሆይ! ለሚስቶችህ፣ ለሴቶች ልጆችህም፣ ለምእምናን ሚስቶችም ከመከናነቢያዎቻቸው በላያቸው ላይ እንዲለቁ ንገራቸው፡፡ ይህ እንዲታወቁና (በባለጌዎች) እንዳይደፈሩ ለመኾን በጣም የቀረበ ነው፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ قُل لِّأَزۡوَٰجِكَ وَبَنَاتِكَ وَنِسَآءِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ يُدۡنِينَ عَلَيۡهِنَّ مِن جَلَٰبِيبِهِنَّۚ ذَٰلِكَ أَدۡنَىٰٓ أَن يُعۡرَفۡنَ فَلَا يُؤۡذَيۡنَۗ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورٗا رَّحِيمٗا ٥٩

60. መናፍቃንና እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ (የአመንዝራነት) በሽታ ያለባቸው በመዲናም ውስጥ (በወሬ) አሸባሪዎቹ (ከዚህ ሥራቸው) ባይከለከሉ በእነርሱ ላይ በእርግጥ እንቀሰቅስሃለን፡፡ ከዚያም በእርሷ ውስጥ ጥቂትን እንጂ አይጎራበቱህም፡፡

۞لَّئِن لَّمۡ يَنتَهِ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ وَٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ وَٱلۡمُرۡجِفُونَ فِي ٱلۡمَدِينَةِ لَنُغۡرِيَنَّكَ بِهِمۡ ثُمَّ لَا يُجَاوِرُونَكَ فِيهَآ إِلَّا قَلِيلٗا ٦٠

61. የተረገሙ ኾነው እንጂ (አይጎራበቱህም)፡፡ በየትም ስፍራ ቢገኙ ይያዛሉ፡፡ መገደልንም ይገደላሉ፡፡

مَّلۡعُونِينَۖ أَيۡنَمَا ثُقِفُوٓاْ أُخِذُواْ وَقُتِّلُواْ تَقۡتِيلٗا ٦١

62. (ይህቺ) በእነዚያ በፊት ባለፉት (ላይ የደነገጋት) የአላህ ድንጋጌ ናት፡፡ ለአላህም ድንጋጌ ፈጽሞ መለወጥን አታገኝም፡፡

سُنَّةَ ٱللَّهِ فِي ٱلَّذِينَ خَلَوۡاْ مِن قَبۡلُۖ وَلَن تَجِدَ لِسُنَّةِ ٱللَّهِ تَبۡدِيلٗا ٦٢

63. ሰዎች ከሰዓቲቱ ይጠይቁሃል፡፡ «ዕውቀትዋ አላህ ዘንድ ብቻ ነው፤» በላቸው፡፡ የሚያሳውቅህም ምንድን ነው! ሰዓቲቱ በቅርብ ጊዜ ልትኾን ይከጀላል፡፡

يَسۡـَٔلُكَ ٱلنَّاسُ عَنِ ٱلسَّاعَةِۖ قُلۡ إِنَّمَا عِلۡمُهَا عِندَ ٱللَّهِۚ وَمَا يُدۡرِيكَ لَعَلَّ ٱلسَّاعَةَ تَكُونُ قَرِيبًا ٦٣

64. አላህ ከሓዲዎችን በእርግጥ ረግሟቸዋል፡፡ ለእነርሱም የተጋጋመችን እሳት አዘጋጅቷል፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ لَعَنَ ٱلۡكَٰفِرِينَ وَأَعَدَّ لَهُمۡ سَعِيرًا ٦٤

65. በእርሷ ውስጥ ዘለዓለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ፤ ወዳጅም ረዳትም አያገኙም፡፡

خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۖ لَّا يَجِدُونَ وَلِيّٗا وَلَا نَصِيرٗا ٦٥

66. ፊቶቻቸው በእሳት ውስጥ በሚገለባበጡ ቀን «ዋ ምኞታችን! አላህን በተገዛን መልክተኛውንም በታዘዝን ኖሮ» እያሉ ይጸጸታሉ፡፡

يَوۡمَ تُقَلَّبُ وُجُوهُهُمۡ فِي ٱلنَّارِ يَقُولُونَ يَٰلَيۡتَنَآ أَطَعۡنَا ٱللَّهَ وَأَطَعۡنَا ٱلرَّسُولَا۠ ٦٦

67. ይላሉም «ጌታችን ሆይ! እኛ ጌቶቻችንንና ታላላቆቻችንን ታዘዝን፡፡ መንገዱንም አሳሳቱን፡፡

وَقَالُواْ رَبَّنَآ إِنَّآ أَطَعۡنَا سَادَتَنَا وَكُبَرَآءَنَا فَأَضَلُّونَا ٱلسَّبِيلَا۠ ٦٧

68. «ጌታችን ሆይ! ከቅጣቱ እጥፍን ስጣቸው፡፡ ታላቅን እርግማንም እርገማቸው፡፡»

رَبَّنَآ ءَاتِهِمۡ ضِعۡفَيۡنِ مِنَ ٱلۡعَذَابِ وَٱلۡعَنۡهُمۡ لَعۡنٗا كَبِيرٗا ٦٨

69. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! እንደእነዚያ ሙሳን እንዳሰቃዩት ሰዎች አትኹኑ፡፡ ካሉትም ነገር ሁሉ አላህ አጠራው፡፡ አላህም ዘንድ ባለሞገስ ነበር፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ ءَاذَوۡاْ مُوسَىٰ فَبَرَّأَهُ ٱللَّهُ مِمَّا قَالُواْۚ وَكَانَ عِندَ ٱللَّهِ وَجِيهًا ٦٩

70. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ ትክክለኛንም ንግግር ተናገሩ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَقُولُواْ قَوۡلًا سَدِيدًا ٧٠

71. ሥራዎቻችሁን ለእናንተ ያበጅላችኋልና፡፡ ኀጢአቶቻችሁንም ለእናንተ ይምርላችኋል፡፡ አላህንና መልክተኛውን የሚታዘዝም ሰው በእርግጥ ታላቅን እድል አገኘ፡፡

يُصۡلِحۡ لَكُمۡ أَعۡمَٰلَكُمۡ وَيَغۡفِرۡ لَكُمۡ ذُنُوبَكُمۡۗ وَمَن يُطِعِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ فَقَدۡ فَازَ فَوۡزًا عَظِيمًا ٧١

72. እኛ አደራን በሰማያትና በምድር፣ በተራራዎችም ላይ አቀረብናት፡፡ መሸከሟንም እንቢ አሉ፡፡ ከእርሷም ፈሩ፡፡ ሰውም ተሸከማት፡፡ እርሱ በጣም በደለኛ ተሳሳች ነውና፡፡

إِنَّا عَرَضۡنَا ٱلۡأَمَانَةَ عَلَى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَٱلۡجِبَالِ فَأَبَيۡنَ أَن يَحۡمِلۡنَهَا وَأَشۡفَقۡنَ مِنۡهَا وَحَمَلَهَا ٱلۡإِنسَٰنُۖ إِنَّهُۥ كَانَ ظَلُومًا جَهُولًا ٧٢

73. መናፍቃንንና መናፍቃትን፣ ወንዶች አጋሪዎችንና ሴቶች አጋሪዎችንም አላህ ሊቀጣና በምእምናንና በምእምናትም ላይ አላህ ንስሓን ሊቀበል (አደራዋን ሰው ተሸከማት)፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

لِّيُعَذِّبَ ٱللَّهُ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ وَٱلۡمُنَٰفِقَٰتِ وَٱلۡمُشۡرِكِينَ وَٱلۡمُشۡرِكَٰتِ وَيَتُوبَ ٱللَّهُ عَلَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِۗ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورًا رَّحِيمًۢا ٧٣

## ሱረቱ ሰበእ

## سورة سبإ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ምስጋና ለዚያ በሰማያትም ያለ በምድርም ያለ ሁሉ የርሱ ለኾነው ለአላህ ይገባው፡፡ በመጨረሻይቱም ዓለም ምስጋና ለእርሱ ብቻ ነው፡፡ እርሱም ብልሃተኛው ውስጠ ዐዋቂው ነው፡፡

ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ ٱلَّذِي لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَهُ ٱلۡحَمۡدُ فِي ٱلۡأٓخِرَةِۚ وَهُوَ ٱلۡحَكِيمُ ٱلۡخَبِيرُ ١

2. በምድር ውስጥ የሚገባውን ሁሉ ከእርሷም የሚወጣውን ከሰማይም የሚወርደውን በእርሷም ውስጥ የሚያርገውን ሁሉ ያውቃል፡፡ እርሱም አዛኙ መሓሪው ነው፡፡

يَعۡلَمُ مَا يَلِجُ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا يَخۡرُجُ مِنۡهَا وَمَا يَنزِلُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ وَمَا يَعۡرُجُ فِيهَاۚ وَهُوَ ٱلرَّحِيمُ ٱلۡغَفُورُ ٢

3. እነዚያ የካዱትም «ሰዓቲቱ አትመጣብንም» አሉ፡፡ በላቸው «አይደለም፤ ሩቁን ሁሉ ዐዋቂ በኾነው ጌታዬ እምላለሁ፡፡ በእርግጥ ትመጣባችኋለች፡፡ የብናኝ ክብደት ያክል እንኳ በሰማያትና በምድር ውስጥ ከእርሱ አይርቅም፡፡ ከዚህ ያነሰም ኾነ የበለጠ የለም በግልጹ መጽሐፍ ውስጥ የተመዘገበ ቢኾን እንጅ፡፡»

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَا تَأۡتِينَا ٱلسَّاعَةُۖ قُلۡ بَلَىٰ وَرَبِّي لَتَأۡتِيَنَّكُمۡ عَٰلِمِ ٱلۡغَيۡبِۖ لَا يَعۡزُبُ عَنۡهُ مِثۡقَالُ ذَرَّةٖ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَلَا فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَآ أَصۡغَرُ مِن ذَٰلِكَ وَلَآ أَكۡبَرُ إِلَّا فِي كِتَٰبٖ مُّبِينٖ ٣

4. እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን ሊመነዳ (ሰዓቲቱ ትመጣባችኋለች)፤ እነዚያ ለእነርሱ ምህረትና የከበረ ሲሳይ አላቸው፡፡

لِّيَجۡزِيَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَرِزۡقٞ كَرِيمٞ ٤

5. እነዚያም የሚያመልጡ መስሏቸው አንቀጾቻችንን ለማፍረስ የጣሩ እነዚያ ለእነርሱ ከመጥፎ ቅጣት የኾነ አሳማሚ ስቃይ አላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ سَعَوۡ فِيٓ ءَايَٰتِنَا مُعَٰجِزِينَ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٞ مِّن رِّجۡزٍ أَلِيمٞ ٥

6. እነዚያም ዕውቀትን የተሰጡት ያንን ከጌታህ ወዳንተ የተወረደውን እርሱ እውነትና አሸናፊ ምስጉን ወደ ኾነው አላህ መንገድ የሚመራ መኾኑን ያውቃሉ፡፡

وَيَرَى ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡعِلۡمَ ٱلَّذِيٓ أُنزِلَ إِلَيۡكَ مِن رَّبِّكَ هُوَ ٱلۡحَقَّ وَيَهۡدِيٓ إِلَىٰ صِرَٰطِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَمِيدِ ٦

7. እነዚያም የካዱት «(ሙታችሁ) መበጣጠስን ሁሉ በተበጣጠሳችሁ ጊዜ እናንተ በአዲስ መፈጠር ውስጥ ትኾናላችሁ ብሎ የሚነግራችሁን ሰው እናሳያችሁን?» አሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ هَلۡ نَدُلُّكُمۡ عَلَىٰ رَجُلٖ يُنَبِّئُكُمۡ إِذَا مُزِّقۡتُمۡ كُلَّ مُمَزَّقٍ إِنَّكُمۡ لَفِي خَلۡقٖ جَدِيدٍ ٧

8. በአላህ ላይ ውሸትን ቀጠፈን? ወይስ በእርሱ ዕብደት አለበትን? (አሉ)፡፡ እንዳሉት አይደለም፡፡ እነዚያ በመጨረሻይቱ (ዓለም) የማያምኑት (በእርሷ) በቅጣት ውስጥ (አሁን) በሩቅ ስህተትም ውስጥ ናቸው፡፡

أَفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبًا أَم بِهِۦ جِنَّةُۢۗ بَلِ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ فِي ٱلۡعَذَابِ وَٱلضَّلَٰلِ ٱلۡبَعِيدِ ٨

9. ከሰማይና ከምድር በፊታቸውና በኋላቸው ወዳለው ሁሉ አይመለከቱምን? ብንሻ በእነርሱ ምድርን እንደረባባቸዋለን፡፡ ወይም በእነርሱ ላይ ከሰማይ ቁራጭን እንጥልባቸዋለን፤ በዚህ ውስጥ (ወደ ጌታው) ተመላሽ ለኾነ ባሪያ ሁሉ ምልክት አለበት፡፡

أَفَلَمۡ يَرَوۡاْ إِلَىٰ مَا بَيۡنَ أَيۡدِيهِمۡ وَمَا خَلۡفَهُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِۚ إِن نَّشَأۡ نَخۡسِفۡ بِهِمُ ٱلۡأَرۡضَ أَوۡ نُسۡقِطۡ عَلَيۡهِمۡ كِسَفٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَةٗ لِّكُلِّ عَبۡدٖ مُّنِيبٖ ٩

10. ለዳውድም ከእኛ የኾነን ችሮታ በእርግጥ ሰጠነው፡ ፡ (አልንም)፡-«ተራራዎች ሆይ! ከእርሱ ጋር ውዳሴን መላልሱ፡፡ በራሪዎችንም (ገራንለት)፡፡ ብረትንም ለእርሱ አለዘብንለት፡፡»

۞وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا دَاوُۥدَ مِنَّا فَضۡلٗاۖ يَٰجِبَالُ أَوِّبِي مَعَهُۥ وَٱلطَّيۡرَۖ وَأَلَنَّا لَهُ ٱلۡحَدِيدَ ١٠

11. ሰፋፊዎችን ጥሩሮች ሥራ፡፡ በአሠራርዋም መጥን፡ ፡ መልካምንም ሥራ ሥሩ፡፡ እኔ የምትሠሩትን ነገር ሁሉ ተመልካች ነኝና (አልነው)፡፡

أَنِ ٱعۡمَلۡ سَٰبِغَٰتٖ وَقَدِّرۡ فِي ٱلسَّرۡدِۖ وَٱعۡمَلُواْ صَٰلِحًاۖ إِنِّي بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ١١

وَلِسُلَيۡمَٰنَ ٱلرِّيحَ غُدُوُّهَا شَهۡرٞ وَرَوَاحُهَا شَهۡرٞۖ وَأَسَلۡنَا لَهُۥ عَيۡنَ ٱلۡقِطۡرِۖ وَمِنَ ٱلۡجِنِّ مَن يَعۡمَلُ بَيۡنَ يَدَيۡهِ بِإِذۡنِ رَبِّهِۦۖ وَمَن يَزِغۡ مِنۡهُمۡ عَنۡ أَمۡرِنَا نُذِقۡهُ مِنۡ عَذَابِ ٱلسَّعِيرِ ١٢

12. ለሱለይማንም ነፋስን የቀትር በፊት ጉዞዋ የወር መንገድ የቀትር በኋላ ጉዞዋም የወር መንገድ ሲኾን ገራንለት፡፡ የነሐስንም ምንጭ ለእርሱ አፈሰስንለት፡፡ ከጋኔኖችም በጌታው ፈቃድ በፊቱ የሚሠሩን (አደረግንለት)፡፡ ከነርሱም ውስጥ ከትእዛዛችን ዝንፍ የሚል ከነዲድ እሳት ቅጣት እናቀምሰዋለን፡፡

يَعۡمَلُونَ لَهُۥ مَا يَشَآءُ مِن مَّحَٰرِيبَ وَتَمَٰثِيلَ وَجِفَانٖ كَٱلۡجَوَابِ وَقُدُورٖ رَّاسِيَٰتٍۚ ٱعۡمَلُوٓاْ ءَالَ دَاوُۥدَ شُكۡرٗاۚ وَقَلِيلٞ مِّنۡ عِبَادِيَ ٱلشَّكُورُ ١٣

13. ከምኩራቦች፣ ከምስሎችም እንደ ገንዳ ከኾኑ ገበታዎችም፣ ከተደላደሉ ታላላቅ ድስቶችም የሚሻውን ሁሉ ይሠሩለታል፡፡ (አልናቸውም) «የዳውድ ቤተሰቦች ሆይ! አመስጋኞች ኾናችሁ (ለጌታችሁ) ሥሩ፡፡» ከባሮቼ በጣም አመስጋኞቹም ጥቂቶች ናቸው፡፡

فَلَمَّا قَضَيۡنَا عَلَيۡهِ ٱلۡمَوۡتَ مَا دَلَّهُمۡ عَلَىٰ مَوۡتِهِۦٓ إِلَّا دَآبَّةُ ٱلۡأَرۡضِ تَأۡكُلُ مِنسَأَتَهُۥۖ فَلَمَّا خَرَّ تَبَيَّنَتِ ٱلۡجِنُّ أَن لَّوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٱلۡغَيۡبَ مَا لَبِثُواْ فِي ٱلۡعَذَابِ ٱلۡمُهِينِ ١٤

14. በእርሱም ላይ ሞትን በፈጸምንበት ጊዜ መሞቱን በትሩን የምትበላ ተንቀሳቃሽ ምስጥ እንጂ ሌላ አላመለከታቸውም፡፡ በወደቀ ጊዜም ጋኔኖች ሩቅን ምስጢር የሚያወቁ በኾኑ ኖሮ በአዋራጅ ስቃይ ውስጥ የማይቆዩ እንደነበሩ ተረዱ፡፡

لَقَدۡ كَانَ لِسَبَإٖ فِي مَسۡكَنِهِمۡ ءَايَةٞۖ جَنَّتَانِ عَن يَمِينٖ وَشِمَالٖۖ كُلُواْ مِن رِّزۡقِ رَبِّكُمۡ وَٱشۡكُرُواْ لَهُۥۚ بَلۡدَةٞ طَيِّبَةٞ وَرَبٌّ غَفُورٞ ١٥

15. ለሰበእ በመኖሪያቸው በእውነት አስደናቂ ምልክት ነበራቸው፡፡ ከግራና ከቀኝ ሁለት አትክልቶች (ነበሯቸው)፡፡ «ከጌታችሁ ሲሳይ ብሉ፡፡ ለእርሱም አመስግኑ፡፡ (አገራችሁ) ውብ አገር ናት፡፡ (ጌታችሁ) መሓሪ ጌታም ነው» (ተባሉ)፡፡

فَأَعۡرَضُواْ فَأَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ سَيۡلَ ٱلۡعَرِمِ وَبَدَّلۡنَٰهُم بِجَنَّتَيۡهِمۡ جَنَّتَيۡنِ ذَوَاتَيۡ أُكُلٍ خَمۡطٖ وَأَثۡلٖ وَشَيۡءٖ مِّن سِدۡرٖ قَلِيلٖ ١٦

16. (ከማመስገን) ዞሩም፡፡ በእነርሱም ላይ የግድቡን ጎርፍ ለቀቅንባቸው፡፡ በአትክልቶቻቸውም ሁለት አትክልቶች፣ ባለመርጋጋ ፍሬዎችን፣ ባለጠደቻና ከቁርቁራም ባለጥቂት ዛፎችን ለወጥናቸው፡፡

ذَٰلِكَ جَزَيۡنَٰهُم بِمَا كَفَرُواْۖ وَهَلۡ نُجَٰزِيٓ إِلَّا ٱلۡكَفُورَ ١٧

17. በመካዳቸው ይህንን መነዳናቸው፤ (እንዲህ ያለውን ቅጣት) በጣም ከሓዲን እንጂ ሌላውን እንቀጣለን?

وَجَعَلۡنَا بَيۡنَهُمۡ وَبَيۡنَ ٱلۡقُرَى ٱلَّتِي بَٰرَكۡنَا فِيهَا قُرٗى ظَٰهِرَةٗ وَقَدَّرۡنَا فِيهَا ٱلسَّيۡرَۖ سِيرُواْ فِيهَا لَيَالِيَ وَأَيَّامًا ءَامِنِينَ ١٨

18. በእነርሱና በዚያች በውስጧ በረከትን ባደረግንባት አገር (በሻም) መካከልም ቅጥልጥል ከተሞችን አደረግን፡፡ በእርሷም ጉዞን ወሰንን፡፡ «ጸጥተኞች ኾናችሁ በሌሊቶችም በቀኖችም ተጓዙ፤» (አልን)፡፡

فَقَالُواْ رَبَّنَا بَٰعِدۡ بَيۡنَ أَسۡفَارِنَا وَظَلَمُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ فَجَعَلۡنَٰهُمۡ أَحَادِيثَ وَمَزَّقۡنَٰهُمۡ كُلَّ مُمَزَّقٍۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّكُلِّ صَبَّارٖ شَكُورٖ ١٩

19. «ጌታችን ሆይ! በጉዞዎቻችን መካከል አራርቅልን» አሉም፡፡ ነፍሶቻቸውንም በደሉ፡፡ (መገረሚያ) ወሬዎችም አደረግናቸው፡፡ መበታተንንም ሁሉ በታተንናቸው፡፡ በዚህ ውስጥ በጣም ታጋሽና አመስጋኝ ለሆነ ሁሉ መገሰጫዎች አሉበት፡፡

20. ኢብሊስም በእነርሱ ላይ ምኞቱን በእርግጥ ፈጸመ፤ ከአመኑትም የሆኑት ጭፍሮች በስተቀር ተከተሉት፡፡

وَلَقَدْ صَدَّقَ عَلَيْهِمْ إِبْلِيسُ ظَنَّهُۥ فَٱتَّبَعُوهُ إِلَّا فَرِيقًا مِّنَ ٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿٢٠﴾

21. በመጨረሻይቱም ዓለም የሚያምነውን ከዚያ እርሱ ከእርሷ በመጠራጠር ውስጥ ከሆነው ሰው ለይተን እንድናውቅ እንጅ በእነርሱ ላይ ለእርሱ ምንም ስልጣን አልነበረውም፡፡ ጌታህም በነገሩ ሁሉ ላይ ተጠባባቂ ነው፡፡

وَمَا كَانَ لَهُۥ عَلَيْهِم مِّن سُلْطَٰنٍ إِلَّا لِنَعْلَمَ مَن يُؤْمِنُ بِٱلْءَاخِرَةِ مِمَّنْ هُوَ مِنْهَا فِى شَكٍّ ۗ وَرَبُّكَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ حَفِيظٌ ﴿٢١﴾

22. «እነዚያን ከአላህ ሌላ (አማልክት ብላችሁ) የምታስቧቸውን ጥሩ፡፡ በሰማያትም በምድርም ውስጥ የብናኝ ክብደት ያክል ምንንም አይችሉም፡፡ ለእነርሱም በሁለቱም ውስጥ ምንም ሽርክና የላቸውም፡፡ ከእነርሱም ለእርሱ ምንም ኢጋዥ የለውም፤» በላቸው፡፡

قُلِ ٱدْعُوا۟ ٱلَّذِينَ زَعَمْتُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ ۖ لَا يَمْلِكُونَ مِثْقَالَ ذَرَّةٍ فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَلَا فِى ٱلْأَرْضِ وَمَا لَهُمْ فِيهِمَا مِن شِرْكٍ وَمَا لَهُۥ مِنْهُم مِّن ظَهِيرٍ ﴿٢٢﴾

23. ምልጃም እርሱ ለፈቀደለት ሰው ብቻ ቢሆን እንጂ እርሱ ዘንድ ምንም አትጠቅምም፡፡ ከልቦቻቸው ላይ ድንጋጤው በተገለጸም ጊዜ (ተማላጆቹ) «ጌታችሁ ምን አለ?» ይላሉ፡፡ (አማላጆቹ) «እውነትን አለ፤ እርሱም ከፍተኛው ታላቁ ጌታ ነው» ይላሉ፡፡

وَلَا تَنفَعُ ٱلشَّفَٰعَةُ عِندَهُۥٓ إِلَّا لِمَنْ أَذِنَ لَهُۥ ۚ حَتَّىٰٓ إِذَا فُزِّعَ عَن قُلُوبِهِمْ قَالُوا۟ مَاذَا قَالَ رَبُّكُمْ ۖ قَالُوا۟ ٱلْحَقَّ ۖ وَهُوَ ٱلْعَلِىُّ ٱلْكَبِيرُ ﴿٢٣﴾

24. «ከሰማያትና ከምድር (ዝናብንና በቃይን) የሚሰጣችሁ ማነው?» በላቸው፡፡ «አላህ ነው፡፡ እኛ ወይም እናንተ በትክክለኛው መንገድ ላይ ወይም በግልጽ መሳሳት ውስጥ ነን» በላቸው፡፡

۞ قُلْ مَن يَرْزُقُكُم مِّنَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۖ قُلِ ٱللَّهُ ۖ وَإِنَّآ أَوْ إِيَّاكُمْ لَعَلَىٰ هُدًى أَوْ فِى ضَلَٰلٍ مُّبِينٍ ﴿٢٤﴾

25. «ከአጠፋነው ጥፋት አትጠየቁም፡፡ ከምትሠሩትም ሥራ አንጠየቅም» በላቸው፡፡

قُل لَّا تُسْـَٔلُونَ عَمَّآ أَجْرَمْنَا وَلَا نُسْـَٔلُ عَمَّا تَعْمَلُونَ ﴿٢٥﴾

26. «ጌታችን በመካከላችን ይሰበስባል፡፡ ከዚያም በመካከላችን በእውነት ይፈርዳል፡፡ እርሱም በትክክል ፈራጁ ዐዋቂው ነው» በላቸው፡፡

قُلْ يَجْمَعُ بَيْنَنَا رَبُّنَا ثُمَّ يَفْتَحُ بَيْنَنَا بِٱلْحَقِّ وَهُوَ ٱلْفَتَّاحُ ٱلْعَلِيمُ ﴿٢٦﴾

27. «እነዚያን ተጋሪዎች አድርጋችሁ በእርሱ ያስጠጋችኋቸውን (ጣዖታት) አሳዩኝ፡፡ ተዉ (ኢታጋሩ)፤ በእውነቱ እርሱ አሸናፊው ብልሃተኛው አላህ ነው» በላቸው፡፡

قُلْ أَرُونِىَ ٱلَّذِينَ أَلْحَقْتُم بِهِۦ شُرَكَآءَ ۖ كَلَّا ۚ بَلْ هُوَ ٱللَّهُ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ﴿٢٧﴾

28. አንተንም ለሰዎች ሁሉ በመላ አብሳሪና አስፈራሪ አድርገን ቢሆን እንጂ አላከንህም፡፡ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

وَمَآ أَرْسَلْنَٰكَ إِلَّا كَآفَّةً لِّلنَّاسِ بَشِيرًا وَنَذِيرًا وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعْلَمُونَ ﴿٢٨﴾

29. «እውነተኞችም እንደ ሆናችሁ ይህ ቀጠሮ መቼ ነው?» ይላሉ፡፡

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلْوَعْدُ إِن كُنتُمْ صَٰدِقِينَ ﴿٢٩﴾

30. «ለእናንተ ከእርሱ አንዲትንም ሰዓት የማትዘገዩበት የማትቀድሙበትም የቀጠሮ ቀን አላችሁ» በላቸው፡፡

قُل لَّكُم مِّيعَادُ يَوۡمٖ لَّا تَسۡتَـٔۡخِرُونَ عَنۡهُ سَاعَةٗ وَلَا تَسۡتَقۡدِمُونَ ٣٠

31. እነዚያ የካዱትም በዚህ ቁርአን በዚያ ከበፊቱ ባለውም (መጽሐፍ) በጭራሽ አናምንም አሉ፡፡ በዳዮችም ከፊላቸው ወደ ከፊሉ ንግግርን የሚመላለሱ ሆነው በጌታቸው ዘንድ በሚቆሙ ጊዜ ብታይ ኖሮ፤ (አስደናቂን ነገር ታይ ነበር)፡፡ እነዚያ የተዋረዱት ለእነዚያ ለኮሩት «እናንተ ባልነበራችሁ ኖሮ አማኞች በኾን ነበር» ይላሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَن نُّؤۡمِنَ بِهَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ وَلَا بِٱلَّذِي بَيۡنَ يَدَيۡهِۗ وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذِ ٱلظَّٰلِمُونَ مَوۡقُوفُونَ عِندَ رَبِّهِمۡ يَرۡجِعُ بَعۡضُهُمۡ إِلَىٰ بَعۡضٍ ٱلۡقَوۡلَ يَقُولُ ٱلَّذِينَ ٱسۡتُضۡعِفُواْ لِلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُواْ لَوۡلَآ أَنتُمۡ لَكُنَّا مُؤۡمِنِينَ ٣١

32. እነዚያ የኮሩት ለእነዚያ ለተዋረዱት «ከትክክለኛው እምነት ከመጣላችሁ በኋላ እኛ ከለከልናችሁን? አይደለም (እናንተው) ከሓዲዎች ነበራችሁ» ይሏቸዋል፡፡

قَالَ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُواْ لِلَّذِينَ ٱسۡتُضۡعِفُوٓاْ أَنَحۡنُ صَدَدۡنَٰكُمۡ عَنِ ٱلۡهُدَىٰ بَعۡدَ إِذۡ جَآءَكُمۖ بَلۡ كُنتُم مُّجۡرِمِينَ ٣٢

33. እነዚያም የተዋረዱት ለእነዚያ ለኮሩት «አይደለም፤ በአላህ እንድንክድና ለእርሱ ባላንጣዎችን እንድናደርግ ስታዙን (የከለከለን) የሌሊትና የቀን ዱለታችሁ ነው» ይላሉ፡፡ ቅጣቱንም ባዩ ጊዜ ጸጸትን ይገልጻሉ፡፡ በእነዚያም በካዱት አንገቶች ላይ እንዛዝሎችን እናደርጋለን፡፡ ይሠሩት የነበሩትን እንጂ ሌላን ይመነዳሉን?

وَقَالَ ٱلَّذِينَ ٱسۡتُضۡعِفُواْ لِلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُواْ بَلۡ مَكۡرُ ٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِ إِذۡ تَأۡمُرُونَنَآ أَن نَّكۡفُرَ بِٱللَّهِ وَنَجۡعَلَ لَهُۥٓ أَندَادٗاۚ وَأَسَرُّواْ ٱلنَّدَامَةَ لَمَّا رَأَوُاْ ٱلۡعَذَابَۚ وَجَعَلۡنَا ٱلۡأَغۡلَٰلَ فِيٓ أَعۡنَاقِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْۖ هَلۡ يُجۡزَوۡنَ إِلَّا مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٣٣

34. በከተማም አስፈራሪን አልላክንም፡፡ ነዋሪዎችዋ «እኛ በዚያ በርሱ በተላካችሁበት ከሓዲዎች ነን» ያሉ ቢኾኑ እንጂ፡፡

وَمَآ أَرۡسَلۡنَا فِي قَرۡيَةٖ مِّن نَّذِيرٍ إِلَّا قَالَ مُتۡرَفُوهَآ إِنَّا بِمَآ أُرۡسِلۡتُم بِهِۦ كَٰفِرُونَ ٣٤

35. «እኛም በገንዘቦችና በልጆች ይበልጥ የበዛን ነን፡፡ እኛም የምንቀጣ አይደለንም» አሉ፡፡

وَقَالُواْ نَحۡنُ أَكۡثَرُ أَمۡوَٰلٗا وَأَوۡلَٰدٗا وَمَا نَحۡنُ بِمُعَذَّبِينَ ٣٥

36. በላቸው «ጌታዬ ሲሳይን ለሚሻው ሰው ያሰፋል፤ ያጠባልም፡፡ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች አያውቁም፡፡»

قُلۡ إِنَّ رَبِّي يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقۡدِرُ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٣٦

37. ገንዘቦቻችሁና ልጆቻችሁም ያች እኛ ዘንድ መቅረብን የምታቀርባችሁ አይደለችም፡፡ ያመነና መልካምን የሠራ ብቻ ሲቀር፡፡ እነዚያ ለእነርሱ በሠሩት መልካም ሥራ እጥፍ ምንዳ አልላቸው፡፡ እነርሱም በገነት ሰገነቶች ውስጥ ጸጥተኞች ናቸው፡፡

وَمَآ أَمۡوَٰلُكُمۡ وَلَآ أَوۡلَٰدُكُم بِٱلَّتِي تُقَرِّبُكُمۡ عِندَنَا زُلۡفَىٰٓ إِلَّا مَنۡ ءَامَنَ وَعَمِلَ صَٰلِحٗا فَأُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ جَزَآءُ ٱلضِّعۡفِ بِمَا عَمِلُواْ وَهُمۡ فِي ٱلۡغُرُفَٰتِ ءَامِنُونَ ٣٧

38. እነዚያም የሚያቅቱ መስሏቸው አንቀጾቻችንን ለማበላሸት የሚጥሩት እነዚያ በቅጣቱ ውስጥ የሚጣዱ ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يَسۡعَوۡنَ فِيٓ ءَايَٰتِنَا مُعَٰجِزِينَ أُوْلَٰٓئِكَ فِي ٱلۡعَذَابِ مُحۡضَرُونَ ٣٨

39. «ጌታዬ ሲሳይን ከባሮቹ ለሚሻው ሰው ያሰፋል፡፡ ለእርሱም ያጠብባል፡፡ ከማንኛውም ነገር የምትለግሱትን እርሱ ይተካዋል፡፡ እርሱም ከሲሳይ ሰጪዎች ሁሉ በላጭ ነው» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّ رَبِّي يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦ وَيَقۡدِرُ لَهُۥۚ وَمَآ أَنفَقۡتُم مِّن شَيۡءٖ فَهُوَ يُخۡلِفُهُۥۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ٣٩

وَيَوۡمَ يَحۡشُرُهُمۡ جَمِيعٗا ثُمَّ يَقُولُ لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ أَهَٰٓؤُلَآءِ إِيَّاكُمۡ كَانُواْ يَعۡبُدُونَ ﴿٤٠﴾

40. ሁሉንም በሚሰበስባቸውና ከዚያም ለመላእክቶቹ «እነዚህ እናንተን ይግገዙ ነበሩን?» በሚላቸው ቀን (የሚኾነውን አስታውስ)፡፡

قَالُواْ سُبۡحَٰنَكَ أَنتَ وَلِيُّنَا مِن دُونِهِمۖ بَلۡ كَانُواْ يَعۡبُدُونَ ٱلۡجِنَّۖ أَكۡثَرُهُم بِهِم مُّؤۡمِنُونَ ﴿٤١﴾

41. (መላእክቶቹም) «ጥራት ይገባህ ከእነርሱ ሌላ ረዳታችን አንተ ብቻ ነህ፡፡ (እንደሚሉት) አይደለም ይልቁንም ጋኔንን ይግገዙ ነበሩ፡፡ አብዛኞቻቸው በእነርሱ አማኞች ናቸው» ይላሉ፡፡

فَٱلۡيَوۡمَ لَا يَمۡلِكُ بَعۡضُكُمۡ لِبَعۡضٖ نَّفۡعٗا وَلَا ضَرّٗا وَنَقُولُ لِلَّذِينَ ظَلَمُواْ ذُوقُواْ عَذَابَ ٱلنَّارِ ٱلَّتِي كُنتُم بِهَا تُكَذِّبُونَ ﴿٤٢﴾

42. ዛሬም ከፊላችሁ ለከፊሉ መጥቀምንም ኾነ መጉዳትን አይችሉም፡፡ ለእነዚያም ለበደሉት «ያችን በእርሷ ታስተባብሉባት የነበራችሁትን የእሳት ቅጣት ቅመሱ» እንላቸዋለን፡፡

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُنَا بَيِّنَٰتٖ قَالُواْ مَا هَٰذَآ إِلَّا رَجُلٞ يُرِيدُ أَن يَصُدَّكُمۡ عَمَّا كَانَ يَعۡبُدُ ءَابَآؤُكُمۡ وَقَالُواْ مَا هَٰذَآ إِلَّآ إِفۡكٞ مُّفۡتَرٗىۚ وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لِلۡحَقِّ لَمَّا جَآءَهُمۡ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا سِحۡرٞ مُّبِينٞ ﴿٤٣﴾

43. በእነርሱም ላይ አንቀጾቻችን ግልጽ ኾነው በተነበቡላቸው ጊዜ «ይህ አባቶቻችሁ ይግገዙት ከነበሩት ነገር ሊከለክላችሁ የሚፈልግ ሰው እንጂ ሌላ አይደለም» አሉ፡፡ «ይህም (ቁርአን) የተቀጣጠፈ ውሸት ነው እንጂ ሌላ አይደለም» አሉ፡፡ እነዚያም የካዱት እውነቱ በመጣላቸው ጊዜ «ይህ ግልጽ ድግምት ነው እንጂ ሌላ አይደለም» አሉ፡፡

وَمَآ ءَاتَيۡنَٰهُم مِّن كُتُبٖ يَدۡرُسُونَهَاۖ وَمَآ أَرۡسَلۡنَآ إِلَيۡهِمۡ قَبۡلَكَ مِن نَّذِيرٖ ﴿٤٤﴾

44. የሚያጠኑዋቸው የኾኑ መጽሐፍቶችንም ምንም አልሰጠናቸውም፡፡ ከአንተ በፊትም አስፈራሪ ነቢይን ወደእነርሱ አልላክንም፡፡

وَكَذَّبَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ وَمَا بَلَغُواْ مِعۡشَارَ مَآ ءَاتَيۡنَٰهُمۡ فَكَذَّبُواْ رُسُلِيۖ فَكَيۡفَ كَانَ نَكِيرِ ﴿٤٥﴾

45. እነዚያም ከእነርሱ በፊት የነበሩት አስተባብለዋል፡፡ የሰጠናቸውንም ከዐስር አንዱን (እነዚህ) አልደረሱም፡፡ መልክተኞቼንም አስተባበሉ፤ (ነቀፍኳቸውም)፡፡ መንቀፌም እንዴት ነበር!

۞قُلۡ إِنَّمَآ أَعِظُكُم بِوَٰحِدَةٍۖ أَن تَقُومُواْ لِلَّهِ مَثۡنَىٰ وَفُرَٰدَىٰ ثُمَّ تَتَفَكَّرُواْۚ مَا بِصَاحِبِكُم مِّن جِنَّةٍۚ إِنۡ هُوَ إِلَّا نَذِيرٞ لَّكُم بَيۡنَ يَدَيۡ عَذَابٖ شَدِيدٖ ﴿٤٦﴾

46. «የምገስጻችሁ ባንዲት ነገር ብቻ ነው፡፡ (እርሷም) ሁለት ሁለት አንድ አንድም ኾናችሁ ለአላህ እንድትነሱ ከዚያም በጓደኛችሁ (በሙሐመድ) ምንም ዕብደት የሌለበት መኾኑን መርምራችሁ እንድትረረዱ ነው፡፡ እርሱ ለእናንተ ከብርቱ ቅጣት በስተፊት አስጠንቃቂ ነው እንጂ ሌላ አይደለም» በላቸው፡፡

قُلۡ مَا سَأَلۡتُكُم مِّنۡ أَجۡرٖ فَهُوَ لَكُمۡۖ إِنۡ أَجۡرِيَ إِلَّا عَلَى ٱللَّهِۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ شَهِيدٞ ﴿٤٧﴾

47. «ከዋጋ ማንኛውም የጠየቅኋችሁ ቢኖር እርሱ ለእናንተው ነው፤ ዋጋዬ በአላህ ላይ እንጂ በሌላ ላይ አይደለም፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّ رَبِّي يَقۡذِفُ بِٱلۡحَقِّ عَلَّٰمُ ٱلۡغُيُوبِ ﴿٤٨﴾

48. «ጌታዬ እውነትን ያወርዳል፡፡ ሩቅ የኾኑትን ምስጢሮች ሁሉ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

قُلۡ جَآءَ ٱلۡحَقُّ وَمَا يُبۡدِئُ ٱلۡبَٰطِلُ وَمَا يُعِيدُ ﴿٤٩﴾

49. «እውነቱ መጣ፡፡ ውሸትም መነሻም መድረሻም የለውም (ተወገደ)» በላቸው፡፡

50. «ብሳሳት የምሳሳተው በራሴ ላይ ብቻ ነው፡፡ ብመራም ጌታዬ ወደኔ በሚያወርደው ነው፡፡ እርሱ ሰሚ ቅርብ ነውና» በላቸው፡፡

قُلۡ إِن ضَلَلۡتُ فَإِنَّمَآ أَضِلُّ عَلَىٰ نَفۡسِيۖ وَإِنِ ٱهۡتَدَيۡتُ فَبِمَا يُوحِيٓ إِلَيَّ رَبِّيٓۚ إِنَّهُۥ سَمِيعٞ قَرِيبٞ ﴿٥٠﴾

51. በደነገጡና ማምለጫ በሌላቸው ጊዜ ከቅርብ ስፍራም በተያዙ ጊዜ (ኹኔታቸውን) ብታይ ኖሮ (አስደናቂን ነገር ባየህ ነበር)፡፡

وَلَوۡ تَرَىٰٓ إِذۡ فَزِعُواْ فَلَا فَوۡتَ وَأُخِذُواْ مِن مَّكَانٖ قَرِيبٖ ﴿٥١﴾

52. «በእርሱም (አሁን) አመንን» ይላሉ፡፡ ለእነርሱም ከሩቅ ስፍራ (እምነትን) በቀላል ማግኘት ከየታቸው?

وَقَالُوٓاْ ءَامَنَّا بِهِۦ وَأَنَّىٰ لَهُمُ ٱلتَّنَاوُشُ مِن مَّكَانِۭ بَعِيدٖ ﴿٥٢﴾

53. በፊትም በእርሱ በእርግጥ ከደዋል፡፡ ከሩቅ ስፍራም በግምት ንግግርን ይጥላሉ፡፡

وَقَدۡ كَفَرُواْ بِهِۦ مِن قَبۡلُۖ وَيَقۡذِفُونَ بِٱلۡغَيۡبِ مِن مَّكَانِۭ بَعِيدٖ ﴿٥٣﴾

54. ከዚህ ቀደም በመሰሎቻቸው እንደ ተሠራውም ብጤ በእነርሱና በሚፈልጉት መካከል ተጋረደ፡፡ እነርሱ በእርግጥ በአወላዋይ ጥርጣሬ ውስጥ ነበሩና፡፡

وَحِيلَ بَيۡنَهُمۡ وَبَيۡنَ مَا يَشۡتَهُونَ كَمَا فُعِلَ بِأَشۡيَاعِهِم مِّن قَبۡلُۚ إِنَّهُمۡ كَانُواْ فِي شَكّٖ مُّرِيبِۭ ﴿٥٤﴾

## ሱረቱ ፋጢር

## سورة فاطر

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ምስጋና ሰማያትንና ምድርን ፈጣሪ፣ መላእክትን ባለ ሁለት ሁለት፣ ባለ ሶስት ሶስትም፣ ባለ አራት አራትም ክንፎች የኾኑ መልክተኞች አድራጊ ለኾነው አላህ ይገባው፡፡ በፍጥረቱ ውስጥ የሚሻውን ይጨምራል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ فَاطِرِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ جَاعِلِ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةِ رُسُلًا أُوْلِيٓ أَجۡنِحَةٖ مَّثۡنَىٰ وَثُلَٰثَ وَرُبَٰعَۚ يَزِيدُ فِي ٱلۡخَلۡقِ مَا يَشَآءُۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ﴿١﴾

2. አላህ ለሰዎች ከችሮታ የሚከፍታት ለእርሷ ምንም አጋጅ የላትም፡፡ የሚያግደውም ከእርሱ በኋላ ለእርሱ ምንም ለቃቂ የለውም፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

مَّا يَفۡتَحِ ٱللَّهُ لِلنَّاسِ مِن رَّحۡمَةٖ فَلَا مُمۡسِكَ لَهَاۖ وَمَا يُمۡسِكۡ فَلَا مُرۡسِلَ لَهُۥ مِنۢ بَعۡدِهِۦۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ﴿٢﴾

3. እናንተ ሰዎች ሆይ! በእናንተ ላይ (ያለውን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ፡፡ ከአላህ ሌላ ፈጣሪ አለን? ከሰማይና ከምድርም ሲሳይን የሚሰጣችሁ አለን? ከእርሱ በስተቀር አምላክ (ሰጪም) የለም፡፡ ታዲያ ወዴት ትዞራላችሁ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ٱذۡكُرُواْ نِعۡمَتَ ٱللَّهِ عَلَيۡكُمۡۚ هَلۡ مِنۡ خَٰلِقٍ غَيۡرُ ٱللَّهِ يَرۡزُقُكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِۚ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ فَأَنَّىٰ تُؤۡفَكُونَ ﴿٣﴾

4. ቢያስተባብሉህም ከአንተ በፊት የነበሩ መልክተኞች በእርግጥ ተስተባብለዋል፡፡ ወደ አላህም ነገሮች ሁሉ ይመለሳሉ፡፡

وَإِن يُكَذِّبُوكَ فَقَدۡ كُذِّبَتۡ رُسُلٞ مِّن قَبۡلِكَۚ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرۡجَعُ ٱلۡأُمُورُ ﴿٤﴾

5. እናንተ ሰዎች ሆይ! የአላህ ቀጠሮ እውነት ነው:: የቅርቢቱም ሕይወት አታታላችሁ:: አታላዩም (ሰይጣን) በአላህ (መታገስ) አያታላችሁ::

6. ሰይጣን ለናንተ ጠላት ነው:: ስለዚህ ጠላት አድርጋችሁ ያዙት:: ተከታዮቹን የሚጠራው ከእሳት ጓዶች እንዲኾኑ ብቻ ነው::

7. እነዚያ የካዱት ለእነርሱ ብርቱ ቅጣት አልላቸው:: እነዚያም ያመኑትና በጎ ስራዎችን የሠሩት ለእነርሱ ምሕረትና ታላቅ ምንዳ አልላቸው::

8. መጥፎ ሥራው የተሸለመለትና መልካም አድርጎ ያየው ሰው (አላህ እንዳቀናው ሰው ነውን?) አላህም የሚሻውን ሰው ያጠምማል:: የሚሻውንም ያቀናል:: ስለዚህ በእነርሱ ላይ (ባለመቅናታቸው) ስለመቆላጨት ነፍስህ አትጥፋ:: አላህ የሚሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነውና::

9. አላህም ያ ነፋሶችን የላከ ነው:: ደመናዎችንም ትቀሰቅሳለች፤ ወደ ሙት (ድርቅ) አገርም እንነዳዋለን:: በእርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው እናደርጋታለን:: ሙታንንም መቀስቀስ እንደዚሁ ነው::

10. ማሸነፍን የሚፈልግ የኾነ ሰው አሸናፊነት ለአላህ ብቻ ነው፤ (እርሱን በመግገዛት ይፈልገው):: መልካም ንግግር ወደርሱ ይወጣል:: በጎ ሥራም ከፍ ያደርገዋል:: እነዚያም መጥፎ ሥራዎችን የሚዶልቱ ለእነሱ ብርቱ ቅጣት አልላቸው:: የእነዚያም ተንኮል እርሱ ይጠፋል::

11. አላህም ከዐፈር፣ ከዚያም ከፍትወት ጠብታ ፈጠራችሁ:: ከዚያም ጎሳዎች አደረጋችሁ:: ሴትም አታረግዝም አትወልድምም በዕውቀቱ ቢኾን እንጂ:: ዕድሜው ከሚረዘምም አንድም አይረዘምም ከዕድሜውም አይጎደልም በመጽሐፉ ውስጥ ያለ ቢኾን እንጂ:: ይህ በአላህ ላይ ገር ነው::

12. ሁለቱ ባሕሮችም አይተካከሉም! ይህ ጣፋጭ፣ ጥምን ቆራጭ፣ መጠጡ በገር ተዋጭ ነው:: ይህኛውም ጨው መርጋጋ ነው:: እርጥብ ስጋንም ከሁሉም ትበላላችሁ:: (ከጨው ባሕር) የምትለብሷትንም ጌጥ ታወጣላችሁ:: ከችሮታው ልትፈልጉና ልታመሰግኑም መርከቦችን በእርሱ ውስጥ ውሃውን ቀዳጆች ኾነው (ሲንሻለሉ) ታያለህ::

13. ሌሊትን በቀን ውስጥ ያስገባል:: ቀንንም በሌሊት ውሰጥ ያስገባል፤ ፀሐይንና ጨረቃንም ገራ:: ሁሉም እተወሰነ ጊዜ ድረስ ይሮጣሉ:: ይህ ጌታችሁ አላህ ነው:: ንግሥናው የእርሱ ብቻ ነው:: እነዚያም ከእርሱ ሌላ የምትግገዟቸው የተምር ፍሬ ሽፋን እንኳ አይኖራቸውም::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِنَّ وَعْدَ ٱللَّهِ حَقٌّۖ فَلَا تَغُرَّنَّكُمُ ٱلْحَيَوٰةُ ٱلدُّنْيَا وَلَا يَغُرَّنَّكُم بِٱللَّهِ ٱلْغَرُورُ ﴿٥﴾

إِنَّ ٱلشَّيْطَـٰنَ لَكُمْ عَدُوٌّ فَٱتَّخِذُوهُ عَدُوًّاۚ إِنَّمَا يَدْعُواْ حِزْبَهُۥ لِيَكُونُواْ مِنْ أَصْحَـٰبِ ٱلسَّعِيرِ ﴿٦﴾

ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَهُمْ عَذَابٌ شَدِيدٌۖ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّـٰلِحَـٰتِ لَهُم مَّغْفِرَةٌ وَأَجْرٌ كَبِيرٌ ﴿٧﴾

أَفَمَن زُيِّنَ لَهُۥ سُوٓءُ عَمَلِهِۦ فَرَءَاهُ حَسَنًاۖ فَإِنَّ ٱللَّهَ يُضِلُّ مَن يَشَآءُ وَيَهْدِى مَن يَشَآءُۖ فَلَا تَذْهَبْ نَفْسُكَ عَلَيْهِمْ حَسَرَٰتٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌۢ بِمَا يَصْنَعُونَ ﴿٨﴾

وَٱللَّهُ ٱلَّذِىٓ أَرْسَلَ ٱلرِّيَـٰحَ فَتُثِيرُ سَحَابًا فَسُقْنَـٰهُ إِلَىٰ بَلَدٍ مَّيِّتٍ فَأَحْيَيْنَا بِهِ ٱلْأَرْضَ بَعْدَ مَوْتِهَاۚ كَذَٰلِكَ ٱلنُّشُورُ ﴿٩﴾

مَن كَانَ يُرِيدُ ٱلْعِزَّةَ فَلِلَّهِ ٱلْعِزَّةُ جَمِيعًاۚ إِلَيْهِ يَصْعَدُ ٱلْكَلِمُ ٱلطَّيِّبُ وَٱلْعَمَلُ ٱلصَّـٰلِحُ يَرْفَعُهُۥۚ وَٱلَّذِينَ يَمْكُرُونَ ٱلسَّيِّـَٔاتِ لَهُمْ عَذَابٌ شَدِيدٌۖ وَمَكْرُ أُوْلَـٰٓئِكَ هُوَ يَبُورُ ﴿١٠﴾

وَٱللَّهُ خَلَقَكُم مِّن تُرَابٍ ثُمَّ مِن نُّطْفَةٍ ثُمَّ جَعَلَكُمْ أَزْوَٰجًاۚ وَمَا تَحْمِلُ مِنْ أُنثَىٰ وَلَا تَضَعُ إِلَّا بِعِلْمِهِۦۚ وَمَا يُعَمَّرُ مِن مُّعَمَّرٍ وَلَا يُنقَصُ مِنْ عُمُرِهِۦٓ إِلَّا فِى كِتَـٰبٍۚ إِنَّ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٌ ﴿١١﴾

وَمَا يَسْتَوِى ٱلْبَحْرَانِ هَـٰذَا عَذْبٌ فُرَاتٌ سَآئِغٌ شَرَابُهُۥ وَهَـٰذَا مِلْحٌ أُجَاجٌۖ وَمِن كُلٍّ تَأْكُلُونَ لَحْمًا طَرِيًّا وَتَسْتَخْرِجُونَ حِلْيَةً تَلْبَسُونَهَاۖ وَتَرَى ٱلْفُلْكَ فِيهِ مَوَاخِرَ لِتَبْتَغُواْ مِن فَضْلِهِۦ وَلَعَلَّكُمْ تَشْكُرُونَ ﴿١٢﴾

يُولِجُ ٱلَّيْلَ فِى ٱلنَّهَارِ وَيُولِجُ ٱلنَّهَارَ فِى ٱلَّيْلِ وَسَخَّرَ ٱلشَّمْسَ وَٱلْقَمَرَ كُلٌّ يَجْرِى لِأَجَلٍ مُّسَمًّىۚ ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبُّكُمْ لَهُ ٱلْمُلْكُۚ وَٱلَّذِينَ تَدْعُونَ مِن دُونِهِۦ مَا يَمْلِكُونَ مِن قِطْمِيرٍ

۝١٣

14. ብትጠሩዋቸው ጥሪያችሁን አይሰሙም፡፡ ቢሰሙም ኖሮ ለእናንተ አይመልሱላችሁም፡፡ በትንሣኤም ቀን (እነርሱን በአላህ) ማጋራታችሁን ይክዳሉ፡፡ እንደ ውስጠ ዐዋቂው ማንም አይነግርህም፡፡

إِن تَدۡعُوهُمۡ لَا يَسۡمَعُواْ دُعَآءَكُمۡ وَلَوۡ سَمِعُواْ مَا ٱسۡتَجَابُواْ لَكُمۡۖ وَيَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ يَكۡفُرُونَ بِشِرۡكِكُمۡۚ وَلَا يُنَبِّئُكَ مِثۡلُ خَبِيرٖ ۝١٤

15. እናንተ ሰዎች ሆይ! እናንተ (ሁል ጊዜ) ወደ አላህ ከጃዮች ናችሁ፡፡ አላህም እርሱ ተብቃቂው ምስጉኑ ነው፡፡

۞يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ أَنتُمُ ٱلۡفُقَرَآءُ إِلَى ٱللَّهِۖ وَٱللَّهُ هُوَ ٱلۡغَنِيُّ ٱلۡحَمِيدُ ۝١٥

16. ቢሻ ያስወግዳችኋል፡፡ አዲስንም ፍጡር ያመጣል፡፡

إِن يَشَأۡ يُذۡهِبۡكُمۡ وَيَأۡتِ بِخَلۡقٖ جَدِيدٖ ۝١٦

17. ይህም በአላህ ላይ ምንም አስቸጋሪ አይደለም፡፡

وَمَا ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ بِعَزِيزٖ ۝١٧

18. ኀጢአትን ተሸካሚም (ነፍስ) የሌላዋን ሸክም አትሸከምም፡፡ የተከበደችም (ነፍስ) ወደ ሸክሟ ብትጣራ (ተጠሪው) የቅርብ ዝምድና ባለቤት ቢኾንም እንኳ ከእርሷ አንዳችን የሚሸከምላት አታገኝም፡፡ የምታስጠነቅቀው እነዚያን ጌታቸውን በሩቅ የሚፈሩትን፣ ሶላትንም አስተካክለው ያደረሱትን ብቻ ነው፡፡ የተጥራራም ሰው የሚጥራራው ለራሱ ብቻ ነው፡፡ መመለሻም ወደ አላህ ብቻ ነው፡፡

وَلَا تَزِرُ وَازِرَةٞ وِزۡرَ أُخۡرَىٰۚ وَإِن تَدۡعُ مُثۡقَلَةٌ إِلَىٰ حِمۡلِهَا لَا يُحۡمَلۡ مِنۡهُ شَيۡءٞ وَلَوۡ كَانَ ذَا قُرۡبَىٰٓۗ إِنَّمَا تُنذِرُ ٱلَّذِينَ يَخۡشَوۡنَ رَبَّهُم بِٱلۡغَيۡبِ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَۚ وَمَن تَزَكَّىٰ فَإِنَّمَا يَتَزَكَّىٰ لِنَفۡسِهِۦۚ وَإِلَى ٱللَّهِ ٱلۡمَصِيرُ ۝١٨

19. ዕውሩና የሚያየውም አይስተካከሉም፡፡

وَمَا يَسۡتَوِي ٱلۡأَعۡمَىٰ وَٱلۡبَصِيرُ ۝١٩

20. ጨለማዎችና ብርሃንም፤ (እንደዚሁ)፡፡

وَلَا ٱلظُّلُمَٰتُ وَلَا ٱلنُّورُ ۝٢٠

21. ጥላና ሐሩርም፡፡

وَلَا ٱلظِّلُّ وَلَا ٱلۡحَرُورُ ۝٢١

22. ሕያዋንና ሙታንም አይስተካከሉም፡፡ አላህ የሚሻውን ሰው ያሰማል፡፡ አንተም በመቃብር ውስጥ ያሉትን አሰሚ አይደለህም፡፡

وَمَا يَسۡتَوِي ٱلۡأَحۡيَآءُ وَلَا ٱلۡأَمۡوَٰتُۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُسۡمِعُ مَن يَشَآءُۖ وَمَآ أَنتَ بِمُسۡمِعٖ مَّن فِي ٱلۡقُبُورِ ۝٢٢

23. አንተ አስጠንቃቂ እንጂ ሌላ አይደለህም፡፡

إِنۡ أَنتَ إِلَّا نَذِيرٌ ۝٢٣

24. እኛ አብሳሪና አስፈራሪ አድርገን በእውነቱ (መምሪያ) ላክንህ፡፡ ማንኛይቱም ሕዝብ በውስጧ አስፈራሪ ያላለፈባት የለችም፡፡

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَٰكَ بِٱلۡحَقِّ بَشِيرٗا وَنَذِيرٗاۚ وَإِن مِّنۡ أُمَّةٍ إِلَّا خَلَا فِيهَا نَذِيرٞ ۝٢٤

25. ቢያስተባብሉህም እነዚያ ከበፊታቸው የነበሩት በእርግጥ አስተባብለዋል፡፡ መልክተኞቻቸው በግልጽ ማስረጃዎችን፣ በጽሑፎችም፣ አብራሪ በኾነ መጽሐፍም መጥተዋቸዋል፡፡

وَإِن يُكَذِّبُوكَ فَقَدْ كَذَّبَ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ جَآءَتْهُمْ رُسُلُهُم بِٱلْبَيِّنَٰتِ وَبِٱلزُّبُرِ وَبِٱلْكِتَٰبِ ٱلْمُنِيرِ ﴿٢٥﴾

26. ከዚያም እነዚያን የካዱትን ያዝኳቸው፡፡ ቅጣቴም እንዴት ነበር! (በስፍራው ነው)፡፡

ثُمَّ أَخَذْتُ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ ۖ فَكَيْفَ كَانَ نَكِيرِ ﴿٢٦﴾

27. አላህ ከሰማይ ውሃን ማውረዱን አላየህምን? በእርሱም ዓይነቶቻቸው የተለያዩ ፍሬዎችን አወጣን፡፡ ከጋራዎችም መልኮቻቸው የተለያዩ ነጮች፣ ቀዮችም፣ በጣም ጥቁሮችም የኾኑ መንገዶች አልሉ፡፡

أَلَمْ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءً فَأَخْرَجْنَا بِهِۦ ثَمَرَٰتٍ مُّخْتَلِفًا أَلْوَٰنُهَا ۚ وَمِنَ ٱلْجِبَالِ جُدَدٌۢ بِيضٌ وَحُمْرٌ مُّخْتَلِفٌ أَلْوَٰنُهَا وَغَرَابِيبُ سُودٌ ﴿٢٧﴾

28. ከሰዎችም፣ ከተንቀሳቃሾችም፣ ከቤት እንስሳዎችም እንደዚሁ መልኮቻቸው የተለያዩ አልሉ፡፡ አላህን ከባሮቹ ውስጥ የሚፈሩት ዐዋቂዎቹ ብቻ ናቸው፡፡ አላህ አሸናፊ መሓሪ ነው፡፡

وَمِنَ ٱلنَّاسِ وَٱلدَّوَآبِّ وَٱلْأَنْعَٰمِ مُخْتَلِفٌ أَلْوَٰنُهُۥ كَذَٰلِكَ ۗ إِنَّمَا يَخْشَى ٱللَّهَ مِنْ عِبَادِهِ ٱلْعُلَمَٰٓؤُا۟ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ عَزِيزٌ غَفُورٌ ﴿٢٨﴾

29. እነዚያ የአላህን መጽሐፍ የሚያነቡ፣ ሶላትንም አስተካክለው ያደረሱ፣ ከሰጠናቸውም ሲሳይ በምስጢርም ኾነ በግልጽ የለገሱ፣ በፍጹም የማትከስርን ንግድ ተስፋ ያደርጋሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَتْلُونَ كِتَٰبَ ٱللَّهِ وَأَقَامُوا۟ ٱلصَّلَوٰةَ وَأَنفَقُوا۟ مِمَّا رَزَقْنَٰهُمْ سِرًّا وَعَلَانِيَةً يَرْجُونَ تِجَٰرَةً لَّن تَبُورَ ﴿٢٩﴾

30. ምንዳዎቻቸውን ሊሞላላቸው፣ ከችሮታውም ሊጨምርላቸው (ተስፋ ያደርጋሉ)፡፡ እርሱ በጣም መሓሪ አመስጋኝ ነውና፡፡

لِيُوَفِّيَهُمْ أُجُورَهُمْ وَيَزِيدَهُم مِّن فَضْلِهِۦٓ ۚ إِنَّهُۥ غَفُورٌ شَكُورٌ ﴿٣٠﴾

31. ያም ከመጽሐፉ ወዳንተ ያወረድንልህ ከበፊቱ ላለው አረጋጋጭ ሲኾን እርሱ እውነት ነው፡፡ አላህ በርግጥ በባሮቹ ውስጥ ዐዋቂ ተመልካች ነው፡፡

وَٱلَّذِىٓ أَوْحَيْنَآ إِلَيْكَ مِنَ ٱلْكِتَٰبِ هُوَ ٱلْحَقُّ مُصَدِّقًا لِّمَا بَيْنَ يَدَيْهِ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ بِعِبَادِهِۦ لَخَبِيرٌۢ بَصِيرٌ ﴿٣١﴾

32. ከዚያም እነዚያን ከባሮቻችን የመረጥናቸውን መጽሐፉን አወረስናቸው፡፡ ከእነርሱም ነፍሱን በዳይ አልለ፡፡ ከእነርሱም መካከለኛ አልለ፡፡ ከእነሱም በአላህ ፈቃድ በበጎ ሥራዎች ቀዳሚ አልለ፡፡ ያ (ማውረስ)፤ እርሱ ታላቅ ችሮታ ነው፡፡

ثُمَّ أَوْرَثْنَا ٱلْكِتَٰبَ ٱلَّذِينَ ٱصْطَفَيْنَا مِنْ عِبَادِنَا ۖ فَمِنْهُمْ ظَالِمٌ لِّنَفْسِهِۦ وَمِنْهُم مُّقْتَصِدٌ وَمِنْهُمْ سَابِقٌۢ بِٱلْخَيْرَٰتِ بِإِذْنِ ٱللَّهِ ۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلْفَضْلُ ٱلْكَبِيرُ ﴿٣٢﴾

33. የመኖሪያ ገነቶችን በውስጧ የወርቅ አንባሮችን፣ ሉልንም የሚሸለሙ ኾነው ይገቡባታል፡፡ በእርሷ ውስጥ አልባሳታቸውም ሐር ነው፡፡

جَنَّٰتُ عَدْنٍ يَدْخُلُونَهَا يُحَلَّوْنَ فِيهَا مِنْ أَسَاوِرَ مِن ذَهَبٍ وَلُؤْلُؤًا ۖ وَلِبَاسُهُمْ فِيهَا حَرِيرٌ ﴿٣٣﴾

34. ይላሉም «ምስጋና ለእዚያ ከእኛ ላይ ሐዘንን ላስወገደልን አላህ ይገባው፡፡ ጌታችን በጣም መሓሪ አመስጋኝ ነውና፡፡

وَقَالُوا۟ ٱلْحَمْدُ لِلَّهِ ٱلَّذِىٓ أَذْهَبَ عَنَّا ٱلْحَزَنَ ۖ إِنَّ رَبَّنَا لَغَفُورٌ شَكُورٌ ﴿٣٤﴾

35. (እርሱም) ያ ከችሮታው የዘላለም መኖሪያን አገር ያሰፈረን ነው፡፡ በእርሷ ውስጥ መከራ አይነካንም፡፡ በእርሷም ውስጥ ድካም አይነካንም፡፡»

ٱلَّذِىٓ أَحَلَّنَا دَارَ ٱلْمُقَامَةِ مِن فَضْلِهِۦ لَا يَمَسُّنَا فِيهَا نَصَبٌ وَلَا يَمَسُّنَا فِيهَا لُغُوبٌ ﴿٣٥﴾

36. እነዚያ የካዱትም ለእነርሱ የገሀነም እሳት አልላቸው፡፡ ይሞቱ ዘንድ በእነርሱ ላይ (በሞት) አይፈረድም፡፡ ከቅጣቷም ከእነርሱ አይቀለልላቸውም፡፡ እንደዚሁ ከሓዲን ሁሉ እንመነዳለን፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَهُمْ نَارُ جَهَنَّمَ لَا يُقْضَىٰ عَلَيْهِمْ فَيَمُوتُواْ وَلَا يُخَفَّفُ عَنْهُم مِّنْ عَذَابِهَاۚ كَذَٰلِكَ نَجْزِي كُلَّ كَفُورٖ ٣٦

37. እነርሱም በርሷ ውስጥ እርዳታን በመፈለግ በኀይል ይጮሃሉ፡፡ «ጌታችን ሆይ! ከእዚያ እንሠራው ከነበርነው ሌላ በጎ ሥራን እንሠራ ዘንድ አውጣን» (ይላሉ)፡፡ «በእርሱ ውስጥ ያስታወሰ ሰው የሚገሰጽበትን ዕድሜ አላቆየናችሁምን? አስጠንቃቂውም መጥቶላችኋል (አስተባብላችኋልም)፡፡ ስለዚህ ቅመሱ፡፡ ለበደለኞችም ምንም ረዳት የላቸውም» (ይባላሉ)፡፡

وَهُمْ يَصْطَرِخُونَ فِيهَا رَبَّنَآ أَخْرِجْنَا نَعْمَلْ صَٰلِحًا غَيْرَ ٱلَّذِي كُنَّا نَعْمَلُۚ أَوَلَمْ نُعَمِّرْكُم مَّا يَتَذَكَّرُ فِيهِ مَن تَذَكَّرَ وَجَآءَكُمُ ٱلنَّذِيرُۖ فَذُوقُواْ فَمَا لِلظَّٰلِمِينَ مِن نَّصِيرٍ ٣٧

38. አላህ የሰማያትንና የምድርን ምስጢር በእርግጥ ዐዋቂ ነው፡፡ እርሱ በልቦች ውስጥ ያለን ሁሉ ዐዋቂ ነውና፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ عَٰلِمُ غَيْبِ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِۚ إِنَّهُۥ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٣٨

39. እርሱ ያ በምድር ውስጥ ምትኮች ያደረጋችሁ ነው፡፡ የካደም ሰው ክህደቱ በእርሱው ላይ ብቻ ነው፡፡ ከሓዲዎችንም ክሕደታቸው ከጌታቸው ዘንድ መጠላትን እንጂ ሌላ አይጨምርላቸውም፡፡ ከሓዲዎችንም ክሕደታቸው ከሳራን እንጂ አይጨምርላቸውም፡፡

هُوَ ٱلَّذِي جَعَلَكُمْ خَلَٰٓئِفَ فِي ٱلْأَرْضِۚ فَمَن كَفَرَ فَعَلَيْهِ كُفْرُهُۥۖ وَلَا يَزِيدُ ٱلْكَٰفِرِينَ كُفْرُهُمْ عِندَ رَبِّهِمْ إِلَّا مَقْتٗاۖ وَلَا يَزِيدُ ٱلْكَٰفِرِينَ كُفْرُهُمْ إِلَّا خَسَارٗا ٣٩

40. በላቸው «እነዚያን ከአላህ ሌላ የምትግገዟቸውን ተጋሪዎቻችሁን አያችሁን? ከምድር ምንን እንደ ፈጠሩ አሳዩኝ፡፡ ወይስ ለእነርሱ በሰማያት ውስጥ ሽርክና አላቸውን? ወይስ መጽሐፍን ሰጠናቸውና እነርሱ ከርሱ በግልጽ አስረጅ ላይ ናቸውን? አይደለም በደለኞች ከፊላቸው ከፊሉን ማታለልን እንጂ አይቀጥሩም፡፡»

قُلْ أَرَءَيْتُمْ شُرَكَآءَكُمُ ٱلَّذِينَ تَدْعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَرُونِي مَاذَا خَلَقُواْ مِنَ ٱلْأَرْضِ أَمْ لَهُمْ شِرْكٞ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ أَمْ ءَاتَيْنَٰهُمْ كِتَٰبٗا فَهُمْ عَلَىٰ بَيِّنَتٖ مِّنْهُۚ بَلْ إِن يَعِدُ ٱلظَّٰلِمُونَ بَعْضُهُم بَعْضًا إِلَّا غُرُورًا ٤٠

41. አላህ ሰማያትንና ምድርን እንዳይወገዱ ይይዛቸዋል፡፡ ቢወገዱም ከእርሱ ሌላ አንድም የሚይዛቸው የለም፡፡ እነሆ እርሱ ታጋሽ መሐሪ ነውና፡፡

۞إِنَّ ٱللَّهَ يُمْسِكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ أَن تَزُولَاۚ وَلَئِن زَالَتَآ إِنْ أَمْسَكَهُمَا مِنْ أَحَدٖ مِّنۢ بَعْدِهِۦٓۚ إِنَّهُۥ كَانَ حَلِيمًا غَفُورٗا ٤١

42. አስፈራሪም ቢመጣላቸው ከሕዝቦቹ ሁሉ ከአንደኛዋ ይበልጥ የተመሩ ሊኾኑ የመሓላቸውን ድካ አድርሰው በአላህ ማሉ፡፡ አስፈራሪም በመጣላቸው ጊዜ መበርገግን እንጂ ሌላ አልጨመረላቸውም፡፡

وَأَقْسَمُواْ بِٱللَّهِ جَهْدَ أَيْمَٰنِهِمْ لَئِن جَآءَهُمْ نَذِيرٞ لَّيَكُونُنَّ أَهْدَىٰ مِنْ إِحْدَى ٱلْأُمَمِۖ فَلَمَّا جَآءَهُمْ نَذِيرٞ مَّا زَادَهُمْ إِلَّا نُفُورًا ٤٢

ٱسْتِكْبَارًا فِى ٱلْأَرْضِ وَمَكْرَ ٱلسَّيِّئِ ۚ وَلَا يَحِيقُ ٱلْمَكْرُ ٱلسَّيِّئُ إِلَّا بِأَهْلِهِۦ ۚ فَهَلْ يَنظُرُونَ إِلَّا سُنَّتَ ٱلْأَوَّلِينَ ۚ فَلَن تَجِدَ لِسُنَّتِ ٱللَّهِ تَبْدِيلًا ۖ وَلَن تَجِدَ لِسُنَّتِ ٱللَّهِ تَحْوِيلًا ﴿٤٣﴾

43. በምድር ላይ ኩራትንና በክፉ (ተንኮል) መዶለትንም (እንጂ አልጨመረላቸውም:: ክፉ ተንኮልም በባለቤቱ ላይ እንጂ በሌላ ላይ አይሰፍርም:: የቀድሞዎቹን ደንብ እንጂ ይጠባበቃሉን? ለአላህ ደንብም መልለወጥን አታገኝም:: ለአላህ ደንብም መዛወርን አታገኝም::

أَوَلَمْ يَسِيرُوا۟ فِى ٱلْأَرْضِ فَيَنظُرُوا۟ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ وَكَانُوٓا۟ أَشَدَّ مِنْهُمْ قُوَّةً ۚ وَمَا كَانَ ٱللَّهُ لِيُعْجِزَهُۥ مِن شَىْءٍ فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَلَا فِى ٱلْأَرْضِ ۚ إِنَّهُۥ كَانَ عَلِيمًا قَدِيرًا ﴿٤٤﴾

44. በምድር ላይ አይኼዱምና የእነዚያን ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ሰዎች መጨረሻ እንዴት እንደ ነበረ አይመለከቱምን? ከእነርሱም በኀይል የበረቱ ነበሩ:: አላህም በሰማያትም ኾነ በምድር ውስጥ ምንም ነገር የሚያቅተው አይደለም:: እርሱ ዐዋቂ ቻይ ነውና::

وَلَوْ يُؤَاخِذُ ٱللَّهُ ٱلنَّاسَ بِمَا كَسَبُوا۟ مَا تَرَكَ عَلَىٰ ظَهْرِهَا مِن دَآبَّةٍ وَلَٰكِن يُؤَخِّرُهُمْ إِلَىٰٓ أَجَلٍ مُّسَمًّى ۖ فَإِذَا جَآءَ أَجَلُهُمْ فَإِنَّ ٱللَّهَ كَانَ بِعِبَادِهِۦ بَصِيرًۢا ﴿٤٥﴾

45. አላህም ሰዎችን በሠሩት ኀጢአት ቢይዝ ኖሮ በወለሏ (በምድር) ላይ ምንም ተንቀሳቃሽ ባልተወ ነበር:: ግን እተወሰነ ጊዜ ድረስ ያቆያቸዋል:: ጊዜያቸውም በመጣ ወቅት (በኀጢአታቸው ይቀጣቸዋል):: አላህ በባሮቹ (ኹኔታ) ተመልካች ነውና::

# سورة يس

# ሱረቱ ያሲን

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

يسٓ ﴿١﴾

1. የ.ሰ.(ያ ሲን)

وَٱلْقُرْءَانِ ٱلْحَكِيمِ ﴿٢﴾

2. ጥበብ በተመላበት ቁርአን እምላለሁ::

إِنَّكَ لَمِنَ ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿٣﴾

3. አንተ በእርግጥ ከመልክተኞቹ ነህ::

عَلَىٰ صِرَٰطٍ مُّسْتَقِيمٍ ﴿٤﴾

4. በቀጥታም መንገድ ላይ ነህ::

تَنزِيلَ ٱلْعَزِيزِ ٱلرَّحِيمِ ﴿٥﴾

5. አሸናፊ አዛኝ ከሆነው አምላክ መወረድን ተወረደ::

لِتُنذِرَ قَوْمًا مَّآ أُنذِرَ ءَابَآؤُهُمْ فَهُمْ غَٰفِلُونَ ﴿٦﴾

6. አባቶቻቸው ያልተስፈራሩትን ሕዝቦች ልታስጠነቅቅበት (ተወረደ):: እነርሱ ዘንጊዎች ናቸውና::

لَقَدۡ حَقَّ ٱلۡقَوۡلُ عَلَىٰٓ أَكۡثَرِهِمۡ فَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ٧

7. በአብዛኞቻቸው ላይ ቃሉ በእውነት ተረጋገጠ፡፡ ስለዚህ እነርሱ አያምኑም፡፡

إِنَّا جَعَلۡنَا فِيٓ أَعۡنَٰقِهِمۡ أَغۡلَٰلٗا فَهِيَ إِلَى ٱلۡأَذۡقَانِ فَهُم مُّقۡمَحُونَ ٨

8. እኛ በአንገቶቻቸው ላይ እንዛዝላዎችን አደረግን፡፡ እርሷም (እንዛዝላይቱ) ወደ አገጮቻቸው ደራሽ ናት፡፡ እነርሱም ራሶቻቸውን ያንጋጠጡ ናቸው፡፡

وَجَعَلۡنَا مِنۢ بَيۡنِ أَيۡدِيهِمۡ سَدّٗا وَمِنۡ خَلۡفِهِمۡ سَدّٗا فَأَغۡشَيۡنَٰهُمۡ فَهُمۡ لَا يُبۡصِرُونَ ٩

9. ከስተፊታቸውም ግርዶን ከስተኋላቸውም ግርዶን አደረግን፡፡ ሸፈንናቸውም፡፡ ስለዚህ እነሱ አያዩም፡፡

وَسَوَآءٌ عَلَيۡهِمۡ ءَأَنذَرۡتَهُمۡ أَمۡ لَمۡ تُنذِرۡهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ١٠

10. ብታስጠነቅቃቸውም ባታስጠነቅቃቸውም በእነርሱ ላይ እኩል ነው፡፡ አያምኑም፡፡

إِنَّمَا تُنذِرُ مَنِ ٱتَّبَعَ ٱلذِّكۡرَ وَخَشِيَ ٱلرَّحۡمَٰنَ بِٱلۡغَيۡبِۖ فَبَشِّرۡهُ بِمَغۡفِرَةٖ وَأَجۡرٖ كَرِيمٍ ١١

11. የምታስጠነቅቀው ግሳጼን የተከተለንና አልረሕማንን በሩቅ የፈራን ሰው ብቻ ነው፡፡ በምሕረትና በመልካም ምንዳም አብስረው፡፡

إِنَّا نَحۡنُ نُحۡيِ ٱلۡمَوۡتَىٰ وَنَكۡتُبُ مَا قَدَّمُواْ وَءَاثَٰرَهُمۡۚ وَكُلَّ شَيۡءٍ أَحۡصَيۡنَٰهُ فِيٓ إِمَامٖ مُّبِينٖ ١٢

12. እኛ ሙታንን እኛ በእርግጥ ሕያው እናደርጋለን፡፡ ያስቀደሙትንም ሥራ ፈለጎቻቸውንም እንጽፋለን፡፡ ነገሩንም ሁሉ ገላጭ መሪ በኾነ መጽሐፍ ውስጥ አጠቃለልነው፡፡

وَٱضۡرِبۡ لَهُم مَّثَلًا أَصۡحَٰبَ ٱلۡقَرۡيَةِ إِذۡ جَآءَهَا ٱلۡمُرۡسَلُونَ ١٣

13. ለእነርሱም የከተማይቱን (የአንጾኪያን) ሰዎች ምሳሌ መልክተኞቹ በመጧት ጊዜ (የኾነውን) ግለጽላቸው፡፡

إِذۡ أَرۡسَلۡنَآ إِلَيۡهِمُ ٱثۡنَيۡنِ فَكَذَّبُوهُمَا فَعَزَّزۡنَا بِثَالِثٖ فَقَالُوٓاْ إِنَّآ إِلَيۡكُم مُّرۡسَلُونَ ١٤

14. ወደእነርሱ ሁለትን ሰዎች በላክንና ባስተባበሉዋቸው ጊዜ በሶስተኛም በአበረታንና እኛ ወደ እናንተ መልክተኞች ነን ባሏቸው ጊዜ (የኾነውን ምሳሌ ግለጽላቸው)፡፡

قَالُواْ مَآ أَنتُمۡ إِلَّا بَشَرٞ مِّثۡلُنَا وَمَآ أَنزَلَ ٱلرَّحۡمَٰنُ مِن شَيۡءٍ إِنۡ أَنتُمۡ إِلَّا تَكۡذِبُونَ ١٥

15. እናንተ መሰላችን ሰዎች እንጂ ሌላ አይደላችሁም፡፡ አልረሕማንም ምንም ነገር አላወረደም፡፡ እናንተ የምትዋሹ እንጂ ሌላ አይደላችሁም አሉዋቸው፡፡

قَالُواْ رَبُّنَا يَعۡلَمُ إِنَّآ إِلَيۡكُمۡ لَمُرۡسَلُونَ ١٦

16. (መልክተኞቹም) አሉ «ጌታችን ያውቃል፡፡ እኛ ወደእናንተ በእርግጥ መልክተኞች ነን፡፡

وَمَا عَلَيۡنَآ إِلَّا ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ١٧

17. «በእኛ ላይም ግልጽ የኾነ ማድረስ እንጂ ሌላ የለብንም፡፡»

قَالُوٓاْ إِنَّا تَطَيَّرۡنَا بِكُمۡۖ لَئِن لَّمۡ تَنتَهُواْ لَنَرۡجُمَنَّكُمۡ وَلَيَمَسَّنَّكُم مِّنَّا عَذَابٌ أَلِيمٞ ١٨

18. (ሕዝቦቹም) «እኛ በእናንተ ገደ ቢሶች ኾን፡፡ ባትከለከሉ በእርግጥ እንወግራችኋለን፡፡ ከእኛም አሳማሚ ቅጣት በእርግጥ ያገኛችኋል» አሉ፡፡

19. «ገደ ቢስነታችሁ ከእናንተው ጋር ነው፡፡ ብትገሰጹ (ትዝታላችሁን?) በእውነቱ እናንተ ወሰን አላፊዎች ሕዝቦች ናችሁ» አሏቸው፡፡

قَالُواْ طَٰٓئِرُكُم مَّعَكُمۡۚ أَئِن ذُكِّرۡتُمۚ بَلۡ أَنتُمۡ قَوۡمٞ مُّسۡرِفُونَ ١٩

20. ከከተማይቱም ሩቅ ዳርቻ የሚሮጥ ሰው መጣ፡፡ «ወገኖቼ ሆይ! መልክተኞቹን ተከተሉ» አለ፡፡

وَجَآءَ مِنۡ أَقۡصَا ٱلۡمَدِينَةِ رَجُلٞ يَسۡعَىٰ قَالَ يَٰقَوۡمِ ٱتَّبِعُواْ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ٢٠

21. «እነርሱ ቅኑን መንገድ የተመሩ ሲኾኑ ዋጋን የማየጠይቁዋችሁን ሰዎች ተከተሉ» (አላቸው)፡፡

ٱتَّبِعُواْ مَن لَّا يَسۡـَٔلُكُمۡ أَجۡرٗا وَهُم مُّهۡتَدُونَ ٢١

22. «ያንንም የፈጠረኝን፤ ወደርሱም የምትመለሱበትን (ጌታ) የማልገዛ ለእኔ ምን አለኝ?» (አለ)፡፡

وَمَا لِيَ لَآ أَعۡبُدُ ٱلَّذِي فَطَرَنِي وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٢٢

23. «ከእርሱ ሌላ አማልክትን እይዛለሁን? አልረህማን በጉዳት ቢሻኝ ምልጃቸው ከእኔ (ለመመለስ) ምንም አትጠቅመኝም፤ አያድኑኝምም፡፡

ءَأَتَّخِذُ مِن دُونِهِۦٓ ءَالِهَةً إِن يُرِدۡنِ ٱلرَّحۡمَٰنُ بِضُرّٖ لَّا تُغۡنِ عَنِّي شَفَٰعَتُهُمۡ شَيۡـٔٗا وَلَا يُنقِذُونِ ٢٣

24. «እኔ ያን ጊዜ በግልጽ ስህተት ውስጥ ነኝ፡፡

إِنِّيٓ إِذٗا لَّفِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ٢٤

25. «እኔ በጌታችሁ አመንኩ፤ ስሙኝም፤» (አለ)፡፡

إِنِّيٓ ءَامَنتُ بِرَبِّكُمۡ فَٱسۡمَعُونِ ٢٥

26. «ገነትን ግባ» ተባለ፡፡ (እርሱም) አለ፡- «ወገኖቼ ቢያውቁ እመኛለሁ፡፡

قِيلَ ٱدۡخُلِ ٱلۡجَنَّةَۖ قَالَ يَٰلَيۡتَ قَوۡمِي يَعۡلَمُونَ ٢٦

27. «ጌታዬ ለእኔ ምሕረት ያደረገልኝና ከተከበሩትም ያደረገኝ መኾኑን፡፡»

بِمَا غَفَرَ لِي رَبِّي وَجَعَلَنِي مِنَ ٱلۡمُكۡرَمِينَ ٢٧

28. ከእርሱም በኋላ በሕዝቦቹ ላይ (ልናጠፋቸው) ሰራዊትን ከሰማይ አላወረድንም፡፡ (በማንም ላይ) አወራጆችም አልነበርንም፡፡

۞وَمَآ أَنزَلۡنَا عَلَىٰ قَوۡمِهِۦ مِنۢ بَعۡدِهِۦ مِن جُندٖ مِّنَ ٱلسَّمَآءِ وَمَا كُنَّا مُنزِلِينَ ٢٨

29. (ቅጣታቸው) አንዲት ጩኸት እንጂ ሌላ አልነበረችም፡፡ ወዲያውኑም እነርሱ ጠፊዎች ኾኑ፡፡

إِن كَانَتۡ إِلَّا صَيۡحَةٗ وَٰحِدَةٗ فَإِذَا هُمۡ خَٰمِدُونَ ٢٩

30. በባሮቹ ላይ ዋ ቁልጭት! ከመልክተኛ አንድም አይመጣቸውም በእርሱ የሚሳለቁበት ቢኾኑ እንጅ፡፡

يَٰحَسۡرَةً عَلَى ٱلۡعِبَادِۚ مَا يَأۡتِيهِم مِّن رَّسُولٍ إِلَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ٣٠

31. ከእነርሱ በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙዎችን ማጥፋታችንንና እነርሱ ወደነርሱ የማይመለሱ መኾናቸውን አላወቁምን?

أَلَمۡ يَرَوۡاْ كَمۡ أَهۡلَكۡنَا قَبۡلَهُم مِّنَ ٱلۡقُرُونِ أَنَّهُمۡ إِلَيۡهِمۡ لَا يَرۡجِعُونَ ٣١

32. ሁሉም እኛ ዘንድ የሚሰበሰቡ የሚቀረቡ እንጂ ሌላ አይደሉም፡፡

وَإِن كُلّٞ لَّمَّا جَمِيعٞ لَّدَيۡنَا مُحۡضَرُونَ ٣٢

33. የሞተችውም ምድር ለእነርሱ ምልክት ናት! ሕያው አደረግናት፡፡ ከእርሷም ፍሬን አወጣን፤ ከርሱም ይበላሉ፡፡

وَءَايَةٞ لَّهُمُ ٱلۡأَرۡضُ ٱلۡمَيۡتَةُ أَحۡيَيۡنَٰهَا وَأَخۡرَجۡنَا مِنۡهَا حَبّٗا فَمِنۡهُ يَأۡكُلُونَ ٣٣

34. በእርሷም ውሰጥ ከዘምበባዎችና ከወይኖች የኾኑ አትክልቶችን አደረግን፡፡ በእርሷም ውስጥ ምንጮችን አፈለቅን፡፡

وَجَعَلۡنَا فِيهَا جَنَّٰتٖ مِّن نَّخِيلٖ وَأَعۡنَٰبٖ وَفَجَّرۡنَا فِيهَا مِنَ ٱلۡعُيُونِ ٣٤

35. ከፍሬውና እጆቻቸው ከሠሩትም ይበሉ ዘንድ (ይህን አደረግን)፤ አያመሰግኑምን?

لِيَأۡكُلُواْ مِن ثَمَرِهِۦ وَمَا عَمِلَتۡهُ أَيۡدِيهِمۡۚ أَفَلَا يَشۡكُرُونَ ٣٥

36. ያ ምድር ከምታበቅለው ከነፍሶቻቸውም ከማያውቁትም ነገር ዓይነቶችን ሁሏንም የፈጠረ (አምላክ) ጥራት ይገባው፡፡

سُبۡحَٰنَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلۡأَزۡوَٰجَ كُلَّهَا مِمَّا تُنۢبِتُ ٱلۡأَرۡضُ وَمِنۡ أَنفُسِهِمۡ وَمِمَّا لَا يَعۡلَمُونَ ٣٦

37. ሌሊቱም ለእነርሱ ምልክት ነው፡፡ ከእርሱ ላይ ቀንን እንገፍፋለን፡፡ ወዲያውኑም እነርሱ በጨለማ ውስጥ ይገባሉ፡፡

وَءَايَةٞ لَّهُمُ ٱلَّيۡلُ نَسۡلَخُ مِنۡهُ ٱلنَّهَارَ فَإِذَا هُم مُّظۡلِمُونَ ٣٧

38. ፀሐይም ለእርሷ ወደ ሆነው መርጊያ ትሮጣለች፡፡ ይህ የአሸናፊው የዐዋቂው አምላክ ውሳኔ ነው፡፡

وَٱلشَّمۡسُ تَجۡرِي لِمُسۡتَقَرّٖ لَّهَاۚ ذَٰلِكَ تَقۡدِيرُ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡعَلِيمِ ٣٨

39. ጨረቃንም የመስፈሪያዎች ባለቤት ሲኾን እንደ ዘንባባ አሮጌ ቀንዘል እስኪኾን ድረስ (መኼዱን) ለካነው፡፡

وَٱلۡقَمَرَ قَدَّرۡنَٰهُ مَنَازِلَ حَتَّىٰ عَادَ كَٱلۡعُرۡجُونِ ٱلۡقَدِيمِ ٣٩

40. ፀሐይ ጨረቃን ልትደርስበት አይገባትም፡፡ ሌሊትም ቀንን (ያለ ጊዜው) ቀዳሚ አይኾንም፡፡ ሁሉም በመዞሪያቸው ውስጥ ይዋኛሉ፡፡

لَا ٱلشَّمۡسُ يَنۢبَغِي لَهَآ أَن تُدۡرِكَ ٱلۡقَمَرَ وَلَا ٱلَّيۡلُ سَابِقُ ٱلنَّهَارِۚ وَكُلّٞ فِي فَلَكٖ يَسۡبَحُونَ ٤٠

41. እኛም (የቀድሞ) ትውልዳቸውን በተሞላች መርከብ ውስጥ የጫን መኾናችን ለእነርሱ ምልክት ነው፡፡

وَءَايَةٞ لَّهُمۡ أَنَّا حَمَلۡنَا ذُرِّيَّتَهُمۡ فِي ٱلۡفُلۡكِ ٱلۡمَشۡحُونِ ٤١

42. ከመሰሉም በእርሱ የሚሳፈሩበትን ለእነርሱ ፈጠርንላቸው፡፡

وَخَلَقۡنَا لَهُم مِّن مِّثۡلِهِۦ مَا يَرۡكَبُونَ ٤٢

43. ብንሻም እናሰጥማቸዋለን፡፡ ለእነርሱም ረዳት የላቸውም፡፡ እነርሱም የሚድዳኑ አይደሉም፡፡

وَإِن نَّشَأۡ نُغۡرِقۡهُمۡ فَلَا صَرِيخَ لَهُمۡ وَلَا هُمۡ يُنقَذُونَ ٤٣

44. ግን ከእኛ ለኾነው ችሮታና እስከ ጊዜ ሞታቸው ለማጣቀም (አዳንናቸው)፡፡

إِلَّا رَحۡمَةٗ مِّنَّا وَمَتَٰعًا إِلَىٰ حِينٖ ٤٤

45. ለእነርሱም «በስተፊታችሁና በኋላችሁ ያለውን ነገር ተጠንቀቁ ይታዘንላችኋልና» በተባሉ ጊዜ (ፊታቸውን ያዞራሉ)፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمُ ٱتَّقُواْ مَا بَيۡنَ أَيۡدِيكُمۡ وَمَا خَلۡفَكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تُرۡحَمُونَ ٤٥

46. ከጌታቸውም ተዓምራት ማንኛይቱም ተዓምር አትመጣላቸውም፤ ከእርሷ የሚሸሹ ቢኾኑ እንጅ፡፡

وَمَا تَأۡتِيهِم مِّنۡ ءَايَةٖ مِّنۡ ءَايَٰتِ رَبِّهِمۡ إِلَّا كَانُواْ عَنۡهَا مُعۡرِضِينَ ٤٦

47. ለእነርሱም «አላህ ከሰጣችሁ ሲሳይ ለግሱ» በተባሉ ጊዜ እነዚያ የካዱት ለእነዚያ ላመኑት «አላህ ቢሻ ኖሮ የሚያበላውን ሰው እናበላለን? እናንተ በግልጽ ስህተት ውስጥ እንጂ በሌላ ላይ አይደላችሁም» ይላሉ፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمۡ أَنفِقُواْ مِمَّا رَزَقَكُمُ ٱللَّهُ قَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لِلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَنُطۡعِمُ مَن لَّوۡ يَشَآءُ ٱللَّهُ أَطۡعَمَهُۥٓ إِنۡ أَنتُمۡ إِلَّا فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ٤٧

48. «እውነተኞችም እንደኾናችሁ ይህ ቀጠሮ መቼ ነው?» ይላሉ፡፡

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلۡوَعۡدُ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٤٨

49. እነርሱ የሚከራከሩ ሲኾኑ በድንገት የምትይዛቸው የኾነችን አንዲትን ጩኸት እንጂ ሌላን አይጠባበቁም፡፡

مَا يَنظُرُونَ إِلَّا صَيۡحَةٗ وَٰحِدَةٗ تَأۡخُذُهُمۡ وَهُمۡ يَخِصِّمُونَ ٤٩

50. (ያን ጊዜ) መናዘዝንም አይችሉም፡፡ ወደ ቤተሰቦቻቸውም አይመለሱም፡፡

فَلَا يَسۡتَطِيعُونَ تَوۡصِيَةٗ وَلَآ إِلَىٰٓ أَهۡلِهِمۡ يَرۡجِعُونَ ٥٠

51. በቀንዱም ይነፋል፡፡ ወዲያውኑም እነርሱ ከመቃብሮቻቸው ወደ ጌታቸው በፍጥነት ይገሰግሳሉ፡፡

وَنُفِخَ فِي ٱلصُّورِ فَإِذَا هُم مِّنَ ٱلۡأَجۡدَاثِ إِلَىٰ رَبِّهِمۡ يَنسِلُونَ ٥١

52. «ወይ ጥፋታችን! ከመኝታችን ማን ቀሰቀሰን? ይህ ያ አዛኙ ጌታ (በእርሱ) የቀጠረን መልክተኞቹም እውነትን የነገሩን ነው» ይላሉ፡፡

قَالُواْ يَٰوَيۡلَنَا مَنۢ بَعَثَنَا مِن مَّرۡقَدِنَاۜۗ هَٰذَا مَا وَعَدَ ٱلرَّحۡمَٰنُ وَصَدَقَ ٱلۡمُرۡسَلُونَ ٥٢

53. (እርሷ) አንዲት ጩኸት እንጂ አይደለችም፡፡ ወዲያውኑም እነርሱ እኛ ዘንድ የሚሰበሰቡ የሚቀርቡ ናቸው፡፡

إِن كَانَتۡ إِلَّا صَيۡحَةٗ وَٰحِدَةٗ فَإِذَا هُمۡ جَمِيعٞ لَّدَيۡنَا مُحۡضَرُونَ ٥٣

54. «ዛሬም ማንኛይቱም ነፍስ ምንም አትበደልም፡፡ ትሠሩትም የነበራችሁትን እንጂ ሌላን አትመነዱም» (ይባላሉ)፡፡

فَٱلۡيَوۡمَ لَا تُظۡلَمُ نَفۡسٞ شَيۡـٔٗا وَلَا تُجۡزَوۡنَ إِلَّا مَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٥٤

55. የገነት ሰዎች ዛሬ በእርግጥ በሥራዎች ውስጥ ተደሳቾች ናቸው፡፡

إِنَّ أَصۡحَٰبَ ٱلۡجَنَّةِ ٱلۡيَوۡمَ فِي شُغُلٖ فَٰكِهُونَ ٥٥

56. እነርሱም ሚስቶቻቸውም በጥላዎች ውስጥ ናቸው፡፡ ባለ አጎበር አልጋዎች ላይ ተደጋፊዎች ናቸው፡፡

هُمۡ وَأَزۡوَٰجُهُمۡ فِي ظِلَٰلٍ عَلَى ٱلۡأَرَآئِكِ مُتَّكِـُٔونَ ٥٦

57. በውስጧ ለእነርሱ ፍራፍሬዎች አሏቸው፡፡ ለእነርሱም የሚፈልጉት ሁሉ አልላቸው፡፡

لَهُمۡ فِيهَا فَٰكِهَةٞ وَلَهُم مَّا يَدَّعُونَ ٥٧

58. (ለእነርሱም) አዛኝ ከሆነው ጌታ በቃል ሰላምታ አላቸው።

سَلَٰمٞ قَوۡلٗا مِّن رَّبّٖ رَّحِيمٖ ٥٨

59. (ይላልም) «እናንተ አመጸኞች ሆይ! ዛሬ (ከምእምናን) ተለዩ፡፡»

وَٱمۡتَٰزُواْ ٱلۡيَوۡمَ أَيُّهَا ٱلۡمُجۡرِمُونَ ٥٩

60. የአደም ልጆች ሆይ! ሰይጣንን አትገዙ፤ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና በማለት ወደእናንተ አላዘዝኩምን?

۞أَلَمۡ أَعۡهَدۡ إِلَيۡكُمۡ يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ أَن لَّا تَعۡبُدُواْ ٱلشَّيۡطَٰنَۖ إِنَّهُۥ لَكُمۡ عَدُوّٞ مُّبِينٞ ٦٠

61. ተገዙኝም፤ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው፤ (በማለትም)፡፡

وَأَنِ ٱعۡبُدُونِيۚ هَٰذَا صِرَٰطٞ مُّسۡتَقِيمٞ ٦١

62. ከእናንተም ብዙን ፍጡር በእርግጥ አሳስቷል፡፡ የምታውቁም አልነበራችሁምን?

وَلَقَدۡ أَضَلَّ مِنكُمۡ جِبِلّٗا كَثِيرًاۖ أَفَلَمۡ تَكُونُواْ تَعۡقِلُونَ ٦٢

63. ይህቺ ያቺ ትቀጠሩዋት የነበረችው ገሀነም ናት፡፡

هَٰذِهِۦ جَهَنَّمُ ٱلَّتِي كُنتُمۡ تُوعَدُونَ ٦٣

64. ትክዱ በነበራችሁት ምክንያት ዛሬ ግቧት (ይባላሉ)፡፡

ٱصۡلَوۡهَا ٱلۡيَوۡمَ بِمَا كُنتُمۡ تَكۡفُرُونَ ٦٤

65. ዛሬ በአፎቻቸው ላይ እናትምና እጆቻቸው ያነጋግሩናል፡፡ እግሮቻቸውም ይሠሩት በነበሩት ሁሉ ይመሰክራሉ፡፡

ٱلۡيَوۡمَ نَخۡتِمُ عَلَىٰٓ أَفۡوَٰهِهِمۡ وَتُكَلِّمُنَآ أَيۡدِيهِمۡ وَتَشۡهَدُ أَرۡجُلُهُم بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ٦٥

66. ብንሻም ኖሮ በዐይኖቻቸው ላይ በአበስን ነበር፡፡ መንገድንም (እንደ ልመዳቸው) በተሽቀዳደሙ ነበር፡፡ እንዴትም ያያሉ?

وَلَوۡ نَشَآءُ لَطَمَسۡنَا عَلَىٰٓ أَعۡيُنِهِمۡ فَٱسۡتَبَقُواْ ٱلصِّرَٰطَ فَأَنَّىٰ يُبۡصِرُونَ ٦٦

67. ብንሻም ኖሮ በስፍራቸው ላይ እንዳሉ ወደ ሌላ ፍጥረት በለወጥናቸው ነበር፡፡ መኼድንም መመለስንም ባልቻሉም ነበር፡፡

وَلَوۡ نَشَآءُ لَمَسَخۡنَٰهُمۡ عَلَىٰ مَكَانَتِهِمۡ فَمَا ٱسۡتَطَٰعُواْ مُضِيّٗا وَلَا يَرۡجِعُونَ ٦٧

68. ዕድሜውንም የምናረዝመውን ሰው በፍጥረቱ (ወደ ደካማነት) እንመልሰዋለን፤ አያውቁምን?

وَمَن نُّعَمِّرۡهُ نُنَكِّسۡهُ فِي ٱلۡخَلۡقِۚ أَفَلَا يَعۡقِلُونَ ٦٨

69. (ሙሐመድን) ቅኔንም አላስተማርነውም፡፡ ለእርሱም አይገባውም፡፡ እርሱ (መጽሐፉ) መገሰጫና ገላጭ ቁርኣን እንጅ (ቅኔ) አይደለም፡፡

وَمَا عَلَّمۡنَٰهُ ٱلشِّعۡرَ وَمَا يَنۢبَغِي لَهُۥٓۚ إِنۡ هُوَ إِلَّا ذِكۡرٞ وَقُرۡءَانٞ مُّبِينٞ ٦٩

70. (ግሣጼነቱም ልቡ) ሕያው የኾነን ሰው ሊያስፈራራበትና ቃሉም በከሓዲዎች ላይ ይፈጸም ዘንድ ነው፡፡

لِّيُنذِرَ مَن كَانَ حَيّٗا وَيَحِقَّ ٱلۡقَوۡلُ عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ ٧٠

71. እኛ እጆቻችን (ኃይሎቻችን) ከሠሩት ለእነርሱ እንስሳዎችን መፍጠራችንን አያውቁምን? እነርሱም ለእርሷ ባለ ሙብቶች ናቸው፡፡

أَوَ لَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّا خَلَقۡنَا لَهُم مِّمَّا عَمِلَتۡ أَيۡدِينَآ أَنۡعَٰمٗا فَهُمۡ لَهَا مَٰلِكُونَ ٧١

72. ለእነርሱም ገራናት፡፡ ስለዚህ ከእርሷ ውስጥ የሚጋልቡት አልለ፡፡ ከእርሷም ይበላሉ፡፡

وَذَلَّلۡنَٰهَا لَهُمۡ فَمِنۡهَا رَكُوبُهُمۡ وَمِنۡهَا يَأۡكُلُونَ ٧٢

73. ለእነርሱም በእርሷ ውስጥ (ሌሎች) ጥቅሞች መጠጦችም አሉዋቸው፡፡ ታዲያ አያመሰግኑምን;

وَلَهُمۡ فِيهَا مَنَٰفِعُ وَمَشَارِبُۚ أَفَلَا يَشۡكُرُونَ ٧٣

74. መረዳትንም በመከጀል ከአላህ ሌላ አማልክትን ያዙ፡፡

وَٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ ءَالِهَةٗ لَّعَلَّهُمۡ يُنصَرُونَ ٧٤

75. መርዳታቸውን አይችሉም፡፡ እነርሱም ለእርሳቸው (ወደ እሳት) የተቀረቡ ሰራዊት ናቸው፡፡

لَا يَسۡتَطِيعُونَ نَصۡرَهُمۡ وَهُمۡ لَهُمۡ جُندٞ مُّحۡضَرُونَ ٧٥

76. ንግግራቸውም አያሳዝንህ፡፡ እኛ የሚደብቁትንም የሚገልጹትንም እናውቃለንና፡፡

فَلَا يَحۡزُنكَ قَوۡلُهُمۡۘ إِنَّا نَعۡلَمُ مَا يُسِرُّونَ وَمَا يُعۡلِنُونَ ٧٦

77. ሰውየው እኛ ከፍቶት ጠብታ የፈጠርነው መኾናችንን አላወቀምን? ወዲያውም እርሱ (ትንሣኤን በመካድ) ግልጽ ተከራካሪ ይኾናልን?

أَوَ لَمۡ يَرَ ٱلۡإِنسَٰنُ أَنَّا خَلَقۡنَٰهُ مِن نُّطۡفَةٖ فَإِذَا هُوَ خَصِيمٞ مُّبِينٞ ٧٧

78. ለእኛም ምሳሌን አደረገልን፡፡ መፈጠሩንም ረሳ፡፡ «አጥንቶችን እነርሱ የበሰበሱ ሲኾኑ ሕያው የሚያደርጋቸው ማነው?» አለ፡፡

وَضَرَبَ لَنَا مَثَلٗا وَنَسِيَ خَلۡقَهُۥۖ قَالَ مَن يُحۡيِ ٱلۡعِظَٰمَ وَهِيَ رَمِيمٞ ٧٨

79. «ያ በመጀመሪያ ጊዜ (ከኢምንት) ያስገኛት ሕያው ያደርጋታል፡፡ እርሱም በፍጡሩ ሁሉ (ኹኔታ) ዐዋቂ ነው» በለው፡፡

قُلْ يُحْيِيهَا ٱلَّذِىٓ أَنشَأَهَآ أَوَّلَ مَرَّةٍ ۖ وَهُوَ بِكُلِّ خَلْقٍ عَلِيمٌ ﴿٧٩﴾

80. ያ ለእናንተ በእርጥብ ዛፍ እሳትን ያደረገላችሁ ነው፡፡ ወዲያውኑም እናንተ ከእርሱ ታቀጣጥላላችሁ፡፡

ٱلَّذِى جَعَلَ لَكُم مِّنَ ٱلشَّجَرِ ٱلْأَخْضَرِ نَارًا فَإِذَآ أَنتُم مِّنْهُ تُوقِدُونَ ﴿٨٠﴾

81. ያ ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ ብጤያቸውን በመፍጠር ላይ ቻይ አይደለምን? ነው እንጅ፡፡ እርሱም በብዙ ፈጣሪው ዐዋቂው ነው፡፡

أَوَلَيْسَ ٱلَّذِى خَلَقَ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ بِقَـٰدِرٍ عَلَىٰٓ أَن يَخْلُقَ مِثْلَهُم ۚ بَلَىٰ وَهُوَ ٱلْخَلَّـٰقُ ٱلْعَلِيمُ ﴿٨١﴾

82. ነገሩም አንዳችን በሻ ጊዜ ኹን ማለት ነው፡፡ ወዲያው ይኾናልም፡፡

إِنَّمَآ أَمْرُهُۥٓ إِذَآ أَرَادَ شَيْـًٔا أَن يَقُولَ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ﴿٨٢﴾

83. ያ የነገሩ ሁሉ ስልጣን በእጁ የኾነው ጌታ ጥራት ይገባው፡፡ ወደእርሱም ትመለሳላችሁ፡፡

فَسُبْحَـٰنَ ٱلَّذِى بِيَدِهِۦ مَلَكُوتُ كُلِّ شَىْءٍ وَإِلَيْهِ تُرْجَعُونَ ﴿٨٣﴾

## ሱረቱ አል ሷፋት

## سورة الصّافات

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَـٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. መሰለፍን በሚሰለፉት፡፡

وَٱلصَّـٰٓفَّـٰتِ صَفًّا ﴿١﴾

2. መገሠጽንም በሚገሥጹት፤

فَٱلزَّٰجِرَٰتِ زَجْرًا ﴿٢﴾

3. ቁርኣንንም በሚያነቡት እምላለሁ፡፡

فَٱلتَّـٰلِيَـٰتِ ذِكْرًا ﴿٣﴾

4. አምላካችሁ በእርግጥ አንድ ነው፡፡

إِنَّ إِلَـٰهَكُمْ لَوَٰحِدٌ ﴿٤﴾

5. የሰማያትና የምድር በመካከላቸው ያለውም ፍጡር ሁሉ ጌታ ነው፡፡ የምሥራቆችም ጌታ ነው፡፡

رَّبُّ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ وَمَا بَيْنَهُمَا وَرَبُّ ٱلْمَشَـٰرِقِ ﴿٥﴾

6. እኛ ቅርቢቱን ሰማይ በከዋክብት ጌጥ አጌጥናት፡፡

إِنَّا زَيَّنَّا ٱلسَّمَآءَ ٱلدُّنْيَا بِزِينَةٍ ٱلْكَوَاكِبِ ﴿٦﴾

7. አመጸኛም ከሆነ ሰይጣን ሁሉ መጠበቅን ጠበቅናት፡፡

وَحِفْظًا مِّن كُلِّ شَيْطَـٰنٍ مَّارِدٍ ﴿٧﴾

8. ወደላይኛው ሰራዊት አያዳምጡም:: ከየወገኑም ሁሉ ችቦ ይጣልባቸዋል::

لَّا يَسَّمَّعُونَ إِلَى ٱلْمَلَإِ ٱلْأَعْلَىٰ وَيُقْذَفُونَ مِن كُلِّ جَانِبٍ ٨

9. የሚባረሩ ሲሆኑ (ይጣልባቸዋል):: ለእነሱም ዘውታሪ ቅጣት አላቸው::

دُحُورًا ۖ وَلَهُمْ عَذَابٌ وَاصِبٌ ٩

10. ንጥቂያን የነጠቀ ወዲያውም አብሪ ኮከብ የተከተለው ሲቀር፤ (እርሱ ይሰማዋል)::

إِلَّا مَنْ خَطِفَ ٱلْخَطْفَةَ فَأَتْبَعَهُۥ شِهَابٌ ثَاقِبٌ ١٠

11. ጠይቃቸውም፤ እነርሱ በአፈጣጠር ይበልጥ የበረቱ ናቸውን? ወይስ እኛ (ከእነርሱ በፊት) የፈጠርነው? (ፍጡር) እኛ ከሚጣበቅ ጭቃ ፈጠርናቸው::

فَٱسْتَفْتِهِمْ أَهُمْ أَشَدُّ خَلْقًا أَم مَّنْ خَلَقْنَآ ۚ إِنَّا خَلَقْنَٰهُم مِّن طِينٍ لَّازِبٍ ١١

12. ይልቁንም (በማስተባበላቸው) ተደነቅህ፤ (ከመደነቅህ) ይሳለቃሉም::

بَلْ عَجِبْتَ وَيَسْخَرُونَ ١٢

13. በተገሠጹም ጊዜ አይመለሱም::

وَإِذَا ذُكِّرُوا۟ لَا يَذْكُرُونَ ١٣

14. ተዓምርን ባዩም ጊዜ ለመሳለቅ ይጠራራሉ::

وَإِذَا رَأَوْا۟ ءَايَةً يَسْتَسْخِرُونَ ١٤

15. ይላሉም «ይህ ግልጽ ድግምት እንጂ ሌላ አይደለም::

وَقَالُوٓا۟ إِنْ هَٰذَآ إِلَّا سِحْرٌ مُّبِينٌ ١٥

16. «በሞትንና ዐፈርና አጥንቶችም በኾን ጊዜ እኛ የምንቀሰቀስ ነን?

أَءِذَا مِتْنَا وَكُنَّا تُرَابًا وَعِظَٰمًا أَءِنَّا لَمَبْعُوثُونَ ١٦

17. «የቀድሞዎቹ አባቶችንም? (ይላሉ)::

أَوَ ءَابَآؤُنَا ٱلْأَوَّلُونَ ١٧

18. «አዎን እናንተ ወራዶች ሆናችሁ (ትነሳላችሁ)» በላቸው::

قُلْ نَعَمْ وَأَنتُمْ دَٰخِرُونَ ١٨

19. እርሷም አንዲት ጩኸት ብቻ ናት:: እነርሱም ወዲያውኑ (ምን እንደሚፈጸምባቸው) ያያሉ::

فَإِنَّمَا هِىَ زَجْرَةٌ وَٰحِدَةٌ فَإِذَا هُمْ يَنظُرُونَ ١٩

20. «ዋ ጥፋታችን! ይህ የፍርዱ ቀን ነው» ይላሉም::

وَقَالُوا۟ يَٰوَيْلَنَا هَٰذَا يَوْمُ ٱلدِّينِ ٢٠

21. «ይህ ያ በእርሱ ታስተባብሉ የነበራችሁት መለያው ቀን ነው» (ይባላሉ)::

هَٰذَا يَوْمُ ٱلْفَصْلِ ٱلَّذِى كُنتُم بِهِۦ تُكَذِّبُونَ ٢١

22. (ለመላእክቶችም) «እነዚያን ነፍሶቻቸውን የበደሉትን ሰዎች ጓደኞቻቸውንም ይግገዟቸው የነበሩትንም (ጣዖታት) ሰብስቡ::

۞ ٱحْشُرُوا۟ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوا۟ وَأَزْوَٰجَهُمْ وَمَا كَانُوا۟ يَعْبُدُونَ ٢٢

23. «ከአላህ ሌላ (የሚገዙዋቸውን ሰብስቧቸው) ወደ እሳት መንገድም ምሩዋቸው::

مِن دُونِ ٱللَّهِ فَٱهْدُوهُمْ إِلَىٰ صِرَٰطِ ٱلْجَحِيمِ ٢٣

24. «አቁሟቸውም:: እነርሱ ተጠያቂዎች ናቸውና» (ይባላል)::

وَقِفُوهُمْ ۖ إِنَّهُم مَّسْـُٔولُونَ ٢٤

25. (ለእነርሱም) «የማትረዳዱት ለእናንተ ምን አላችሁ? (ይባላሉ)፡፡

مَا لَكُمْ لَا تَنَاصَرُونَ ﴿٢٥﴾

26. በእርግጥ እነርሱ ዛሬ እጃቸውን የሰጡ ወራዳዎች ናቸው፡፡

بَلْ هُمُ ٱلْيَوْمَ مُسْتَسْلِمُونَ ﴿٢٦﴾

27. የሚወቃቀሱም ሆነው ከፊላቸው በከፊሉ ላይ ይመጣሉ፡፡

وَأَقْبَلَ بَعْضُهُمْ عَلَىٰ بَعْضٍ يَتَسَآءَلُونَ ﴿٢٧﴾

28. (ለአስከታዮቹ) እናንተ ከስተቀኝ ትመጡብን ነበር ይላሉ፡፡

قَالُوٓاْ إِنَّكُمْ كُنتُمْ تَأْتُونَنَا عَنِ ٱلْيَمِينِ ﴿٢٨﴾

29. (አስከታዮቹም) ይላሉ «አይደለም ፈጽሞ ምእምናን አልነበራችሁም፡፡

قَالُواْ بَل لَّمْ تَكُونُواْ مُؤْمِنِينَ ﴿٢٩﴾

30. «ለእኛም በእናንተ ላይ ምንም ስልጣን አልነበረንም፡፡ በእርግጥ እናንተ ጠማሞች ሕዝቦች ነበራችሁ፡፡

وَمَا كَانَ لَنَا عَلَيْكُم مِّن سُلْطَٰنٍۭ ۖ بَلْ كُنتُمْ قَوْمًا طَٰغِينَ ﴿٣٠﴾

31. «በእኛም ላይ የጌታችን ቃል ተረጋገጠብን፤ እኛ (ሁላችንም ቅጣቱን) ቀማሾች ነን፡፡

فَحَقَّ عَلَيْنَا قَوْلُ رَبِّنَآ ۖ إِنَّا لَذَآئِقُونَ ﴿٣١﴾

32. «ወደ ጥምመት ጠራናችሁም፡፡ እኛ ጠማሞች ነበርንና» (ይላሉ)፡፡

فَأَغْوَيْنَٰكُمْ إِنَّا كُنَّا غَٰوِينَ ﴿٣٢﴾

33. ስለዚህ እነርሱ በዚያ ቀን በቅጣቱ ነጋሪዎች ናቸው፡ ፡

فَإِنَّهُمْ يَوْمَئِذٍ فِى ٱلْعَذَابِ مُشْتَرِكُونَ ﴿٣٣﴾

34. እኛ በአመጸኞች ሁሉ እንደዚሁ እንሠራለን፡፡

إِنَّا كَذَٰلِكَ نَفْعَلُ بِٱلْمُجْرِمِينَ ﴿٣٤﴾

35. እነርሱ ከአላህ ሌላ አምላክ የለም በተባሉ ጊዜ ይኮሩ ነበሩ፡፡

إِنَّهُمْ كَانُوٓاْ إِذَا قِيلَ لَهُمْ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا ٱللَّهُ يَسْتَكْبِرُونَ ﴿٣٥﴾

36. እኛ ለዕብድ ባለቅኔ ብለን አማልክቶቻችንን የምንተው ነን? ይሉም ነበር፡፡

وَيَقُولُونَ أَئِنَّا لَتَارِكُوٓاْ ءَالِهَتِنَا لِشَاعِرٍ مَّجْنُونٍ ﴿٣٦﴾

37. አይደለም እውነቱን (ሃይማኖት) አመጣ፡፡ መልክተኞቹንም እውነተኛነታቸውን አረጋገጠ፡፡

بَلْ جَآءَ بِٱلْحَقِّ وَصَدَّقَ ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿٣٧﴾

38. እናንተ አሳማሚውን ቅጣት በእርግጥ ቀማሾች ናችሁ፡፡

إِنَّكُمْ لَذَآئِقُواْ ٱلْعَذَابِ ٱلْأَلِيمِ ﴿٣٨﴾

39. ትሠሩትም የነበራችሁትን እንጂ ሌላን አትመነዱም፡፡

وَمَا تُجْزَوْنَ إِلَّا مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ﴿٣٩﴾

40. ግን ምርጥ የሆኑት የአላህ ባሮች (ቅጣትን አይቀምሱም)፡፡

إِلَّا عِبَادَ ٱللَّهِ ٱلْمُخْلَصِينَ ﴿٤٠﴾

41. እነዚያ ለእነርሱ የታወቀ ሲሳይ አላቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمْ رِزْقٌ مَّعْلُومٌ ﴿٤١﴾

42. ፍራፍሬዎች (አሏቸው) እነርሱም የተከበሩ ናቸው፤

فَوَٰكِهُ وَهُم مُّكْرَمُونَ ﴿٤٢﴾

43. በድሎት ገነቶች ውስጥ፡፡

فِي جَنَّٰتِ ٱلنَّعِيمِ ٤٣

44. ፊት ለፊት የሚታያዩ ሲሆኑ በአልጋዎች ላይ (ይንፈላሰሳሉ)፡፡

عَلَىٰ سُرُرٖ مُّتَقَٰبِلِينَ ٤٤

45. ከሚመነጭ ወይን ጠጅ በያዘ ብርጭቆ በእነርሱ ላይ ይዞርባቸዋል፡፡

يُطَافُ عَلَيۡهِم بِكَأۡسٖ مِّن مَّعِينِۭ ٤٥

46. ነጭ ለጠጪዎች ጣፋጭ ከኾነች፡፡

بَيۡضَآءَ لَذَّةٖ لِّلشَّٰرِبِينَ ٤٦

47. በእርሷ ውስጥም ምታት የለባትም፡፡ እነርሱም ከእርሷ የሚሰክሩ አይደሉም፡፡

لَا فِيهَا غَوۡلٞ وَلَا هُمۡ عَنۡهَا يُنزَفُونَ ٤٧

48. እነርሱም ዘንድ ዓይናቸውን (በባሎቻቸው ላይ) አሳጣሪዎች የኾኑ ዓይናማዎች አልሉ፡፡

وَعِندَهُمۡ قَٰصِرَٰتُ ٱلطَّرۡفِ عِينٞ ٤٨

49. እነርሱ ልክ የተሸፈነ (የሰጎን) ዕንቁላል ይመስላሉ፡፡

كَأَنَّهُنَّ بَيۡضٞ مَّكۡنُونٞ ٤٩

50. የሚጠያየቁም ሆነው ከፊላቸው ወደ ከፊሉ ይመጣሉ፡፡

فَأَقۡبَلَ بَعۡضُهُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖ يَتَسَآءَلُونَ ٥٠

51. ከእነርሱ የሆነ ተናጋሪ ይላል «እኔ ጓደኛ ነበረኝ፡፡

قَالَ قَآئِلٞ مِّنۡهُمۡ إِنِّي كَانَ لِي قَرِينٞ ٥١

52. «በእርግጥ አንተ ከሚያምኑት ነህን? የሚል፡፡

يَقُولُ أَءِنَّكَ لَمِنَ ٱلۡمُصَدِّقِينَ ٥٢

53. «በሞትንና ዐፈር አጥንቶችም በሆን ጊዜ እኛ በእርግጥ እንመረመራለን?» (የሚል)፡፡

أَءِذَا مِتۡنَا وَكُنَّا تُرَابٗا وَعِظَٰمًا أَءِنَّا لَمَدِينُونَ ٥٣

54. እናንተ ተመልካቾች ናችሁን? ይላል፡፡

قَالَ هَلۡ أَنتُم مُّطَّلِعُونَ ٥٤

55. ይመለከታልም፤ በገሀነም መካከልም (ጓደኛውን) ያየዋል፡፡

فَٱطَّلَعَ فَرَءَاهُ فِي سَوَآءِ ٱلۡجَحِيمِ ٥٥

56. ይላል «በአላህ እምላለሁ፤ በእርግጥ ልታጠፋኝ ቀርበህ ነበር፡፡

قَالَ تَٱللَّهِ إِن كِدتَّ لَتُرۡدِينِ ٥٦

57. «የጌታየም ጸጋ ባልነበረ ኖሮ ወደ እሳት ከሚቀርቡት እሆን ነበር፡፡»

وَلَوۡلَا نِعۡمَةُ رَبِّي لَكُنتُ مِنَ ٱلۡمُحۡضَرِينَ ٥٧

58. (የገነት ሰዎች ይላሉ) «እኛ የምንሞት አይደለንምን?

أَفَمَا نَحۡنُ بِمَيِّتِينَ ٥٨

59. «የመጀመሪያይቱ መሞታችን ብቻ ስትቀር፡፡ እኛም የምንቅቀጣ አይደለንምን?» (ይላሉ)፡፡

إِلَّا مَوۡتَتَنَا ٱلۡأُولَىٰ وَمَا نَحۡنُ بِمُعَذَّبِينَ ٥٩

60. ይህ (ለገነት ሰዎች የተወሳው) እርሱ በእርግጥ ታላቅ ዕድል ነው፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَهُوَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ٦٠

61. ለዚህ ብጤ ሠሪዎች ይሥሩ፡፡

لِمِثۡلِ هَٰذَا فَلۡيَعۡمَلِ ٱلۡعَٰمِلُونَ ٦١

62. በመስተንግዶነት ይህ ይበልጣልን? ወይስ የዘቁም ዛፍ?

أَذَٰلِكَ خَيۡرٞ نُّزُلًا أَمۡ شَجَرَةُ ٱلزَّقُّومِ ٦٢

63. እኛ ለበዳዮች ፈተና አድርገናታል፡፡

إِنَّا جَعَلۡنَٰهَا فِتۡنَةٗ لِّلظَّٰلِمِينَ ٦٣

64. እርሷ በገሀነም አዘቅት ውስጥ የምትወጣ ዛፍ ናት፡፡

إِنَّهَا شَجَرَةٞ تَخۡرُجُ فِيٓ أَصۡلِ ٱلۡجَحِيمِ ٦٤

65. እንቡጧ ልክ የሰይጣናት ራሶች ይመስላል፡፡

طَلۡعُهَا كَأَنَّهُۥ رُءُوسُ ٱلشَّيَٰطِينِ ٦٥

66. እነርሱም ከእርሷ በይዎች ናቸው፤ ሆዶችንም ከእርሷ ሞይዎች ናቸው፡፡

فَإِنَّهُمۡ لَأٓكِلُونَ مِنۡهَا فَمَالِـُٔونَ مِنۡهَا ٱلۡبُطُونَ ٦٦

67. ከዚያም ለእነርሱ በእርሷ ላይ ከተኳሳ ውሃ ቅልቅል (መጠጥ) አልላቸው፡፡

ثُمَّ إِنَّ لَهُمۡ عَلَيۡهَا لَشَوۡبٗا مِّنۡ حَمِيمٖ ٦٧

68. ከዚያም መመለሻቸው ወደ ተጋጋመች እሳት ነው፡፡

ثُمَّ إِنَّ مَرۡجِعَهُمۡ لَإِلَى ٱلۡجَحِيمِ ٦٨

69. እነሱ አባቶቻቸውን የተሳሳቱ ሆነው አግኝተዋልና፡፡

إِنَّهُمۡ أَلۡفَوۡاْ ءَابَآءَهُمۡ ضَآلِّينَ ٦٩

70. እነሱም በፈለጎቻቸው ላይ ይገሰግሳሉና፡፡

فَهُمۡ عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِمۡ يُهۡرَعُونَ ٧٠

71. ከእነርሱ በፊትም የቀድሞዎቹ (ሕዝቦች) አብዛኞቻቸው በእርግጥ ተሳስተዋል፡፡

وَلَقَدۡ ضَلَّ قَبۡلَهُمۡ أَكۡثَرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٧١

72. በውስጣቸውም አስፈራሪዎችን በእርግጥ ልከናል፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا فِيهِم مُّنذِرِينَ ٧٢

73. የተስፈራሪዎቹም መጨረሻ እንዴት እንደነበረ ተመልከት፡፡

فَٱنظُرۡ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلۡمُنذَرِينَ ٧٣

74. ምርጥ የሆኑት የአላህ ባሮች ብቻ ሲቀሩ፡፡

إِلَّا عِبَادَ ٱللَّهِ ٱلۡمُخۡلَصِينَ ٧٤

75. ኑሕም በእርግጥ ጠራን፡፡ ጥሪውን ተቀባዮቹም ምንኛ አማርን!

وَلَقَدۡ نَادَىٰنَا نُوحٞ فَلَنِعۡمَ ٱلۡمُجِيبُونَ ٧٥

76. እርሱንም ቤተሰቦቹንም ከከባድ ጭንቅ አዳንን፡፡

وَنَجَّيۡنَٰهُ وَأَهۡلَهُۥ مِنَ ٱلۡكَرۡبِ ٱلۡعَظِيمِ ٧٦

77. ዘሮቹንም እነርሱን ብቻ ቀሪዎች አደረግን፤

وَجَعَلۡنَا ذُرِّيَّتَهُۥ هُمُ ٱلۡبَاقِينَ ٧٧

78. በርሱም ላይ በኋለኞቹ ሕዝቦች ውስጥ (መልካም ዝናን) ተውን፡፡

وَتَرَكۡنَا عَلَيۡهِ فِي ٱلۡأٓخِرِينَ ٧٨

| | |
|---|---|
| 79. «በዓለማት ውስጥ ሰላም በኑሕ ላይ ይኹን፡፡» | سَلَٰمٌ عَلَىٰ نُوحٖ فِي ٱلۡعَٰلَمِينَ ٧٩ |
| 80. እኛ እንደዚሁ መልካም ሠሪዎችን እንመነዳለን፡፡ | إِنَّا كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ٨٠ |
| 81. እርሱ ከምእምናን ባሮቻችን ነውና፡፡ | إِنَّهُۥ مِنۡ عِبَادِنَا ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٨١ |
| 82. ከዚያም ሌሎቹን አሰጠምን፡፡ | ثُمَّ أَغۡرَقۡنَا ٱلۡأٓخَرِينَ ٨٢ |
| 83. ኢብራሂምም በእርግጥ ከተከታዮቹ ነው፡፡ | ۞وَإِنَّ مِن شِيعَتِهِۦ لَإِبۡرَٰهِيمَ ٨٣ |
| 84. ወደ ጌታው በቅን ልብ በመጣ ጊዜ (የኾነውን አስታውስ)፡፡፡ | إِذۡ جَآءَ رَبَّهُۥ بِقَلۡبٖ سَلِيمٍ ٨٤ |
| 85. «ለአባቱና ለሕዝቦቹ ምንን ትግገዛላችሁ?» ባለ ጊዜ፡፡ | إِذۡ قَالَ لِأَبِيهِ وَقَوۡمِهِۦ مَاذَا تَعۡبُدُونَ ٨٥ |
| 86. «ለቅጥፈት ብላችሁ ከአላህ ሌላ አማልክትን ትሻላችሁን? | أَئِفۡكًا ءَالِهَةٗ دُونَ ٱللَّهِ تُرِيدُونَ ٨٦ |
| 87. «በዓለማትም ጌታ ሃሳባችሁ ምንድን ነው?» አለ፡፡ | فَمَا ظَنُّكُم بِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٨٧ |
| 88. በከዋክብትም መመልከትን ተመለከተ፡፡ | فَنَظَرَ نَظۡرَةٗ فِي ٱلنُّجُومِ ٨٨ |
| 89. «እኔ በሽተኛ ነኝም» አለ፡፡ | فَقَالَ إِنِّي سَقِيمٞ ٨٩ |
| 90. ከእርሱም የሸሹ ሆነው ኼዱ፡፡ | فَتَوَلَّوۡاْ عَنۡهُ مُدۡبِرِينَ ٩٠ |
| 91. ወደ አማልክቶቻቸውም ተዘነበለ፡፡ አለም፡- «አትበሉምን?» | فَرَاغَ إِلَىٰٓ ءَالِهَتِهِمۡ فَقَالَ أَلَا تَأۡكُلُونَ ٩١ |
| 92. «የማትናገሩት ለናንተ ምን አላችሁ?» | مَا لَكُمۡ لَا تَنطِقُونَ ٩٢ |
| 93. በኀይል የሚመታቸውም ሆኖ በእነርሱ ላይ በድብቅ ተዘነበለ፡፡ | فَرَاغَ عَلَيۡهِمۡ ضَرۡبَۢا بِٱلۡيَمِينِ ٩٣ |
| 94. ወደእርሱም (ሰዎቹ) እየሮጡ መጡ፡፡ | فَأَقۡبَلُوٓاْ إِلَيۡهِ يَزِفُّونَ ٩٤ |
| 95. አላቸው «የምትጠርቡትን ትግገዛላችሁን?» | قَالَ أَتَعۡبُدُونَ مَا تَنۡحِتُونَ ٩٥ |
| 96. «አላህ እናንተንም የምትሠሩትንም የፈጠረ ሲኾን፡፡» | وَٱللَّهُ خَلَقَكُمۡ وَمَا تَعۡمَلُونَ ٩٦ |

97. «ለእርሱም ግንብን ገንቡ በእሳት ነበልባል ውስጥ ጣሉትም» አሉ፡፡

قَالُواْ ٱبۡنُواْ لَهُۥ بُنۡيَٰنٗا فَأَلۡقُوهُ فِي ٱلۡجَحِيمِ ۝٩٧

98. በእርሱም ተንኮልን አሰቡ፡፡ ዝቅተኞችም አደረግናቸው፡፡

فَأَرَادُواْ بِهِۦ كَيۡدٗا فَجَعَلۡنَٰهُمُ ٱلۡأَسۡفَلِينَ ۝٩٨

99. አለም «እኔ ወደ ጌታዬ ኼያጅ ነኝ፡፡ በእርግጥ ይመራኛልና፡፡»

وَقَالَ إِنِّي ذَاهِبٌ إِلَىٰ رَبِّي سَيَهۡدِينِ ۝٩٩

100. ጌታዬ ሆይ! ከመልካሞቹ የሆነን (ልጅ) ስጠኝ፡፡

رَبِّ هَبۡ لِي مِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ۝١٠٠

101. ታጋሽ በሆነ ወጣት ልጅም አበሰርነው፡፡

فَبَشَّرۡنَٰهُ بِغُلَٰمٍ حَلِيمٖ ۝١٠١

102. ከእርሱ ጋርም ለሥራ በደረሰ ጊዜ «ልጄ ሆይ! እኔ በሕልሜ እኔ የማርድህ ሆኜ አያለሁ፡፡ ተመልከትም፤ ምን ታያለህ?» አለው፡፡ «አባቴ ሆይ! የታዘዝከውን ሥራ፡፡ አላህ ቢሻ ከታጋሾቹ ሆኜ ታገኘኛለህ» አለ፡፡

فَلَمَّا بَلَغَ مَعَهُ ٱلسَّعۡيَ قَالَ يَٰبُنَيَّ إِنِّيٓ أَرَىٰ فِي ٱلۡمَنَامِ أَنِّيٓ أَذۡبَحُكَ فَٱنظُرۡ مَاذَا تَرَىٰۚ قَالَ يَٰٓأَبَتِ ٱفۡعَلۡ مَا تُؤۡمَرُۖ سَتَجِدُنِيٓ إِن شَآءَ ٱللَّهُ مِنَ ٱلصَّٰبِرِينَ ۝١٠٢

103. ሁለቱም ትዕዛዙን በተቀበሉና በግንባሩም ጎን ላይ በጣለው ጊዜ (የሆነው ሆነ)፡፡

فَلَمَّآ أَسۡلَمَا وَتَلَّهُۥ لِلۡجَبِينِ ۝١٠٣

104. ጠራነውም፤ (አልነው) «ኢብራሂም ሆይ!

وَنَٰدَيۡنَٰهُ أَن يَٰٓإِبۡرَٰهِيمُ ۝١٠٤

105. ራእይቱን በእውነት አረጋገጥክ፡፡» እኛ እንደዚሁ መልካም ሠሪዎችን እንመነዳለን፡፡

قَدۡ صَدَّقۡتَ ٱلرُّءۡيَآۚ إِنَّا كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ۝١٠٥

106. ይህ እርሱ በእውነት ግልጽ ፈተና ነው፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَهُوَ ٱلۡبَلَٰٓؤُاْ ٱلۡمُبِينُ ۝١٠٦

107. በታላቅ ዕርድም (መስዋዕት) ተቤዠነው፡፡

وَفَدَيۡنَٰهُ بِذِبۡحٍ عَظِيمٖ ۝١٠٧

108. በእርሱም ላይ በኋለኞቹ ሕዝቦች ውስጥ መልካም ዝናን አስቀረንለት፡፡

وَتَرَكۡنَا عَلَيۡهِ فِي ٱلۡأٓخِرِينَ ۝١٠٨

109. ሰላም በኢብራሂም ላይ ይሁን፡፡

سَلَٰمٌ عَلَىٰٓ إِبۡرَٰهِيمَ ۝١٠٩

110. እንደዚሁ መልካም ሠሪዎችን ሁሉ እንመነዳለን፡፡

كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ۝١١٠

111. እርሱ በእርግጥ ካመኑት ባሮቻችን ነው፡፡

إِنَّهُۥ مِنۡ عِبَادِنَا ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ۝١١١

112. በኢስሐቅም አበሰርነው፡፡ ከመልካሞቹ የሆነ ነቢይ ሲሆን፡፡

وَبَشَّرۡنَٰهُ بِإِسۡحَٰقَ نَبِيّٗا مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ۝١١٢

113. በእርሱና በኢስሐቅ ላይም ባረክን፡፡ ከሁለቱም ዘሮች በጎ ሠሪ አልለ፡፡ ለነፍሱ ግልጽ በዳይም አለ፡፡

وَبَٰرَكۡنَا عَلَيۡهِ وَعَلَىٰٓ إِسۡحَٰقَۚ وَمِن ذُرِّيَّتِهِمَا مُحۡسِنٞ وَظَالِمٞ لِّنَفۡسِهِۦ مُبِينٞ ١١٣

114. በሙሳና በሃሩን ላይም በእርግጥ ለገስን፡፡

وَلَقَدۡ مَنَنَّا عَلَىٰ مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ١١٤

115. እነርሱንም ሕዝቦቻቸውንም ከታላቅ ጭንቅ አዳንን፡፡

وَنَجَّيۡنَٰهُمَا وَقَوۡمَهُمَا مِنَ ٱلۡكَرۡبِ ٱلۡعَظِيمِ ١١٥

116. ረዳናቸውም፡፡ እነርሱም አሸናፊዎች ነበሩ፡፡

وَنَصَرۡنَٰهُمۡ فَكَانُواْ هُمُ ٱلۡغَٰلِبِينَ ١١٦

117. በጣም የተብራራውንም መጽሐፍ ሰጠናቸው፡፡

وَءَاتَيۡنَٰهُمَا ٱلۡكِتَٰبَ ٱلۡمُسۡتَبِينَ ١١٧

118. ቀጥተኛውንም መንገድ መራናቸው፡፡

وَهَدَيۡنَٰهُمَا ٱلصِّرَٰطَ ٱلۡمُسۡتَقِيمَ ١١٨

119. በሁለቱም ላይ በኋለኞቹ ሕዝቦች ውስጥ መልካም ዝናን ተውንላቸው፡፡

وَتَرَكۡنَا عَلَيۡهِمَا فِي ٱلۡأٓخِرِينَ ١١٩

120. ሰላም በሙሳና በሃሩን ላይ ይሁን፡፡

سَلَٰمٌ عَلَىٰ مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ١٢٠

121. እኛ እንደዚሁ በጎ አድራጊዎችን ሁሉ እንመነዳለን፡፡

إِنَّا كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٢١

122. ሁለቱም በእርግጥ ከአመኑት ባሮቻችን ናቸው፡፡

إِنَّهُمَا مِنۡ عِبَادِنَا ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٢٢

123. ኢልያስም በእርግጥ ከመልክተኞቹ ነው፡፡

وَإِنَّ إِلۡيَاسَ لَمِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٢٣

124. ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፤ አላህን አትፈሩምን?

إِذۡ قَالَ لِقَوۡمِهِۦٓ أَلَا تَتَّقُونَ ١٢٤

125. በዐልን ትገዛላችሁን? ከሰዓሊዎቹ ሁሉ ይበልጥ በጣም አሳማሪ የሆነውንም አምላክ ትተዋላችሁን?

أَتَدۡعُونَ بَعۡلٗا وَتَذَرُونَ أَحۡسَنَ ٱلۡخَٰلِقِينَ ١٢٥

126. አላህን ጌታችሁንና የቀድሞዎቹ አባቶቻችሁን ጌታ (ትተዋላችሁን)?

ٱللَّهَ رَبَّكُمۡ وَرَبَّ ءَابَآئِكُمُ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٢٦

127. አስተባበሉትም፡፡ ስለዚህ እነርሱ (ለቅጣት) የሚጣዱ ናቸው፡፡

فَكَذَّبُوهُ فَإِنَّهُمۡ لَمُحۡضَرُونَ ١٢٧

128. ንጹሕ የተደረጉት የአላህ ባሮች ብቻ ሲቀሩ፡፡

إِلَّا عِبَادَ ٱللَّهِ ٱلۡمُخۡلَصِينَ ١٢٨

129. በእርሱ ላይም በኋለኞቹ ሕዝቦች ውስጥ መልካም ዝናን ተውንለት፡፡

وَتَرَكۡنَا عَلَيۡهِ فِي ٱلۡأٓخِرِينَ ١٢٩

130. ሰላም በኢልያሲን ላይ ይሁን፡፡

سَلَٰمٌ عَلَىٰٓ إِلۡ يَاسِينَ ١٣٠

131. እኛ እንደዚሁ መልካም ሠሪዎችን እንመነዳለን፡፡

إِنَّا كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ١٣١

132. እርሱ በእርግጥ ከምእመናን ባሮቻችን ነው፡፡

إِنَّهُۥ مِنۡ عِبَادِنَا ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ١٣٢

133. ሉጥም በእርግጥ ከመልክተኞቹ ነው፡፡

وَإِنَّ لُوطٗا لَّمِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٣٣

134. እርሱንና ቤተሰቦቹን ሁሉንም በአዳንናቸው ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ نَجَّيۡنَٰهُ وَأَهۡلَهُۥٓ أَجۡمَعِينَ ١٣٤

135. (በቅጣቱ ውስጥ) ከቀሪዎቹ የሆነችው አሮጊት ብቻ ስትቀር፡፡

إِلَّا عَجُوزٗا فِي ٱلۡغَٰبِرِينَ ١٣٥

136. ከዚያም ሌሎቹን አጠፋን፡፡

ثُمَّ دَمَّرۡنَا ٱلۡأٓخَرِينَ ١٣٦

137. እናንተም ያነጋችሁ ስትሆኑ በእነርሱ (መኖሪያዎች) ላይ (በቀን) ታልፋላችሁ፡፡

وَإِنَّكُمۡ لَتَمُرُّونَ عَلَيۡهِم مُّصۡبِحِينَ ١٣٧

138. በሌሊትም (ታልፋላችሁ)፤ ልብም አታደርጉምን?

وَبِٱلَّيۡلِۚ أَفَلَا تَعۡقِلُونَ ١٣٨

139. ዩኑስም በእርግጥ ከመልክተኞቹ ነው፡፡

وَإِنَّ يُونُسَ لَمِنَ ٱلۡمُرۡسَلِينَ ١٣٩

140. ወደ ተመላው መርከብ በኮበለለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ أَبَقَ إِلَى ٱلۡفُلۡكِ ٱلۡمَشۡحُونِ ١٤٠

141. ዕጣም ተጣጣለ፡፡ ከተሸነፉትም ሆነ፡፡

فَسَاهَمَ فَكَانَ مِنَ ٱلۡمُدۡحَضِينَ ١٤١

142. እርሱም ተወቃሽ ሲሆን ዐሳው ዋጠው፡፡

فَٱلۡتَقَمَهُ ٱلۡحُوتُ وَهُوَ مُلِيمٞ ١٤٢

143. እርሱ ለጌታው ከአወዳሾቹ ባልሆነም ኖሮ፤

فَلَوۡلَآ أَنَّهُۥ كَانَ مِنَ ٱلۡمُسَبِّحِينَ ١٤٣

144. እስከሚቀሰቀሱበት ቀን ድረስ በሆዱ ውስጥ በቆየ ነበር፡፡

لَلَبِثَ فِي بَطۡنِهِۦٓ إِلَىٰ يَوۡمِ يُبۡعَثُونَ ١٤٤

145. እርሱ በሽተኛ ሆኖ በቃይ በሌለው (በባሕር) ዳርቻ ላይ ጣልነውም፡፡

۞فَنَبَذۡنَٰهُ بِٱلۡعَرَآءِ وَهُوَ سَقِيمٞ ١٤٥

146. በእርሱም ላይ (በአጠገቡ) ከቅል የሆነችን ዛፍ አበቀልን፡፡

وَأَنۢبَتۡنَا عَلَيۡهِ شَجَرَةٗ مِّن يَقۡطِينٖ ١٤٦

147. ወደ መቶ ሺሕ ሰዎችም (ዳግመኛ) ላክነው፡፡ ከቶውንም ይጨምራሉ፡፡

وَأَرۡسَلۡنَٰهُ إِلَىٰ مِاْئَةِ أَلۡفٍ أَوۡ يَزِيدُونَ ١٤٧

148. አመኑም፡፡ እስከ ጊዜ ድረስም አጣቀምናቸው፡፡

فَـَٔامَنُواْ فَمَتَّعۡنَٰهُمۡ إِلَىٰ حِينٖ ١٤٨

149. (የመካን ሰዎች) ጠይቃቸውም፡፡ «ለጌታህ ሴቶች ልጆች ለእነርሱም ወንዶች ልጆች ይኖራልን?»

فَٱسۡتَفۡتِهِمۡ أَلِرَبِّكَ ٱلۡبَنَاتُ وَلَهُمُ ٱلۡبَنُونَ ١٤٩

150. ወይስ እኛ እነርሱ የተጣዱ ሆነው መላእክትን ሴቶች አድርገን ፈጠርን?

أَمۡ خَلَقۡنَا ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ إِنَٰثٗا وَهُمۡ شَٰهِدُونَ ١٥٠

151. ንቁ! እነርሱ ከቅጥፈታቸው (የተነሳ) ይላሉ:-

أَلَآ إِنَّهُم مِّنۡ إِفۡكِهِمۡ لَيَقُولُونَ ١٥١

152. «አላህ (መላእክትን) ወለደ፡፡» እነርሱም በእርግጥ ውሸታሞች ናቸው፡፡

وَلَدَ ٱللَّهُ وَإِنَّهُمۡ لَكَٰذِبُونَ ١٥٢

153. በወንዶች ልጆች ላይ ይልቅ ሴቶችን ልጆች መረጥን?

أَصۡطَفَى ٱلۡبَنَاتِ عَلَى ٱلۡبَنِينَ ١٥٣

154. ለእናንተ ምን (አስረጅ) አላችሁ? እንዴት ትፈርዳላችሁ!

مَا لَكُمۡ كَيۡفَ تَحۡكُمُونَ ١٥٤

155. አትገነዘቡምን?

أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ١٥٥

156. ወይስ ለእናንተ ግልጽ አስረጅ አላችሁን?

أَمۡ لَكُمۡ سُلۡطَٰنٞ مُّبِينٞ ١٥٦

157. «እውነተኞች እንደ ሆናችሁ መጽሐፋችሁን አምጡ» (በላቸው)፡፡

فَأۡتُواْ بِكِتَٰبِكُمۡ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ١٥٧

158. በአላህና በአጋንንት መካከልም ዝምድናን አደረጉ፡፡ አጋንንትም እነርሱ (ይህን ባዮች በእሳት) የሚጣዱ መሆናቸውን በእርግጥ ዐውቀዋል፡፡

وَجَعَلُواْ بَيۡنَهُۥ وَبَيۡنَ ٱلۡجِنَّةِ نَسَبٗاۚ وَلَقَدۡ عَلِمَتِ ٱلۡجِنَّةُ إِنَّهُمۡ لَمُحۡضَرُونَ ١٥٨

159. አላህ ከሚመጥኑት ሁሉ ጠራ፡፡

سُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ عَمَّا يَصِفُونَ ١٥٩

160. ግን የተመረጡት የአላህ ባሮች (በአላህ ላይ አይዋሹም)፡፡

إِلَّا عِبَادَ ٱللَّهِ ٱلۡمُخۡلَصِينَ ١٦٠

161. እናንተም የምትገዟቸውም ሁሉ፤

فَإِنَّكُمۡ وَمَا تَعۡبُدُونَ ١٦١

162. በእርሱ (በአላህ) ላይ አንድንም አጥማሚዎች አይደላችሁም፡፡

مَآ أَنتُمۡ عَلَيۡهِ بِفَٰتِنِينَ ١٦٢

163. ያንን እርሱ ገሀነምን ገቢ የሆነውን ሰው ቢሆን እንጅ፡፡

إِلَّا مَنۡ هُوَ صَالِ ٱلۡجَحِيمِ ١٦٣

164. (ጂብሪል አለ) ከእኛም አንድም የለም፤ ለእርሱ የታወቀ ደረጃ ያለው ቢሆን እንጅ፡፡

وَمَا مِنَّآ إِلَّا لَهُۥ مَقَامٞ مَّعۡلُومٞ ١٦٤

165. እኛም (ጌታን ለመግገዛት) ተሰላፊዎቹ እኛ ነን፡፡

وَإِنَّا لَنَحۡنُ ٱلصَّآفُّونَ ١٦٥

166. እኛም (አላህን) አጥሪዎቹ እኛ ነን፡፡

وَإِنَّا لَنَحۡنُ ٱلۡمُسَبِّحُونَ ١٦٦

167. እነርሱም (ከሓዲዎቹ) በእርግጥ ይሉ ነበሩ:-

وَإِن كَانُواْ لَيَقُولُونَ ١٦٧

168. «ከቀድሞዎቹ (መጻሕፍት) ገሳጭ መጽሐፍ እኛ ዘንድ በነበረን ኖሮ፤

لَوْ أَنَّ عِندَنَا ذِكْرًا مِّنَ ٱلْأَوَّلِينَ ﴿١٦٨﴾

169. «የአላህ ምርጦች ባሮች በሆን ነበር፡፡»

لَكُنَّا عِبَادَ ٱللَّهِ ٱلْمُخْلَصِينَ ﴿١٦٩﴾

170. ግን (ቁርኣኑ በመጣላቸው ጊዜ) በእርሱ ካዱ፡፡ ወደፊትም በእርግጥ ያውቃሉ፡፡

فَكَفَرُوا۟ بِهِۦ ۖ فَسَوْفَ يَعْلَمُونَ ﴿١٧٠﴾

171. (የእርዳታ) ቃላችንም መልክተኞች ለሆኑት ባሮቻችን በእውነት አልፋለች፡፡

وَلَقَدْ سَبَقَتْ كَلِمَتُنَا لِعِبَادِنَا ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿١٧١﴾

172. እነርሱ ተረጂዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡

إِنَّهُمْ لَهُمُ ٱلْمَنصُورُونَ ﴿١٧٢﴾

173. ሰራዊቶቻችንም በእርግጥ አሸናፊዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡

وَإِنَّ جُندَنَا لَهُمُ ٱلْغَٰلِبُونَ ﴿١٧٣﴾

174. ከእነርሱም (ከመካ ከሓዲዎች) እስከ ጥቂት ጊዜ ድረስ ዙር (ተዋቸው)፡፡

فَتَوَلَّ عَنْهُمْ حَتَّىٰ حِينٍ ﴿١٧٤﴾

175. እያቸውም ወደፊትም (የሚደርስባቸውን) ያያሉ፡፡

وَأَبْصِرْهُمْ فَسَوْفَ يُبْصِرُونَ ﴿١٧٥﴾

176. በቅጣታችንም ያቻኩላሉን?

أَفَبِعَذَابِنَا يَسْتَعْجِلُونَ ﴿١٧٦﴾

177. በቀያቸውም በወረደ ጊዜ የተስፈራሪዎቹ ንጋት ከፋ!

فَإِذَا نَزَلَ بِسَاحَتِهِمْ فَسَآءَ صَبَاحُ ٱلْمُنذَرِينَ ﴿١٧٧﴾

178. እነርሱንም እስከ (ጥቂት) ጊዜ ድረስ ተዋቸው፡፡

وَتَوَلَّ عَنْهُمْ حَتَّىٰ حِينٍ ﴿١٧٨﴾

179. ተመልከትም በእርግጥም ያያሉ፡፡

وَأَبْصِرْ فَسَوْفَ يُبْصِرُونَ ﴿١٧٩﴾

180. የማሸነፍ ጌታ የሆነው ጌታህ ከሚሉት ሁሉ ጠራ፡፡

سُبْحَٰنَ رَبِّكَ رَبِّ ٱلْعِزَّةِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿١٨٠﴾

181. በመልክተኞቹም ላይ ሰላም ይኹኑ፤

وَسَلَٰمٌ عَلَى ٱلْمُرْسَلِينَ ﴿١٨١﴾

182. ምስጋናም ለዓለማት ጌታ ለአላህ ይሁን፡፡

وَٱلْحَمْدُ لِلَّهِ رَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿١٨٢﴾

# ሱረቱ ሷድ

# سورة ص

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

1. ጸ. (ሷድ) የክብር ባለቤት በሆነው ቁርኣን እምላለሁ (ብዙ አማልክት አሉ እንደሚሉት አይደለም)::

2. ይልቁንም እነዚያ የካዱት ሰዎች በትዕቢትና በክርክር ውስጥ ናቸው::

3. ከእነርሱ በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙን አጥፍተናል:: (ጊዜው) የመሸሻና የማምለጫ ጊዜ ሳይሆንም (ለእርዳታ) ተጣሩ::

4. ከእነርሱ የሆነ አስፈራሪም ስለ መጣላቸው ተደነቁ:: ከሓዲዎቹም «ይህ ድግምተኛ (ጠንቋይ) ውሸታም ነው» አሉ::

5. «አማልክቶቹን አንድ አምላክ አደረጋቸውን? ይህ አስደናቂ ነገር ነው» (አሉ)::

6. ከእነርሱም መኳንንቶቹ «ሂዱ፤ በአማልክቶቻችሁም (መግገዛት) ላይ ታገሱ:: ይህ (ከእኛ) የሚፈለግ ነገር ነውና» እያሉ አዘገሙ::

7. «ይህንንም በኋለኛይቱ ሃይማኖት አልሰማንም:: ይህ ውሸትን መፍጠር እንጅ ሌላ አይደለም» (እያሉም)::

8. «ከመካከላችን በእርሱ ላይ ቁርኣን ተወረደን?» (አሉ):: በእውነት እነርሱ ከግሳጼዬ (ከቁርኣን) በመጠራጠር ውስጥ ናቸው:: በእርግጥም ቅጣቴን ገና አልቀመሱም::

9. ይልቁንም የአሸናፊውና የለጋሱ ጌታህ የችሮታው መጋዘኖች እነርሱ ዘንድ ናቸውን?

10. ወይስ የሰማያትና የምድር የመካከላቸውም ንግሥና የእነርሱ ነውን? (ነው ቢሉ) በመሰላሎችም ይውጡ::

11. እዚያ ዘንድ ከአሕዛብ የሆኑ ተሸናፊ ሰራዊት ናቸው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

صٓۚ وَٱلۡقُرۡءَانِ ذِي ٱلذِّكۡرِ ١

بَلِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فِي عِزَّةٖ وَشِقَاقٖ ٢

كَمۡ أَهۡلَكۡنَا مِن قَبۡلِهِم مِّن قَرۡنٖ فَنَادَواْ وَّلَاتَ حِينَ مَنَاصٖ ٣

وَعَجِبُوٓاْ أَن جَآءَهُم مُّنذِرٞ مِّنۡهُمۡۖ وَقَالَ ٱلۡكَٰفِرُونَ هَٰذَا سَٰحِرٞ كَذَّابٌ ٤

أَجَعَلَ ٱلۡأٓلِهَةَ إِلَٰهٗا وَٰحِدًاۖ إِنَّ هَٰذَا لَشَيۡءٌ عُجَابٞ ٥

وَٱنطَلَقَ ٱلۡمَلَأُ مِنۡهُمۡ أَنِ ٱمۡشُواْ وَٱصۡبِرُواْ عَلَىٰٓ ءَالِهَتِكُمۡۖ إِنَّ هَٰذَا لَشَيۡءٞ يُرَادُ ٦

مَا سَمِعۡنَا بِهَٰذَا فِي ٱلۡمِلَّةِ ٱلۡأٓخِرَةِ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا ٱخۡتِلَٰقٌ ٧

أَءُنزِلَ عَلَيۡهِ ٱلذِّكۡرُ مِنۢ بَيۡنِنَاۚ بَلۡ هُمۡ فِي شَكّٖ مِّن ذِكۡرِيۚ بَل لَّمَّا يَذُوقُواْ عَذَابِ ٨

أَمۡ عِندَهُمۡ خَزَآئِنُ رَحۡمَةِ رَبِّكَ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡوَهَّابِ ٩

أَمۡ لَهُم مُّلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَاۖ فَلۡيَرۡتَقُواْ فِي ٱلۡأَسۡبَٰبِ ١٠

جُندٞ مَّا هُنَالِكَ مَهۡزُومٞ مِّنَ ٱلۡأَحۡزَابِ ١١

كَذَّبَتۡ قَبۡلَهُمۡ قَوۡمُ نُوحٖ وَعَادٞ وَفِرۡعَوۡنُ ذُو ٱلۡأَوۡتَادِ ١٢

12. ከእነርሱ በፊት የኑሕ ሕዝቦች፣ ዓድም፣ የችካሎች ባለቤት የሆነው ፈርዖንም አስተባበሉ፡፡

وَثَمُودُ وَقَوۡمُ لُوطٖ وَأَصۡحَٰبُ لۡـَٔيۡكَةِۚ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلۡأَحۡزَابُ ١٣

13. ሰሙድም፣ የሉጥ ሰዎችም፣ የአይከት ሰዎችም (አስተባበሉ)፡፡ እነዚህ አሕዛቦቹ ናቸው፡፡

إِن كُلٌّ إِلَّا كَذَّبَ ٱلرُّسُلَ فَحَقَّ عِقَابِ ١٤

14. ሁሉም መልክተኞቹን ያስዋሹ እንጅ ሌላ አይደሉም፡፡ ቅጣቴም ተረጋገጠባቸው፡፡

وَمَا يَنظُرُ هَٰٓؤُلَآءِ إِلَّا صَيۡحَةٗ وَٰحِدَةٗ مَّا لَهَا مِن فَوَاقٖ ١٥

15. እነዚህም ለእርሷ መመለስ የሌላትን አንዲትን ጩኸት እንጅ ሌላን አይጠባበቁም፡፡

وَقَالُواْ رَبَّنَا عَجِّل لَّنَا قِطَّنَا قَبۡلَ يَوۡمِ ٱلۡحِسَابِ ١٦

16. «ጌታችን ሆይ! ከምርመራው ቀን በፊት መጽሐፋችንን አስቸኩልልን» አሉም፡፡

ٱصۡبِرۡ عَلَىٰ مَا يَقُولُونَ وَٱذۡكُرۡ عَبۡدَنَا دَاوُۥدَ ذَا ٱلۡأَيۡدِۖ إِنَّهُۥٓ أَوَّابٌ ١٧

17. በሚሉት ነገር ላይ ታገስ፡፡ የኀይል ባለቤት የሆነውን ባሪያችንንም ዳውድን አውሳላቸው፡፡ እርሱ በጣም መላሳ ነውና፡፡

إِنَّا سَخَّرۡنَا ٱلۡجِبَالَ مَعَهُۥ يُسَبِّحۡنَ بِٱلۡعَشِيِّ وَٱلۡإِشۡرَاقِ ١٨

18. እኛ ተራራዎችን ከቀትር በኋላና በረፋድም ከእርሱ ጋር የሚያወድሱ ሲሆኑ ገራንለት፡፡

وَٱلطَّيۡرَ مَحۡشُورَةٗۖ كُلّٞ لَّهُۥٓ أَوَّابٞ ١٩

19. በራሪዎችንም (አእዋፍን) የሚሰበሰቡ ሆነው (ገራንለት)፡፡ ሁሉም ለእርሱ (ማወደስ) የሚመላለስ ነው፡፡

وَشَدَدۡنَا مُلۡكَهُۥ وَءَاتَيۡنَٰهُ ٱلۡحِكۡمَةَ وَفَصۡلَ ٱلۡخِطَابِ ٢٠

20. መንግሥቱንም አበረታንለት፡፡ ጥበብንም ንግግርን መለየትንም ሰጠነው፡፡

۞وَهَلۡ أَتَىٰكَ نَبَؤُاْ ٱلۡخَصۡمِ إِذۡ تَسَوَّرُواْ ٱلۡمِحۡرَابَ ٢١

21. የተከራካሪዎቹም ወሬ መጥቶልሃልን? ምኩራቡን በተንጠላጠሉ ጊዜ፡፡

إِذۡ دَخَلُواْ عَلَىٰ دَاوُۥدَ فَفَزِعَ مِنۡهُمۡۖ قَالُواْ لَا تَخَفۡۖ خَصۡمَانِ بَغَىٰ بَعۡضُنَا عَلَىٰ بَعۡضٖ فَٱحۡكُم بَيۡنَنَا بِٱلۡحَقِّ وَلَا تُشۡطِطۡ وَٱهۡدِنَآ إِلَىٰ سَوَآءِ ٱلصِّرَٰطِ ٢٢

22. በዳውድ ላይም በገቡ ጊዜ ከእነርሱም በደነገጠ ጊዜ «አትፍራ፤ (እኛ) ከፊላችን በከፊሉ ላይ ወሰን ያለፈ ሁለት ተከራካሪዎች ነን፡፡ በመካከላችንም በእውነት ፍረድ፡፡ አታዳላም፡፡ ወደ መካከለኛውም መንገድ ምራን፤» አሉት፡፡

إِنَّ هَٰذَآ أَخِي لَهُۥ تِسۡعٞ وَتِسۡعُونَ نَعۡجَةٗ وَلِيَ نَعۡجَةٞ وَٰحِدَةٞ فَقَالَ أَكۡفِلۡنِيهَا وَعَزَّنِي فِي ٱلۡخِطَابِ ٢٣

23. «ይህ ወንድሜ ነው፤ ለእርሱ ዘጠና ዘጠኝ ሴቶች በጎች አሉት፡፡ ለኔም አንዲት ሴት በግ አለችኝ፡፡ እርሷንም ዕድሌ አድርጋት አለኝ፡፡ በንግግርም አሸነፈኝ» አለው፡፡

قَالَ لَقَدۡ ظَلَمَكَ بِسُؤَالِ نَعۡجَتِكَ إِلَىٰ نِعَاجِهِۦۖ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلۡخُلَطَآءِ لَيَبۡغِي بَعۡضُهُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٍ إِلَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَقَلِيلٞ مَّا هُمۡۗ وَظَنَّ دَاوُۥدُ أَنَّمَا فَتَنَّٰهُ فَٱسۡتَغۡفَرَ رَبَّهُۥ وَخَرَّۤ رَاكِعٗاۤ وَأَنَابَ۩ ٢٤

24. «ሴት በግህን ወደ በጎቹ (ለመቀላቀል) በመጠየቁ በእርግጥ በደለህ፡፡ ከተጋሪዎችም ብዙዎቹ ከፊላቸው በከፊሉ ላይ ወሰን ያልፋሉ፡፡ እነዚያ ያመኑትና መልካሞችን የሠሩት ብቻ ሲቀሩ፡፡ እነርሱም በጣም ጥቂቶች ናቸው» አለ፡፡ ዳውድም የፈተንነው መኾኑን ዐወቀ፡፡ ጌታውንም ምሕረትን ለመነ፡፡ ሰጋጅ ኾኖ ወደቀም፡፡ በመጸጸት ተመለሰም፡፡

25. ለእርሱም እኛ ዘንድ መቅረብ (ክብር) መልካም መመለሻም አለው፡፡

فَغَفَرْنَا لَهُۥ ذَٰلِكَۖ وَإِنَّ لَهُۥ عِندَنَا لَزُلْفَىٰ وَحُسْنَ مَـَٔابٍ ﴿٢٥﴾

26. ዳውድ ሆይ! እኛ በምድር ላይ ምትክ አድርገንሃልና በሰዎች መካከል በእውነት ፍረድ፡፡ ዝንባሌህንም አትከተል፤ከአላህ መንገድ ያሳሳትሃልና፡፡ እነዚያ ከአላህ መንገድ የሚሳሳቱ የምርመራውን ቀን በመርሳታቸው ለእነርሱ ብርቱ ቅጣት አላቸው፡፡

يَٰدَاوُۥدُ إِنَّا جَعَلْنَٰكَ خَلِيفَةً فِى ٱلْأَرْضِ فَٱحْكُم بَيْنَ ٱلنَّاسِ بِٱلْحَقِّ وَلَا تَتَّبِعِ ٱلْهَوَىٰ فَيُضِلَّكَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَضِلُّونَ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ لَهُمْ عَذَابٌ شَدِيدٌۢ بِمَا نَسُوا۟ يَوْمَ ٱلْحِسَابِ ﴿٢٦﴾

27. ሰማይንና ምድርን በመካከላቸውም ያለውን ሁሉ ለከንቱ አልፈጠርንም፡፡ ይህ የእነዚያ የካዱት ሰዎች ጥርጣሬ ነው፡፡ ለእነዚያም ለካዱት ሰዎች ከእሳት ወዮላቸው!

وَمَا خَلَقْنَا ٱلسَّمَآءَ وَٱلْأَرْضَ وَمَا بَيْنَهُمَا بَٰطِلًاۚ ذَٰلِكَ ظَنُّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ۚ فَوَيْلٌ لِّلَّذِينَ كَفَرُوا۟ مِنَ ٱلنَّارِ ﴿٢٧﴾

28. በእውነቱ እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን በምድር ውስጥ እንደሚያጠፉት እናደርጋለን? ወይስ አላህን ፈሪዎቹን እንደ ከሓዲዎቹ እናደርጋለን?

أَمْ نَجْعَلُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَعَمِلُوا۟ ٱلصَّٰلِحَٰتِ كَٱلْمُفْسِدِينَ فِى ٱلْأَرْضِ أَمْ نَجْعَلُ ٱلْمُتَّقِينَ كَٱلْفُجَّارِ ﴿٢٨﴾

29. (ይህ) ወዳንተ ያወረድነው ብሩክ መጽሐፍ ነው፡፡ አንቀጾቹን እንዲያስተነትኑና የአእምሮዎች ባለቤቶችም እንዲገሰጹ (አወረድነው)፡፡

كِتَٰبٌ أَنزَلْنَٰهُ إِلَيْكَ مُبَٰرَكٌ لِّيَدَّبَّرُوٓا۟ ءَايَٰتِهِۦ وَلِيَتَذَكَّرَ أُو۟لُوا۟ ٱلْأَلْبَٰبِ ﴿٢٩﴾

30. ለዳውድም ሱለይማንን ሰጠነው፡፡ ምን ያምር ባሪያ! (ሱለይማን)፣ እርሱ መላሳ ነው፡፡

وَوَهَبْنَا لِدَاوُۥدَ سُلَيْمَٰنَۚ نِعْمَ ٱلْعَبْدُ إِنَّهُۥٓ أَوَّابٌ ﴿٣٠﴾

31. በእርሱ ላይ ከቀትር በኋላ በሦስት እግሮችና በአራተኛዋ ኮቴ ጫፍ የሚቆሙ ጮሌዎች ፈረሶች በተቀረቡለት ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذْ عُرِضَ عَلَيْهِ بِٱلْعَشِىِّ ٱلصَّٰفِنَٰتُ ٱلْجِيَادُ ﴿٣١﴾

32. አለም «እኔ (ፀሐይ) በግርዶ እስከ ተደበቀች ድረስ ከጌታዬ ማስታወስ ፋንታ ፈረስን መውደድን መረጥኩ፡ ፡»

فَقَالَ إِنِّىٓ أَحْبَبْتُ حُبَّ ٱلْخَيْرِ عَن ذِكْرِ رَبِّى حَتَّىٰ تَوَارَتْ بِٱلْحِجَابِ ﴿٣٢﴾

33. «በእኔ ላይ መልሷት» (አለ) አጋዶችዋንና አንገቶችዋንም ማበስ ያዘ፡፡

رُدُّوهَا عَلَىَّۖ فَطَفِقَ مَسْحًۢا بِٱلسُّوقِ وَٱلْأَعْنَاقِ ﴿٣٣﴾

34. ሱለይማንንም በእርግጥ ፈተንነው፡፡ በመንበሩም ላይ አካልን ጣልን፡፡ ከዚያም በመጸጸት ተመለሰ፡፡

وَلَقَدْ فَتَنَّا سُلَيْمَٰنَ وَأَلْقَيْنَا عَلَىٰ كُرْسِيِّهِۦ جَسَدًا ثُمَّ أَنَابَ ﴿٣٤﴾

35. «ጌታዬ ሆይ! ለእኔ ማር፡፡ ከእኔ በኋላ ለአንድም የማይገባንም ንግሥና ስጠኝ፡፡ አንተ ለጋሱ አንተ ብቻ ነህና» አለ፡፡

قَالَ رَبِّ ٱغْفِرْ لِى وَهَبْ لِى مُلْكًا لَّا يَنۢبَغِى لِأَحَدٍ مِّنۢ بَعْدِىٓۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلْوَهَّابُ ﴿٣٥﴾

36. ነፋስንም በትእዛዙ ወደፈለገበት ስፍራ ልዝብ ኾና የምትፈስ ስትኾን ገራንለት፡፡

فَسَخَّرْنَا لَهُ ٱلرِّيحَ تَجْرِى بِأَمْرِهِۦ رُخَآءً حَيْثُ أَصَابَ ﴿٣٦﴾

| | |
|---|---|
| 37. ሰይጣናትንም ገንቢዎችንና ሰጣሚዎችን ሁሉ (ገራንለት)፡፡ | وَٱلشَّيَٰطِينَ كُلَّ بَنَّآءٖ وَغَوَّاصٖ ﴿٣٧﴾ |
| 38. ሌሎችንም በፍንጆች ተቆራኞችን (ገራንለት)፡፡ | وَءَاخَرِينَ مُقَرَّنِينَ فِي ٱلۡأَصۡفَادِ ﴿٣٨﴾ |
| 39. «ይህ ስጦታችን ነው፡፡ ያለግምት ለግስ፤ ወይም ጨብጥ» (አልነው)፡፡ | هَٰذَا عَطَآؤُنَا فَٱمۡنُنۡ أَوۡ أَمۡسِكۡ بِغَيۡرِ حِسَابٖ ﴿٣٩﴾ |
| 40. ለእርሱም እኛ ዘንድ መቅረብ፤ መልካም መመለሻም በእርግጥ አልለው፡፡ | وَإِنَّ لَهُۥ عِندَنَا لَزُلۡفَىٰ وَحُسۡنَ مَـَٔابٖ ﴿٤٠﴾ |
| 41. ባሪያችንን አዩብንም አውሳላቸው፡፡ «እኔ ሰይጣን በጉዳትና በስቃይ ነካኝ» ሲል ጌታውን በተጣራ ጊዜ፡፡ | وَٱذۡكُرۡ عَبۡدَنَآ أَيُّوبَ إِذۡ نَادَىٰ رَبَّهُۥٓ أَنِّي مَسَّنِيَ ٱلشَّيۡطَٰنُ بِنُصۡبٖ وَعَذَابٍ ﴿٤١﴾ |
| 42. «በእግርህ (ምድርን) ምታ፡፡ ይህ ቀዝቃዛ መታጠቢያ መጠጥም ነው» (ተባለ)፡፡ | ٱرۡكُضۡ بِرِجۡلِكَۖ هَٰذَا مُغۡتَسَلُۢ بَارِدٞ وَشَرَابٞ ﴿٤٢﴾ |
| 43. ለእርሱም ከእኛ ዘንድ ለችሮታ ባለአእምሮዎችንም ለመገሠጽ ቤተሰቦቹን ከእነርሱም ጋር መሰላቸውን ሰጠነው፡፡ | وَوَهَبۡنَا لَهُۥٓ أَهۡلَهُۥ وَمِثۡلَهُم مَّعَهُمۡ رَحۡمَةٗ مِّنَّا وَذِكۡرَىٰ لِأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ ﴿٤٣﴾ |
| 44. «በእጅህም ጭብጥ አርጩሜን ያዝ፡፡ በእርሱም (ሚስትህን) ምታ፡፡ ማላህንም አታፍርስ» (አልነው)፡፡ እኛ ታጋሽ ኾኖ አገኘነው፡፡ ምን ያምር ባሪያ እርሱ በጣም መላሳ ነው፡፡ | وَخُذۡ بِيَدِكَ ضِغۡثٗا فَٱضۡرِب بِّهِۦ وَلَا تَحۡنَثۡۗ إِنَّا وَجَدۡنَٰهُ صَابِرٗاۚ نِّعۡمَ ٱلۡعَبۡدُ إِنَّهُۥٓ أَوَّابٞ ﴿٤٤﴾ |
| 45. ባሮቻችንንም ኢብራሂምን፣ ኢስሐቅንና ያዕቆብንም፣ የኀይልና የማስተዋል ባለቤቶች የኾኑን አውሳላቸው፡፡ | وَٱذۡكُرۡ عِبَٰدَنَآ إِبۡرَٰهِيمَ وَإِسۡحَٰقَ وَيَعۡقُوبَ أُوْلِي ٱلۡأَيۡدِي وَٱلۡأَبۡصَٰرِ ﴿٤٥﴾ |
| 46. እኛ ጥሩ በኾነች ጠባይ መረጥናቸው፡፡ (እርሷም) የመጨረሻይቱን አገር ማስታወስ ናት፡፡ | إِنَّآ أَخۡلَصۡنَٰهُم بِخَالِصَةٖ ذِكۡرَى ٱلدَّارِ ﴿٤٦﴾ |
| 47. እነርሱም እኛ ዘንድ ከመልካሞቹ ምርጦች ናቸው፡ ፡ | وَإِنَّهُمۡ عِندَنَا لَمِنَ ٱلۡمُصۡطَفَيۡنَ ٱلۡأَخۡيَارِ ﴿٤٧﴾ |
| 48. ኢስማዒልንም፣ አልየሰዕንም፣ ዙልኪፍልንም አውሳ፡፡ ሁሉም ከበላጮቹ ናቸው፡፡ | وَٱذۡكُرۡ إِسۡمَٰعِيلَ وَٱلۡيَسَعَ وَذَا ٱلۡكِفۡلِۖ وَكُلّٞ مِّنَ ٱلۡأَخۡيَارِ ﴿٤٨﴾ |
| 49. ይህ መልካም ዝና ነው፡፡ ለአላህ ፈሪዎችም በእርግጥ ውብ የኾነ መመለሻ አላቸው፡፡ | هَٰذَا ذِكۡرٞۚ وَإِنَّ لِلۡمُتَّقِينَ لَحُسۡنَ مَـَٔابٖ ﴿٤٩﴾ |
| 50. በሮቻቸው ለእነርሱ የተከፈቱ ሲኾኑ የመኖሪያ ገነቶች አሏቸው፡፡ | جَنَّٰتِ عَدۡنٖ مُّفَتَّحَةٗ لَّهُمُ ٱلۡأَبۡوَٰبُ ﴿٥٠﴾ |
| 51. በእርሷ ውስጥ የተደገፉ ኾነው በውስጧ በብዙ እሸቶችና በመጠጥም ያዝዛሉ፡፡ | مُتَّكِـِٔينَ فِيهَا يَدۡعُونَ فِيهَا بِفَٰكِهَةٖ كَثِيرَةٖ وَشَرَابٖ ﴿٥١﴾ |
| 52. እነርሱ ዘንድም ዓይኖቻቸውን (በባሎቻቸው ላይ) አሳጣሪዎች እኩያዎች (ሴቶች) አሉሉ፡፡ | ۞وَعِندَهُمۡ قَٰصِرَٰتُ ٱلطَّرۡفِ أَتۡرَابٌ ﴿٥٢﴾ |

53. ይህ ለምርመራው ቀን የምትቀጠሩት ተሰፋ ነው፡፡

هَٰذَا مَا تُوعَدُونَ لِيَوۡمِ ٱلۡحِسَابِ ٥٣

54. ይህ ሲሳያችን ነው፡፡ ለእርሱ ምንም ማለቅ የለውም፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَرِزۡقُنَا مَا لَهُۥ مِن نَّفَادٍ ٥٤

55. ይህ (ለአማኞች ነው)፡፡ ለጠማሞችም በጣም የከፋ መመለሻ አላቸው፡፡

هَٰذَاۚ وَإِنَّ لِلطَّٰغِينَ لَشَرَّ مَـَٔابٖ ٥٥

56. የሚገቧት ስትኾን ገሀነም (አለቻቸው)፡፡ ምንጣፊቱም ምንኛ ከፋች፡፡

جَهَنَّمَ يَصۡلَوۡنَهَا فَبِئۡسَ ٱلۡمِهَادُ ٥٦

57. ይህ (ለከሓዲዎች ነው)፡፡ ይቅመሱትም፡፡ የፈላ ውሃና እኸ ነው፡፡

هَٰذَا فَلۡيَذُوقُوهُ حَمِيمٞ وَغَسَّاقٞ ٥٧

58. ሌላም ከመሰሉ ዓይነቶች አልሉ፡፡

وَءَاخَرُ مِن شَكۡلِهِۦٓ أَزۡوَٰجٌ ٥٨

59. ይህ ከእናንተ ጋር በመጋፈጥ ገቢ ጭፍራ ነው፤ (ይባላሉ)፡፡ ለእነርሱ አይስፋቸው፡፡ እነርሱ እሳትን ገቢዎች ናቸውና (ይላሉ)፡፡

هَٰذَا فَوۡجٞ مُّقۡتَحِمٞ مَّعَكُمۡ لَا مَرۡحَبَۢا بِهِمۡۚ إِنَّهُمۡ صَالُواْ ٱلنَّارِ ٥٩

60. (ተከታዮቹ) ይላሉ «ይልቁን እናንተ አይስፋችሁ፡፡ እናንተ (ክህደቱን) ለእኛ አቀረባችሁት፡፡ መርጊያይቱም (ገሀነም) ከፋች፡፡»

قَالُواْ بَلۡ أَنتُمۡ لَا مَرۡحَبَۢا بِكُمۡۖ أَنتُمۡ قَدَّمۡتُمُوهُ لَنَاۖ فَبِئۡسَ ٱلۡقَرَارُ ٦٠

61. «ጌታችን ሆይ! ይህንን ያቀረበልንን ሰው በእሳት ውስጥ እጥፍን ቅጣት ጨምርለት» ይላሉ፡፡

قَالُواْ رَبَّنَا مَن قَدَّمَ لَنَا هَٰذَا فَزِدۡهُ عَذَابٗا ضِعۡفٗا فِي ٱلنَّارِ ٦١

62. ይላሉም «ለእኛ ምን አለን? ከመጥፎዎች እንቆጥራቸው የነበሩትን ሰዎች (እዚህ) አናይምሳ፡፡»

وَقَالُواْ مَا لَنَا لَا نَرَىٰ رِجَالٗا كُنَّا نَعُدُّهُم مِّنَ ٱلۡأَشۡرَارِ ٦٢

63. «መቀለጃ አድርገን ያዝናቸውን? ወይስ ዓይኖቻችን ከእነሱ ዋለሉ?»

أَتَّخَذۡنَٰهُمۡ سِخۡرِيًّا أَمۡ زَاغَتۡ عَنۡهُمُ ٱلۡأَبۡصَٰرُ ٦٣

64. ይህ በእርግጥ እምነት ነው፡፡ (እርሱም) የእሳት ሰዎች (የእርስ በእርስ) መካሰስ ነው፡፡

إِنَّ ذَٰلِكَ لَحَقّٞ تَخَاصُمُ أَهۡلِ ٱلنَّارِ ٦٤

65. «እኔ አስፈራሪ ብቻ ነኝ፡፡ ኀያል አንድ ከኾነው አላህ በቀር ምንም አምላክ የለም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّمَآ أَنَا۠ مُنذِرٞۖ وَمَا مِنۡ إِلَٰهٍ إِلَّا ٱللَّهُ ٱلۡوَٰحِدُ ٱلۡقَهَّارُ ٦٥

66. «የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ጌታ አሸናፊው መሓሪው ነው፡፡»

رَبُّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَا ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡغَفَّٰرُ ٦٦

67. በላቸው «እርሱ (ቁርኣን) ታላቅ ዜና ነው፡፡

قُلۡ هُوَ نَبَؤٌاْ عَظِيمٌ ٦٧

68. «እናንተ ከእርሱ ዘንጊዎች ናችሁ፡፡

أَنتُمۡ عَنۡهُ مُعۡرِضُونَ ٦٨

| | |
|---|---|
| 69. (በአደም ነገር) «በሚከራከሩ ጊዜ በላይኛው ሰራዊት ለእኔ ምንም ዕውቀት አልነበረኝም፡፡ | مَا كَانَ لِيَ مِنۡ عِلۡمِۭ بِٱلۡمَلَإِ ٱلۡأَعۡلَىٰٓ إِذۡ يَخۡتَصِمُونَ ۝٦٩ |
| 70. «ወደእኔም አስፈራሪ ገላጭ መኾኔ እንጂ ሌላ አይወረድልኝም» (በል)፡፡ | إِن يُوحَىٰٓ إِلَيَّ إِلَّآ أَنَّمَآ أَنَا۠ نَذِيرٞ مُّبِينٌ ۝٧٠ |
| 71. ጌታህ «ለመላእክት እኔ ሰውን ከጭቃ ፈጣሪ ነኝ ባለ ጊዜ» (አስታውስ)፡፡ | إِذۡ قَالَ رَبُّكَ لِلۡمَلَٰٓئِكَةِ إِنِّي خَٰلِقُۢ بَشَرٗا مِّن طِينٖ ۝٧١ |
| 72. «ፍጥረቱንም ባስተካከልኩና ከመንፈሴ በነፋሁበት ጊዜ ለእርሱ ሰጋጆች ኾናችሁ ውደቁ» (አልኩ)፡፡ | فَإِذَا سَوَّيۡتُهُۥ وَنَفَخۡتُ فِيهِ مِن رُّوحِي فَقَعُواْ لَهُۥ سَٰجِدِينَ ۝٧٢ |
| 73. መላእክትም መላውም ባንድነት ሰገዱ፡፡ | فَسَجَدَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ كُلُّهُمۡ أَجۡمَعُونَ ۝٧٣ |
| 74. ኢብሊስ ብቻ ሲቀር፡፡ ኮራ፤ ከከሓዲዎቹም ነበር፡፡ | إِلَّآ إِبۡلِيسَ ٱسۡتَكۡبَرَ وَكَانَ مِنَ ٱلۡكَٰفِرِينَ ۝٧٤ |
| 75. (አላህም) «ኢብሊስ ሆይ! በሁለት እጆቼ (በኃይሌ) ለፈጠርኩት ከመስገድ ምን ከለከለህ? (አሁን) ኮራህን? ወይስ (ፊቱኑ) ከትዕቢተኞቹ ነበርክ?» አለው፡፡ | قَالَ يَٰٓإِبۡلِيسُ مَا مَنَعَكَ أَن تَسۡجُدَ لِمَا خَلَقۡتُ بِيَدَيَّۖ أَسۡتَكۡبَرۡتَ أَمۡ كُنتَ مِنَ ٱلۡعَالِينَ ۝٧٥ |
| 76. «እኔ ከእርሱ በላጭ ነኝ፡፡ ከእሳት ፈጠርከኝ፤ ከጭቃም ፈጠርከው» አለ፡፡ | قَالَ أَنَا۠ خَيۡرٞ مِّنۡهُ خَلَقۡتَنِي مِن نَّارٖ وَخَلَقۡتَهُۥ مِن طِينٖ ۝٧٦ |
| 77. (አላህ) አለው «ከእርሷ ውጣ፤ አንተ የተባረርክ ነህና፡፡» | قَالَ فَٱخۡرُجۡ مِنۡهَا فَإِنَّكَ رَجِيمٞ ۝٧٧ |
| 78. «እርግማኔም እስከ ፍርዱ ቀን ድረስ ባንተ ላይ ይኹን፡፡» | وَإِنَّ عَلَيۡكَ لَعۡنَتِيٓ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلدِّينِ ۝٧٨ |
| 79. «ጌታዬ ሆይ! እስከሚቀሰቀሱበት ቀን ድረስ አቆየኝም» አለ፡፡ | قَالَ رَبِّ فَأَنظِرۡنِيٓ إِلَىٰ يَوۡمِ يُبۡعَثُونَ ۝٧٩ |
| 80. (አላህም) አለው «አንተ ከሚቆዩት ነህ፡፡» | قَالَ فَإِنَّكَ مِنَ ٱلۡمُنظَرِينَ ۝٨٠ |
| 81. «እስከ ታወቀው ወቅት ቀን ድረስ፡፡» | إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡوَقۡتِ ٱلۡمَعۡلُومِ ۝٨١ |
| 82. (እርሱም) አለ «በአሸናፊነትህ ይኹንብኝ፤ በመላ አሳስታቸዋለሁ፡፡» | قَالَ فَبِعِزَّتِكَ لَأُغۡوِيَنَّهُمۡ أَجۡمَعِينَ ۝٨٢ |
| 83. «ከእነርሱ ምርጥ የኾኑት ባሮችህ ብቻ ሲቀሩ፡፡» | إِلَّا عِبَادَكَ مِنۡهُمُ ٱلۡمُخۡلَصِينَ ۝٨٣ |
| 84. (አላህ) አለው «እውነቱም (ከኔ ነው)፡፡ እውነትንም እላለሁ፡፡ | قَالَ فَٱلۡحَقُّ وَٱلۡحَقَّ أَقُولُ ۝٨٤ |
| 85. ከአንተና ከእነርሱ ውስጥ ከተከተሉህ ባንድ ላይ ገሀነምን በእርግጥ እሞላታለሁ፡፡» | لَأَمۡلَأَنَّ جَهَنَّمَ مِنكَ وَمِمَّن تَبِعَكَ مِنۡهُمۡ أَجۡمَعِينَ ۝٨٥ |

86. በላቸው «በእርሱ ላይ ምንም ዋጋ አልጠይቃችሁም፤ እኔም ከተግደርዳሪዎቹ አይደለሁም፡፡

قُلْ مَآ أَسْـَٔلُكُمْ عَلَيْهِ مِنْ أَجْرٍ وَمَآ أَنَا۠ مِنَ ٱلْمُتَكَلِّفِينَ ﴿٨٦﴾

87. «እርሱ (ቁርኣን) ለዓለማት መገሠጫ እንጂ ሌላ አይደለም፡፡

إِنْ هُوَ إِلَّا ذِكْرٌ لِّلْعَـٰلَمِينَ ﴿٨٧﴾

88. «ትንቢቱንም (እውነት መኾኑን) ከጊዜ በኋላ በእርግጥ ታውቁታላችሁ፡፡»

وَلَتَعْلَمُنَّ نَبَأَهُۥ بَعْدَ حِينٍۭ ﴿٨٨﴾

# ሱረቱ አል ዙመር

# سورة الزمر

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَـٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. የመጽሐፉ መወረድ አሸናፊው ጥበበኛው ከኾነው አላህ ነው፡፡

تَنزِيلُ ٱلْكِتَـٰبِ مِنَ ٱللَّهِ ٱلْعَزِيزِ ٱلْحَكِيمِ ﴿١﴾

2. እኛ ወደ አንተ መጽሐፉን በእውነት (የተመላ) ሲኾን አወረድነው፡፡ አላህንም ሃይማኖትን ለእርሱ ብቻ ያጠራህ ኾነህ ተገዛው፡፡

إِنَّآ أَنزَلْنَآ إِلَيْكَ ٱلْكِتَـٰبَ بِٱلْحَقِّ فَٱعْبُدِ ٱللَّهَ مُخْلِصًا لَّهُ ٱلدِّينَ ﴿٢﴾

3. ንቁ! ፍጹም ጥሩ የኾነው ሃይማኖት የአላህ ብቻ ነው፡፡ እነዚያም ከእርሱ ሌላ (ጣዖታትን) ረዳቶች የያዙት «ወደ አላህ ማቃረብን እንዲያቀርቡን እንጅ ለሌላ አንገዛቸውም» (ይላሉ)፡፡ አላህ በዚያ እነርሱ በእርሱ በሚለያዩበት ነገር በመካከላቸው ይፈርዳል፡፡ አላህ እርሱ ውሸታም ከሓዲ የኾነን ሰው አያቀናም፡፡

أَلَا لِلَّهِ ٱلدِّينُ ٱلْخَالِصُ ۚ وَٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُوا۟ مِن دُونِهِۦٓ أَوْلِيَآءَ مَا نَعْبُدُهُمْ إِلَّا لِيُقَرِّبُونَآ إِلَى ٱللَّهِ زُلْفَىٰٓ إِنَّ ٱللَّهَ يَحْكُمُ بَيْنَهُمْ فِى مَا هُمْ فِيهِ يَخْتَلِفُونَ ۗ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهْدِى مَنْ هُوَ كَـٰذِبٌ كَفَّارٌ ﴿٣﴾

4. አላህ ልጅን መያዝ በፈለገ ኖሮ ከሚፈጥረው ውስጥ የሚሻውን ይመርጥ ነበር፡፡ ጥራት ተገባው፡፡ እርሱ አሸናፊው አንዱ አላህ ነው፡፡

لَّوْ أَرَادَ ٱللَّهُ أَن يَتَّخِذَ وَلَدًا لَّٱصْطَفَىٰ مِمَّا يَخْلُقُ مَا يَشَآءُ ۚ سُبْحَـٰنَهُۥ ۖ هُوَ ٱللَّهُ ٱلْوَٰحِدُ ٱلْقَهَّارُ ﴿٤﴾

5. ሰማያትንና ምድርን በእውነት ፈጠረ፡፡ ሌሊትን በቀን ላይ ይጠቀልላል፡፡ ቀንንም በሌሊት ላይ ይጠቀልላል፤ ፀሐይንና ጨረቃንም ገራ፡፡ ሁሉም ለተወሰነ ጊዜ ይሮጣሉ፡፡ ንቁ! እርሱ አሸናፊው መሓሪው ነው፡፡

خَلَقَ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ بِٱلْحَقِّ ۖ يُكَوِّرُ ٱلَّيْلَ عَلَى ٱلنَّهَارِ وَيُكَوِّرُ ٱلنَّهَارَ عَلَى ٱلَّيْلِ ۖ وَسَخَّرَ ٱلشَّمْسَ وَٱلْقَمَرَ ۖ كُلٌّ يَجْرِى لِأَجَلٍ مُّسَمًّى ۗ أَلَا هُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْغَفَّـٰرُ ﴿٥﴾

6. ከአንዲት ነፍስ ፈጠራችሁ፡፡ ከዚያም ከእርሷ መቀናጆዋን አደረገ፡፡ ለእናንተም ከግመልና ከከብት፣ ከፍየል፣ ከበግ ስምንት ዓይነቶችን (ወንድና ሴት) አወረደ፡፡ በእናቶቻችሁ ሆዶች ውስጥ በሦስት ጨለማዎች ውስጥ ከመፍጠር በኋላ (ሙሉ) መፍጠርን ይፈጠራችኋል፡፡ ይህ ጌታችሁ አላህ ነው፡፡ ስልጣኑ የርሱ ብቻ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ ታዲያ ወዴት ትዞራላችሁ፡፡

خَلَقَكُم مِّن نَّفۡسٖ وَٰحِدَةٖ ثُمَّ جَعَلَ مِنۡهَا زَوۡجَهَا وَأَنزَلَ لَكُم مِّنَ ٱلۡأَنۡعَٰمِ ثَمَٰنِيَةَ أَزۡوَٰجٖۚ يَخۡلُقُكُمۡ فِي بُطُونِ أُمَّهَٰتِكُمۡ خَلۡقٗا مِّنۢ بَعۡدِ خَلۡقٖ فِي ظُلُمَٰتٖ ثَلَٰثٖۚ ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبُّكُمۡ لَهُ ٱلۡمُلۡكُۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ فَأَنَّىٰ تُصۡرَفُونَ ٦

7. ብትክዱ አላህ ከእናንተ የተብቃቃ ነው፡፡ ለባሪያዎቹም ክህደትን አይወድም፡፡ ብታመሰግኑም፤ እርሱን ይወድላችኋል፡፡ ማንኛይቱም ኃጢአትን ተሸካሚ ነፍስ የሌላይቱን ኃጢአት አትሸከምም፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደ ጌታችሁ ነው፡፡ ትሠሩት የነበራችሁትንም ይነግራችኋል፡፡ እርሱ በልቦች ውስጥ ያሉትን ዐዋቂ ነውና፡፡

إِن تَكۡفُرُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَنِيٌّ عَنكُمۡۖ وَلَا يَرۡضَىٰ لِعِبَادِهِ ٱلۡكُفۡرَۖ وَإِن تَشۡكُرُواْ يَرۡضَهُ لَكُمۡۗ وَلَا تَزِرُ وَازِرَةٞ وِزۡرَ أُخۡرَىٰۚ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّكُم مَّرۡجِعُكُمۡ فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَۚ إِنَّهُۥ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٧

8. ሰውንም ጉዳት ባገኘው ጊዜ ጌታውን ወደርሱ ተመላሽ ኾኖ ይጠራል፡፡ ከዚያም ከእርሱ ዘንድ ጸጋን በሰጠው ጊዜ ያንን ከዚያ በፊት ወደርሱ ይጸልይበት የነበረውን (መከራ) ይረሳል፡፡ ከመንገዱ ለማሳሳትም ለአላህ ባላንጣዎችን ያደርጋል፡፡ «በክህደትህ ጥቂትን ተጣቀም፡፡ አንተ በእርግጥ ከእሳት ጓዶች ነህ» በለው፡፡

۞وَإِذَا مَسَّ ٱلۡإِنسَٰنَ ضُرّٞ دَعَا رَبَّهُۥ مُنِيبًا إِلَيۡهِ ثُمَّ إِذَا خَوَّلَهُۥ نِعۡمَةٗ مِّنۡهُ نَسِيَ مَا كَانَ يَدۡعُوٓاْ إِلَيۡهِ مِن قَبۡلُ وَجَعَلَ لِلَّهِ أَندَادٗا لِّيُضِلَّ عَن سَبِيلِهِۦۚ قُلۡ تَمَتَّعۡ بِكُفۡرِكَ قَلِيلًا إِنَّكَ مِنۡ أَصۡحَٰبِ ٱلنَّارِ ٨

9. እርሱ የመጨረሻይቱን ዓለም (ቅጣት) የሚፈራ የጌታውንም ችሮታ የሚከጅል ሲኾን በሌሊት ሰዓቶች ሰጋጅና ቋሚ ኾኖ ለጌታው የሚገዛ ሰው (እንደ ተስፋ ቢሱ ከሓዲ ነውን? በለው)፡፡ «እነዚያ የሚያውቁና እነዚያ የማያውቁ ይስተካከላሉን?» በላቸው፡፡ የሚገነዘቡት ባለ አእምሮዎቹ ብቻ ናቸው፡፡

أَمَّنۡ هُوَ قَٰنِتٌ ءَانَآءَ ٱلَّيۡلِ سَاجِدٗا وَقَآئِمٗا يَحۡذَرُ ٱلۡأٓخِرَةَ وَيَرۡجُواْ رَحۡمَةَ رَبِّهِۦۗ قُلۡ هَلۡ يَسۡتَوِي ٱلَّذِينَ يَعۡلَمُونَ وَٱلَّذِينَ لَا يَعۡلَمُونَۗ إِنَّمَا يَتَذَكَّرُ أُوْلُواْ ٱلۡأَلۡبَٰبِ ٩

10. (ጌታችሁ) «እናንተ ያመናችሁ ባሮቼ ሆይ! ጌታችሁን ፍሩ፡፡ ለነዚያ በዚህች በቅርቢቱ ዓለም መልካም ለሠሩት መልካም ምንዳ አላቸው፡፡ የአላህ ምድርም ሰፊ ናት፤ (ብትቸገሩ ተሰደዱ)፡፡ ታጋሾቹ ምንዳቸውን የሚሰጡት ያለግምት ነው» (ይላል) በላቸው፡፡

قُلۡ يَٰعِبَادِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ رَبَّكُمۡۚ لِلَّذِينَ أَحۡسَنُواْ فِي هَٰذِهِ ٱلدُّنۡيَا حَسَنَةٞۗ وَأَرۡضُ ٱللَّهِ وَٰسِعَةٌۗ إِنَّمَا يُوَفَّى ٱلصَّٰبِرُونَ أَجۡرَهُم بِغَيۡرِ حِسَابٖ ١٠

11. በል «እኔ አላህን ሃይማኖትን ለርሱ ያጠራሁ ኾኜ እንድግገዛው ታዘዝኩ፡፡

قُلۡ إِنِّيٓ أُمِرۡتُ أَنۡ أَعۡبُدَ ٱللَّهَ مُخۡلِصٗا لَّهُ ٱلدِّينَ ١١

12. «የሙስሊሞችም መጀመሪያ እንድኾን ታዘዝኩ፡፡»

وَأُمِرۡتُ لِأَنۡ أَكُونَ أَوَّلَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ١٢

13. «እኔ ከጌታዬ ባምጽ የታላቁን ቀን ቅጣት እፈራለሁ» በል፡፡

قُلۡ إِنِّيٓ أَخَافُ إِنۡ عَصَيۡتُ رَبِّي عَذَابَ يَوۡمٍ عَظِيمٖ ١٣

14. አላህን «ሃይማኖቴን ለእርሱ ያጠራሁ ኾኜ እግገዛዋለሁ» በል፡፡

قُلِ ٱللَّهَ أَعۡبُدُ مُخۡلِصٗا لَّهُۥ دِينِي ١٤

15. «ከእርሱ ሌላ የሻችሁትን ተገዙ፡፡ ከሳሪዎች ማለት እነዚያ በትንሣኤ ቀን ነፍሶቻቸውንና ቤተሰቦቻቸውን ያከሰሩ ናቸው፡፡ ንቁ! ይህ እርሱ ግልጽ ከሳራ ነው» በላቸው፡፡

فَٱعۡبُدُواْ مَا شِئۡتُم مِّن دُونِهِۦۗ قُلۡ إِنَّ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ وَأَهۡلِيهِمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۗ أَلَا ذَٰلِكَ هُوَ ٱلۡخُسۡرَانُ ٱلۡمُبِينُ ١٥

16. ለእነርሱ ከበላያቸው ከእሳት የኾኑ (ድርብርብ) ጥላዎች አልሏቸው፡፡ ከበታቻቸውም ጥላዎች አልሏቸው። ይህ አላህ ባሮቹን (እንዲጠነቀቁ) በእርሱ ያስፈራራበታል፡፡ «ባሮቼ ሆይ! ስለዚህ ፍሩኝ፡፡»

لَهُم مِّن فَوۡقِهِمۡ ظُلَلٞ مِّنَ ٱلنَّارِ وَمِن تَحۡتِهِمۡ ظُلَلٞۚ ذَٰلِكَ يُخَوِّفُ ٱللَّهُ بِهِۦ عِبَادَهُۥۚ يَٰعِبَادِ فَٱتَّقُونِ ١٦

17. እነዚያም ጣዖታትን የሚግገዟት ከመኾን የራቁ ወደ አላህም የዞሩ ለእነርሱ ብስራት አልላቸው፡፡ ስለዚህ ባሮቼን አብስር፡፡

وَٱلَّذِينَ ٱجۡتَنَبُواْ ٱلطَّٰغُوتَ أَن يَعۡبُدُوهَا وَأَنَابُوٓاْ إِلَى ٱللَّهِ لَهُمُ ٱلۡبُشۡرَىٰۚ فَبَشِّرۡ عِبَادِ ١٧

18. እነዚያን ንግግርን የሚያዳምጡትንና መልካሙን የሚከተሉትን (አብስር)፡፡ እነዚያ እነርሱ አላህ የመራቸው ናቸው፡፡ እነዚያም እነርሱ ባለአእምሮዎቹ ናቸው፡፡

ٱلَّذِينَ يَسۡتَمِعُونَ ٱلۡقَوۡلَ فَيَتَّبِعُونَ أَحۡسَنَهُۥٓۚ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ هَدَىٰهُمُ ٱللَّهُۖ وَأُوْلَٰٓئِكَ هُمۡ أُوْلُواْ ٱلۡأَلۡبَٰبِ ١٨

19. በእርሱ ላይ የቅጣት ቃል የተረጋገጠችበትን ሰው (ትመራዋለህን?) አንተ በእሳት ውስጥ ያለን ሰው ታድናለህን?

أَفَمَنۡ حَقَّ عَلَيۡهِ كَلِمَةُ ٱلۡعَذَابِ أَفَأَنتَ تُنقِذُ مَن فِي ٱلنَّارِ ١٩

20. ግን እነዚያ ጌታቸውን የፈሩ ለእነርሱ ከበላያቸው የታነጹ ሰገነቶች ያሏቸው ሰገነቶች ከስሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው የኾኑ አልሏቸው፡፡ (ይህንን) አላህ ቃል ገባላቸው፡፡ አላህ ቃሉን አያፈርስም፡፡

لَٰكِنِ ٱلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْ رَبَّهُمۡ لَهُمۡ غُرَفٞ مِّن فَوۡقِهَا غُرَفٞ مَّبۡنِيَّةٞ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۖ وَعۡدَ ٱللَّهِ لَا يُخۡلِفُ ٱللَّهُ ٱلۡمِيعَادَ ٢٠

21. አላህ ከሰማይ ውሃን እንዳወረደና በምድርም ውስጥ ምንጮች አድርጎ እንዳስገባው አላየህምን? ከዚያም በእርሱ ዓይነቶቹ የተለያዩን አዝመራ ያወጣል፡፡ ከዚያም ይደርቃል፡፡ ገርጥቶም ታየዋለህ፡፡ ከዚያም ስብርብር ያደርገዋል፡፡ በዚህ ውስጥ ለባለ አእምሮዎች ግሣጼ አለበት፡፡

أَلَمۡ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ أَنزَلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ فَسَلَكَهُۥ يَنَٰبِيعَ فِي ٱلۡأَرۡضِ ثُمَّ يُخۡرِجُ بِهِۦ زَرۡعٗا مُّخۡتَلِفًا أَلۡوَٰنُهُۥ ثُمَّ يَهِيجُ فَتَرَىٰهُ مُصۡفَرّٗا ثُمَّ يَجۡعَلُهُۥ حُطَٰمًاۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَذِكۡرَىٰ لِأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ ٢١

22. አላህ ደረቱን ለእስልምና ያስፋለትና እርሱም ከጌታው ዘንድ በብርሃን ላይ የኾነ ሰው (ልቡ እንደ ደረቀ ሰው ነውን?) ልቦቻቸውም ከአላህ መወሳት ለደረቁ ሰዎች ወዮላቸው፡፡ እነዚያ በግልጽ መሳሳት ውስጥ ናቸው፡፡

أَفَمَن شَرَحَ ٱللَّهُ صَدۡرَهُۥ لِلۡإِسۡلَٰمِ فَهُوَ عَلَىٰ نُورٖ مِّن رَّبِّهِۦۚ فَوَيۡلٞ لِّلۡقَٰسِيَةِ قُلُوبُهُم مِّن ذِكۡرِ ٱللَّهِۚ أُوْلَٰٓئِكَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ٢٢

23. አላህ ከዜና ሁሉ መልካምን፣ ተመሳሳይ፣ ተደጋጋሚ የኾነን መጽሐፍ አወረደ፡፡ ከእርሱ (ግሣጼ) የእነዚያ ጌታቸውን የሚፈሩት ሰዎች ቆዳዎች ይኮማተራሉ፡፡ ከዚያም ቆዳዎቻቸውና ልቦቻቸው ወደ አላህ (ተስፋ) ማስታወስ ይለዝባሉ፡፡ ይህ የአላህ መምሪያ ነው፡፡ በእርሱ የሚሻውን ሰው ይመራበታል፡፡ አላህም የሚያጠመው ሰው ለእርሱ ምንም አቅኚ የለውም፡፡

ٱللَّهُ نَزَّلَ أَحۡسَنَ ٱلۡحَدِيثِ كِتَٰبٗا مُّتَشَٰبِهٗا مَّثَانِيَ تَقۡشَعِرُّ مِنۡهُ جُلُودُ ٱلَّذِينَ يَخۡشَوۡنَ رَبَّهُمۡ ثُمَّ تَلِينُ جُلُودُهُمۡ وَقُلُوبُهُمۡ إِلَىٰ ذِكۡرِ ٱللَّهِۚ ذَٰلِكَ هُدَى ٱللَّهِ يَهۡدِي بِهِۦ مَن يَشَآءُۚ وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِنۡ هَادٍ ٢٣

24. በትንሣኤ ቀን ከፉን ቅጣት በፊቱ የሚመክት ሰው (ከቅጣት እንደሚድን ነውን?) ለበዳዮችም «ትሠሩት የነበራችሁትን (ቅጣቱን) ቅመሱ» ይባላሉ፡፡

أَفَمَن يَتَّقِي بِوَجۡهِهِۦ سُوٓءَ ٱلۡعَذَابِ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۚ وَقِيلَ لِلظَّٰلِمِينَ ذُوقُواْ مَا كُنتُمۡ تَكۡسِبُونَ ٢٤

25. ከእነሱ በፊት የነበሩት አስተባበሉ፡፡ ቅጣቱም ከማያውቁት በኩል መጣባቸው፡፡

كَذَّبَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ فَأَتَىٰهُمُ ٱلۡعَذَابُ مِنۡ حَيۡثُ لَا يَشۡعُرُونَ ٢٥

26. አላህም በቅርቢቱ ሕይወት ውርደትን አቀመሳቸው፡፡ የመጨረሻይቱም ዓለም ቅጣት በጣም ትልቅ ነው፡፡ የሚያውቁ ቢኾኑ ኖሮ (አያስተባብሉም ነበር)፡፡

فَأَذَاقَهُمُ ٱللَّهُ ٱلۡخِزۡيَ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَعَذَابُ ٱلۡأٓخِرَةِ أَكۡبَرُۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٢٦

27. በዚህም ቁርኣን ውስጥ ለሰዎች ይገሠጹ ዘንድ ከየምሳሌው ሁሉ በእርግጥ አብራራን፡፡

وَلَقَدۡ ضَرَبۡنَا لِلنَّاسِ فِي هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ مِن كُلِّ مَثَلٖ لَّعَلَّهُمۡ يَتَذَكَّرُونَ ٢٧

28. መዛባት የሌለበት ዐረብኛ ቁርኣን ሲኾን (አብራራነው)፡፡ ሊጠነቀቁ ይከጀላልና፡፡

قُرۡءَانًا عَرَبِيًّا غَيۡرَ ذِي عِوَجٖ لَّعَلَّهُمۡ يَتَّقُونَ ٢٨

29. አላህ በእርሱ ተጨቃጫቂዎች የኾኑ ተጋሪዎች ያሉትን ባሪያና ለአንድ ሰው ብቻ ንጹሕ የኾነን ባሪያ (ለሚያጋራና ባንድነቱ ለሚያምን ሰው) ምሳሌ አደረገ፡፡ በምሳሌ ይስተካከላሉን? ምስጋና ለአላህ ይገባው፡፡ በእውነቱ አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

ضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلٗا رَّجُلٗا فِيهِ شُرَكَآءُ مُتَشَٰكِسُونَ وَرَجُلٗا سَلَمٗا لِّرَجُلٍ هَلۡ يَسۡتَوِيَانِ مَثَلًاۚ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِۚ بَلۡ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٢٩

30. አንተ ሟች ነህ፤ እነርሱም ሟቾች ናቸው፡፡

إِنَّكَ مَيِّتٞ وَإِنَّهُم مَّيِّتُونَ ٣٠

31. ከዚያም እናንተ በትንሣኤ ቀን እጌታችሁ ዘንድ ትከራከራላችሁ፡፡

ثُمَّ إِنَّكُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ عِندَ رَبِّكُمۡ تَخۡتَصِمُونَ ٣١

32. በአላህም ላይ ከዋሸ እውነቱንም በመጣለት ጊዜ ካስተባበለ ሰው ይበልጥ በዳይ ማን ነው? በገሀነም ውስጥ ለከሓዲዎች መኖሪያ የለምን? (አለ እንጅ)፡፡

۞فَمَنۡ أَظۡلَمُ مِمَّن كَذَبَ عَلَى ٱللَّهِ وَكَذَّبَ بِٱلصِّدۡقِ إِذۡ جَآءَهُۥٓۚ أَلَيۡسَ فِي جَهَنَّمَ مَثۡوٗى لِّلۡكَٰفِرِينَ ٣٢

33. ያም በእውነት የመጣው በእርሱ ያመነውም እነዚያ እነርሱ አላህን ፈሪዎች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِي جَآءَ بِٱلصِّدۡقِ وَصَدَّقَ بِهِۦٓ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُتَّقُونَ ٣٣

34. ለእነርሱ በጌታቸው ዘንድ የሚሹት ሁሉ አልላቸው፡፡ ይህ የበጎ አድራጊዎች ምንዳ ነው፡፡

لَهُم مَّا يَشَآءُونَ عِندَ رَبِّهِمْۚ ذَٰلِكَ جَزَآءُ ٱلْمُحْسِنِينَ ﴿٣٤﴾

35. አላህ ያንን (በስሕተት) የሠሩትን መጥፎ ሥራ ከእነርሱ ሊሰርይላቸው በዚያም ይሠሩት በነበሩት በመልካሙ ሥራ ምንዳቸውን ሊመነዳቸው (ይህንን አደረገ)፡፡

لِيُكَفِّرَ ٱللَّهُ عَنْهُمْ أَسْوَأَ ٱلَّذِى عَمِلُوا۟ وَيَجْزِيَهُمْ أَجْرَهُم بِأَحْسَنِ ٱلَّذِى كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ﴿٣٥﴾

36. አላህ ባሪያውን በቂ አይደለምን? በእነዚያ ከእርሱ ሌላ በኾኑትም (ጣዖታት) ያስፈራሩሃል፡፡ አላህ የሚያጠመውም ሰው ለርሱ ምንም አቅኚ የለውም፡፡

أَلَيْسَ ٱللَّهُ بِكَافٍ عَبْدَهُۥ ۖ وَيُخَوِّفُونَكَ بِٱلَّذِينَ مِن دُونِهِۦ ۚ وَمَن يُضْلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِنْ هَادٍ ﴿٣٦﴾

37. አላህ የሚያቀናውም ሰው ለእርሱ ምንም አጥማሚ የለውም፡፡ አላህ አሸናፊ የመበቀል ባለቤት አይደለምን?

وَمَن يَهْدِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِن مُّضِلٍّ ۗ أَلَيْسَ ٱللَّهُ بِعَزِيزٍ ذِى ٱنتِقَامٍ ﴿٣٧﴾

38. ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ ማን እንደ ኾነ ብትጠይቃቸው «አላህ ነው» ይሉሃል፡፡ «ከአላህ ሌላ የምትግገዟቸውን (ጣዖታት) አያችሁን? (ንገሩኝ) አላህ በጉዳት ቢፈልገኝ እነርሱ ጉዳቱን ገላጮች ናቸውን? ወይስ በችሮታው ቢፈቅደኝ እነርሱ ችሮታውን አጋጆች ናቸውን?» በላቸው፡፡ «አላህ በቂዬ ነው፡፡ በእርሱ ላይ ተመኪዎች ይመካሉ» በል፡፡

وَلَئِن سَأَلْتَهُم مَّنْ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُ ۚ قُلْ أَفَرَءَيْتُم مَّا تَدْعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ إِنْ أَرَادَنِىَ ٱللَّهُ بِضُرٍّ هَلْ هُنَّ كَٰشِفَٰتُ ضُرِّهِۦٓ أَوْ أَرَادَنِى بِرَحْمَةٍ هَلْ هُنَّ مُمْسِكَٰتُ رَحْمَتِهِۦ ۚ قُلْ حَسْبِىَ ٱللَّهُ ۖ عَلَيْهِ يَتَوَكَّلُ ٱلْمُتَوَكِّلُونَ ﴿٣٨﴾

39. (ሙሐመድ ሆይ!) በላቸው «ሕዝቦቼ ሆይ! ባላችሁበት ኹኔታ ላይ ሥሩ፡፡ እኔ ሠሪ ነኝና፡፡ ወደፊትም ታውቃላችሁ፡፡»

قُلْ يَٰقَوْمِ ٱعْمَلُوا۟ عَلَىٰ مَكَانَتِكُمْ إِنِّى عَٰمِلٌ ۖ فَسَوْفَ تَعْلَمُونَ ﴿٣٩﴾

40. ያንን የሚያሳፍረው ቅጣት የሚመጠበትንና በእርሱ ላይ ዘውታሪ ቅጣት የሚሰፍርበትን (ታውቃላችሁ)

مَن يَأْتِيهِ عَذَابٌ يُخْزِيهِ وَيَحِلُّ عَلَيْهِ عَذَابٌ مُّقِيمٌ ﴿٤٠﴾

41. እኛ መጽሐፉን ባንተ ላይ ለሰዎች (ጥቅም) በእውነት አወረድነው፡፡ የተመራም ሰው ለነፍሱ ነው፡፡ የጠመመም ሰው የሚጠምመው (ጉዳቱ) በእርሷ ላይ ነው፡፡ አንተም (ታስገድዳቸው ዘንድ) በእነርሱ ላይ ጠባቂ አይደለህም፡፡

إِنَّآ أَنزَلْنَا عَلَيْكَ ٱلْكِتَٰبَ لِلنَّاسِ بِٱلْحَقِّ ۖ فَمَنِ ٱهْتَدَىٰ فَلِنَفْسِهِۦ ۖ وَمَن ضَلَّ فَإِنَّمَا يَضِلُّ عَلَيْهَا ۖ وَمَآ أَنتَ عَلَيْهِم بِوَكِيلٍ ﴿٤١﴾

42. አላህ ነፍሶችን በሞታቸው ጊዜ ይወስዳል፡፡ ያችንም ያልሞተችውን በእንቅልፏ ጊዜ (ይወስዳታል)፡፡ ታዲያ ያችን ሞትን የፈረደባትን ይይዛታል፡፡ ሌላይቱንም እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ ይለቅቃታል፡፡ በዚህ ውስጥ ለሚያስተነትኑ ሕዝቦች ምልክቶች አልሉበት፡፡

ٱللَّهُ يَتَوَفَّى ٱلْأَنفُسَ حِينَ مَوْتِهَا وَٱلَّتِى لَمْ تَمُتْ فِى مَنَامِهَا ۖ فَيُمْسِكُ ٱلَّتِى قَضَىٰ عَلَيْهَا ٱلْمَوْتَ وَيُرْسِلُ ٱلْأُخْرَىٰٓ إِلَىٰٓ أَجَلٍ مُّسَمًّى ۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَٰتٍ لِّقَوْمٍ يَتَفَكَّرُونَ ﴿٤٢﴾

43. ይልቁንም (ቁረይሾች) ከአላህ ሌላ አማላጆችን ያዙ፡፡ «እነርሱ ምንንም የማይችሉና የማያውቁ ቢኾኑም?» በላቸው፡፡

أَمِ ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ شُفَعَآءَۚ قُلْ أَوَلَوْ كَانُواْ لَا يَمْلِكُونَ شَيْـًٔا وَلَا يَعْقِلُونَ ﴿٤٣﴾

44. «ምልጃ መላውም የአላህ ብቻ ነው፡፡ የሰማያትና የምድር ሥልጣን የእርሱ ብቻ ነው፡፡ ከዚያም ወደእርሱ ትመለሳላችሁ» በላቸው፡፡

قُل لِّلَّهِ ٱلشَّفَٰعَةُ جَمِيعًاۖ لَّهُۥ مُلْكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِۖ ثُمَّ إِلَيْهِ تُرْجَعُونَ ﴿٤٤﴾

45. አላህም ብቻውን በተወሳ ጊዜ የእነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት ሰዎች ልቦች ይሸማቀቃሉ፤ (ይደነብራሉ)፡፡ እነዚያም ከእርሱ ሌላ የኾኑት (ጣዖታት) በተወሱ ጊዜ እነርሱ ወዲያውኑ ይደሰታሉ፡፡

وَإِذَا ذُكِرَ ٱللَّهُ وَحْدَهُ ٱشْمَأَزَّتْ قُلُوبُ ٱلَّذِينَ لَا يُؤْمِنُونَ بِٱلْـَٔاخِرَةِۖ وَإِذَا ذُكِرَ ٱلَّذِينَ مِن دُونِهِۦٓ إِذَا هُمْ يَسْتَبْشِرُونَ ﴿٤٥﴾

46. «ሰማያትንና ምድርን የፈጠርክ ሩቁንም ቅርቡንም ዐዋቂ የኾንክ አላህ ሆይ! አንተ በባሮችህ መካከል በእዚያ በእርሱ ይለያዩበት በነበሩት ነገር ትፈርዳለህ» በል፡፡

قُلِ ٱللَّهُمَّ فَاطِرَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ عَٰلِمَ ٱلْغَيْبِ وَٱلشَّهَٰدَةِ أَنتَ تَحْكُمُ بَيْنَ عِبَادِكَ فِى مَا كَانُواْ فِيهِ يَخْتَلِفُونَ ﴿٤٦﴾

47. ለእነዚያም ለበደሉት በምድር ያለው ሁሉ መላውም ከእርሱ ጋር መሰሉም ቢኖራቸው ኖሮ በትንሣኤ ቀን ከቅጣቱ ክፋት የተነሳ በእርሱ ነፍሶቻቸውን በተበገዙበት ነበር፡፡ ለእነርሱም ከአላህ ዘንድ ያስቡት ያልነበሩት ሁሉ ይገለጽላቸዋል፡፡

وَلَوْ أَنَّ لِلَّذِينَ ظَلَمُواْ مَا فِى ٱلْأَرْضِ جَمِيعًا وَمِثْلَهُۥ مَعَهُۥ لَٱفْتَدَوْاْ بِهِۦ مِن سُوٓءِ ٱلْعَذَابِ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِۚ وَبَدَا لَهُم مِّنَ ٱللَّهِ مَا لَمْ يَكُونُواْ يَحْتَسِبُونَ ﴿٤٧﴾

48. ለእነርሱም የሠሩዋቸው መጥፎዎቹ ይገለጹላቸዋል፡፡ በእነርሱም ላይ በእርሱ ያላግጡበት የነበሩት ቅጣት ይሰፍርባቸዋል፡፡

وَبَدَا لَهُمْ سَيِّـَٔاتُ مَا كَسَبُواْ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ﴿٤٨﴾

49. ሰውም ጉዳት ባገኘው ጊዜ ይጠራናል፡፡ ከዚያም ከእኛ የኾነውን ጸጋ በሰጠነው ጊዜ «እርሱን የተሰጠሁት፤ በዕውቀት ብቻ ነው» ይላል፡፡ ይልቁንም እርሷ (ጸጋይቱ) መፈተኛ ናት፡፡ ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

فَإِذَا مَسَّ ٱلْإِنسَٰنَ ضُرٌّ دَعَانَا ثُمَّ إِذَا خَوَّلْنَٰهُ نِعْمَةً مِّنَّا قَالَ إِنَّمَآ أُوتِيتُهُۥ عَلَىٰ عِلْمٍۭۚ بَلْ هِىَ فِتْنَةٌ وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَهُمْ لَا يَعْلَمُونَ ﴿٤٩﴾

50. እነዚያ ከእነርሱ በፊት የነበሩት ሕዝቦች በእርግጥ ብለዋታል፡፡ ይሠሩት የነበሩትም ነገር ከእነርሱ አልጠቀማቸውም፡፡

قَدْ قَالَهَا ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ فَمَآ أَغْنَىٰ عَنْهُم مَّا كَانُواْ يَكْسِبُونَ ﴿٥٠﴾

51. የሠሩዋቸውም መጥፎዎች (ቅጣት) አገኛቸው፡፡ ከእነዚህም እነዚያ የበደሉት የሠሩዋቸው መጥፎዎች (ፍዳ) በእርግጥ ይነካቸዋል፡፡ እነርሱም አምላጮች አይደሉም፡፡

فَأَصَابَهُمْ سَيِّـَٔاتُ مَا كَسَبُواْۚ وَٱلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنْ هَٰٓؤُلَآءِ سَيُصِيبُهُمْ سَيِّـَٔاتُ مَا كَسَبُواْ وَمَا هُم بِمُعْجِزِينَ ﴿٥١﴾

52. አላህ ሲሳዩን ለሚሻው ሰው የሚያሰፋ የሚያጠብም መኾኑን አያውቁምን? በዚህ ውስጥ ለሚያምኑት ሕዝቦች ግሣጼዎች አሉበት፡፡

أَوَ لَمْ يَعْلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ يَبْسُطُ ٱلرِّزْقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقْدِرُۚ إِنَّ فِى ذَٰلِكَ لَءَايَٰتٍ لِّقَوْمٍ يُؤْمِنُونَ ﴿٥٢﴾

53. በላቸው «እናንተ በነፍሶቻችሁ ላይ ድንበር ያለፋችሁ ባሮቼ ሆይ! ከአላህ እዝነት ተስፋ አትቁረጡ፡ ፡ አላህ ኃጢአቶችን በመላ ይምራልና፡፡ እነሆ እርሱ መሓሪው አዛኙ ነውና፡፡

۞ قُلْ يَٰعِبَادِىَ ٱلَّذِينَ أَسْرَفُواْ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمْ لَا تَقْنَطُواْ مِن رَّحْمَةِ ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَغْفِرُ ٱلذُّنُوبَ جَمِيعًاۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلْغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٥٣﴾

54. «ቅጣቱም ወደእናንተ ከመምጣቱና ከዚያም የማትርረዱ ከመኾናችሁ በፊት ወደ ጌታችሁ (በመጸጸት) ተመለሱ፡፡ ለእርሱም ታዘዙ፡፡

وَأَنِيبُوٓاْ إِلَىٰ رَبِّكُمْ وَأَسْلِمُواْ لَهُۥ مِن قَبْلِ أَن يَأْتِيَكُمُ ٱلْعَذَابُ ثُمَّ لَا تُنصَرُونَ ﴿٥٤﴾

55. «እናንተ የማታውቁ ስትኾኑም ቅጣቱ በድንገት ሳይመጣባችሁ በፊት ከጌታችሁ ወደናንተ የተወረደውን መልካሙን (መጽሐፍ) ተከተሉ፡፡»

وَٱتَّبِعُوٓاْ أَحْسَنَ مَآ أُنزِلَ إِلَيْكُم مِّن رَّبِّكُم مِّن قَبْلِ أَن يَأْتِيَكُمُ ٱلْعَذَابُ بَغْتَةً وَأَنتُمْ لَا تَشْعُرُونَ ﴿٥٥﴾

56. (የካደች) ነፍስ «እኔ ከሚሳለቁት የነበርኩ ስኾን በአላህ በኩል ባጓደልኩት ዋ ጸጸቴ» ማለቷን (ለመፍራት)፤

أَن تَقُولَ نَفْسٌ يَٰحَسْرَتَىٰ عَلَىٰ مَا فَرَّطتُ فِى جَنۢبِ ٱللَّهِ وَإِن كُنتُ لَمِنَ ٱلسَّٰخِرِينَ ﴿٥٦﴾

57. ወይም «አላህ በመራኝ ኖሮ ከሚጠነቀቁት እኾን ነበር» ማለቷን (ለመፍራት)፡፡

أَوْ تَقُولَ لَوْ أَنَّ ٱللَّهَ هَدَىٰنِى لَكُنتُ مِنَ ٱلْمُتَّقِينَ ﴿٥٧﴾

58. ወይም ቅጣቱን በምታይ ጊዜ «ለእኔ (ወደ ምድረ ዓለም) አንድ ጊዜ መመለስ በኖረኝና ከበጎ አድራጊዎቹ በኾንኩ» ማለቷን (ለመፍራት መልካሙን ተከተሉ)፡፡

أَوْ تَقُولَ حِينَ تَرَى ٱلْعَذَابَ لَوْ أَنَّ لِى كَرَّةً فَأَكُونَ مِنَ ٱلْمُحْسِنِينَ ﴿٥٨﴾

59. የለም ተመርተሃል፡፡ አንቀጾቼ በእርግጥ መጥተውልሃል፡፡ በእነርሱም አስተባብለሃል፡፡ ኮርተሃልም፡፡ ከከሓዲዎቹም ኾነሃል፤ (ይባላል)፡፡

بَلَىٰ قَدْ جَآءَتْكَ ءَايَٰتِى فَكَذَّبْتَ بِهَا وَٱسْتَكْبَرْتَ وَكُنتَ مِنَ ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿٥٩﴾

60. በትንሣኤ ቀንም እነዚያን በአላህ ላይ የዋሹትን ፊቶቻቸው የጠቆሩ ኾነው ታያቸዋለህ፡፡ በገሀነም ውስጥ ለትዕቢተኞች መኖሪያ የለምን?

وَيَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ تَرَى ٱلَّذِينَ كَذَبُواْ عَلَى ٱللَّهِ وُجُوهُهُم مُّسْوَدَّةٌۚ أَلَيْسَ فِى جَهَنَّمَ مَثْوًى لِّلْمُتَكَبِّرِينَ ﴿٦٠﴾

61. እነዚያንም የተጠነቀቁትን በማግኛቸው ስፍራ ኾነው አላህ ያድናቸዋል፡፡ ክፉ ነገር አይነካቸውም፡፡ እነርሱም አያዝኑም፡፡

وَيُنَجِّى ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ٱتَّقَوْاْ بِمَفَازَتِهِمْ لَا يَمَسُّهُمُ ٱلسُّوٓءُ وَلَا هُمْ يَحْزَنُونَ ﴿٦١﴾

62. አላህ የነገሩ ሁሉ ፈጣሪ ነው፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ አስተናባሪ ነው፡፡

ٱللَّهُ خَٰلِقُ كُلِّ شَىْءٍۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ وَكِيلٌ ﴿٦٢﴾

63. የሰማያትና የምድር (ድልብ) መክፈቻዎች የእርሱ ብቻ ናቸው፡፡ እነዚያም በአላህ አንቀጾች የካዱት እነዚያ እነሱ ከሳሪዎቹ ናቸው፡፡

لَّهُۥ مَقَالِيدُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِۗ وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلْخَٰسِرُونَ ﴿٦٣﴾

64. «እናንተ መሃይማን ሆይ! ከአላህ ሌላን እንድግገዛ ታዙኛላችሁን?» በላቸው፡፡

قُلْ أَفَغَيْرَ ٱللَّهِ تَأْمُرُوٓنِّىٓ أَعْبُدُ أَيُّهَا ٱلْجَٰهِلُونَ ﴿٦٤﴾

65. ብታጋራ ሥራህ በእርግጥ ይታበሳል፡፡ በእርግጥም ከከሓዲዎቹ ትኾናለህ ማለት ወደ አንተም ወደእነዚያም ካንተ በፊት ወደነበሩት በእርግጥ ተወርዷል፡፡

وَلَقَدْ أُوحِىَ إِلَيْكَ وَإِلَى ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِكَ لَئِنْ أَشْرَكْتَ لَيَحْبَطَنَّ عَمَلُكَ وَلَتَكُونَنَّ مِنَ ٱلْخَٰسِرِينَ ﴿٦٥﴾

66. ይልቅ አላህን ብቻ ተገዛም፡፡ ከአመስጋኞቹም ኹን፡፡

بَلِ ٱللَّهَ فَٱعْبُدْ وَكُن مِّنَ ٱلشَّٰكِرِينَ ﴿٦٦﴾

67. አላህንም በትንሣኤ ቀን ምድር በመላ ጭብጡ ስትኾን፤ ሰማያትም በኀይሉ የሚጠቀለሉ ሲኾኑ (ከርሱ ጋር ሌላን በማጋራታቸው) ተገቢ ክብሩን አላከበሩትም፡፡ ከሚያጋሩት ጠራ፤ ላቀም፡፡

وَمَا قَدَرُوا۟ ٱللَّهَ حَقَّ قَدْرِهِۦ وَٱلْأَرْضُ جَمِيعًا قَبْضَتُهُۥ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ وَٱلسَّمَٰوَٰتُ مَطْوِيَّٰتٌۢ بِيَمِينِهِۦ ۚ سُبْحَٰنَهُۥ وَتَعَٰلَىٰ عَمَّا يُشْرِكُونَ ﴿٦٧﴾

68. በቀንዱም ይንነፋል፡፡ በሰማያት ውስጥ ያለው ፍጡርና በምድርም ውስጥ ያለው ፍጡር ሁሉ አላህ የሻው ሲቀር በድንጋጤ ይሞታል፡፡ ከዚያም በእርሱ ሌላ (መንነፋት) ይንነፋል፡፡ ወዲያውም እነርሱ (የሚሠራባቸውን) የሚጠባበቁ ኾነው ቋሚዎች ይኾናሉ፡፡

وَنُفِخَ فِى ٱلصُّورِ فَصَعِقَ مَن فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَن فِى ٱلْأَرْضِ إِلَّا مَن شَآءَ ٱللَّهُ ۖ ثُمَّ نُفِخَ فِيهِ أُخْرَىٰ فَإِذَا هُمْ قِيَامٌ يَنظُرُونَ ﴿٦٨﴾

69. ምድርም በጌታዋ ብርሃን ታበራለች፡፡ መጽሐፉም ይቅቀረባል፡፡ ነቢያቱና ምስክሮቹም ይመጣሉ፡፡ በመካከላቸውም በእውነት ይፈረዳል፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

وَأَشْرَقَتِ ٱلْأَرْضُ بِنُورِ رَبِّهَا وَوُضِعَ ٱلْكِتَٰبُ وَجِا۟ىٓءَ بِٱلنَّبِيِّۦنَ وَٱلشُّهَدَآءِ وَقُضِىَ بَيْنَهُم بِٱلْحَقِّ وَهُمْ لَا يُظْلَمُونَ ﴿٦٩﴾

70. ነፍስም ሁሉ የሠራችውን ሥራ ትሞላለች፤ (ትሰፈራለች)፡፡ እርሱም የሚሠሩትን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

وَوُفِّيَتْ كُلُّ نَفْسٍ مَّا عَمِلَتْ وَهُوَ أَعْلَمُ بِمَا يَفْعَلُونَ ﴿٧٠﴾

71. እነዚያ የካዱትም የተከፋፈሉ ጭፍሮች ኾነው ወደ ገሀነም ይንነዳሉ፡፡ በመጧትም ጊዜ ደጃፎችዋ ይከፈታሉ፡፡ ዘበኞችዋም «ከእናንተ የኾኑ መልክተኞች የጌታችሁን አንቀጾች በናንተ ላይ የሚያነቡላችሁ የዚህንም ቀን መገናኘት የሚያስጠነቅቋችሁ አልመጡዋ ችሁምን?» ይሏቸዋል፡፡ «የለም መጥተውናል፤ ግን የቅጣቲቱ ቃል በከሓዲዎች ላይ ተረጋገጠች» ይላሉ፡፡

وَسِيقَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ إِلَىٰ جَهَنَّمَ زُمَرًا ۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءُوهَا فُتِحَتْ أَبْوَٰبُهَا وَقَالَ لَهُمْ خَزَنَتُهَآ أَلَمْ يَأْتِكُمْ رُسُلٌ مِّنكُمْ يَتْلُونَ عَلَيْكُمْ ءَايَٰتِ رَبِّكُمْ وَيُنذِرُونَكُمْ لِقَآءَ يَوْمِكُمْ هَٰذَا ۚ قَالُوا۟ بَلَىٰ وَلَٰكِنْ حَقَّتْ كَلِمَةُ ٱلْعَذَابِ عَلَى ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿٧١﴾

72. «የገሀነምን ደጃፎች በውስጧ ዘውታሪዎች ስትኾኑ ግቡ፡፡ የትዕቢተኞችም መኖሪያ ምን ትከፋ!» ይባላሉ፡፡

قِيلَ ٱدْخُلُوٓا۟ أَبْوَٰبَ جَهَنَّمَ خَٰلِدِينَ فِيهَا ۖ فَبِئْسَ مَثْوَى ٱلْمُتَكَبِّرِينَ ﴿٧٢﴾

73. እነዚያም ጌታቸውን የፈሩት የተከፋፈሉ ጭፍሮች ኾነው ወደ ገነት ይንነዳሉ፡፡ በመጧትም ጊዜ ደጃፎችዋ የተከፈቱ ሲኾኑ ዘበኞችዋም ለእነርሱ «ሰላም በናንተ ላይ ይኹን፡፡ ተዋባችሁ፡፡ ዘውታሪዎች ኾናችሁ ግቧት» በሏቸው ጊዜ (ይገቧታል)፡፡

وَسِيقَ ٱلَّذِينَ ٱتَّقَوۡاْ رَبَّهُمۡ إِلَى ٱلۡجَنَّةِ زُمَرًاۖ حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءُوهَا وَفُتِحَتۡ أَبۡوَٰبُهَا وَقَالَ لَهُمۡ خَزَنَتُهَا سَلَٰمٌ عَلَيۡكُمۡ طِبۡتُمۡ فَٱدۡخُلُوهَا خَٰلِدِينَ ﴿٧٣﴾

74. «ምስጋና ለአላህ ለዚያ ተስፋ ቃሉን ለሞላልን፡፡ የገነትን ምድር በምንሻው ስፍራ የምንሰፍር ስንኾን ላወረሰን ይገባው» ይላሉም፡፡ የሠሪዎችም ምንዳ ምን ያምር!

وَقَالُواْ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ ٱلَّذِي صَدَقَنَا وَعۡدَهُۥ وَأَوۡرَثَنَا ٱلۡأَرۡضَ نَتَبَوَّأُ مِنَ ٱلۡجَنَّةِ حَيۡثُ نَشَآءُۖ فَنِعۡمَ أَجۡرُ ٱلۡعَٰمِلِينَ ﴿٧٤﴾

75. መላእክትንም በጌታቸው ምስጋና ቀላቅለው የሚያጠሩ ሲኾኑ በዐርሹ ዙሪያ ከባቢዎች ኾነው ታያለህ፡፡ በመካከላቸው በእውነት ይፈረዳል፡፡ ይባላልም፤ «ምስጋና ለአላህ ለዓለማት ጌታ ይገባው፡፡»

وَتَرَى ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ حَآفِّينَ مِنۡ حَوۡلِ ٱلۡعَرۡشِ يُسَبِّحُونَ بِحَمۡدِ رَبِّهِمۡۚ وَقُضِيَ بَيۡنَهُم بِٱلۡحَقِّۚ وَقِيلَ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٧٥﴾

# ሱረቱ አል ጋፊር

# سورة غافر

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሓ.ሚም)፤

حمٓ ﴿١﴾

2. የመጽሐፉ መወረድ አሸናፊ ዐዋቂ ከሆነው አላህ ነው፡፡

تَنزِيلُ ٱلۡكِتَٰبِ مِنَ ٱللَّهِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡعَلِيمِ ﴿٢﴾

3. ኀጢአትን መሓሪ፣ ጸጸትንም ተቀባይ፣ ቅጣተ ብርቱ፣ የልግስና ባለቤት ከኾነው (አላህ የወረደ ነው)፡፡ ከእርሱ በቀር አምላክ የለም፡፡ መመለሻው ወደርሱ ብቻ ነው፡፡

غَافِرِ ٱلذَّنۢبِ وَقَابِلِ ٱلتَّوۡبِ شَدِيدِ ٱلۡعِقَابِ ذِي ٱلطَّوۡلِۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ إِلَيۡهِ ٱلۡمَصِيرُ ﴿٣﴾

4. በአላህ አንቀጾች እነዚያ የካዱት ቢኾኑ እንጅ ማንም (በመዝለፍ) አይከራከርም፡፡ በያገሮችም ውስጥ መዘዋወራቸው አይሸንግልህ፡፡

مَا يُجَٰدِلُ فِيٓ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ إِلَّا ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَلَا يَغۡرُرۡكَ تَقَلُّبُهُمۡ فِي ٱلۡبِلَٰدِ ﴿٤﴾

5. ከእነርሱ በፊት የኑሕ ሕዝቦች ከኋላቸውም አሕዛቦቹ አስተባባሉ፡፡ ሕዝቦችም ሁሉ መልክተኛቸውን ሊይዙ አሰቡ፡፡ በውሸትም በእርሱ እውነትን ሊያጠፉበት ተከራከሩ፡፡ ያዝኳቸውም፡፡ ታዲያ ቅጣቴ እንዴት ነበር?

كَذَّبَتۡ قَبۡلَهُمۡ قَوۡمُ نُوحٖ وَٱلۡأَحۡزَابُ مِنۢ بَعۡدِهِمۡۖ وَهَمَّتۡ كُلُّ أُمَّةِۭ بِرَسُولِهِمۡ لِيَأۡخُذُوهُۖ وَجَٰدَلُواْ بِٱلۡبَٰطِلِ لِيُدۡحِضُواْ بِهِ ٱلۡحَقَّ فَأَخَذۡتُهُمۡۖ فَكَيۡفَ كَانَ عِقَابِ ﴿٥﴾

6. እንደዚሁም የጌታህ ቃል በእነዚያ በካዱት ላይ እነርሱ የእሳት ጓዶች ናቸው ማለት ተረጋገጠች፡፡

وَكَذَٰلِكَ حَقَّتۡ كَلِمَتُ رَبِّكَ عَلَى ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَنَّهُمۡ

أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِ ٦

7. እነዚያ ዐርሹን የሚሸከሙት እነዚያም በዙሪያው ያሉት በጌታቸው ምስጋና ያወድሳሉ፡፡ በእርሱም ያምናሉ፡፡ «ጌታችን ሆይ! ነገሩን ሁሉ በእዝነትና በዕውቀት ከበሃል፡፡ ስለዚህ ለእነዚያ ለተጸጸቱት መንገድህንም ለተከተሉት ምሕረት አድርግላቸው፡፡ የእሳትንም ቅጣት ጠብቃቸው፡፡» እያሉ ለእነዚያ ላመኑት ምሕረትን ይለምናሉ፡፡

ٱلَّذِينَ يَحۡمِلُونَ ٱلۡعَرۡشَ وَمَنۡ حَوۡلَهُۥ يُسَبِّحُونَ بِحَمۡدِ رَبِّهِمۡ وَيُؤۡمِنُونَ بِهِۦ وَيَسۡتَغۡفِرُونَ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْۖ رَبَّنَا وَسِعۡتَ كُلَّ شَيۡءٖ رَّحۡمَةٗ وَعِلۡمٗا فَٱغۡفِرۡ لِلَّذِينَ تَابُواْ وَٱتَّبَعُواْ سَبِيلَكَ وَقِهِمۡ عَذَابَ ٱلۡجَحِيمِ ٧

8. «ጌታችን ሆይ! እነርሱንም፣ ከአባቶቻቸውና ከሚስቶቻቸውም፣ ከዝርዮቻቸውም፣ የበጀውን ሁሉ እነዚያን ቃል የገባህላቸውን የመኖሪያ ገነቶች አግባቸው፡፡ አንተ አሸናፊው ጥበበኛው አንተ ነህና፡፡

رَبَّنَا وَأَدۡخِلۡهُمۡ جَنَّٰتِ عَدۡنٍ ٱلَّتِي وَعَدتَّهُمۡ وَمَن صَلَحَ مِنۡ ءَابَآئِهِمۡ وَأَزۡوَٰجِهِمۡ وَذُرِّيَّٰتِهِمۡۚ إِنَّكَ أَنتَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٨

9. «ከቅጣቶችም ጠብቃቸው፡፡ በዚያ ቀንም የምትጠብቃውን ሰው በእርግጥ አዘንክለት፡፡» ይህም እርሱ ታላቅ ማግኘት ነው፡፡

وَقِهِمُ ٱلسَّيِّـَٔاتِۚ وَمَن تَقِ ٱلسَّيِّـَٔاتِ يَوۡمَئِذٖ فَقَدۡ رَحِمۡتَهُۥۚ وَذَٰلِكَ هُوَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ٩

10. እነዚያ የካዱት ሰዎች «ወደ እምነት በምትጠሩና በምትክዱ ጊዜ አላህ (እናንተን) መጥላቱ ነፍሶቻችሁን (ዛሬ) ከመጥላታችሁ የበለጠ ነው» በማለት ይጥጠራሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يُنَادَوۡنَ لَمَقۡتُ ٱللَّهِ أَكۡبَرُ مِن مَّقۡتِكُمۡ أَنفُسَكُمۡ إِذۡ تُدۡعَوۡنَ إِلَى ٱلۡإِيمَٰنِ فَتَكۡفُرُونَ ١٠

11. «ጌታችን ሆይ! ሁለትን ሞት አሞትከን፡፡ ሁለትንም ሕይወት ሕያው አደረግከን፡፡ በኃጢአቶቻችንም መሰከርን፡፡ ታዲያ (ከእሳት) ወደ መውጣት መንገድ አለን?» ይላሉ፡፡

قَالُواْ رَبَّنَآ أَمَتَّنَا ٱثۡنَتَيۡنِ وَأَحۡيَيۡتَنَا ٱثۡنَتَيۡنِ فَٱعۡتَرَفۡنَا بِذُنُوبِنَا فَهَلۡ إِلَىٰ خُرُوجٖ مِّن سَبِيلٖ ١١

12. «ይህ እነሆ አላህ ብቻውን በተጠራ ጊዜ ስለ ካዳችሁ በእርሱም ተጋሪ ቢደረግ የምታምኑ ስለ ኾናችሁ ነው፡፡ ስለዚህ ፍርዱ ከፍተኛ ታላቅ ለኾነው አላህ ብቻ ነው፡፡»

ذَٰلِكُم بِأَنَّهُۥٓ إِذَا دُعِيَ ٱللَّهُ وَحۡدَهُۥ كَفَرۡتُمۡ وَإِن يُشۡرَكۡ بِهِۦ تُؤۡمِنُواْۚ فَٱلۡحُكۡمُ لِلَّهِ ٱلۡعَلِيِّ ٱلۡكَبِيرِ ١٢

13. እርሱ ያ (ለአምላክነቱ) ምልክቶቹን የሚያሳያችሁ ለእናንተም ከሰማይ ሲሳይን የሚያወርድላችሁ ነው፡፡ ወደእርሱም የሚመለስ ሰው ቢኾን እንጂ ሌላው አይገሰጽም፡፡

هُوَ ٱلَّذِي يُرِيكُمۡ ءَايَٰتِهِۦ وَيُنَزِّلُ لَكُم مِّنَ ٱلسَّمَآءِ رِزۡقٗاۚ وَمَا يَتَذَكَّرُ إِلَّا مَن يُنِيبُ ١٣

14. አላህንም ከሓዲዎች ቢጠሉም ሃይማኖትን ለእርሱ አጥሪዎች ኾናችሁ ተገዙት፡፡

فَٱدۡعُواْ ٱللَّهَ مُخۡلِصِينَ لَهُ ٱلدِّينَ وَلَوۡ كَرِهَ ٱلۡكَٰفِرُونَ ١٤

15. (እርሱ) ደረጃዎችን ከፍ አድራጊ የዐርሹ ባለቤት ነው፡፡ የመገናኛውን ቀን ያስፈራራ ዘንድ ከባሮቹ በሚሻው ሰው ላይ ከትዕዛዙ መንፈስን (ራእይን) ያወርዳል፡፡

رَفِيعُ ٱلدَّرَجَٰتِ ذُو ٱلۡعَرۡشِ يُلۡقِي ٱلرُّوحَ مِنۡ أَمۡرِهِۦ عَلَىٰ مَن يَشَآءُ مِنۡ عِبَادِهِۦ لِيُنذِرَ يَوۡمَ ٱلتَّلَاقِ ١٥

16. እነርሱ (ከመቃብር) በሚወጡበት ቀን በአላህ ላይ ከእነርሱ ምንም ነገር አይደበቅም፡፡ «ንግሥናው ዛሬ ለማን ነው?» (ይባላል፤)፡፡ «ለአሸናፊው ለአንዱ አላህ ብቻ ነው» (ይባላል)፡፡

يَوۡمَ هُم بَٰرِزُونَۖ لَا يَخۡفَىٰ عَلَى ٱللَّهِ مِنۡهُمۡ شَيۡءٞۚ لِّمَنِ ٱلۡمُلۡكُ ٱلۡيَوۡمَۖ لِلَّهِ ٱلۡوَٰحِدِ ٱلۡقَهَّارِ ١٦

17. «ዛሬ ነፍስ ሁሉ በሠራችው ሥራ ትምመነዳለች፡፡ ዛሬ በደል የለም፡፡ አላህ በእርግጥ ምርመራው ፈጣን ነው» (ይባላል)፡፡

ٱلۡيَوۡمَ تُجۡزَىٰ كُلُّ نَفۡسِۭ بِمَا كَسَبَتۡۚ لَا ظُلۡمَ ٱلۡيَوۡمَۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَرِيعُ ٱلۡحِسَابِ ١٧

18. ቅርቢቱንም (የትንሣኤን) ቀን ልቦች ጭንቀትን የተመሉ ኾነው ላንቃዎች ዘንድ የሚደርሱበትን ጊዜ አስጠንቅቃቸው፡፡ ለበዳዮች ምንም ወዳጅና ተሰሚ አማላጅ የላቸውም፡፡

وَأَنذِرۡهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡأٓزِفَةِ إِذِ ٱلۡقُلُوبُ لَدَى ٱلۡحَنَاجِرِ كَٰظِمِينَۚ مَا لِلظَّٰلِمِينَ مِنۡ حَمِيمٖ وَلَا شَفِيعٖ يُطَاعُ ١٨

19. (አላህ) የዓይኖችን ክዳት ልቦችም የሚደብቁትን ሁሉ ያውቃል፡፡

يَعۡلَمُ خَآئِنَةَ ٱلۡأَعۡيُنِ وَمَا تُخۡفِي ٱلصُّدُورُ ١٩

20. አላህም በእውነት ይፈርዳል፡፡ እነዚያም ከእርሱ ሌላ የሚግገዟቸው በምንም አይፈርዱም፡፡ አላህ እርሱ ሰሚው ተመልካቹ ነው፡፡

وَٱللَّهُ يَقۡضِي بِٱلۡحَقِّۖ وَٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ مِن دُونِهِۦ لَا يَقۡضُونَ بِشَيۡءٍۗ إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡبَصِيرُ ٢٠

21. የእነዚያን ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ሕዝቦች ፍጻሜ እንዴት እንደነበረ ይመለከቱ ዘንድ በምድር ላይ አይኼዱምን? በኀይልና በምድር ላይ በተዋቸው ምልክቶች፤ ከእነርሱ ይበልጥ የበረቱ ነበሩ፡፡ አላህም በኀጢአቶቻቸው ያዛቸው፡፡ ለእነርሱም ከአላህ (ቅጣት) ምንም ጠባቂ አልነበራቸውም፡፡

۞أَوَلَمۡ يَسِيرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَيَنظُرُواْ كَيۡفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ كَانُواْ مِن قَبۡلِهِمۡۚ كَانُواْ هُمۡ أَشَدَّ مِنۡهُمۡ قُوَّةٗ وَءَاثَارٗا فِي ٱلۡأَرۡضِ فَأَخَذَهُمُ ٱللَّهُ بِذُنُوبِهِمۡ وَمَا كَانَ لَهُم مِّنَ ٱللَّهِ مِن وَاقٖ ٢١

22. ይህ (መያዝ) እነርሱ መልክተኞቻቸው በተዓምራቶች ይመጡባቸው ስለነበሩና ስለ ካዱ ነው፡፡ አላህም ያዛቸው፡፡ እርሱ ኀያል ቅጣተ ብርቱ ነውና፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ كَانَت تَّأۡتِيهِمۡ رُسُلُهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَكَفَرُواْ فَأَخَذَهُمُ ٱللَّهُۚ إِنَّهُۥ قَوِيّٞ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٢٢

23. ሙሳንም በተዓምራቶቻችንና በግልጽ ማስረጃ በእርግጥ ላክነው፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا مُوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَا وَسُلۡطَٰنٖ مُّبِينٍ ٢٣

24. ወደ ፈርዖንና ወደ ሃማን፤ ወደ ቃሩንም (ላክነው)፡ ፡ «ድግምተኛ ውሸታም ነው» አሉም፡፡

إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ وَهَٰمَٰنَ وَقَٰرُونَ فَقَالُواْ سَٰحِرٞ كَذَّابٞ ٢٤

25. ከእኛ ዘንድ እውነትን ይዞ በመጣላቸውም ጊዜ «የእነዚያን ከእርሱ ጋር ያመኑትን ሰዎች ወንዶች ልጆች ግደሉ፤ ሴቶቻቸውንም አስቀሩ» አሉ፡፡ የከሓዲዎችም ተንኮል በጥፋት ውስጥ እንጅ አይደለም፡፡

فَلَمَّا جَآءَهُم بِٱلۡحَقِّ مِنۡ عِندِنَا قَالُواْ ٱقۡتُلُوٓاْ أَبۡنَآءَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مَعَهُۥ وَٱسۡتَحۡيُواْ نِسَآءَهُمۡۚ وَمَا كَيۡدُ ٱلۡكَٰفِرِينَ إِلَّا فِي ضَلَٰلٖ ٢٥

26. ፈርዖንም «ተዉኝ፤ ሙሳን ልግደል፡፡ ጌታውንም ይጥራ፡፡ ያድነው እንደኾነ፡፡ እኔ ሃይማኖታችሁን ሊለውጥ፤ ወይም በምድር ውስጥ ጥፋትን ሊያሰራጭ እፈራለሁና» አለ፡፡

وَقَالَ فِرۡعَوۡنُ ذَرُونِيٓ أَقۡتُلۡ مُوسَىٰ وَلۡيَدۡعُ رَبَّهُۥٓۖ إِنِّيٓ أَخَافُ أَن يُبَدِّلَ دِينَكُمۡ أَوۡ أَن يُظۡهِرَ فِي ٱلۡأَرۡضِ ٱلۡفَسَادَ ٢٦

27. ሙሳም «እኔ በምርመራው ቀን ከማያምን ትዕቢተኛ ሁሉ በጌታዬና በጌታችሁ ተጠበቅሁ» አለ፡፡

وَقَالَ مُوسَىٰٓ إِنِّي عُذۡتُ بِرَبِّي وَرَبِّكُم مِّن كُلِّ مُتَكَبِّرٖ لَّا يُؤۡمِنُ بِيَوۡمِ ٱلۡحِسَابِ ٢٧

28. ከፈርዖንም ቤተሰቦች አንድ እምነቱን የሚደብቅ ምእመን ሰው አለ፡- «ሰውየውን ከጌታችሁ በተዓምራቶች በእርግጥ የመጣለችሁ ሲኾን ‹ጌታዬ አላህ ነው› ስለሚል ትገድላላችሁን? ውሸታምም ቢኾን ውሸቱ በርሱው ላይ ነው፡፡ እውነተኛ ቢኾን ግን የዚያ የሚያስፈራራችሁ ከፊሉ ያገኛችኋል፡፡ አላህ ያንን እርሱ ድንበር አላፊ ውሸታም የኾነውን አይመራምና፡፡

وَقَالَ رَجُلٞ مُّؤۡمِنٞ مِّنۡ ءَالِ فِرۡعَوۡنَ يَكۡتُمُ إِيمَٰنَهُۥٓ أَتَقۡتُلُونَ رَجُلًا أَن يَقُولَ رَبِّيَ ٱللَّهُ وَقَدۡ جَآءَكُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ مِن رَّبِّكُمۡۖ وَإِن يَكُ كَٰذِبٗا فَعَلَيۡهِ كَذِبُهُۥۖ وَإِن يَكُ صَادِقٗا يُصِبۡكُم بَعۡضُ ٱلَّذِي يَعِدُكُمۡۖ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي مَنۡ هُوَ مُسۡرِفٞ كَذَّابٞ ٢٨

29. «ወገኖቼ ሆይ! በምድር ላይ አሸናፊዎች ስትኾኑ ዛሬ መንግስቱ የእናንተ ነው፡፡ ታዲያ ከአላህ ቅጣት ቢመጣብን የሚያድነን ማን ነው?» (አለ)፡፡ ፈርዖን «የማየውን ነገር እንጅ፤ አላመለከታችሁም፡፡ ቅኑንም መንገድ እንጅ አልመራችሁም» አላቸው፡፡

يَٰقَوۡمِ لَكُمُ ٱلۡمُلۡكُ ٱلۡيَوۡمَ ظَٰهِرِينَ فِي ٱلۡأَرۡضِ فَمَن يَنصُرُنَا مِنۢ بَأۡسِ ٱللَّهِ إِن جَآءَنَاۚ قَالَ فِرۡعَوۡنُ مَآ أُرِيكُمۡ إِلَّا مَآ أَرَىٰ وَمَآ أَهۡدِيكُمۡ إِلَّا سَبِيلَ ٱلرَّشَادِ ٢٩

30. ያም ያመነው ሰው አለ «እኔ በናንተ ላይ የአሕዛቦቹን ቀን ብጤ እፈራላችኋለሁ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِيٓ ءَامَنَ يَٰقَوۡمِ إِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُم مِّثۡلَ يَوۡمِ ٱلۡأَحۡزَابِ ٣٠

31. «የኑሕን ሕዝቦች፣ የዓድንና የሰሙድንም፣ የእነዚያንም ከኋላቸው የነበሩትን ልማድ ብጤ (እፈራላችኋለሁ)፡፡ አላህም ለባሮቹ መበደልን የሚሻ አይደለም፡፡

مِثۡلَ دَأۡبِ قَوۡمِ نُوحٖ وَعَادٖ وَثَمُودَ وَٱلَّذِينَ مِنۢ بَعۡدِهِمۡۚ وَمَا ٱللَّهُ يُرِيدُ ظُلۡمٗا لِّلۡعِبَادِ ٣١

32. «ወገኖቼ ሆይ! እኔ በእናንተ ላይ የመጠራሪያን ቀን እፈራለሁ፡፡»

وَيَٰقَوۡمِ إِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ يَوۡمَ ٱلتَّنَادِ ٣٢

33. ወደ ኋላ ዞራችሁ በምትሸሹበት ቀን፤ ለናንተ ከአላህ (ቅጣት) ምንም ጠባቂ የላችሁም፡፡ አላህም የሚያጠመው ሰው ለርሱ ምንም አቅኚ የለውም፡፡

يَوۡمَ تُوَلُّونَ مُدۡبِرِينَ مَا لَكُم مِّنَ ٱللَّهِ مِنۡ عَاصِمٖۗ وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِنۡ هَادٖ ٣٣

34. ዩሱፍም ከዚህ በፊት ግልጽ ማስረጃዎችን በእርግጥ አመጣላችሁ፡፡ ከዚያም እርሱ ካመጣላችሁ ነገር ከመጠራጠር አልተወገዳችሁም፡፡ በጠፋም ጊዜ «አላህ ከእርሱ ኋላ መልክተኛን በጭራሽ አይልክም» አላችሁ፡፡ አላህ እንደዚሁ ድንበር አላፊ ተጠራጣሪ የኾነን ሰው ያሳስታል፡፡

وَلَقَدۡ جَآءَكُمۡ يُوسُفُ مِن قَبۡلُ بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَمَا زِلۡتُمۡ فِي شَكّٖ مِّمَّا جَآءَكُم بِهِۦۖ حَتَّىٰٓ إِذَا هَلَكَ قُلۡتُمۡ لَن يَبۡعَثَ ٱللَّهُ مِنۢ بَعۡدِهِۦ رَسُولٗاۚ كَذَٰلِكَ يُضِلُّ ٱللَّهُ مَنۡ هُوَ مُسۡرِفٞ مُّرۡتَابٌ ٣٤

35. እነዚያ፤ የመጣላቸው አስረጅ ሳይኖር በአላህ ተዓምራቶች የሚከራከሩ (ክርክራቸው) አላህ ዘንድና እነዚያም አመኑት ዘንድ መጠላቱ በጣም ተለቀ፡፡ እንደዚሁ አላህ በኩሩ ጨካኝ (ሰው) ልብ ሁሉ ላይ ያትማል፡፡

ٱلَّذِينَ يُجَٰدِلُونَ فِيٓ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ بِغَيۡرِ سُلۡطَٰنٍ أَتَىٰهُمۡۖ كَبُرَ مَقۡتًا عِندَ ٱللَّهِ وَعِندَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۚ كَذَٰلِكَ يَطۡبَعُ ٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ قَلۡبِ مُتَكَبِّرٖ جَبَّارٖ ﴿٣٥﴾

36. ፈርዖንም አለ «ሃማን ሆይ! መንገዶችን እደርስ ዘንድ ረዢም ሕንጻን ለእኔ ካብልኝ፡፡

وَقَالَ فِرۡعَوۡنُ يَٰهَٰمَٰنُ ٱبۡنِ لِي صَرۡحٗا لَّعَلِّيٓ أَبۡلُغُ ٱلۡأَسۡبَٰبَ ﴿٣٦﴾

37. «የሰማያትን መንገዶች (እደርስ ዘንድ)፣ ወደ ሙሳም አምላክ እመለከት ዘንድ፡፡ እኔም ውሸታም ነው ብዬ በእርግጥ እጠረጥረዋለሁ» (አለ)፡፡ እንደዚሁም ለፈርዖን መጥፎ ሥራው ተሸለመለት፡፡ ከቅን መንገድም ታገደ፡፡ የፈርዖንም ተንኮል በከሳራ ውስጥ እንጅ አይደለም፡፡

أَسۡبَٰبَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ فَأَطَّلِعَ إِلَىٰٓ إِلَٰهِ مُوسَىٰ وَإِنِّي لَأَظُنُّهُۥ كَٰذِبٗاۚ وَكَذَٰلِكَ زُيِّنَ لِفِرۡعَوۡنَ سُوٓءُ عَمَلِهِۦ وَصُدَّ عَنِ ٱلسَّبِيلِۚ وَمَا كَيۡدُ فِرۡعَوۡنَ إِلَّا فِي تَبَابٖ ﴿٣٧﴾

38. ያም ያመነው አለ «ወገኖቼ ሆይ! ተከተሉኝ፡፡ ቀጥታውን መንገድ እመራችኋለሁና፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِيٓ ءَامَنَ يَٰقَوۡمِ ٱتَّبِعُونِ أَهۡدِكُمۡ سَبِيلَ ٱلرَّشَادِ ﴿٣٨﴾

39. «ወገኖቼ ሆይ! ይህቺ ቅርቢቱ ሕይወት (ጥቂት) መጣቀሚያ ብቻ ናት፡፡ መጨረሻይቱም ዓለም እርሷ መርጊያ አገር ናት፡፡»

يَٰقَوۡمِ إِنَّمَا هَٰذِهِ ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا مَتَٰعٞ وَإِنَّ ٱلۡأٓخِرَةَ هِيَ دَارُ ٱلۡقَرَارِ ﴿٣٩﴾

40. «መጥፎን የሠራ ሰው ብጤዋን እንጅ አይምመነዳም፡፡ እርሱ ምእመን ኾኖ ከወንድ ወይም ከሴት በጎን የሠራም ሰው እነዚያ ገነትን ይገባሉ፡፡ በእርሷ ውስጥ ያለ ቁጥጥር ይመገባሉ፡፡

مَنۡ عَمِلَ سَيِّئَةٗ فَلَا يُجۡزَىٰٓ إِلَّا مِثۡلَهَاۖ وَمَنۡ عَمِلَ صَٰلِحٗا مِّن ذَكَرٍ أَوۡ أُنثَىٰ وَهُوَ مُؤۡمِنٞ فَأُوْلَٰٓئِكَ يَدۡخُلُونَ ٱلۡجَنَّةَ يُرۡزَقُونَ فِيهَا بِغَيۡرِ حِسَابٖ ﴿٤٠﴾

41. «ወገኖቼም ሆይ! ወደ መዳን የምጠራችሁ ስኾን ወደ እሳትም የምትጠሩኝ ስትኾኑ ለኔ ምን አለኝ!

۞وَيَٰقَوۡمِ مَا لِيٓ أَدۡعُوكُمۡ إِلَى ٱلنَّجَوٰةِ وَتَدۡعُونَنِيٓ إِلَى ٱلنَّارِ ﴿٤١﴾

42. «በአላህ ልክድና በእርሱም ለእኔ ዕውቀት የሌለኝን ነገር በእርሱ እንዳጋራ ትጠሩኛላችሁ፡፡ እኔም ወደ አሸናፊው፣ መሓሪው (አላህ) እጠራችኋለሁ፡፡

تَدۡعُونَنِي لِأَكۡفُرَ بِٱللَّهِ وَأُشۡرِكَ بِهِۦ مَا لَيۡسَ لِي بِهِۦ عِلۡمٞ وَأَنَا۠ أَدۡعُوكُمۡ إِلَى ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡغَفَّٰرِ ﴿٤٢﴾

43. «በእርግጥ ወደእርሱ የምትጠሩብኝ (ጣዖት) ለእርሱ በቅርቢቱም ኾነ በመጨረሻይቱ ዓለም (ተሰሚ) ጥሪ የለውም፡፡ መመለሻችንም በእርግጥ ወደ አላህ ነው፡፡ ወሰን አላፊዎቹም እነሱ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡

لَا جَرَمَ أَنَّمَا تَدۡعُونَنِيٓ إِلَيۡهِ لَيۡسَ لَهُۥ دَعۡوَةٞ فِي ٱلدُّنۡيَا وَلَا فِي ٱلۡأٓخِرَةِ وَأَنَّ مَرَدَّنَآ إِلَى ٱللَّهِ وَأَنَّ ٱلۡمُسۡرِفِينَ هُمۡ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِ ﴿٤٣﴾

44. «ወደ ፊትም ለእናንተ የምላችሁን ምክር (ቅጣትን በምታዩ ጊዜ) ታስታውሳላችሁ፡፡ ነገሬንም ሁሉ ወደ አላህ አስጠጋለሁ፡፡ አላህ ባሮቹን ተመልካች ነውና፡፡»

فَسَتَذۡكُرُونَ مَآ أَقُولُ لَكُمۡۚ وَأُفَوِّضُ أَمۡرِيٓ إِلَى ٱللَّهِۚ إِنَّ ٱللَّهَ بَصِيرُۢ بِٱلۡعِبَادِ ﴿٤٤﴾

45. ከመከሩዋቸውም መጥፎዎች አላህ ጠበቀው:: በፈርዖን ቤተሰቦችም ላይ ክፉ ቅጣት ሰፈረባቸው::

فَوَقَىٰهُ ٱللَّهُ سَيِّـَٔاتِ مَا مَكَرُواْۖ وَحَاقَ بِـَٔالِ فِرۡعَوۡنَ سُوٓءُ ٱلۡعَذَابِ ٤٥

46. እሳት በጧትና በማታ በእርሷ ላይ ይቀርባሉ:: ሰዓቲቱም በምትኾንበት ቀን «የፈርዖንን ቤተሰቦች ብርቱን ቅጣት (ገሀነምን) አግቡዋቸው» (ይባላል)::

ٱلنَّارُ يُعۡرَضُونَ عَلَيۡهَا غُدُوّٗا وَعَشِيّٗاۚ وَيَوۡمَ تَقُومُ ٱلسَّاعَةُ أَدۡخِلُوٓاْ ءَالَ فِرۡعَوۡنَ أَشَدَّ ٱلۡعَذَابِ ٤٦

47. በእሳትም ውስጥ የሚከራከሩበትን ጊዜ (አስታውስ):: ደካማዎቹም ለእነዚያ ለኮሩት «እኛ ለእናንተ ተከታዮች ነበርንና እናንተ (አሁን) ከእሳት ከፊሉን ከእኛ ላይ ገፍታሪዎች ናችሁን?» ይላሉ::

وَإِذۡ يَتَحَآجُّونَ فِي ٱلنَّارِ فَيَقُولُ ٱلضُّعَفَٰٓؤُاْ لِلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُوٓاْ إِنَّا كُنَّا لَكُمۡ تَبَعٗا فَهَلۡ أَنتُم مُّغۡنُونَ عَنَّا نَصِيبٗا مِّنَ ٱلنَّارِ ٤٧

48. እነዚያም የኮሩት «እኛ ሁላችንም በውስጧ ነን:: አላህ በባሮቹ መካከል በእርግጥ ፈረደ» ይላሉ::

قَالَ ٱلَّذِينَ ٱسۡتَكۡبَرُوٓاْ إِنَّا كُلّٞ فِيهَآ إِنَّ ٱللَّهَ قَدۡ حَكَمَ بَيۡنَ ٱلۡعِبَادِ ٤٨

49. እነዚያም በእሳት ውስጥ ያሉት ለገሀነም ዘበኞች «ጌታችሁን ለምኑልን፤ ከእኛ ላይ ከቅጣቱ አንድን ቀን ያቃልልን» ይላሉ::

وَقَالَ ٱلَّذِينَ فِي ٱلنَّارِ لِخَزَنَةِ جَهَنَّمَ ٱدۡعُواْ رَبَّكُمۡ يُخَفِّفۡ عَنَّا يَوۡمٗا مِّنَ ٱلۡعَذَابِ ٤٩

50. (ዘበኞቹም) «መልእክተኞቻችሁ በተዓምራቶች ይመጡላችሁ አልነበሩምን?» ይላሉ:: (ከሓዲዎቹም) «እንዴታ መጥተውናል እንጅ፤ (ግን አስተባበልናቸው)» ይላሉ:: «እንግዲያውስ ጸልዩ:: የከሓዲዎችም ጸሎት በከንቱ እንጅ አይደለም» ይሏቸዋል::

قَالُوٓاْ أَوَلَمۡ تَكُ تَأۡتِيكُمۡ رُسُلُكُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِۖ قَالُواْ بَلَىٰۚ قَالُواْ فَٱدۡعُواْۗ وَمَا دُعَٰٓؤُاْ ٱلۡكَٰفِرِينَ إِلَّا فِي ضَلَٰلٍ ٥٠

51. እኛ መልክተኞቻችንን፣ እነዚያንም ያመኑትን በቅርቢቱ ሕይወት ምስክሮችም በሚቆሙበት ቀን በእርግጥ እንረዳለን::

إِنَّا لَنَنصُرُ رُسُلَنَا وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَيَوۡمَ يَقُومُ ٱلۡأَشۡهَٰدُ ٥١

52. በደለኞችን ምክንያታቸው በማይጠቅማቸው ቀን (እንረዳለን):: ለእነርሱም ርግማን አልላቸው:: ለእነርሱም መጥፎ አገር አልላቸው::

يَوۡمَ لَا يَنفَعُ ٱلظَّٰلِمِينَ مَعۡذِرَتُهُمۡۖ وَلَهُمُ ٱللَّعۡنَةُ وَلَهُمۡ سُوٓءُ ٱلدَّارِ ٥٢

53. ሙሳንም መምሪያን በእርግጥ ሰጠነው:: የእስራኤልንም ልጆች መጽሐፉን አወረስናቸው::

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡهُدَىٰ وَأَوۡرَثۡنَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱلۡكِتَٰبَ ٥٣

54. ለባለ አእምሮዎች መሪና ገሳጭ ሲኾን::

هُدٗى وَذِكۡرَىٰ لِأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ ٥٤

55. (ሙሐመድ ሆይ!) ታገስም የአላህ ተስፋ እውነት ነውና:: ለስህተትህም ምሕረትን ለምን:: ከቀትር በኋላም በማለዳም ጌታህን ከማመስገን ጋር አጥራው::

فَٱصۡبِرۡ إِنَّ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٞ وَٱسۡتَغۡفِرۡ لِذَنۢبِكَ وَسَبِّحۡ بِحَمۡدِ رَبِّكَ بِٱلۡعَشِيِّ وَٱلۡإِبۡكَٰرِ ٥٥

56. እነዚያ የመጣላቸው አስረጅ ሳይኖር በአላህ አንቀጾች የሚከራከሩ በልቦቻቸው ውስጥ እነርሱ ደራሾቹ ያልኾኑት ኩራት ብቻ እንጅ ምንም የለም፡፡ በአላህም ተጠበቅ፡፡ እነሆ እርሱ ሰሚው ተመልካቹ ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُجَٰدِلُونَ فِيٓ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ بِغَيۡرِ سُلۡطَٰنٍ أَتَىٰهُمۡ إِن فِي صُدُورِهِمۡ إِلَّا كِبۡرٞ مَّا هُم بِبَٰلِغِيهِۚ فَٱسۡتَعِذۡ بِٱللَّهِۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡبَصِيرُ ٥٦

57. ሰማያትንና ምድርን መፍጠር ሰዎችን ከመፍጠር ይልቅ ታላቅ ነው፡፡ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች አያውቁም፡፡

لَخَلۡقُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ أَكۡبَرُ مِنۡ خَلۡقِ ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعۡلَمُونَ ٥٧

58. ዕውርና የሚያይ እነዚያም አምነው መልካሞችን የሠሩና መጥፎ ሠሪው አይስተካከሉም፡፡ በጣም ጥቂትን ብቻ ትገሰጻላችሁ፡፡

وَمَا يَسۡتَوِي ٱلۡأَعۡمَىٰ وَٱلۡبَصِيرُ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَلَا ٱلۡمُسِيٓءُۚ قَلِيلٗا مَّا تَتَذَكَّرُونَ ٥٨

59. ሰዓቲቱ በእርግጥ መጪ ናት፡፡ በእርሷ ጥርጥር የለም፡፡ ግን አብዛኞቹ ሰዎች አያምኑም፡፡

إِنَّ ٱلسَّاعَةَ لَأٓتِيَةٞ لَّا رَيۡبَ فِيهَا وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يُؤۡمِنُونَ ٥٩

60. ጌታችሁም አለ «ለምኑኝ፤ እቀበላችኋለሁና፡፡ እነዚያ እኔን ከመግገዛት የሚኮሩት ተዋራጆች ኾነው ገሀነምን በእርግጥ ይገባሉ፡፡

وَقَالَ رَبُّكُمُ ٱدۡعُونِيٓ أَسۡتَجِبۡ لَكُمۡۚ إِنَّ ٱلَّذِينَ يَسۡتَكۡبِرُونَ عَنۡ عِبَادَتِي سَيَدۡخُلُونَ جَهَنَّمَ دَاخِرِينَ ٦٠

61. አላህ ያ ለእናንተ ሌሊትን በውስጡ ልታርፉበት (ጨለማ) ቀንንም (ልትሠሩበት) የሚያሳይ ያደረገላችሁ ነው፡፡ አላህ በሰዎች ላይ በእርግጥ የችሮታ ባለቤት ነውና፡፡ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች አያመሰግኑም፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلَّيۡلَ لِتَسۡكُنُواْ فِيهِ وَٱلنَّهَارَ مُبۡصِرًاۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَذُو فَضۡلٍ عَلَى ٱلنَّاسِ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَشۡكُرُونَ ٦١

62. ይሃችሁ ጌታችሁ አላህ ነው፤ የነገሩ ሁሉ ፈጣሪ ነው፤ ከርሱ ሌላ አምላክ የለም፤ ታዲያ (ከእምነት) ወዴት ትመለሳላችሁ፡፡

ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبُّكُمۡ خَٰلِقُ كُلِّ شَيۡءٖ لَّآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ فَأَنَّىٰ تُؤۡفَكُونَ ٦٢

63. እንደዚሁ እነዚያ በአላህ አንቀጾች ይክዱ የነበሩት (ከእምነት) ይመለሳሉ፡፡

كَذَٰلِكَ يُؤۡفَكُ ٱلَّذِينَ كَانُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ يَجۡحَدُونَ ٦٣

64. አላህ ያ ምድርን መርጊያ ሰማይንም ጣሪያ ያደረገላችሁ ነው፡፡ የቀረጻችኁም ቅርጻችሁንም ያሳመረ ከጣፋጮችም ሲሳዮች የሰጣችሁ ነው፡፡ ይሃችሁ ጌታችሁ አላህ ነው፡፡ የዓለማትም ጌታ አላህ ላቀ፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ قَرَارٗا وَٱلسَّمَآءَ بِنَآءٗ وَصَوَّرَكُمۡ فَأَحۡسَنَ صُوَرَكُمۡ وَرَزَقَكُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِۚ ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبُّكُمۡۖ فَتَبَارَكَ ٱللَّهُ رَبُّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٦٤

65. እርሱ ብቻ (ሁል ጊዜ) ሕያው ነው፤ ከርሱ ሌላ አምላክ የለም፤ ሃይማኖትንም ለእርሱ ያጠራችሁ ስትኾኑ «ምስጋና ለዓለማት ጌታ ለአላህ ይኹን» የምትሉ ኾናችሁ ተገዙት፡፡

هُوَ ٱلۡحَيُّ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ فَٱدۡعُوهُ مُخۡلِصِينَ لَهُ ٱلدِّينَۗ ٱلۡحَمۡدُ لِلَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٦٥

66. «እኔ ከጌታዬ አስረጂዎች በመጡልኝ ጊዜ እነዚያን ከአላህ ሌላ የምትገዙዋቸውን እንዳልገዛ ተከልክያለሁ፡፡ ለዓለማት ጌታም እንድገዛ ታዝዣለሁ» በላቸው፡፡

۞قُلۡ إِنِّي نُهِيتُ أَنۡ أَعۡبُدَ ٱلَّذِينَ تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ لَمَّا جَآءَنِيَ ٱلۡبَيِّنَٰتُ مِن رَّبِّي وَأُمِرۡتُ أَنۡ أُسۡلِمَ لِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٦٦

67. እርሱ ያ ከዐፈር ከዚያም ከፍትወት ጠብታ ከዚያም ከረጋ ደም የፈጠራችሁ ነው፡፡ ከዚያም ሕጻናት አድርጎ ያወጣችኋል፡፡ ከዚያም ጥንካሬያችሁን ትደርሱ ዘንድ፤ ከዚያም ሽማግሌዎች ትኾኑ ዘንድ (ያቆያችኋል)፡፡ ከእናንተም ውስጥ ከዚህ በፊት የሚሞት አልለ፡፡ (ይህንንም ያደረገው ልትኖሩና) የተወሰነ ጊዜንም ልትደርሱ ታውቁም ዘንድ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِى خَلَقَكُم مِّن تُرَابٍ ثُمَّ مِن نُّطْفَةٍ ثُمَّ مِنْ عَلَقَةٍ ثُمَّ يُخْرِجُكُمْ طِفْلًا ثُمَّ لِتَبْلُغُوٓاْ أَشُدَّكُمْ ثُمَّ لِتَكُونُواْ شُيُوخًا ۚ وَمِنكُم مَّن يُتَوَفَّىٰ مِن قَبْلُ ۖ وَلِتَبْلُغُوٓاْ أَجَلًا مُّسَمًّى وَلَعَلَّكُمْ تَعْقِلُونَ ﴿٦٧﴾

68. እርሱ ያ ሕያው የሚያደርግ የሚገድልም ነው፡፡ አንዳችን ነገር በሻም ጊዜ ለእርሱ የሚለውን «ኹን» ነው፤ ወዲያውም ይኾናል፡፡

هُوَ ٱلَّذِى يُحْىِۦ وَيُمِيتُ ۖ فَإِذَا قَضَىٰٓ أَمْرًا فَإِنَّمَا يَقُولُ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ﴿٦٨﴾

69. ወደእነዚያ በአላህ አንቀጾች ወደሚከራከሩት (ከእምነት) እንዴት እንደሚመለሱ አታይምን?

أَلَمْ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ يُجَٰدِلُونَ فِىٓ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ أَنَّىٰ يُصْرَفُونَ ﴿٦٩﴾

70. ወደእነዚያ በመጽሐፉ በዚያም መልክተኞቻችንን በእርሱ በላክንበት ወዳስተባበሉት (አታይምን?) ወደፊትም ያውቃሉ፡፡

ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِٱلْكِتَٰبِ وَبِمَآ أَرْسَلْنَا بِهِۦ رُسُلَنَا ۖ فَسَوْفَ يَعْلَمُونَ ﴿٧٠﴾

71. እንዛዝላዎቹና ሰንሰለቶቹ በአንገቶቻቸው ላይ በተደረጉ ጊዜ (በእርሷ) ይጎተታሉ፡፡

إِذِ ٱلْأَغْلَٰلُ فِىٓ أَعْنَٰقِهِمْ وَٱلسَّلَٰسِلُ يُسْحَبُونَ ﴿٧١﴾

72. በገሀነም ውስጥ (ይጎተታሉ)፤ ከዚያም በእሳት ውስጥ ይማገዳሉ፡፡

فِى ٱلْحَمِيمِ ثُمَّ فِى ٱلنَّارِ يُسْجَرُونَ ﴿٧٢﴾

73. ከዚያም ለእነርሱ ይባላሉ (በአላህ) «ታጋሯቸው የነበራችሁት የታሉ?»

ثُمَّ قِيلَ لَهُمْ أَيْنَ مَا كُنتُمْ تُشْرِكُونَ ﴿٧٣﴾

74. «ከአላህ ሌላ (የምታጋሩዋቸው)፤ ከኛ ተሰወሩን?» «ከቶ ከዚህ በፊት ምንንም የምንገዛ አልነበርንም» ይላሉ፤ እንደዚሁ አላህ ከሓዲዎችን ያሳስታል፡፡

مِن دُونِ ٱللَّهِ ۖ قَالُواْ ضَلُّواْ عَنَّا بَل لَّمْ نَكُن نَّدْعُواْ مِن قَبْلُ شَيْـًٔا ۚ كَذَٰلِكَ يُضِلُّ ٱللَّهُ ٱلْكَٰفِرِينَ ﴿٧٤﴾

75. ይህ (ቅጣት) ያላግባብ በምድር ውስጥ ትደሰቱ በነበራችሁትና ትንበጣረሩ በነበራችሁት ነው (ይባላሉ)፡፡

ذَٰلِكُم بِمَا كُنتُمْ تَفْرَحُونَ فِى ٱلْأَرْضِ بِغَيْرِ ٱلْحَقِّ وَبِمَا كُنتُمْ تَمْرَحُونَ ﴿٧٥﴾

76. የገሀነምን በሮች በውስጧ ዘውታሪዎች ስትኾኑ ግቡ (ይባላሉ)፡፡ የትዕቢተኞችም መኖሪያ (ገሀነም) ምን ትከፋ!

ٱدْخُلُوٓاْ أَبْوَٰبَ جَهَنَّمَ خَٰلِدِينَ فِيهَا ۖ فَبِئْسَ مَثْوَى ٱلْمُتَكَبِّرِينَ ﴿٧٦﴾

77. ታገስም የአላህ ቀጠሮ እውነት ነውና፡፡ የዚያንም የምናስፈራራቸውን ከፊሉን (በሕይወትህ) ብናሳይህ (መልካም ነው)፡፡ ወይም ብንገድልህ ወደኛ ይመለሳሉ፡፡

فَٱصْبِرْ إِنَّ وَعْدَ ٱللَّهِ حَقٌّ ۚ فَإِمَّا نُرِيَنَّكَ بَعْضَ ٱلَّذِى نَعِدُهُمْ أَوْ نَتَوَفَّيَنَّكَ فَإِلَيْنَا يُرْجَعُونَ ﴿٧٧﴾

78. ካንተ በፊትም መልክተኞችን በእርግጥ ልከናል፡፡ ከእነርሱ ባንተ ላይ የተረክንልህ አልለ፡፡ ከእነርሱም ባንተ ላይ ያልተረክነው አልለ፡፡ ለማንኛውም መልክተኛ በአላህ ፈቃድ ካልኾነ ተዓምርን ሊያመጣ አይገባውም፡፡ የአላህም ትእዛዝ በመጣ ጊዜ በእውነት ይፈረዳል፡፡ እዚያ ዘንድም አጥፊዎቹ ይከስራሉ፡፡

وَلَقَدْ أَرْسَلْنَا رُسُلًا مِّن قَبْلِكَ مِنْهُم مَّن قَصَصْنَا عَلَيْكَ وَمِنْهُم مَّن لَّمْ نَقْصُصْ عَلَيْكَ ۗ وَمَا كَانَ لِرَسُولٍ أَن يَأْتِىَ بِـَٔايَةٍ إِلَّا بِإِذْنِ ٱللَّهِ ۚ فَإِذَا جَآءَ أَمْرُ ٱللَّهِ قُضِىَ بِٱلْحَقِّ وَخَسِرَ هُنَالِكَ ٱلْمُبْطِلُونَ ﴿٧٨﴾

79. አላህ ያ ለእናንተ ግመልን ከብትንና ፍየልን ከእርሷ (ከፊሷን) ልትጋልቡ የፈጠረላችሁ ነው፡፡ ከእርሷም ትበላላችሁ፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِى جَعَلَ لَكُمُ ٱلْأَنْعَٰمَ لِتَرْكَبُوا۟ مِنْهَا وَمِنْهَا تَأْكُلُونَ ﴿٧٩﴾

80. ለእናንተም በእርሷ ውስጥ ጥቅሞች አልሏችሁ፡፡ በእርሷም ላይ (እቃን በመጫን) በልቦቻችሁ ያሰባችሁትን ጉዳይ ትደርሱ ዘንድ (ፈጠረላችሁ)፡፡ በእርሷም ላይ በመርከቦችም ላይ ትሳፈራላችሁ፡፡

وَلَكُمْ فِيهَا مَنَٰفِعُ وَلِتَبْلُغُوا۟ عَلَيْهَا حَاجَةً فِى صُدُورِكُمْ وَعَلَيْهَا وَعَلَى ٱلْفُلْكِ تُحْمَلُونَ ﴿٨٠﴾

81. ተዓምራቱንም ያሳያችኋል፡፡ ታዲያ ከአላህ ተዓምራት የትኛውን ትክዳላችሁ?

وَيُرِيكُمْ ءَايَٰتِهِۦ فَأَىَّ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ تُنكِرُونَ ﴿٨١﴾

82. የእነዚያን ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ሕዝቦች ፍጻሜ እንዴት እንደነበረ ይመለከቱ ዘንድ በምድር ላይ አይኼዱምን? ከእነርሱ ይበልጥ ብዙዎች በኀይልና በምድር ላይ በተዋቸው ምልክቶችም በጣም ብርቱዎች ነበሩ፡፡ ያም ይሠሩት የነበሩት ከእነርሱ ምንም አልጠቀማቸውም፡፡

أَفَلَمْ يَسِيرُوا۟ فِى ٱلْأَرْضِ فَيَنظُرُوا۟ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ ۚ كَانُوٓا۟ أَكْثَرَ مِنْهُمْ وَأَشَدَّ قُوَّةً وَءَاثَارًا فِى ٱلْأَرْضِ فَمَآ أَغْنَىٰ عَنْهُم مَّا كَانُوا۟ يَكْسِبُونَ ﴿٨٢﴾

83. መልክተኞቻቸውም ተዓምራቶችን ባመጡላቸው ጊዜ እነርሱ ዘንድ ባለው ዕውቀት ተደሰቱ፡፡ በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩት ቅጣትም በእነርሱ ላይ ሰፈረባቸው፡፡

فَلَمَّا جَآءَتْهُمْ رُسُلُهُم بِٱلْبَيِّنَٰتِ فَرِحُوا۟ بِمَا عِندَهُم مِّنَ ٱلْعِلْمِ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُوا۟ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ﴿٨٣﴾

84. ብርቱ ቅጣታችንንም ባዩ ጊዜ «በአላህ አንድ ሲኾን አምነናል፤ በእርሱም እናጋራ በነበርነው (ጣዖታት) ክደናል» አሉ፡፡

فَلَمَّا رَأَوْا۟ بَأْسَنَا قَالُوٓا۟ ءَامَنَّا بِٱللَّهِ وَحْدَهُۥ وَكَفَرْنَا بِمَا كُنَّا بِهِۦ مُشْرِكِينَ ﴿٨٤﴾

85. ብርቱ ቅጣታችንን ባዩ ጊዜ ማመናቸውም የሚጠቅማቸው አልነበረም፡፡ የአላህን ደንብ ያችን በባሮቹ ውስጥ ያለፈችውን (ተጠንቀቁ) በዚያ ጊዜም ከሓዲዎች ከሰሩ፡፡

فَلَمْ يَكُ يَنفَعُهُمْ إِيمَٰنُهُمْ لَمَّا رَأَوْا۟ بَأْسَنَا ۖ سُنَّتَ ٱللَّهِ ٱلَّتِى قَدْ خَلَتْ فِى عِبَادِهِۦ ۖ وَخَسِرَ هُنَالِكَ ٱلْكَٰفِرُونَ ﴿٨٥﴾

# ሱረቱ ፉሲለት

# سورة فصّلت

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ.(ሓ ሚም)፡፡

حمٓ ﴿١﴾

2. (ይህ ቁርኣን) እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ ከሆነው (አላህ) የተወረደ ነው፡፡

تَنزِيلٌ مِّنَ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ ﴿٢﴾

3. እንቀጾቹ የተብራሩ የኾነ መጽሐፍ ነው፡፡ ዐረብኛ ቁርኣን ሲኾን ለሚያውቁ ሕዝቦች (የተብራራ) ነው፡፡

كِتَٰبٌ فُصِّلَتْ ءَايَٰتُهُۥ قُرْءَانًا عَرَبِيًّا لِّقَوْمٍ يَعْلَمُونَ ﴿٣﴾

4. አብሳሪና አስፈራሪ ሲኾን (ተወረደ)፡፡ አብዛኛዎቻቸውም ተዉት፡፡ እነርሱም አይሰሙም፡፡

بَشِيرًا وَنَذِيرًا فَأَعْرَضَ أَكْثَرُهُمْ فَهُمْ لَا يَسْمَعُونَ ﴿٤﴾

5. አሉም «ልቦቻችን ከእዚያ ወደእርሱ ከምትጠራን እምነት በመሸፈኛዎች ውስጥ ናቸው፡፡ በጆሮዎቻችንም ላይ ድንቁርና አልለ፤ በእኛና ባንተም መካከል ግርዶሽ አልለ፡፡ (በሃይማኖትህ) ሥስራም፤ እኛ ሠሪዎች ነንና፡፡ »

وَقَالُوا۟ قُلُوبُنَا فِىٓ أَكِنَّةٍ مِّمَّا تَدْعُونَآ إِلَيْهِ وَفِىٓ ءَاذَانِنَا وَقْرٌ وَمِنۢ بَيْنِنَا وَبَيْنِكَ حِجَابٌ فَٱعْمَلْ إِنَّنَا عَٰمِلُونَ ﴿٥﴾

6. (እንዲህ) በላቸው «እኔ መሰላችሁ ሰው ብቻ ነኝ፡፡ አምላካችሁ አንድ አምላክ ብቻ ነው ወደእርሱም ቀጥ በሉ ምሕረትንም ለምኑት ማለት ወደእኔ ይወረድልኛል፡፡ ለአጋሪዎቹም ወዮላቸው፡፡

قُلْ إِنَّمَآ أَنَا۠ بَشَرٌ مِّثْلُكُمْ يُوحَىٰٓ إِلَىَّ أَنَّمَآ إِلَٰهُكُمْ إِلَٰهٌ وَٰحِدٌ فَٱسْتَقِيمُوٓا۟ إِلَيْهِ وَٱسْتَغْفِرُوهُ ۗ وَوَيْلٌ لِّلْمُشْرِكِينَ ﴿٦﴾

7. ለእነዚያ ዘካን ለማይሰጡት እነርሱም በመጨረሻይቱ ዓለም እነርሱ ከሓዲዎች ለኾኑት (ወዮላቸው)፡፡

ٱلَّذِينَ لَا يُؤْتُونَ ٱلزَّكَوٰةَ وَهُم بِٱلْءَاخِرَةِ هُمْ كَٰفِرُونَ ﴿٧﴾

8. እነዚያ ያመኑትና በጎ ሥራዎችን የሠሩት ለእነርሱ የማይቆረጥ ምንዳ አልላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَعَمِلُوا۟ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُمْ أَجْرٌ غَيْرُ مَمْنُونٍ ﴿٨﴾

9. በላቸው «እናንተ በዚያ ምድርን በሁለት ቀኖች ውስጥ በፈጠረው አምላክ በእርግጥ ትክዳላችሁን? ለእርሱም ባለንጣዎችን ታደርጋላችሁን? ያ (ይህንን የሠራው) የዓለማት ጌታ ነው፡፡

۞ قُلْ أَئِنَّكُمْ لَتَكْفُرُونَ بِٱلَّذِى خَلَقَ ٱلْأَرْضَ فِى يَوْمَيْنِ وَتَجْعَلُونَ لَهُۥٓ أَندَادًا ۚ ذَٰلِكَ رَبُّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٩﴾

10. በእርሷም ከበላይዋ የረጉ ጋራዎችን አደረገ፡፡ በእርሷም በረከትን አደረገ፡፡ በውስጧም ምግቦችዋን (ካለፉት ሁለት ቀኖች ጋር) በአራት ቀናት ውስጥ ለጠያቂዎች ትክክል ሲኾኑ ወሰነ፡፡

وَجَعَلَ فِيهَا رَوَٰسِىَ مِن فَوْقِهَا وَبَٰرَكَ فِيهَا وَقَدَّرَ فِيهَآ أَقْوَٰتَهَا فِىٓ أَرْبَعَةِ أَيَّامٍ سَوَآءً لِّلسَّآئِلِينَ ﴿١٠﴾

11. ከዚያም ወደ ሰማይ እርሷ ጭስ ኾና ሳለች አሰበ፡፡ ለእርሷም ለምድርም «ወዳችሁም ኾነ ወይም ጠልታችሁ ኑ» አላቸው፡፡ «ታዛዦች ኾነን መጣን» አሉ፡፡

ثُمَّ ٱسْتَوَىٰٓ إِلَى ٱلسَّمَآءِ وَهِىَ دُخَانٌ فَقَالَ لَهَا وَلِلْأَرْضِ ٱئْتِيَا طَوْعًا أَوْ كَرْهًا قَالَتَآ أَتَيْنَا طَآئِعِينَ ﴿١١﴾

12. በሁለት ቀኖችም ውስጥ ሰባት ሰማያት አደረጋቸው፡፡ በሰማይቱም ሁሉ ነገሯን አዘጋጀ፡፡ ቅርቢቱንም ሰማይ በመብራቶች አጌጥን፡፡ (ከሰይጣናት) መጠበቅንም ጠበቅናት፡፡ ይህ የአሸናፊው የዐዋቂው (ጌታ) ውሳኔ ነው፡፡

فَقَضَىٰهُنَّ سَبْعَ سَمَٰوَاتٍ فِى يَوْمَيْنِ وَأَوْحَىٰ فِى كُلِّ سَمَآءٍ أَمْرَهَا ۚ وَزَيَّنَّا ٱلسَّمَآءَ ٱلدُّنْيَا بِمَصَٰبِيحَ وَحِفْظًا ۚ ذَٰلِكَ تَقْدِيرُ ٱلْعَزِيزِ ٱلْعَلِيمِ ﴿١٢﴾

13. (ከእምነት) እንቢ «ቢሉም እንደ ዓድና ሰሙድ መቅሰፍት ብጤ የኾነን መቅሰፍት አስጠነቅቃችኋለሁ» በላቸው፡፡

فَإِنْ أَعْرَضُوا۟ فَقُلْ أَنذَرْتُكُمْ صَٰعِقَةً مِّثْلَ صَٰعِقَةِ عَادٍ وَثَمُودَ ﴿١٣﴾

إِذۡ جَآءَتۡهُمُ ٱلرُّسُلُ مِنۢ بَيۡنِ أَيۡدِيهِمۡ وَمِنۡ خَلۡفِهِمۡ أَلَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّا ٱللَّهَۖ قَالُواْ لَوۡ شَآءَ رَبُّنَا لَأَنزَلَ مَلَٰٓئِكَةٗ فَإِنَّا بِمَآ أُرۡسِلۡتُم بِهِۦ كَٰفِرُونَ ١٤

14. መልክተኞቹ አላህን እንጅ ሌላን አትግገዙ በማለት ከስተፊታቸውም ከስተኋለቸውም በመጡባቸው ጊዜ «ጌታችን በሻ ኖሮ መላእክትን ባወረደ ነበር:: ስለዚህ እኛ በዚያ በእርሱ በተላካችሁበት ከሓዲዎች ነን» አሉ::

فَأَمَّا عَادٞ فَٱسۡتَكۡبَرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّ وَقَالُواْ مَنۡ أَشَدُّ مِنَّا قُوَّةًۖ أَوَلَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّ ٱللَّهَ ٱلَّذِي خَلَقَهُمۡ هُوَ أَشَدُّ مِنۡهُمۡ قُوَّةٗۖ وَكَانُواْ بِـَٔايَٰتِنَا يَجۡحَدُونَ ١٥

15. ዓድም በምድር ላይ ያለ አግባብ ኮሩ:: «ከእኛ ይበልጥ በኀይል ብርቱ ማን ነው?» አሉም:: ያ የፈጠራቸው አላህ እርሱ በኀይል ከእነርሱ ይበልጥ የበረታ መኾኑን አያዩምን? በተዓምራታችንም ይክዱ ነበሩ::

فَأَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ رِيحٗا صَرۡصَرٗا فِيٓ أَيَّامٖ نَّحِسَاتٖ لِّنُذِيقَهُمۡ عَذَابَ ٱلۡخِزۡيِ فِي ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَعَذَابُ ٱلۡأٓخِرَةِ أَخۡزَىٰۖ وَهُمۡ لَا يُنصَرُونَ ١٦

16. በቅርቢቱ ሕይወት የውርደትን ቅጣት ልናቀምሳቸውም በእነርሱ ላይ የሚንሻሻን ብርቱ ነፋስ መናጢዎች በኾኑ ቀናት ውስጥ ላክንባቸው:: የመጨረሻይቱም (ዓለም) ስቃይ በጣም አዋራጅ ነው:: እነርሱም አይረዱም::

وَأَمَّا ثَمُودُ فَهَدَيۡنَٰهُمۡ فَٱسۡتَحَبُّواْ ٱلۡعَمَىٰ عَلَى ٱلۡهُدَىٰ فَأَخَذَتۡهُمۡ صَٰعِقَةُ ٱلۡعَذَابِ ٱلۡهُونِ بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ١٧

17. ሰሙዶችማ መራናቸው ዕውርነትንም በቅንነት ላይ መረጡ:: ይሠሩትም በነበሩት ኃጢኣት አሳናሽ የኾነችው የመብረቅ ቅጣት ያዘቻቸው::

وَنَجَّيۡنَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَكَانُواْ يَتَّقُونَ ١٨

18. እነዚያንም ያመኑትንና ይጠነቀቁ የነበሩትን አዳንናቸው::

وَيَوۡمَ يُحۡشَرُ أَعۡدَآءُ ٱللَّهِ إِلَى ٱلنَّارِ فَهُمۡ يُوزَعُونَ ١٩

19. የአላህም ጠላቶች ወደ እሳት የሚሰበሰቡበትን ቀን (አስታውስ):: እነርሱም የሚከመከሙ ኾነው ይነዳሉ::

حَتَّىٰٓ إِذَا مَا جَآءُوهَا شَهِدَ عَلَيۡهِمۡ سَمۡعُهُمۡ وَأَبۡصَٰرُهُمۡ وَجُلُودُهُم بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٢٠

20. በመጧትም ጊዜ ጆሮዎቻቸው፣ ዓይኖቻቸውና ቆዳዎቻቸውም ይሠሩት በነበሩት ነገር በእነርሱ ላይ ይመሰክሩባቸዋል::

وَقَالُواْ لِجُلُودِهِمۡ لِمَ شَهِدتُّمۡ عَلَيۡنَاۖ قَالُوٓاْ أَنطَقَنَا ٱللَّهُ ٱلَّذِيٓ أَنطَقَ كُلَّ شَيۡءٖۚ وَهُوَ خَلَقَكُمۡ أَوَّلَ مَرَّةٖ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ٢١

21. ለቆዳዎቻቸውም «በእኛ ላይ ለምን መሰከራችሁብን?» ይላሉ:: «ያ አንዳቹን ነገር ሁሉ ያናገረው አላህ አናገረን:: እርሱም በመጀመሪያ ጊዜ ፈጠራችሁ:: ወደእርሱም ትመለሳላችሁ» ይሏቸዋል::

وَمَا كُنتُمۡ تَسۡتَتِرُونَ أَن يَشۡهَدَ عَلَيۡكُمۡ سَمۡعُكُمۡ وَلَآ أَبۡصَٰرُكُمۡ وَلَا جُلُودُكُمۡ وَلَٰكِن ظَنَنتُمۡ أَنَّ ٱللَّهَ لَا يَعۡلَمُ كَثِيرٗا مِّمَّا تَعۡمَلُونَ ٢٢

22. ጆሮዎቻችሁ ዓይኖቻችሁና ቆዳዎቻችሁም በእናንተ ላይ ከመመስከራቸው የምትደበቁ አልነበራችሁም:: ግን አላህ ከምትሠሩት ብዙውን አያውቅም ብላችሁ ጠረጠራችሁ::

وَذَٰلِكُمۡ ظَنُّكُمُ ٱلَّذِي ظَنَنتُم بِرَبِّكُمۡ أَرۡدَىٰكُمۡ فَأَصۡبَحۡتُم مِّنَ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٢٣

23. ይህም ያ በጌታችሁ የጠረጠራችሁት ጥርጣሪያችሁ አጠፋችሁ:: ከከሳሪዎቹም ኾናችሁ (ይባላሉ)::

24. ቢታገሱም እሳት ለእነርሱ መኖሪያቸው ናት፡፡ ወደሚወዱት መመለስንም ቢጠይቁ እነርሱ ተቀባይ የሚያገኙ አይደሉም፡፡

فَإِن يَصْبِرُوا۟ فَٱلنَّارُ مَثْوًى لَّهُمْ ۖ وَإِن يَسْتَعْتِبُوا۟ فَمَا هُم مِّنَ ٱلْمُعْتَبِينَ ﴿٢٤﴾

25. ለእነርሱም ቁራኛዎችን አዘጋጀንላቸው፡፡ በፊታቸው ያለውንና በኋላቸው ያለውንም ሁሉ ለእነርሱ ሸለሙላቸው፡፡ ከጋኔንና ከሰውም ከእነርሱ በፊት በእርግጥ ካለፉት ሕዝቦች ጋር ኾነው ቃሉ በእነርሱ ላይ ተረጋገጠባቸው፡፡ እነርሱ በእርግጥ ከሳሪዎች ነበሩና፡፡

۞ وَقَيَّضْنَا لَهُمْ قُرَنَآءَ فَزَيَّنُوا۟ لَهُم مَّا بَيْنَ أَيْدِيهِمْ وَمَا خَلْفَهُمْ وَحَقَّ عَلَيْهِمُ ٱلْقَوْلُ فِىٓ أُمَمٍ قَدْ خَلَتْ مِن قَبْلِهِم مِّنَ ٱلْجِنِّ وَٱلْإِنسِ ۖ إِنَّهُمْ كَانُوا۟ خَٰسِرِينَ ﴿٢٥﴾

26. እነዚያም የካዱት «ይህንን ቁርአን አታዳምጡ፡፡ ታሸንፉም ዘንድ (ሲነበብ) በእርሱ ውስጥ ተንጫጩ» አሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ لَا تَسْمَعُوا۟ لِهَٰذَا ٱلْقُرْءَانِ وَٱلْغَوْا۟ فِيهِ لَعَلَّكُمْ تَغْلِبُونَ ﴿٢٦﴾

27. እነዚያንም የካዱትን ብርቱን ቅጣት እናቀምሳቸዋለን፡፡ የእዚያንም ይሠሩት የነበሩትን መጥፎውን (ፍዳ) በእርግጥ እንመነዳቸዋለን፡፡

فَلَنُذِيقَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ عَذَابًا شَدِيدًا وَلَنَجْزِيَنَّهُمْ أَسْوَأَ ٱلَّذِى كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ﴿٢٧﴾

28. ይህ የአላህ ጠላቶች ፍዳ ነው፡፡ እሳት በውስጧ ለእነርሱ የዘላለም መኖሪያ አገር አልላቸው፡፡ ከአንቀጾቻችን ይክዱ በነበሩት ምንዳን (ይምመነዳሉ)፡፡

ذَٰلِكَ جَزَآءُ أَعْدَآءِ ٱللَّهِ ٱلنَّارُ ۖ لَهُمْ فِيهَا دَارُ ٱلْخُلْدِ ۖ جَزَآءًۢ بِمَا كَانُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَا يَجْحَدُونَ ﴿٢٨﴾

29. እነዚያም የካዱት (በእሳት ውስጥ ኾነው) «ጌታችን ሆይ! እነዚያን ከጋኔንና ከሰው ያሳሳቱንን አሳየን፡፡ ከታችኞቹ ይኾኑ ዘንድ ከጫማዎቻችን ሥር እናደርጋቸዋለንና» ይላሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ رَبَّنَآ أَرِنَا ٱلَّذَيْنِ أَضَلَّانَا مِنَ ٱلْجِنِّ وَٱلْإِنسِ نَجْعَلْهُمَا تَحْتَ أَقْدَامِنَا لِيَكُونَا مِنَ ٱلْأَسْفَلِينَ ﴿٢٩﴾

30. እነዚያ «ጌታችን አላህ ነው» ያሉ ከዚያም ቀጥ ያሉ «አትፍሩ፤ አትዘኑም፤ በዚያችም ተስፋ ቃል ትደረግላችሁ በነበራችሁት ገነት ተበሰሩ» በማለት በነሱ ላይ መላእክት ይወርዳሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ قَالُوا۟ رَبُّنَا ٱللَّهُ ثُمَّ ٱسْتَقَٰمُوا۟ تَتَنَزَّلُ عَلَيْهِمُ ٱلْمَلَٰٓئِكَةُ أَلَّا تَخَافُوا۟ وَلَا تَحْزَنُوا۟ وَأَبْشِرُوا۟ بِٱلْجَنَّةِ ٱلَّتِى كُنتُمْ تُوعَدُونَ ﴿٣٠﴾

31. «እኛ በቅርቢቱም ሕይወት በመጨረሻይቱም ረዳቶቻችሁ ነን! ለእናንተም በእርሷ ውስጥ ነፍሶቻችሁ የሚሹት ሁሉ አልላችሁ፡፡ ለእናንተም በእርሷ ውስጥ የምትፈልጉት ሁሉ አልላችሁ፡፡

نَحْنُ أَوْلِيَآؤُكُمْ فِى ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَا وَفِى ٱلْءَاخِرَةِ ۖ وَلَكُمْ فِيهَا مَا تَشْتَهِىٓ أَنفُسُكُمْ وَلَكُمْ فِيهَا مَا تَدَّعُونَ ﴿٣١﴾

32. «መሓሪ አዛኝ ከኾነው አላህ መስተንግዶ ሲኾን» (ይባላሉ)፡፡

نُزُلًا مِّنْ غَفُورٍ رَّحِيمٍ ﴿٣٢﴾

33. ወደ አላህ ከጠራና መልካምንም ከሠራ፣ «እኔ ከሙስሊሞች ነኝ» ካለም ሰው ይበልጥ ቃሉ ያማረ ማን ነው?

وَمَنْ أَحْسَنُ قَوْلًا مِّمَّن دَعَآ إِلَى ٱللَّهِ وَعَمِلَ صَٰلِحًا وَقَالَ إِنَّنِى مِنَ ٱلْمُسْلِمِينَ ﴿٣٣﴾

34. መልካሚቱና ክፉይቱም (ጸባይ) አይተካከሉም፡፡ በዚያች እርሷ መልካም በኾነችው ጸባይ (መጥፎይቱን) ገፍትር፡፡ ያን ጊዜ ያ ባንተና በእርሱ መካከል ጠብ ያለው ሰው እርሱ ልክ እንደ አዛኝ ዘመድ ይኾናል፡፡

وَلَا تَسْتَوِى ٱلْحَسَنَةُ وَلَا ٱلسَّيِّئَةُ ۚ ٱدْفَعْ بِٱلَّتِى هِىَ أَحْسَنُ فَإِذَا ٱلَّذِى بَيْنَكَ وَبَيْنَهُۥ عَدَٰوَةٌ كَأَنَّهُۥ وَلِىٌّ حَمِيمٌ ٣٤

35. (ይህችንም ጠባይ) እነዚያ የታገሱት እንጅ ሌላው አያገኛትም፡፡ የትልቅም ዕድል ባለቤት እንጅ ማንም አይገጠማትም፡፡

وَمَا يُلَقَّىٰهَآ إِلَّا ٱلَّذِينَ صَبَرُوا۟ وَمَا يُلَقَّىٰهَآ إِلَّا ذُو حَظٍّ عَظِيمٍ ٣٥

36. ከሰይጣንም ጉትጎታ ቢያገኝህ (ከመልካም ጠባይም ቢመልስህ) በአላህ ተጠበቅ፡፡ እነሆ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና፡፡

وَإِمَّا يَنزَغَنَّكَ مِنَ ٱلشَّيْطَٰنِ نَزْغٌ فَٱسْتَعِذْ بِٱللَّهِ ۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلْعَلِيمُ ٣٦

37. ሌሊትና ቀንም ፀሐይና ጨረቃም ከምልክቶቹ ናቸው፡፡ ለፀሐይና ለጨረቃ አትስገዱ፡፡ ለእዚያም ለፈጠራቸው አላህ ስገዱ፡፡ እርሱን ብቻ የምትግገዙ እንደ ኾናችሁ (ለሌላ አትስገዱ)፡፡

وَمِنْ ءَايَٰتِهِ ٱلَّيْلُ وَٱلنَّهَارُ وَٱلشَّمْسُ وَٱلْقَمَرُ ۚ لَا تَسْجُدُوا۟ لِلشَّمْسِ وَلَا لِلْقَمَرِ وَٱسْجُدُوا۟ لِلَّهِ ٱلَّذِى خَلَقَهُنَّ إِن كُنتُمْ إِيَّاهُ تَعْبُدُونَ ٣٧

38. ቢኮሩም እነዚያ በጌታህ ዘንድ ያሉት (መላእክት) በቀንም በሌሊትም ለእርሱ ያወድሳሉ፡፡ እነርሱም አይሰለቹም፡፡

فَإِنِ ٱسْتَكْبَرُوا۟ فَٱلَّذِينَ عِندَ رَبِّكَ يُسَبِّحُونَ لَهُۥ بِٱلَّيْلِ وَٱلنَّهَارِ وَهُمْ لَا يَسْـَٔمُونَ ۩ ٣٨

39. አንተ ምድርን ደረቅ ኾና ማየትህም ከምልክቶቹ ነው፡፡ በእርሷም ላይ ውሃን ባወረድን ጊዜ (በቡቃያዎችዋ) ትላወሳለች፡፡ ትነፋለችም፡፡ ያ ሕያው ያደረጋት ጌታ በእርግጥ ሙታንን ሕያው አድራጊ ነው፡፡ እነርሱ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

وَمِنْ ءَايَٰتِهِۦٓ أَنَّكَ تَرَى ٱلْأَرْضَ خَٰشِعَةً فَإِذَآ أَنزَلْنَا عَلَيْهَا ٱلْمَآءَ ٱهْتَزَّتْ وَرَبَتْ ۚ إِنَّ ٱلَّذِىٓ أَحْيَاهَا لَمُحْىِ ٱلْمَوْتَىٰٓ ۚ إِنَّهُۥ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ٣٩

40. እነዚያ አንቀጾቻችንን የሚያጣምሙ በእኛ ላይ አይደበቁም፡፡ (የሚያጣምምና) በእሳት ውስጥ የሚጣለው ሰው ይበልጣልን? ወይስ በትንሣኤ ቀን ጸጥተኛ ኾኖ የሚመጣው ሰው? የሻችሁትን ሥሩ (ዋጋችሁን ታገኛላችሁ)፡፡ እርሱ የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነውና፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُلْحِدُونَ فِىٓ ءَايَٰتِنَا لَا يَخْفَوْنَ عَلَيْنَآ ۗ أَفَمَن يُلْقَىٰ فِى ٱلنَّارِ خَيْرٌ أَم مَّن يَأْتِىٓ ءَامِنًا يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ ۚ ٱعْمَلُوا۟ مَا شِئْتُمْ ۖ إِنَّهُۥ بِمَا تَعْمَلُونَ بَصِيرٌ ٤٠

41. እነዚያ በቁርኣን እርሱ አሸናፊ መጽሐፍ ሲኾን በመጣላቸው ጊዜ የካዱት (ጠፊዎች ናቸው)፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ بِٱلذِّكْرِ لَمَّا جَآءَهُمْ ۖ وَإِنَّهُۥ لَكِتَٰبٌ عَزِيزٌ ٤١

42. ከኋላውም ከፊቱም ውሸት አይመጣበትም፡፡ ጥበበኛ ምስጉን ከኾነው ጌታ የተወረደ ው፡፡

لَّا يَأْتِيهِ ٱلْبَٰطِلُ مِنۢ بَيْنِ يَدَيْهِ وَلَا مِنْ خَلْفِهِۦ ۖ تَنزِيلٌ مِّنْ حَكِيمٍ حَمِيدٍ ٤٢

43. ካንተ በፊት ለነበሩት መልክተኞች የተባለው ብጤ እንጅ ለአንተ ሌላ አይባልም፡፡ ጌታህ የምህረት ባለቤትና የአሳማሚ ቅጣት ባለቤት ነው፡፡

مَّا يُقَالُ لَكَ إِلَّا مَا قَدْ قِيلَ لِلرُّسُلِ مِن قَبْلِكَ ۚ إِنَّ رَبَّكَ لَذُو مَغْفِرَةٍ وَذُو عِقَابٍ أَلِيمٍ ٤٣

44. በአጀምኛ የኾነ ቁርአን ባደረግነው ኖሮ አንቀጾቹ «(በምናውቀው ቋንቋ) አይብራሩም ኖሯልን? (ቁርአኑ) አጀምኛና (መልክተኛው) ዐረባዊ ይኾናልን?» ባሉ ነበር እርሱ ለእነዚያ ለአመኑት መምሪያና መፈወሻ ነው:: እነዚያም የማያምኑት በጆሮዎቻቸው ውስጥ ድንቁርና ነው:: (አይሰሙትም):: እነርሱም በእነርሱ ላይ እውርነት ነው:: እነዚያ ከሩቅ ስፍራ እንደሚጥጠሩ ናቸው::

وَلَوۡ جَعَلۡنَٰهُ قُرۡءَانًا أَعۡجَمِيًّا لَّقَالُواْ لَوۡلَا فُصِّلَتۡ ءَايَٰتُهُۥٓۖ ءَا۬عۡجَمِيٌّ وَعَرَبِيٌّۗ قُلۡ هُوَ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْ هُدٗى وَشِفَآءٞۚ وَٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ فِيٓ ءَاذَانِهِمۡ وَقۡرٞ وَهُوَ عَلَيۡهِمۡ عَمًىۚ أُوْلَٰٓئِكَ يُنَادَوۡنَ مِن مَّكَانِۭ بَعِيدٖ ﴿٤٤﴾

45. ሙሳንም መጽሐፉን በእርግጥ ሰጠነው:: በእርሱም ተለያዩበት:: ከጌታህም ያለፈች ቃል ባልነበረች ኖሮ በመካከላቸው በተፈረደ ነበር:: እነርሱም ከእርሱ አወላዋይ በኾነ ጥርጣሬ ውስጥ ናቸው::

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا مُوسَى ٱلۡكِتَٰبَ فَٱخۡتُلِفَ فِيهِۗ وَلَوۡلَا كَلِمَةٞ سَبَقَتۡ مِن رَّبِّكَ لَقُضِيَ بَيۡنَهُمۡۚ وَإِنَّهُمۡ لَفِي شَكّٖ مِّنۡهُ مُرِيبٖ ﴿٤٥﴾

46. መልካም የሠራ ሰው ለነፍሱ ነው:: ያጠፋም ሰው በእርሷ ላይ ነው:: ጌታህም ለባሮቹ በዳይ አይደለም::

مَّنۡ عَمِلَ صَٰلِحٗا فَلِنَفۡسِهِۦۖ وَمَنۡ أَسَآءَ فَعَلَيۡهَاۗ وَمَا رَبُّكَ بِظَلَّٰمٖ لِّلۡعَبِيدِ ﴿٤٦﴾

47. ጊዜይቱን ማወቅ ወደእርሱ ይመለሳል ከፍሬዎችም ከሽፋኖቻቸው አይወጡም:: ከሴትም አንዲትም አታረግዝም፣ አትወልድምም በዕውቀቱ ቢኾን እንጅ:: «ተጋሪዎቼ የት ናቸው?» በማለት በሚጠራቸው ቀንም «ከእኛ ውስጥ (ባላንጣ አልለ ብሎ) ምንም መስካሪ አለመኖሩን አስታወቅንህ» ይላሉ::

۞إِلَيۡهِ يُرَدُّ عِلۡمُ ٱلسَّاعَةِۚ وَمَا تَخۡرُجُ مِن ثَمَرَٰتٖ مِّنۡ أَكۡمَامِهَا وَمَا تَحۡمِلُ مِنۡ أُنثَىٰ وَلَا تَضَعُ إِلَّا بِعِلۡمِهِۦۚ وَيَوۡمَ يُنَادِيهِمۡ أَيۡنَ شُرَكَآءِي قَالُوٓاْ ءَاذَنَّٰكَ مَا مِنَّا مِن شَهِيدٖ ﴿٤٧﴾

48. ያም በፊት ይግገዙት የነበሩት (ጣዖት) ከእነርሱ ይጠፋቸዋል:: ለእነርሱም ምንም መሸሻ የሌላቸው መኾኑን ያረጋግጣሉ::

وَضَلَّ عَنۡهُم مَّا كَانُواْ يَدۡعُونَ مِن قَبۡلُۖ وَظَنُّواْ مَا لَهُم مِّن مَّحِيصٖ ﴿٤٨﴾

49. ሰው በጎ ነገርን ከመለመን አይሰለችም:: ክፉም ቢያገኘው ወዲያውኑ በጣም ተስፋ ቆራጭ ተበሳጭ ይኾናል::

لَّا يَسۡـَٔمُ ٱلۡإِنسَٰنُ مِن دُعَآءِ ٱلۡخَيۡرِ وَإِن مَّسَّهُ ٱلشَّرُّ فَيَـُٔوسٞ قَنُوطٞ ﴿٤٩﴾

50. ካገኘችውም መከራ በኋላ ከእኛ የኾነን እዝነት ብናቀምሰው «ይህ ለእኔ (በሥራዬ የተገባኝ) ነው:: ሰዓቲቱም መጪ ናት ብዬ አላስብም:: ወደ ጌታየም ብመለስ ለእኔ እርሱ ዘንድ መልካሚቱ (ገነት) በእርግጥ አለችኝ» ይላል:: እነዚያንም የካዱትን ሥራዎቻቸውን በእርግጥ እንነግራቸዋለን:: ከብርቱውም ስቃይ በእርግጥ እናቀምሳቸዋለን::

وَلَئِنۡ أَذَقۡنَٰهُ رَحۡمَةٗ مِّنَّا مِنۢ بَعۡدِ ضَرَّآءَ مَسَّتۡهُ لَيَقُولَنَّ هَٰذَا لِي وَمَآ أَظُنُّ ٱلسَّاعَةَ قَآئِمَةٗ وَلَئِن رُّجِعۡتُ إِلَىٰ رَبِّيٓ إِنَّ لِي عِندَهُۥ لَلۡحُسۡنَىٰۚ فَلَنُنَبِّئَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِمَا عَمِلُواْ وَلَنُذِيقَنَّهُم مِّنۡ عَذَابٍ غَلِيظٖ ﴿٥٠﴾

51. በሰውም ላይ ጸጋችንን በለገስን ጊዜ (ከማመስገን) ይዞራል:: በጎኑም ይርቃል:: መከራም ባገኘው ጊዜ የብዙ ልመና ባለቤት ይኾናል::

وَإِذَآ أَنۡعَمۡنَا عَلَى ٱلۡإِنسَٰنِ أَعۡرَضَ وَنَـَٔا بِجَانِبِهِۦ وَإِذَا مَسَّهُ ٱلشَّرُّ فَذُو دُعَآءٍ عَرِيضٖ ﴿٥١﴾

52. በላቸው «ንገሩኝ (ቁርአኑ) ከአላህ ዘንድ ቢኾን ከዚያም በእርሱ ብትክዱ (ከውነት) በራቀ ጭቅጭቅ ላይ ከኾነ ሰው ይበልጥ የተሳሳተ ማን ነው?»

قُلۡ أَرَءَيۡتُمۡ إِن كَانَ مِنۡ عِندِ ٱللَّهِ ثُمَّ كَفَرۡتُم بِهِۦ مَنۡ أَضَلُّ مِمَّنۡ هُوَ فِي شِقَاقِۭ بَعِيدٖ ﴿٥٢﴾

53. እርሱም (ቁርኣን) እውነት መኾኑ ለእነርሱ እስከሚገለፅላቸው ድረስ በአጽናፎቹ ውስጥና በነፍሶቻቸውም ውስጥ ያሉትን ተዓምራቶቻችንን በእርግጥ እናሳያቸዋለን፡፡ ጌታህም እርሱ በነገሩ ሁሉ ላይ ዐዋቂ መኾኑ አይበቃቸውምን?

سَنُرِيهِمْ ءَايَٰتِنَا فِى ٱلْـَٔافَاقِ وَفِىٓ أَنفُسِهِمْ حَتَّىٰ يَتَبَيَّنَ لَهُمْ أَنَّهُ ٱلْحَقُّ ۗ أَوَلَمْ يَكْفِ بِرَبِّكَ أَنَّهُۥ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ شَهِيدٌ ﴿٥٣﴾

54. ንቁ! እነርሱ ከጌታቸው መገናኘት በመጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡ ንቁ! እርሱ በነገሩ ሁሉ (ዕውቀቱ) ከባቢ ነው፡፡

أَلَآ إِنَّهُمْ فِى مِرْيَةٍ مِّن لِّقَآءِ رَبِّهِمْ ۗ أَلَآ إِنَّهُۥ بِكُلِّ شَىْءٍ مُّحِيطٌۢ ﴿٥٤﴾

# ሱረቱ አል ሹራ

# سورة الشورى

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሐ፡ ሚም)፡፡

حمٓ ﴿١﴾

2. ዐ.ሰ.ቀ (ዓይን ሲን ቃፍ)፤

عٓسٓقٓ ﴿٢﴾

3. እንደዚሁ (በዚህች ሱራ ውስጥ እንዳለው) አሸናፊው ጥበበኛው አላህ ወዳንተ ያወርዳል፡፡ ወደእነዚያም ከአንተ በፊት ወደ ነበሩት ሕዝቦች (አውርዷል)፡፡

كَذَٰلِكَ يُوحِىٓ إِلَيْكَ وَإِلَى ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِكَ ٱللَّهُ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ﴿٣﴾

4. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የእርሱ ነው፡፡ እርሱም የበላዩ ታላቁ ነው፡፡

لَهُۥ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۖ وَهُوَ ٱلْعَلِىُّ ٱلْعَظِيمُ ﴿٤﴾

5. (ከአላህ ፍራቻ) ሰማያት ከበላያቸው ሊቀደዱ ይቀርባሉ፡፡ መላእክትም ጌታቸውን እያመሰገኑ ያወድሳሉ፡፡ በምድርም ላለው ፍጡር ምሕረትን ይለምናሉ፡፡ ንቁ! አላህ እርሱ መሓሪው አዛኙ ነው፡፡

تَكَادُ ٱلسَّمَٰوَٰتُ يَتَفَطَّرْنَ مِن فَوْقِهِنَّ ۚ وَٱلْمَلَٰٓئِكَةُ يُسَبِّحُونَ بِحَمْدِ رَبِّهِمْ وَيَسْتَغْفِرُونَ لِمَن فِى ٱلْأَرْضِ ۗ أَلَآ إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلْغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٥﴾

6. እነዚያም ከእርሱ ሌላ (የጣዖታት) ረዳቶችን የያዙ፤ አላህ በእነርሱ ላይ ተጠባባቂ ነው፡፡ አንተም በእነርሱ ላይ ኀላፊ አይደለህም፡፡

وَٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُوا۟ مِن دُونِهِۦٓ أَوْلِيَآءَ ٱللَّهُ حَفِيظٌ عَلَيْهِمْ وَمَآ أَنتَ عَلَيْهِم بِوَكِيلٍ ﴿٦﴾

7. እንደዚሁም የከተሞች እናት የኾነችውን (የመካን ሰዎች) በአካባቢዋ ያሉትንም ልታስፈራራ የመሰብሰቢያውንም ቀን በእርሱ ጥርጣሬ የሌለበት ሲኾን ልታስጠነቅቅ ዐረብኛ የኾነን ቁርኣን ወደ አንተ አወረድን:: (ከእነርሱም) ከፊሉ በገነት ውስጥ ከፊሉም በእሳት ውስጥ ነው::

وَكَذَٰلِكَ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ قُرۡءَانًا عَرَبِيّٗا لِّتُنذِرَ أُمَّ ٱلۡقُرَىٰ وَمَنۡ حَوۡلَهَا وَتُنذِرَ يَوۡمَ ٱلۡجَمۡعِ لَا رَيۡبَ فِيهِۚ فَرِيقٞ فِي ٱلۡجَنَّةِ وَفَرِيقٞ فِي ٱلسَّعِيرِ ٧

8. አላህም በሻ ኖሮ (ባንድ ሃይማኖት ላይ) አንድ ሕዝብ ባደረጋቸው ነበር:: ግን የሚሻውን ሰው በእዝነቱ ውስጥ ያስገባል:: በዳዮችም ለእነርሱ ወዳጅና ረዳት ምንም የላቸውም::

وَلَوۡ شَآءَ ٱللَّهُ لَجَعَلَهُمۡ أُمَّةٗ وَٰحِدَةٗ وَلَٰكِن يُدۡخِلُ مَن يَشَآءُ فِي رَحۡمَتِهِۦۚ وَٱلظَّٰلِمُونَ مَا لَهُم مِّن وَلِيّٖ وَلَا نَصِيرٍ ٨

9. ከእርሱ ሌላ ረዳቶችን ያዙን? (ረዳቶች አይደሉም):: አላህም ረዳት እርሱ ብቻ ነው:: እርሱም ሙታንን ሕያው ያደርጋል:: እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው::

أَمِ ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِهِۦٓ أَوۡلِيَآءَۖ فَٱللَّهُ هُوَ ٱلۡوَلِيُّ وَهُوَ يُحۡيِ ٱلۡمَوۡتَىٰ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٩

10. ከምንም ነገር ያ በእርሱ የተለያዩበት ፍርዱ ወደ አላህ ነው:: «እርሱ አላህ ጌታዬ ነው:: በእርሱ ላይ ተጠጋሁ፣ ወደርሱም እመለሳለሁ» (በላቸው)::

وَمَا ٱخۡتَلَفۡتُمۡ فِيهِ مِن شَيۡءٖ فَحُكۡمُهُۥٓ إِلَى ٱللَّهِۚ ذَٰلِكُمُ ٱللَّهُ رَبِّي عَلَيۡهِ تَوَكَّلۡتُ وَإِلَيۡهِ أُنِيبُ ١٠

11. ሰማያትንና ምድርን ፈጣሪ ነው:: ከነፍሶቻችሁ ሴቶችን ከቤት እንስሳዎችም ዓይነቶችን (ወንዶችና ሴቶችን) ለእናንተ አደረገላችሁ:: በእርሱ ያበዛችኋል:: የሚመስለው ምንም ነገር የለም:: እርሱም ሰሚው ተመልካቹ ነው::

فَاطِرُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ جَعَلَ لَكُم مِّنۡ أَنفُسِكُمۡ أَزۡوَٰجٗا وَمِنَ ٱلۡأَنۡعَٰمِ أَزۡوَٰجٗا يَذۡرَؤُكُمۡ فِيهِۚ لَيۡسَ كَمِثۡلِهِۦ شَيۡءٞۖ وَهُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡبَصِيرُ ١١

12. የሰማያትና የምድር (ድልቦች) መከፈቻዎች የእርሱ ናቸው:: ሲሳይን ለሚሻው ሰው ያሰፋል፤ ያጠባልም:: እርሱ ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነውና::

لَهُۥ مَقَالِيدُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ يَبۡسُطُ ٱلرِّزۡقَ لِمَن يَشَآءُ وَيَقۡدِرُۚ إِنَّهُۥ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ١٢

13. ለእናንተ ከሃይማኖት ያንን በእርሱ ኑሕን ያዘዘበትን ደነገገላችሁ:: ያንንም ወዳንተ ያወረድነውን ያንንም በእርሱ ኢብራሂምን ሙሳንና ዒሳንም ያዘዝንበትን ሃይማኖትን በትክክል አቋቁሙ በእርሱም አትለያዩ ማለትን (ደነገግን):: በአጋሪዎቹ ላይ ያ ወደርሱ የምትጠራቸው ነገር ከበዳቸው:: አላህ የሚሻውን ሰው ወደእርሱ (እምነት) ይመርጣል:: የሚመለስንም ሰው ወደርሱ ይመራል::

۞شَرَعَ لَكُم مِّنَ ٱلدِّينِ مَا وَصَّىٰ بِهِۦ نُوحٗا وَٱلَّذِيٓ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ وَمَا وَصَّيۡنَا بِهِۦٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَمُوسَىٰ وَعِيسَىٰٓۖ أَنۡ أَقِيمُواْ ٱلدِّينَ وَلَا تَتَفَرَّقُواْ فِيهِۚ كَبُرَ عَلَى ٱلۡمُشۡرِكِينَ مَا تَدۡعُوهُمۡ إِلَيۡهِۚ ٱللَّهُ يَجۡتَبِيٓ إِلَيۡهِ مَن يَشَآءُ وَيَهۡدِيٓ إِلَيۡهِ مَن يُنِيبُ ١٣

14. (የሃይማኖት ሰዎች) ዕውቀቱም ከመጣላቸው በኋላ በመካከላቸው ለምቀኝነት እንጅ ለሌላ አልተለያዩም:: እስከ ተወሰነም ጊዜ (በማቆየት) ከጌታህ ያለፈች ቃል ባልነበረች ኖሮ በእነርሱ መካከል (አሁን) በተፈረደ ነበር:: እነዚያም ከኋላቸው መጽሐፉን እንዲወርሱ የተደረጉት ከእርሱ በእርግጥ በአወላዋይ ጥርጣሬ ውስጥ ናቸው::

وَمَا تَفَرَّقُوٓاْ إِلَّا مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَهُمُ ٱلۡعِلۡمُ بَغۡيَۢا بَيۡنَهُمۡۚ وَلَوۡلَا كَلِمَةٞ سَبَقَتۡ مِن رَّبِّكَ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمّٗى لَّقُضِيَ بَيۡنَهُمۡۚ وَإِنَّ ٱلَّذِينَ أُورِثُواْ ٱلۡكِتَٰبَ مِنۢ بَعۡدِهِمۡ لَفِي شَكّٖ مِّنۡهُ مُرِيبٖ ١٤

15. ለዚህም (ድንጋጌ ሰዎችን) ጥራ፡፡ እንደታዘዝከውም ቀጥ በል፡፡ ዝንባሌዎቻቸውንም አትከተል፡፡ «በላቸውም ከመጽሐፍ አላህ ባወረደው ሁሉ አመንኩ፡፡ በመካከላችሁም ላስተካክል ታዘዝኩ፡፡ አላህ ጌታችን ጌታችሁም ነው፡፡ ለእኛ ሥራዎቻችን አልሉን፡፡ ለእናንተም ሥራዎቻችሁ አልሏችሁ፡፡ በእኛና በእናንተ መካከል ክርክር የለም፡፡ አላህ በመካከላችን ይሰበስባል፡፡ መመለሻም ወደእርሱ ብቻ ነው፡፡»

فَلِذَٰلِكَ فَٱدۡعُۖ وَٱسۡتَقِمۡ كَمَآ أُمِرۡتَۖ وَلَا تَتَّبِعۡ أَهۡوَآءَهُمۡۖ وَقُلۡ ءَامَنتُ بِمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ مِن كِتَٰبٖۖ وَأُمِرۡتُ لِأَعۡدِلَ بَيۡنَكُمُۖ ٱللَّهُ رَبُّنَا وَرَبُّكُمۡۖ لَنَآ أَعۡمَٰلُنَا وَلَكُمۡ أَعۡمَٰلُكُمۡۖ لَا حُجَّةَ بَيۡنَنَا وَبَيۡنَكُمُۖ ٱللَّهُ يَجۡمَعُ بَيۡنَنَاۖ وَإِلَيۡهِ ٱلۡمَصِيرُ ١٥

16. እነዚያም በአላህ (ሃይማኖት) ለእርሱ ተቀባይ ካገኘ በኋላ የሚከራከሩት ማስረጃቸው በጌታቸው ዘንድ ብልሹ ናት፡፡ በእነርሱም ላይ ቁጣ አልለባቸው፡፡ ለእነርሱም ብርቱ ቅጣት አልላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ يُحَآجُّونَ فِي ٱللَّهِ مِنۢ بَعۡدِ مَا ٱسۡتُجِيبَ لَهُۥ حُجَّتُهُمۡ دَاحِضَةٌ عِندَ رَبِّهِمۡ وَعَلَيۡهِمۡ غَضَبٞ وَلَهُمۡ عَذَابٞ شَدِيدٌ ١٦

17. አላህ ያ መጽሐፉን በእውነት ያወረደ ነው፡፡ ሚዛንንም (እንደዚሁ)፡፡ ሰዓቲቱ ምንአልባት ቅርብ መኾንዋን ምን ያሳውቅሃል?

ٱللَّهُ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ ٱلۡكِتَٰبَ بِٱلۡحَقِّ وَٱلۡمِيزَانَۗ وَمَا يُدۡرِيكَ لَعَلَّ ٱلسَّاعَةَ قَرِيبٞ ١٧

18. እነዚያ በእርሷ የማያምኑት በእርሷ ያቻኩላሉ፡፡ እነዚያም ያመኑት ከእርሷ ፈሪዎች ናቸው፡፡ እርሷም እውነት መኾንዋን ያውቃሉ፡፡ ንቁ! እነዚያ በሰዓቲቱ የሚከራከሩት በእርግጥ (ከእውነት) በራቀ ስሕተት ውስጥ ናቸው፡፡

يَسۡتَعۡجِلُ بِهَا ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِهَاۖ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مُشۡفِقُونَ مِنۡهَا وَيَعۡلَمُونَ أَنَّهَا ٱلۡحَقُّۗ أَلَآ إِنَّ ٱلَّذِينَ يُمَارُونَ فِي ٱلسَّاعَةِ لَفِي ضَلَٰلِۭ بَعِيدٍ ١٨

19. አላህ በባሮቹ ሩህሩህ ነው፡፡ ለሚሻው ሰው (በሰፊው) ሲሳይን ይሰጣል፡፡ እርሱም ብርቱው አሸናፊው ነው፡፡

ٱللَّهُ لَطِيفُۢ بِعِبَادِهِۦ يَرۡزُقُ مَن يَشَآءُۖ وَهُوَ ٱلۡقَوِيُّ ٱلۡعَزِيزُ ١٩

20. (በሥራው) የኋለኛይቱን ዓለም አዝመራ የሚፈልግ የኾነ ሰው ለእርሱ በአዝመራው ላይ እንጨምርለታለን፡ ፡ የቅርቢቱንም ዓለም አዝመራ የሚፈልግ የኾነ ሰው ከእርሷ (የተወሰነለትን ብቻ) እንሰጠዋለን፡፡ ለእርሱም በኋለኛይቱ ዓለም ምንም ፋንታ የለውም፡፡

مَن كَانَ يُرِيدُ حَرۡثَ ٱلۡأٓخِرَةِ نَزِدۡ لَهُۥ فِي حَرۡثِهِۦۖ وَمَن كَانَ يُرِيدُ حَرۡثَ ٱلدُّنۡيَا نُؤۡتِهِۦ مِنۡهَا وَمَا لَهُۥ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ مِن نَّصِيبٍ ٢٠

21. ከሃይማኖት አላህ በእርሱ ያልፈቀደውን ለእነርሱ የደነገጉ ተጋሪዎች ለእነርሱ አልሏቸውን? የፍርዱ ቃል ባልነበረ ኖሮ በመካከላቸው (አሁን) በተፈረደ ነበር፡፡ በደለኞችም ለእነርሱ አሳማሚ ቅጣት በእርግጥ አልላቸው፡፡

أَمۡ لَهُمۡ شُرَكَٰٓؤُاْ شَرَعُواْ لَهُم مِّنَ ٱلدِّينِ مَا لَمۡ يَأۡذَنۢ بِهِ ٱللَّهُۚ وَلَوۡلَا كَلِمَةُ ٱلۡفَصۡلِ لَقُضِيَ بَيۡنَهُمۡۗ وَإِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٢١

22. በደለኞችን ከሠሩት ሥራ (ዋጋ በትንሣኤ ቀን) ፈሪዎች ኾነው ታያቸዋለህ፡፡ እርሱም በእነርሱ ላይ ወዳቂ ነው፡፡ እነዚያም ያመኑት መልካሞችንም የሠሩት በገነቶች ጨፌዎች ውስጥ ናቸው፡፡ ለእነርሱ በጌታቸው ዘንድ የሚሹት ሁሉ አልላቸው፡፡ ይህ እርሱ ታላቅ ችሮታ ነው፡፡

تَرَى ٱلظَّٰلِمِينَ مُشۡفِقِينَ مِمَّا كَسَبُواْ وَهُوَ وَاقِعُۢ بِهِمۡۗ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فِي رَوۡضَاتِ ٱلۡجَنَّاتِۖ لَهُم مَّا يَشَآءُونَ عِندَ رَبِّهِمۡۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلۡفَضۡلُ ٱلۡكَبِيرُ ٢٢

23. ይህ (ታላቅ ችሮታ) ያ አላህ እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን ባሮቹን የሚያበስርበት ነው፡፡ «በእርሱ (መልክቴን በማድረሴ) ላይ በዝምድና ውዴታን እንጅ ዋጋን አልጠይቃችሁም» በላቸው፡፡ መልካሚቱንም ሥራ የሚሠራ ሰው ለእርሱ በእርሷ መልካምን ነገር እንጨምርለታለን፡፡ አላህ መሓሪ አመስጋኝ ነውና፡፡

ذَٰلِكَ ٱلَّذِي يُبَشِّرُ ٱللَّهُ عِبَادَهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِۗ قُل لَّآ أَسۡـَٔلُكُمۡ عَلَيۡهِ أَجۡرًا إِلَّا ٱلۡمَوَدَّةَ فِي ٱلۡقُرۡبَىٰۗ وَمَن يَقۡتَرِفۡ حَسَنَةٗ نَّزِدۡ لَهُۥ فِيهَا حُسۡنًاۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ شَكُورٌ ٢٣

24. ይልቁንም «በአላህ ላይ ውሸትን ቀጠፈ» ይላሉን? አላህም ቢሻ በልብህ ላይ ያትማል፡፡ አላህም ውሸቱን ያብብሳል፡፡ እውነቱንም በቃላቱ ያረጋግጣል፡፡ እርሱ በልቦች ውስጥ ያለን ሁሉ ዐዋቂ ነውና፡፡

أَمۡ يَقُولُونَ ٱفۡتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبٗاۖ فَإِن يَشَإِ ٱللَّهُ يَخۡتِمۡ عَلَىٰ قَلۡبِكَۗ وَيَمۡحُ ٱللَّهُ ٱلۡبَٰطِلَ وَيُحِقُّ ٱلۡحَقَّ بِكَلِمَٰتِهِۦٓۚ إِنَّهُۥ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٢٤

25. እርሱም ያ ከባሮቹ ንስሓን የሚቀበል፣ ከኃጢአቶችም ይቅር የሚል፣ የምትሠሩትንም ሁሉ የሚያውቅ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي يَقۡبَلُ ٱلتَّوۡبَةَ عَنۡ عِبَادِهِۦ وَيَعۡفُواْ عَنِ ٱلسَّيِّـَٔاتِ وَيَعۡلَمُ مَا تَفۡعَلُونَ ٢٥

26. እነዚያንም ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን ልመናቸውን ይቀበላል፡፡ ከችሮታውም ይጨምርላቸዋል፡፡ ከሓዲዎቹም ለእነርሱ ብርቱ ቅጣት አልላቸው፡፡

وَيَسۡتَجِيبُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَيَزِيدُهُم مِّن فَضۡلِهِۦۚ وَٱلۡكَٰفِرُونَ لَهُمۡ عَذَابٞ شَدِيدٞ ٢٦

27. አላህም ለባሮቹ (ሁሉ) ሲሳይን በዘረጋ ኖሮ በምድር ውስጥ (ሁሉም) ወሰን ባለፉ ነበር፡፡ ግን የሚሻውን በልክ ያወርዳል፡፡ እርሱ በባሮቹ ውስጥ ዐዋቂ ተመልካች ነውና፡፡

۞وَلَوۡ بَسَطَ ٱللَّهُ ٱلرِّزۡقَ لِعِبَادِهِۦ لَبَغَوۡاْ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَٰكِن يُنَزِّلُ بِقَدَرٖ مَّا يَشَآءُۚ إِنَّهُۥ بِعِبَادِهِۦ خَبِيرُۢ بَصِيرٞ ٢٧

28. እርሱም ያ ተስፋ ከቆረጡ በኋላ ዝናምን የሚያወርድ ችሮታውንም የሚዘረጋ ነው፡፡ እርሱም ረዳቱ ምስጉኑ ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي يُنَزِّلُ ٱلۡغَيۡثَ مِنۢ بَعۡدِ مَا قَنَطُواْ وَيَنشُرُ رَحۡمَتَهُۥۚ وَهُوَ ٱلۡوَلِيُّ ٱلۡحَمِيدُ ٢٨

29. ሰማያትንና ምድርንም መፍጠሩ፣ ከተንቀሳቃሽም በሁለቱ ውስጥ የበተነውን (መፍጠሩ) ከአስደናቂ ምልክቶቹ ነው፡፡ እርሱም በሚሻ ጊዜ እነርሱን በመሰብሰብ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِۦ خَلۡقُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَثَّ فِيهِمَا مِن دَآبَّةٖۚ وَهُوَ عَلَىٰ جَمۡعِهِمۡ إِذَا يَشَآءُ قَدِيرٞ ٢٩

30. ከመከራም ማንኛውም ያገኛችሁ ነገር እጆቻችሁ በሠሩት (ኃጢአት) ምክንያት ነው፡፡ ከብዙውም ይቅር ይላል፡፡

وَمَآ أَصَٰبَكُم مِّن مُّصِيبَةٖ فَبِمَا كَسَبَتۡ أَيۡدِيكُمۡ وَيَعۡفُواْ عَن كَثِيرٖ ٣٠

31. እናንተም በምድር ውስጥ የምታቅቱ አይደላችሁም፡፡ ለእናንተም ከአላህ ሌላ ከዘመድም ከረዳትም ምንም የላችሁም፡፡

وَمَآ أَنتُم بِمُعۡجِزِينَ فِي ٱلۡأَرۡضِۖ وَمَا لَكُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ مِن وَلِيّٖ وَلَا نَصِيرٖ ٣١

32. በባሕር ላይ እንደ ጋራዎች ኾነው ተንሻላዮቹም (መርከቦች) ከአስደናቂ ምልክቶቹ ናቸው፡፡

وَمِنۡ ءَايَٰتِهِ ٱلۡجَوَارِ فِي ٱلۡبَحۡرِ كَٱلۡأَعۡلَٰمِ ٣٢

33. ቢሻ ነፋሱን የረጋ ያደርገዋል፡፡ በባሕሩም ጀርባ ላይ ረጊዎች ይኾናሉ፡፡ በዚህ ውስጥ በጣም ታጋሽና አመስጋኝ ለኾነ ሁሉ በእርግጥ ምልክቶች አሉ፡፡

إِن يَشَأۡ يُسۡكِنِ ٱلرِّيحَ فَيَظۡلَلۡنَ رَوَاكِدَ عَلَىٰ ظَهۡرِهِۦٓۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّكُلِّ صَبَّارٖ شَكُورٍ ٣٣

34. ወይም በሠሩት ኃጢአት ምክንያት (በማስጠም) ያጠፉቸዋል፡፡ ከብዙም ይቅርታ ያደርጋል፡፡

أَوۡ يُوبِقۡهُنَّ بِمَا كَسَبُواْ وَيَعۡفُ عَن كَثِيرٖ ٣٤

35. (ከእነርሱ ለመበቀል)፤ እነዚያንም በአንቀጾቻችን የሚከራከሩትን ለማወቅ (ያጠፉቸዋል)፡፡ ለእነርሱ ምንም መሸሻ የላቸውም፡፡

وَيَعۡلَمَ ٱلَّذِينَ يُجَٰدِلُونَ فِيٓ ءَايَٰتِنَا مَا لَهُم مِّن مَّحِيصٖ ٣٥

36. ከምንም ነገር የተሰጣችሁት የቅርቢቱ ሕይወት መጠቀሚያ ነው፡፡ አላህ ዘንድ ያለውም ምንዳ ለእነዚያ ለአመኑትና በጌታቸው ላይ ለሚጠጉት በላጭና ሁል ጊዜ ነዋሪ ነው፡፡

فَمَآ أُوتِيتُم مِّن شَيۡءٖ فَمَتَٰعُ ٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَاۖ وَمَا عِندَ ٱللَّهِ خَيۡرٞ وَأَبۡقَىٰ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَلَىٰ رَبِّهِمۡ يَتَوَكَّلُونَ ٣٦

37. ለእነዚያም የኀጢአትን ታላላቆችና ጠያፎችን የሚርቁ በተቆጡም ጊዜ እነሱ የሚምሩት ለኾኑት፡፡

وَٱلَّذِينَ يَجۡتَنِبُونَ كَبَٰٓئِرَ ٱلۡإِثۡمِ وَٱلۡفَوَٰحِشَ وَإِذَا مَا غَضِبُواْ هُمۡ يَغۡفِرُونَ ٣٧

38. ለእነዚያም የጌታቸውን ጥሪ ለተቀበሉት፣ ሶላትንም ላዘወተሩት፣ ነገራቸውም በመካከላቸው መመካከር ለኾነው ከሰጠናቸውም ሲሳይ ለሚለግሱት፡፡

وَٱلَّذِينَ ٱسۡتَجَابُواْ لِرَبِّهِمۡ وَأَقَامُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَأَمۡرُهُمۡ شُورَىٰ بَيۡنَهُمۡ وَمِمَّا رَزَقۡنَٰهُمۡ يُنفِقُونَ ٣٨

39. ለእነዚያም በደል በደረሰባቸው ጊዜ እነርሱ (በመሰሉ) የሚመልሱ ለኾኑት (በላጭና ኗሪ ነው)፡፡

وَٱلَّذِينَ إِذَآ أَصَابَهُمُ ٱلۡبَغۡيُ هُمۡ يَنتَصِرُونَ ٣٩

40. የመጥፎም ነገረ ዋጋ ብጤዋ መጥፎ ናት፡፡ ይቅርም ያለና ያሳመረ ሰው ምንዳው በአላህ ላይ ነው፡፡ እርሱ በደለኞችን አይወድም፡፡

وَجَزَٰٓؤُاْ سَيِّئَةٖ سَيِّئَةٞ مِّثۡلُهَاۖ فَمَنۡ عَفَا وَأَصۡلَحَ فَأَجۡرُهُۥ عَلَى ٱللَّهِۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلظَّٰلِمِينَ ٤٠

41. ከተበደሉም በኋላ (በመሰሉ) የተበቀሉ እነዚያ በነርሱ ላይ ምንም (የወቀሳ) መንገድ የለባቸውም፡፡

وَلَمَنِ ٱنتَصَرَ بَعۡدَ ظُلۡمِهِۦ فَأُوْلَٰٓئِكَ مَا عَلَيۡهِم مِّن سَبِيلٍ ٤١

42. (የወቀሳ) መንገዱ በእነዚያ ሰዎችን በሚበድሉት፣ በምድርም ውስጥ ያለ ሕግ ወሰን በሚያልፉት፣ ላይ ብቻ ነው፡፡ እነዚያ ለእነርሱ አሳማሚ ቅጣት አልላቸው፡፡

إِنَّمَا ٱلسَّبِيلُ عَلَى ٱلَّذِينَ يَظۡلِمُونَ ٱلنَّاسَ وَيَبۡغُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ٤٢

43. የታገሰና ምሕረት ያደረገም ሰው ይህ ከምርሮቹ (ከተፈላጊዎቹ) ነገሮች ነው፡፡

وَلَمَن صَبَرَ وَغَفَرَ إِنَّ ذَٰلِكَ لَمِنۡ عَزۡمِ ٱلۡأُمُورِ ٤٣

44. አላህ የሚያጠመውም ሰው ከእርሱ በኋላ ለእርሱ ምንም ረዳት የለውም፡፡ በደለኞችንም ቅጣቱን ባዩ ጊዜ ወደ መመለስ መንገድ አልለን? የሚሉ ሲኾኑ ታያቸዋለህ፡፡

وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِن وَلِيّٖ مِّنۢ بَعۡدِهِۦۗ وَتَرَى ٱلظَّٰلِمِينَ لَمَّا رَأَوُاْ ٱلۡعَذَابَ يَقُولُونَ هَلۡ إِلَىٰ مَرَدّٖ مِّن سَبِيلٖ ٤٤

45. ከውርደት የተነሳ ፈሪዎች ኾነው በዓይን ስርቆት ወደእርሷ (ወደ እሳት) እያስተዋሉ በእርሷ ላይ የሚቀረቡ ሲኾኑ ታያቸዋለህ፡፡ እነዚያም ያመኑት፡- «በእርግጥ ከሳሪዎቹ እነዚያ ነፍሶቻቸውንና ቤተሰቦቻቸውን በትንሣኤ ቀን ያከሰሩት ናቸው» ይላሉ፡፡

وَتَرَىٰهُمۡ يُعۡرَضُونَ عَلَيۡهَا خَٰشِعِينَ مِنَ ٱلذُّلِّ يَنظُرُونَ مِن طَرۡفٍ خَفِيّٖۗ وَقَالَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِنَّ ٱلۡخَٰسِرِينَ ٱلَّذِينَ خَسِرُوٓاْ أَنفُسَهُمۡ وَأَهۡلِيهِمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِۗ أَلَآ إِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ فِي عَذَابٖ مُّقِيمٖ ٤٥

46. ንቁ! በደለኞች በእርግጥ በዘውታሪ ስቃይ ውስጥ ናቸው፡፡ ለእነርሱም ከአላህ ሌላ የሚረዷቸው ዘመዶች ምንም አልነበሩዋቸውም፡፡ አላህም የሚያጠመው ሰው ለእርሱ (ወደ እውነት) ምንም መንገድ የለውም፡፡

وَمَا كَانَ لَهُم مِّنۡ أَوۡلِيَآءَ يَنصُرُونَهُم مِّن دُونِ ٱللَّهِۗ وَمَن يُضۡلِلِ ٱللَّهُ فَمَا لَهُۥ مِن سَبِيلٍ ٤٦

47. ለእርሱ መመለስ የሌለው ቀን ከአላህ ከመምጣቱ በፊት ለጌታችሁ ታዘዙ፡፡ በዚያ ቀን ለእናንተ ምንም መጠጊያ የላችሁም፡፡ ለእናንተም ምንም መካድ የላችሁም፡፡

ٱسۡتَجِيبُواْ لِرَبِّكُم مِّن قَبۡلِ أَن يَأۡتِيَ يَوۡمٞ لَّا مَرَدَّ لَهُۥ مِنَ ٱللَّهِۚ مَا لَكُم مِّن مَّلۡجَإٖ يَوۡمَئِذٖ وَمَا لَكُم مِّن نَّكِيرٖ ٤٧

48. ቢዞሩም (ወቀሳ የለብህም)፡፡ በእነርሱ ላይ ጠባቂ አድርገን አልላክንህምና፡፡ ባንተ ላይ ማድረስ እንጅ ሌላ የለብህም፡፡ እኛም ሰውን ከእኛ የኾነን ጸጋ ባቀመስነው ጊዜ በርሷ ይደሰታል፡፡ እጆቻቸው ባስቀደሙትም ኀጢአት ምክንያት መከራ ብትደርስባቸው (ተስፋ ይቆርጣሉ)፡፡ ሰው (ውለታን) በጣም ከሐዲ ነውና፡፡

فَإِنۡ أَعۡرَضُواْ فَمَآ أَرۡسَلۡنَٰكَ عَلَيۡهِمۡ حَفِيظًاۖ إِنۡ عَلَيۡكَ إِلَّا ٱلۡبَلَٰغُۗ وَإِنَّآ إِذَآ أَذَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ مِنَّا رَحۡمَةٗ فَرِحَ بِهَاۖ وَإِن تُصِبۡهُمۡ سَيِّئَةُۢ بِمَا قَدَّمَتۡ أَيۡدِيهِمۡ فَإِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ كَفُورٞ ٤٨

49. የሰማያትና የምድር ንግሥና የአላህ ነው፡፡ የሚሻውን ይፈጥራል፡፡ ለሚሻው ሰው ሴቶችን (ልጆች) ይሰጣል፡፡ ለሚሻውም ሰው ወንዶችን ይሰጣል፡፡

لِّلَّهِ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ يَخۡلُقُ مَا يَشَآءُۚ يَهَبُ لِمَن يَشَآءُ إِنَٰثٗا وَيَهَبُ لِمَن يَشَآءُ ٱلذُّكُورَ ٤٩

50. ወይም ወንዶችና ሴቶች አድርጎ ያጠናዳቸዋል፡፡ የሚሻውንም ሰው መካን ያደርገዋል፡፡ እርሱ ዐዋቂ ቻይ ነውና፡፡

أَوۡ يُزَوِّجُهُمۡ ذُكۡرَانٗا وَإِنَٰثٗاۖ وَيَجۡعَلُ مَن يَشَآءُ عَقِيمًاۚ إِنَّهُۥ عَلِيمٞ قَدِيرٞ ٥٠

51. ለሰውም አላህ በራእይ፣ ወይም ከግርዶ ወዲያ፣ ወይም መልክተኛን (መልአክን) የሚልክና በፈቃዱ የሚሻውን ነገር የሚያወርድለት ቢኾን እንጅ (በገሃድ) ሊያናግረው ተገቢው አይደለም:: እርሱ የበላይ ጥበበኛ ነውና::

۞وَمَا كَانَ لِبَشَرٍ أَن يُكَلِّمَهُ ٱللَّهُ إِلَّا وَحۡيًا أَوۡ مِن وَرَآيِٕ حِجَابٍ أَوۡ يُرۡسِلَ رَسُولٗا فَيُوحِيَ بِإِذۡنِهِۦ مَا يَشَآءُۚ إِنَّهُۥ عَلِيٌّ حَكِيمٞ ﴿٥١﴾

52. እንደዚሁም ወደ አንተ ከትእዛዛችን ሲኾን መንፈስን (ቁርኣንን) አወረድን:: መጽሐፉም እምነቱም ምን እንደኾነ የምታውቅ አልነበርክም:: ግን (መንፈሱን) ከባሮቻችን የምንሻውን ሰው በእርሱ የምንመራበት ብርሃን አደረግነው:: አንተም ወደ ቀጥተኛው መንገድ በእርግጥ ትመራለህ::

وَكَذَٰلِكَ أَوۡحَيۡنَآ إِلَيۡكَ رُوحٗا مِّنۡ أَمۡرِنَاۚ مَا كُنتَ تَدۡرِي مَا ٱلۡكِتَٰبُ وَلَا ٱلۡإِيمَٰنُ وَلَٰكِن جَعَلۡنَٰهُ نُورٗا نَّهۡدِي بِهِۦ مَن نَّشَآءُ مِنۡ عِبَادِنَاۚ وَإِنَّكَ لَتَهۡدِيٓ إِلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ﴿٥٢﴾

53. ወደዚያ በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ የእርሱ ወደ ኾነው አላህ መንገድ (ትመራለህ):: ንቁ! ነገሮቹ ሁሉ ወደ አላህ ይመለሳሉ::

صِرَٰطِ ٱللَّهِ ٱلَّذِي لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۗ أَلَآ إِلَى ٱللَّهِ تَصِيرُ ٱلۡأُمُورُ ﴿٥٣﴾

# ሱረቱ አል ዙኽሩፍ

# سورة الزخرف

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሓ ሚም)::

حمٓ ﴿١﴾

2. ገላጭ በኾነው መጽሐፍ እምላለሁ::

وَٱلۡكِتَٰبِ ٱلۡمُبِينِ ﴿٢﴾

3. እኛ ታውቁ ዘንድ ዐረብኛ ቁርኣን አደረግነው::

إِنَّا جَعَلۡنَٰهُ قُرۡءَٰنًا عَرَبِيّٗا لَّعَلَّكُمۡ تَعۡقِلُونَ ﴿٣﴾

4. እርሱም በመጽሐፎቹ እናት ውስጥ እኛ ዘንድ በእርግጥ ከፍተኛ ጥበብ የተመላ ነው::

وَإِنَّهُۥ فِيٓ أُمِّ ٱلۡكِتَٰبِ لَدَيۡنَا لَعَلِيٌّ حَكِيمٌ ﴿٤﴾

5. ድንበር አላፊዎች ሕዝቦች ለመኾናችሁ ቁርኣኑን ከእናንተ ማገድን እናግዳለን?

أَفَنَضۡرِبُ عَنكُمُ ٱلذِّكۡرَ صَفۡحًا أَن كُنتُمۡ قَوۡمٗا مُّسۡرِفِينَ ﴿٥﴾

6. በፊተኞቹም ሕዝቦች ውስጥ ከነቢይ ብዙን ልከናል::

وَكَمۡ أَرۡسَلۡنَا مِن نَّبِيّٖ فِي ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿٦﴾

7. ከነቢይም አንድም የሚመጣላቸው አልነበረም በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩ ቢኾኑ እንጅ::

وَمَا يَأۡتِيهِم مِّن نَّبِيٍّ إِلَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ﴿٧﴾

8. ከእነርሱም በኀይል ይበልጥ የበረቱትን አጥፍተናል፡፡ የፊተኞቹም (አጠፋፍ) ምሳሌ አልፏል፡፡

فَأَهۡلَكۡنَآ أَشَدَّ مِنۡهُم بَطۡشٗا وَمَضَىٰ مَثَلُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٨

9. «ሰማያትንና ምድርንም ማን ፈጠራቸው» ብለህ ብትጠይቃቸው «አሸናፊው ዐዋቂው (አላህ) በእርግጥ ፈጠራቸው» ይላሉ፡፡

وَلَئِن سَأَلۡتَهُم مَّنۡ خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ لَيَقُولُنَّ خَلَقَهُنَّ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡعَلِيمُ ٩

10. (እርሱ) ያ ምድርን ለእናንተ ምንጣፍ ያደረገላችሁ በርሷም ውስጥ ትምመሩ ዘንድ ለእናንተ መንገዶችን ያደረገላችሁ ነው፡፡

ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ مَهۡدٗا وَجَعَلَ لَكُمۡ فِيهَا سُبُلٗا لَّعَلَّكُمۡ تَهۡتَدُونَ ١٠

11. ያም ከሰማይ ውሃን በልክ ያወረደላችሁ ነው፡፡ በእርሱም የሞተችውን አገር ሕያው አደረግን፡፡ እንደዚሁ (ከመቃብራችሁ) ትውወጣላችሁ፡፡

وَٱلَّذِي نَزَّلَ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءَۢ بِقَدَرٖ فَأَنشَرۡنَا بِهِۦ بَلۡدَةٗ مَّيۡتٗاۚ كَذَٰلِكَ تُخۡرَجُونَ ١١

12. ያም ዓይነቶችን ሁሉ የፈጠረ ለእናንተም ከመርከቦችና ከቤት እንስሳዎች የምትጋልቧቸውን ያደረገላችሁ ነው፡፡

وَٱلَّذِي خَلَقَ ٱلۡأَزۡوَٰجَ كُلَّهَا وَجَعَلَ لَكُم مِّنَ ٱلۡفُلۡكِ وَٱلۡأَنۡعَٰمِ مَا تَرۡكَبُونَ ١٢

13. በጀርባዎቹ ላይ እንድትደላደሉ ከዚያም በርሱ ላይ የተደላደላችሁ ጊዜ የጌታችሁን ጸጋ እንድታስታውሱ፤ እንድትሉም፡- «ያ ይህንን የማንችለው ስንኾን ለእኛ ያገራለን ጌታ ጥራት ይገባው፡፡

لِتَسۡتَوُۥاْ عَلَىٰ ظُهُورِهِۦ ثُمَّ تَذۡكُرُواْ نِعۡمَةَ رَبِّكُمۡ إِذَا ٱسۡتَوَيۡتُمۡ عَلَيۡهِ وَتَقُولُواْ سُبۡحَٰنَ ٱلَّذِي سَخَّرَ لَنَا هَٰذَا وَمَا كُنَّا لَهُۥ مُقۡرِنِينَ ١٣

14. እኛም በእርግጥ ወደ ጌታችን ተመላሾች፤ነን» (እንድትሉ)፡፡

وَإِنَّآ إِلَىٰ رَبِّنَا لَمُنقَلِبُونَ ١٤

15. ከባሮቹም ለእርሱ ቁራጭን (ልጅን) አደረጉለት፡፡ ሰው በእርግጥ ግልጽ ከሓዲ ነው፡፡

وَجَعَلُواْ لَهُۥ مِنۡ عِبَادِهِۦ جُزۡءًاۚ إِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ لَكَفُورٞ مُّبِينٌ ١٥

16. ከሚፈጥረው ውስጥ ሴቶች ልጆችን ያዘን? በወንዶች ልጆችም (እናንተን) መረጣችሁን?

أَمِ ٱتَّخَذَ مِمَّا يَخۡلُقُ بَنَاتٖ وَأَصۡفَىٰكُم بِٱلۡبَنِينَ ١٦

17. አንዳቸውም ለአልረሕማን ምሳሌ ባደረገው ነገር (በሴት ልጅ) በተበሰረ ጊዜ እርሱ በቁጭት የተመላ ኾኖ ፊቱ የጠቆረ ይኾናል፡፡

وَإِذَا بُشِّرَ أَحَدُهُم بِمَا ضَرَبَ لِلرَّحۡمَٰنِ مَثَلٗا ظَلَّ وَجۡهُهُۥ مُسۡوَدّٗا وَهُوَ كَظِيمٌ ١٧

18. በጌጥ (ተከልሶ) እንዲያድግ የሚደረገውን? እርሱም (ለደካማነቱ) በክርክር የሚያብራራውን ፍጡር (ሴትን) ለአላህ ያደርጋሉን?

أَوَمَن يُنَشَّؤُاْ فِي ٱلۡحِلۡيَةِ وَهُوَ فِي ٱلۡخِصَامِ غَيۡرُ مُبِينٖ ١٨

19. መላእክትንም እነርሱ የአልረሕማን ባሮች የኾኑትን ሴቶች አደረጉ፡፡ ሲፈጠሩ ነበሩን? መመስከራቸው በእርግጥ ትጻፋለች፡፡ ይጠየቃሉም፡፡

وَجَعَلُواْ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ ٱلَّذِينَ هُمۡ عِبَٰدُ ٱلرَّحۡمَٰنِ إِنَٰثًاۚ أَشَهِدُواْ خَلۡقَهُمۡۚ سَتُكۡتَبُ شَهَٰدَتُهُمۡ وَيُسۡـَٔلُونَ ١٩

| | |
|---|---|
| 20. «አልረሕማንም በሻ ኖሮ ባልተገዛናቸው ነበር» አሉ፡፡ ለእነርሱ በዚህ ምንም ዕውቀት የላቸውም፡፡ እነርሱ የሚዋሹ እንጅ ሌላ አይደሉም፡፡ | وَقَالُواْ لَوْ شَآءَ ٱلرَّحْمَٰنُ مَا عَبَدْنَٰهُم مَّا لَهُم بِذَٰلِكَ مِنْ عِلْمٍ إِنْ هُمْ إِلَّا يَخْرُصُونَ ﴿٢٠﴾ |
| 21. ከእርሱ (ከቁርኣን) በፊት መጽሐፍን ሰጠናቸውን? ስለዚህ እነርሱ እርሱን የጨበጡ ናቸውን? | أَمْ ءَاتَيْنَٰهُمْ كِتَٰبًا مِّن قَبْلِهِۦ فَهُم بِهِۦ مُسْتَمْسِكُونَ ﴿٢١﴾ |
| 22. ከቶውንም «እኛ አባቶቻችንን በሃይማኖት ላይ አገኘናቸው፡፡ እኛም በፈለጎቻቸው ላይ ተመሪዎች ነን» አሉ፡፡ | بَلْ قَالُوٓاْ إِنَّا وَجَدْنَآ ءَابَآءَنَا عَلَىٰٓ أُمَّةٍ وَإِنَّا عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِم مُّهْتَدُونَ ﴿٢٢﴾ |
| 23. (ነገሩ) እንደዚሁም ነው፡፡ ከበፊትህ በማንኛይቱም ከተማ ውስጥ አስፈራሪን አልላክንም፤ ቅምጥሎችዋ እኛ አባቶቻችንን በሃይማኖት ላይ አገኘን፤ እኛም በፈለጎቻቸው ላይ ተከታዮች ነን ያሉ ቢኾኑ እንጅ፡፡ | وَكَذَٰلِكَ مَآ أَرْسَلْنَا مِن قَبْلِكَ فِى قَرْيَةٍ مِّن نَّذِيرٍ إِلَّا قَالَ مُتْرَفُوهَآ إِنَّا وَجَدْنَآ ءَابَآءَنَا عَلَىٰٓ أُمَّةٍ وَإِنَّا عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِم مُّقْتَدُونَ ﴿٢٣﴾ |
| 24. (አስፈራሪው) «አባቶቻችሁን በእርሱ ላይ ከአገኛችሁበት ይበልጥ ቀጥተኛን (ሃይማኖት) ባመጣላችሁም?» አላቸው፡፡ «እኛ በእርሱ በተላካችሁበት ነገር ከሓዲዎች ነን» አሉ፡፡ | ۞ قَٰلَ أَوَلَوْ جِئْتُكُم بِأَهْدَىٰ مِمَّا وَجَدتُّمْ عَلَيْهِ ءَابَآءَكُمْ قَالُوٓاْ إِنَّا بِمَآ أُرْسِلْتُم بِهِۦ كَٰفِرُونَ ﴿٢٤﴾ |
| 25. ከእነርሱም ተበቀልን፡፡ ያስተባባዮቹም መጨረሻ እንዴት እንደ ነበረ ተመልከት፡፡ | فَٱنتَقَمْنَا مِنْهُمْ فَٱنظُرْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلْمُكَذِّبِينَ ﴿٢٥﴾ |
| 26. ኢብራሂምም ለአባቱና ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «እኔ ከምትግገዙት ሁሉ ንጹሕ ነኝ፡፡» | وَإِذْ قَالَ إِبْرَٰهِيمُ لِأَبِيهِ وَقَوْمِهِۦٓ إِنَّنِى بَرَآءٌ مِّمَّا تَعْبُدُونَ ﴿٢٦﴾ |
| 27. «ከዚያ ከፈጠረኝ በስተቀር (አልግገዛም)፡፡ እርሱ በእርግጥ ይመራኛልና፡፡» | إِلَّا ٱلَّذِى فَطَرَنِى فَإِنَّهُۥ سَيَهْدِينِ ﴿٢٧﴾ |
| 28. በዝርዮቹም ውስጥ ይመለሱ ዘንድ (ባንድ አምላክ ማመንን) ቀሪ ቃል አደረጋት፡፡ | وَجَعَلَهَا كَلِمَةًۢ بَاقِيَةً فِى عَقِبِهِۦ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ ﴿٢٨﴾ |
| 29. ይልቅ እነዚህን (ቁረይሾችን)፣ አባቶቻቸውንም ቁርኣንና ገላጭ መልክተኛ እስከመጣላቸው ድረስ አጣቀምኳቸው፡፡ | بَلْ مَتَّعْتُ هَٰٓؤُلَآءِ وَءَابَآءَهُمْ حَتَّىٰ جَآءَهُمُ ٱلْحَقُّ وَرَسُولٌ مُّبِينٌ ﴿٢٩﴾ |
| 30. እውነቱም በመጣላቸው ጊዜ «ይህ ድግምት ነው፡፡ እኛም በእርሱ ከሓዲዎች ነን» አሉ፡፡ | وَلَمَّا جَآءَهُمُ ٱلْحَقُّ قَالُواْ هَٰذَا سِحْرٌ وَإِنَّا بِهِۦ كَٰفِرُونَ ﴿٣٠﴾ |
| 31. «ይህም ቁርኣን ከሁለቱ ከተሞች በታላቅ ሰው ላይ አይወረድም ኖሯልን?» አሉ፡፡ | وَقَالُواْ لَوْلَا نُزِّلَ هَٰذَا ٱلْقُرْءَانُ عَلَىٰ رَجُلٍ مِّنَ ٱلْقَرْيَتَيْنِ عَظِيمٍ ﴿٣١﴾ |

32. እነርሱ የጌታህን ችሮታ ያከፈፍላሉን? እኛ በቅርቢቱ ሕይወት ኑሯቸውን በመካከላቸው አከፋፍለናል፡፡ ከፊላቸውም ከፊሉን ሠራተኛ አድርጎ ይይዝ ዘንድ ከፊላቸውን ከከፊሉ በላይ በደረጃዎች (በሀብት) አበለጥን፡፡ የጌታህም ጸጋ (ገነት) ከሚሰበስቡት (ሃብት) በላጪ ናት፡፡

أَهُمْ يَقْسِمُونَ رَحْمَتَ رَبِّكَۚ نَحْنُ قَسَمْنَا بَيْنَهُم مَّعِيشَتَهُمْ فِي ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَاۚ وَرَفَعْنَا بَعْضَهُمْ فَوْقَ بَعْضٍ دَرَجَٰتٍ لِّيَتَّخِذَ بَعْضُهُم بَعْضًا سُخْرِيًّاۗ وَرَحْمَتُ رَبِّكَ خَيْرٌ مِّمَّا يَجْمَعُونَ ﴿٣٢﴾

33. ሰዎችም (በክሕደት) አንድ ሕዝብ የሚኾኑ ባልነበሩ ኖሮ በአልረሕማን ፤ለሚክዱት ሰዎች (በዚህች ዓለም) ለቤቶቻቸው ከብር የኾኑን ጣራዎች በእነርሱ ላይ የሚወጡባቸውንም (የብር) መሰላሎች ባደረግንላቸው ነበር፡፡

وَلَوْلَآ أَن يَكُونَ ٱلنَّاسُ أُمَّةً وَٰحِدَةً لَّجَعَلْنَا لِمَن يَكْفُرُ بِٱلرَّحْمَٰنِ لِبُيُوتِهِمْ سُقُفًا مِّن فِضَّةٍ وَمَعَارِجَ عَلَيْهَا يَظْهَرُونَ ﴿٣٣﴾

34. ለቤቶቻቸውም ደጃፎችን በእነርሱ ላይ የሚደገፉባቸውንም አልጋዎች (ከብር ባደረግንላቸው ነበር)፡፡

وَلِبُيُوتِهِمْ أَبْوَٰبًا وَسُرُرًا عَلَيْهَا يَتَّكِـُٔونَ ﴿٣٤﴾

35. የወርቅ ጌጥንም (ባደረግንላቸው ነበር)፡፡ ይህም ሁሉ የቅርቢቱ ሕይወት መጣቀሚያ እንጅ ሌላ አይደለም፤ (ጠፊ ነው)፡፡ መጨረሻይቱም አገር በጌታህ ዘንድ ለጥንቁቆቹ ናት፡፡

وَزُخْرُفًاۚ وَإِن كُلُّ ذَٰلِكَ لَمَّا مَتَٰعُ ٱلْحَيَوٰةِ ٱلدُّنْيَاۚ وَٱلْءَاخِرَةُ عِندَ رَبِّكَ لِلْمُتَّقِينَ ﴿٣٥﴾

36. ከአልረሕማን ግሣጼ (ከቁርኣን) የሚደናበርም ሰው ለእርሱ ሰይጣንን እናስጠጋለን፡፡ ስለዚህ እርሱ ለእርሱ ቁራኛ ነው፡፡

وَمَن يَعْشُ عَن ذِكْرِ ٱلرَّحْمَٰنِ نُقَيِّضْ لَهُۥ شَيْطَٰنًا فَهُوَ لَهُۥ قَرِينٌ ﴿٣٦﴾

37. እነርሱም (ተደናባሪዎቹ) ተመሪዎች መኾናቸውን የሚያስቡ ሲኾኑ እነርሱ (ሰይጣናት) ከቀጥተኛው መንገድ በእርግጥ ያግዷቸዋል፡፡

وَإِنَّهُمْ لَيَصُدُّونَهُمْ عَنِ ٱلسَّبِيلِ وَيَحْسَبُونَ أَنَّهُم مُّهْتَدُونَ ﴿٣٧﴾

38. (በትንሣኤ) ወደኛ በመጣም ጊዜ (ቁራኛዬ ሆይ!) «በእኔና ባንተ መካከል የምሥራቅና የምዕራብ ርቀት በኖረ ወይ ምኞቴ! ምን የከፋህ ቁራኛ ነህ» ይላል፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا جَآءَنَا قَالَ يَٰلَيْتَ بَيْنِي وَبَيْنَكَ بُعْدَ ٱلْمَشْرِقَيْنِ فَبِئْسَ ٱلْقَرِينُ ﴿٣٨﴾

39. ስለ በደላችሁም ዛሬ እናንተ በቅጣት ተጋሪዎች መኾናችሁ አይጠቅማችሁም፤ (ይባላሉ)፡፡

وَلَن يَنفَعَكُمُ ٱلْيَوْمَ إِذ ظَّلَمْتُمْ أَنَّكُمْ فِي ٱلْعَذَابِ مُشْتَرِكُونَ ﴿٣٩﴾

40. አንተ ደንቆሮዎችን ታሰማለህን? ወይስ ዕውሮችንና በግልጽ ጥመት ውስጥ የኾኑን ሰዎች ትመራለህን?

أَفَأَنتَ تُسْمِعُ ٱلصُّمَّ أَوْ تَهْدِي ٱلْعُمْيَ وَمَن كَانَ فِي ضَلَٰلٍ مُّبِينٍ ﴿٤٠﴾

41. አንተንም (ቅጣታቸውን ስታይ) ብንወስድህ እኛ ከእነርሱ ተበቃዮች ነን፡፡

فَإِمَّا نَذْهَبَنَّ بِكَ فَإِنَّا مِنْهُم مُّنتَقِمُونَ ﴿٤١﴾

42. ወይም ያንን የቀጠርናቸውን ብናሳይህ እኛ በእነርሱ (ቅጣት) ላይ ቻይዎች ነን፡፡

أَوْ نُرِيَنَّكَ ٱلَّذِي وَعَدْنَٰهُمْ فَإِنَّا عَلَيْهِم مُّقْتَدِرُونَ ﴿٤٢﴾

43. ያንንም ወደ አንተ የተወረደልህን አጥብቀህ ያዝ፡፡ አንተ በቀጥተኛው መንገድ ላይ ነህና፡፡

فَٱسْتَمْسِكْ بِٱلَّذِىٓ أُوحِىَ إِلَيْكَ ۖ إِنَّكَ عَلَىٰ صِرَٰطٍ مُّسْتَقِيمٍ ﴿٤٣﴾

44. እርሱም (ቁርአን) ለአንተ፣ ለሕዘቦችህም ታላቅ ክብር ነው፡፡ ወደ ፊትም (ከርሱ) ትጠየቃላችሁ፡፡

وَإِنَّهُۥ لَذِكْرٌ لَّكَ وَلِقَوْمِكَ ۖ وَسَوْفَ تُسْـَٔلُونَ ﴿٤٤﴾

45. ከመልእክተኞቻችንም ካንተ በፊት የላክናቸውን (ተከታዮቻቸውን) ከአልረሕማን ሌላ የሚገዙዋቸው የኾኑን አማልክት አድርገን እንደ ኾነ ጠይቃቸው፡፡

وَسْـَٔلْ مَنْ أَرْسَلْنَا مِن قَبْلِكَ مِن رُّسُلِنَآ أَجَعَلْنَا مِن دُونِ ٱلرَّحْمَٰنِ ءَالِهَةً يُعْبَدُونَ ﴿٤٥﴾

46. ሙሳንም በተዓምራቶቻችን ወደ ፈርዖንና ወደ ሹማምንቶቹ በእርግጥ ላክን፡፡ «እኔ የዓለማት ጌታ መልክተኛ ነኝ» አላቸውም፡፡

وَلَقَدْ أَرْسَلْنَا مُوسَىٰ بِـَٔايَٰتِنَآ إِلَىٰ فِرْعَوْنَ وَمَلَإِي۟هِۦ فَقَالَ إِنِّى رَسُولُ رَبِّ ٱلْعَٰلَمِينَ ﴿٤٦﴾

47. በተዓምራታችንም በመጣባቸው ጊዜ ወዲያውኑ እነርሱ በእርሷ ይስቃሉ፡፡

فَلَمَّا جَآءَهُم بِـَٔايَٰتِنَآ إِذَا هُم مِّنْهَا يَضْحَكُونَ ﴿٤٧﴾

48. ከተዓምርም አንዲትንም አናሳያቸውም እርሷ ከብጤዋ በጣም የበለጠች ብትኾን እንጅ፡፡ (ከክህደታቸው) ይመለሱም ዘንድ በቅጣት ያዝናቸው፡፡

وَمَا نُرِيهِم مِّنْ ءَايَةٍ إِلَّا هِىَ أَكْبَرُ مِنْ أُخْتِهَا ۖ وَأَخَذْنَٰهُم بِٱلْعَذَابِ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ ﴿٤٨﴾

49. «አንተ ድግምተኛ (ዐዋቂ) ሆይ! ጌታህን አንተ ዘንድ ቃል በገባልህ ለእኛ ለምንልን፡፡ እኛ (ቅጣቱን ቢያነሳልን) ተመሪዎች ነን» አሉም፡፡

وَقَالُوا۟ يَـٰٓأَيُّهَ ٱلسَّاحِرُ ٱدْعُ لَنَا رَبَّكَ بِمَا عَهِدَ عِندَكَ إِنَّنَا لَمُهْتَدُونَ ﴿٤٩﴾

50. ስቃዩን ከእነርሱ ላይ በገለጥንም ጊዜ ወዲያውኑ ኪዳናቸውን ያፈርሳሉ፡፡

فَلَمَّا كَشَفْنَا عَنْهُمُ ٱلْعَذَابَ إِذَا هُمْ يَنكُثُونَ ﴿٥٠﴾

51. ፈርዖንም በሕዝቦቹ ውስጥ ተጣራ፡፡ አለም፤ «ሕዝቦቼ ሆይ! የምስር ግዛት የኔ አይደለምን? እነዚህም ጅረቶች ከስሬ የሚፈሱ ሲኾኑ (የኔ አይደሉምን?) አትመለከቱምን?

وَنَادَىٰ فِرْعَوْنُ فِى قَوْمِهِۦ قَالَ يَٰقَوْمِ أَلَيْسَ لِى مُلْكُ مِصْرَ وَهَٰذِهِ ٱلْأَنْهَٰرُ تَجْرِى مِن تَحْتِىٓ ۖ أَفَلَا تُبْصِرُونَ ﴿٥١﴾

52. «በውነቱ እኔ ከዚህ ያ እርሱ ወራዳ ንግግሩንም ሊገልጽ የማይቀርብ ከኾነው በላጭ ነኝ፡፡

أَمْ أَنَا۠ خَيْرٌ مِّنْ هَٰذَا ٱلَّذِى هُوَ مَهِينٌ وَلَا يَكَادُ يُبِينُ ﴿٥٢﴾

53. «በእርሱም ላይ የወርቅ አንባሮች ለምን አልተጣሉበትም ወይም መላእክት ከእርሱ ጋር ተቆራኝተው ለምን አልመጡም» (አለ)፡፡

فَلَوْلَآ أُلْقِىَ عَلَيْهِ أَسْوِرَةٌ مِّن ذَهَبٍ أَوْ جَآءَ مَعَهُ ٱلْمَلَـٰٓئِكَةُ مُقْتَرِنِينَ ﴿٥٣﴾

54. ሕዝቦቹንም አቄላቸው፡፡ ታዘዙትም፡፡ እነርሱ አመጸኞች ሕዝቦች ነበሩና፡፡

فَٱسْتَخَفَّ قَوْمَهُۥ فَأَطَاعُوهُ ۚ إِنَّهُمْ كَانُوا۟ قَوْمًا فَٰسِقِينَ ﴿٥٤﴾

55. ባስቆጡንም ጊዜ ከእነርሱ በተበቀለን፡፡ ሁሉንም አሰጠምናቸውም፡፡

فَلَمَّآ ءَاسَفُونَا ٱنتَقَمْنَا مِنْهُمْ فَأَغْرَقْنَٰهُمْ أَجْمَعِينَ ﴿٥٥﴾

56. (በጥፋት) ቀዳሚዎችና ለኋለኞቹ (መቀጣጫ) ምሳሌም አደረግናቸው፡፡

فَجَعَلۡنَٰهُمۡ سَلَفٗا وَمَثَلٗا لِّلۡأٓخِرِينَ ٥٦

57. የመርየም ልጅም ምሳሌ በተደረገ ጊዜ ሕዝቦችህ (ከሓዲዎቹ) ወዲያውኑ ከእርሱ ይስቃሉ፡፡

۞وَلَمَّا ضُرِبَ ٱبۡنُ مَرۡيَمَ مَثَلًا إِذَا قَوۡمُكَ مِنۡهُ يَصِدُّونَ ٥٧

58. «አማልክቶቻችን ይበልጣሉን ወይስ እርሱ?» አሉም፡፡ ለክርክርም እንጅ ላንተ እርሱን ምሳሌ አላደረጉትም፡፡ በእውነት እነርሱ ክርክረ ብርቱ ሕዝቦች ናቸው፡፡

وَقَالُوٓاْ ءَأَٰلِهَتُنَا خَيۡرٌ أَمۡ هُوَۚ مَا ضَرَبُوهُ لَكَ إِلَّا جَدَلَۢاۚ بَلۡ هُمۡ قَوۡمٌ خَصِمُونَ ٥٨

59. እርሱ በርሱ ላይ የለገስንለት ለእስራኤለም ልጆች ተዓምር ያደረግነው የኾነ ባሪያ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

إِنۡ هُوَ إِلَّا عَبۡدٌ أَنۡعَمۡنَا عَلَيۡهِ وَجَعَلۡنَٰهُ مَثَلٗا لِّبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٥٩

60. ብንሻም ኖሮ በምድር ላይ ከእናንተ ምትክ መላእክትን ባደረግን ነበር፡፡

وَلَوۡ نَشَآءُ لَجَعَلۡنَا مِنكُم مَّلَٰٓئِكَةٗ فِي ٱلۡأَرۡضِ يَخۡلُفُونَ ٦٠

61. እርሱም (ዒሳ) ለሰዓቲቱ (ማወቂያ) በእርግጥ ምልክት ነው፡፡ «በእርሷም አትጠራጠሩ፡፡ ተከተሉኝም፤ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው» (በላቸው)፡፡

وَإِنَّهُۥ لَعِلۡمٞ لِّلسَّاعَةِ فَلَا تَمۡتَرُنَّ بِهَا وَٱتَّبِعُونِۚ هَٰذَا صِرَٰطٞ مُّسۡتَقِيمٞ ٦١

62. ሰይጣንም አያግዳችሁ፡፡ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና፡፡

وَلَا يَصُدَّنَّكُمُ ٱلشَّيۡطَٰنُۖ إِنَّهُۥ لَكُمۡ عَدُوّٞ مُّبِينٞ ٦٢

63. ዒሳ በታምራቶች በመጣ ጊዜም አላቸው «በእርግጥ በጥበብ መጣኋችሁ፡፡ የዚያንም በርሱ የምትለያዩበትን ከፊሉን ለናንተ ላብራራላችሁ (መጣሁ)፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ ታዘዙኝም፡፡

وَلَمَّا جَآءَ عِيسَىٰ بِٱلۡبَيِّنَٰتِ قَالَ قَدۡ جِئۡتُكُم بِٱلۡحِكۡمَةِ وَلِأُبَيِّنَ لَكُم بَعۡضَ ٱلَّذِي تَخۡتَلِفُونَ فِيهِۖ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُونِ ٦٣

64. «አላህ ጌታዬ ጌታችሁም ነውና ተገዙት፡፡ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው፡፡»

إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ رَبِّي وَرَبُّكُمۡ فَٱعۡبُدُوهُۚ هَٰذَا صِرَٰطٞ مُّسۡتَقِيمٞ ٦٤

65. ከመካከላቸውም አሕዛቦቹ ተለያዩ፡፡ ለእነዚያም ለበደሉት ከአሳማሚ ቀን ቅጣት ወዮላቸው፡፡

فَٱخۡتَلَفَ ٱلۡأَحۡزَابُ مِنۢ بَيۡنِهِمۡۖ فَوَيۡلٞ لِّلَّذِينَ ظَلَمُواْ مِنۡ عَذَابِ يَوۡمٍ أَلِيمٍ ٦٥

66. ሰዓቲቱን እነርሱ የማያውቁ ኾነው በድንገት ልትመጣባቸው እንጅ ይጠባበቃሉን?

هَلۡ يَنظُرُونَ إِلَّا ٱلسَّاعَةَ أَن تَأۡتِيَهُم بَغۡتَةٗ وَهُمۡ لَا يَشۡعُرُونَ ٦٦

67. ወዳጆች በዚያ ቀን ከፊላቸው ለከፊሉ ጠላት ነው፡፡ አላህን ፈሪዎች ብቻ ሲቀሩ፡፡

ٱلۡأَخِلَّآءُ يَوۡمَئِذِۭ بَعۡضُهُمۡ لِبَعۡضٍ عَدُوٌّ إِلَّا ٱلۡمُتَّقِينَ ٦٧

68. (ለነርሱስ) «ባሮቼ ሆይ! ዛሬ ቀን በእናንተ ላይ ፍርሃት የለባችሁም እናንተም የምታዝኑ አይደላችሁም» (ይባላሉ)፡፡

يَٰعِبَادِ لَا خَوْفٌ عَلَيْكُمُ ٱلْيَوْمَ وَلَآ أَنتُمْ تَحْزَنُونَ ﴿٦٨﴾

69. እነዚያ በአንቀጾቻችን ያመኑና ፍጹም ታዛዦች የነበሩ (ባሮቼ ሆይ!)

ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ بِـَٔايَٰتِنَا وَكَانُوا۟ مُسْلِمِينَ ﴿٦٩﴾

70. «ገነትን ግቡ እናንተም ሚስቶቻችሁም ትደሰታላችሁ ትከበሩም አላችሁ» (ይባላሉ)፡፡

ٱدْخُلُوا۟ ٱلْجَنَّةَ أَنتُمْ وَأَزْوَٰجُكُمْ تُحْبَرُونَ ﴿٧٠﴾

71. ከወርቅ የኾኑ ሰፋፊ ዝርግ ሳሕኖችና ኩባያዎች በእነርሱ ላይ ይዝዞራሉ፡፡ በእርሷም ውስጥ ነፍሶች የሚከጅሉት፣ ዓይኖችም የሚደሰቱበት ሁሉ አልለ፡፡ እናንተም በውስጧ ዘላለም ዘውታሪዎች ናችሁ፡፡

يُطَافُ عَلَيْهِم بِصِحَافٍ مِّن ذَهَبٍ وَأَكْوَابٍ ۖ وَفِيهَا مَا تَشْتَهِيهِ ٱلْأَنفُسُ وَتَلَذُّ ٱلْأَعْيُنُ ۖ وَأَنتُمْ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿٧١﴾

72. ይህችም ያቺ ትሠሩት በነበራችሁት ዋጋ የተሰጣችኋት ገነት ናት፡፡

وَتِلْكَ ٱلْجَنَّةُ ٱلَّتِىٓ أُورِثْتُمُوهَا بِمَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ﴿٧٢﴾

73. ለእናንተ በውስጧ ብዙ ፍረፍሬዎች በእርግጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

لَكُمْ فِيهَا فَٰكِهَةٌ كَثِيرَةٌ مِّنْهَا تَأْكُلُونَ ﴿٧٣﴾

74. አመጸኞች በገሀነም ስቃይ ውስጥ በእርግጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلْمُجْرِمِينَ فِى عَذَابِ جَهَنَّمَ خَٰلِدُونَ ﴿٧٤﴾

75. ከእነርሱ (ቅጣቱ) አይቀለልላቸውም፡፡ እነርሱም በእርሱ ውስጥ ተሰፋ ቆራጮች ናቸው፡፡

لَا يُفَتَّرُ عَنْهُمْ وَهُمْ فِيهِ مُبْلِسُونَ ﴿٧٥﴾

76. አልበደልናቸውምም፤ ግን በዳዮቹ እነርሱው ነበሩ፡ ፡

وَمَا ظَلَمْنَٰهُمْ وَلَٰكِن كَانُوا۟ هُمُ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٧٦﴾

77. «ማሊክ ሆይ! ጌታህ በኛ ላይ (በሞት) ይፍረድ፡፡» እያሉ ይጣራሉም፡፡ «እናንተ (በቅጣቱ ውስጥ) ዘላለም ነዋሪዎች ናችሁ» ይላቸዋል፡፡

وَنَادَوْا۟ يَٰمَٰلِكُ لِيَقْضِ عَلَيْنَا رَبُّكَ ۖ قَالَ إِنَّكُم مَّٰكِثُونَ ﴿٧٧﴾

78. እውነተኛውን መንገድ በእርግጥ አመጣንላችሁ፡፡ ግን አብዛኞቻችሁ እውነቱን ጠይዎች ናችሁ፡፡

لَقَدْ جِئْنَٰكُم بِٱلْحَقِّ وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَكُمْ لِلْحَقِّ كَٰرِهُونَ ﴿٧٨﴾

79. ይልቁንም (በነቢዩ ላይ በማደም) ነገርን አጠነከሩን? እኛም (ተንኮላቸውን ወደእነርሱ በመመለስ) አጠንካሪዎች ነን፡፡

أَمْ أَبْرَمُوٓا۟ أَمْرًا فَإِنَّا مُبْرِمُونَ ﴿٧٩﴾

80. ወይም እኛ ምስጢራቸውንና ውይይታቸውን የማንሰማ መኾናችንን ያስባሉን? አይደለም፤ መልከተኞቻችንም እነርሱ ዘንድ ይጽፋሉ፡፡

أَمْ يَحْسَبُونَ أَنَّا لَا نَسْمَعُ سِرَّهُمْ وَنَجْوَىٰهُم ۚ بَلَىٰ وَرُسُلُنَا لَدَيْهِمْ يَكْتُبُونَ ﴿٨٠﴾

81. «ለአልረሕማን ልጅ (የለውም እንጅ) ቢኖረው እኔ (ለልጁ) የተገዢዎቹ መጀመሪያ ነኝ» በላቸው፡፡

قُلْ إِن كَانَ لِلرَّحْمَٰنِ وَلَدٌ فَأَنَا۠ أَوَّلُ ٱلْعَٰبِدِينَ ﴿٨١﴾

82. የሰማያትና የምድር ጌታ የዙፋኑ ጌታ ከሚሉት ነገር ሁሉ ጠራ፡፡

سُبۡحَٰنَ رَبِّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ رَبِّ ٱلۡعَرۡشِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿٨٢﴾

83. ተዋቸውም፡፡ ያንን ይስፈራሩበት የነበሩትን ቀናቸውን እስከሚገናኙ ድረስ (በስሕተታቸው ውስጥ) ይዋኙ ይጫዎቱም፡፡

فَذَرۡهُمۡ يَخُوضُواْ وَيَلۡعَبُواْ حَتَّىٰ يُلَٰقُواْ يَوۡمَهُمُ ٱلَّذِي يُوعَدُونَ ﴿٨٣﴾

84. እርሱም ያ በሰማይ ውስጥ ሊግገዙት የሚገባው በምድርም ውስጥ ሊግገዙት የሚገባው አምላክ ነው፡፡ እርሱም ብልሃተኛው ዐዋቂው ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي فِي ٱلسَّمَآءِ إِلَٰهٞ وَفِي ٱلۡأَرۡضِ إِلَٰهٞۚ وَهُوَ ٱلۡحَكِيمُ ٱلۡعَلِيمُ ﴿٨٤﴾

85. ያም የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ንግሥና የእርሱ ብቻ የኾነው አምላክ ላቀ፡፡ የሰዓቲቱም (የመምጫዋ ዘመን) ዕውቀት እርሱ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ ወደእርሱም ትመለሳላችሁ፡፡

وَتَبَارَكَ ٱلَّذِي لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَا وَعِندَهُۥ عِلۡمُ ٱلسَّاعَةِ وَإِلَيۡهِ تُرۡجَعُونَ ﴿٨٥﴾

86. እነዚያም ከአላህ ሌላ የሚግገዟቸው እነርሱ የሚያውቁ ኾነው በእውነት ከመሰከሩት በስተቀር ምልጃን አይችሉም፡፡

وَلَا يَمۡلِكُ ٱلَّذِينَ يَدۡعُونَ مِن دُونِهِ ٱلشَّفَٰعَةَ إِلَّا مَن شَهِدَ بِٱلۡحَقِّ وَهُمۡ يَعۡلَمُونَ ﴿٨٦﴾

87. ማን እንደፈጠራቸውም ብትጠይቃቸው «በእርግጥ አላህ ነው» ይላሉ፡፡ ታዲያ (ከእምነት) ወዴት ይዞራሉ፡፡

وَلَئِن سَأَلۡتَهُم مَّنۡ خَلَقَهُمۡ لَيَقُولُنَّ ٱللَّهُۖ فَأَنَّىٰ يُؤۡفَكُونَ ﴿٨٧﴾

88. (ነቢዩ) ጌታዬ ሆይ! እነዚህ የማያምኑ ሕዝቦች ናቸው፤ የማለቱም (ዕውቀት አላህ ዘንድ ነው)፡፡

وَقِيلِهِۦ يَٰرَبِّ إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ قَوۡمٞ لَّا يُؤۡمِنُونَ ﴿٨٨﴾

89. እነርሱንም ተዋቸው፡፡ ነገሬ ሰላም ነው በልም፡፡ ወደፊትም (የሚመጣባቸውን) ያውቃሉ፡፡

فَٱصۡفَحۡ عَنۡهُمۡ وَقُلۡ سَلَٰمٞۚ فَسَوۡفَ يَعۡلَمُونَ ﴿٨٩﴾

# ሱረቱ አል ዱኻን

# سورة الدخان

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሓ ሚም)፡፡

حمٓ ١

2. አብራሪ በኾነው መጽሐፍ እንምላለን፡፡

وَٱلۡكِتَٰبِ ٱلۡمُبِينِ ٢

3. እኛ (ቁርአኑን) በተባረከች ሌሊት ውስጥ አወረድነው፡፡ እኛ አስፈራሪዎች ነበርንና፡፡

إِنَّآ أَنزَلۡنَٰهُ فِي لَيۡلَةٖ مُّبَٰرَكَةٍۚ إِنَّا كُنَّا مُنذِرِينَ ٣

4. በውስጧ የተወሰነው ነገር ሁሉ ይልለያል፡፡

فِيهَا يُفۡرَقُ كُلُّ أَمۡرٍ حَكِيمٍ ٤

5. ከእኛ ዘንድ የኾነ ትእዛዝ ሲኾን (አወረድነው)፡፡ እኛ (መልክተኞችን) ላኪዎች ነበርን፡፡

أَمۡرٗا مِّنۡ عِندِنَآۚ إِنَّا كُنَّا مُرۡسِلِينَ ٥

6. ከጌታህ በኾነው ችሮታ (ተላኩ)፡፡ እነሆ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና፡፡

رَحۡمَةٗ مِّن رَّبِّكَۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلسَّمِيعُ ٱلۡعَلِيمُ ٦

7. የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ነገር ሁሉ ጌታ ከኾነው (ተላኩ)፡፡ የምታረጋግጡ እንደኾናችሁ (ነገሩ እንዳልነው መኾኑን እወቁ)፡፡

رَبِّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَآۖ إِن كُنتُم مُّوقِنِينَ ٧

8. ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ ሕያው ያደርጋል፡፡ ይገድላልም፡፡ ጌታችሁ የመጀመሪያዎቹ አባቶቻችሁም ጌታ ነው፡፡

لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ يُحۡيِۦ وَيُمِيتُۖ رَبُّكُمۡ وَرَبُّ ءَابَآئِكُمُ ٱلۡأَوَّلِينَ ٨

9. በእውነቱ እነርሱ የሚጫወቱ ሲኾኑ በመጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡

بَلۡ هُمۡ فِي شَكّٖ يَلۡعَبُونَ ٩

10. ሰማይም በግልጽ ጭስ የምትመጣበትን ቀን ተጠባበቅ፡፡

فَٱرۡتَقِبۡ يَوۡمَ تَأۡتِي ٱلسَّمَآءُ بِدُخَانٖ مُّبِينٖ ١٠

11. ሰዎችን የሚሸፍን (በኾነ ጭስ) ይህ አሳማሚ ቅጣት ነው፡፡

يَغۡشَى ٱلنَّاسَۖ هَٰذَا عَذَابٌ أَلِيمٞ ١١

12. «ጌታችን ሆይ! ከእኛ ላይ ቅጣቱን ግለጥልን፡፡ እኛ አማኞች እንኾናለንና» (ይላሉም)፡፡

رَّبَّنَا ٱكۡشِفۡ عَنَّا ٱلۡعَذَابَ إِنَّا مُؤۡمِنُونَ ١٢

13. (ቅጣቱ በወረደ ጊዜ) ለእነርሱ መገገሰጽ እንዴት ይኖራቸዋል? አስረጅ መልክተኛ የመጣቸው ሲኾን (የካዱም ሲኾኑ)::

أَنَّىٰ لَهُمُ ٱلذِّكْرَىٰ وَقَدْ جَآءَهُمْ رَسُولٌ مُّبِينٌ ١٣

14. ከዚያም ከእርሱ የዞሩ፤ (ከሰው) «የተሰተማረ ዕብድ ነው» ያሉም ሲኾኑ::

ثُمَّ تَوَلَّوْاْ عَنْهُ وَقَالُواْ مُعَلَّمٌ مَّجْنُونٌ ١٤

15. እኛ ቅጣቱን ለጥቂት ጊዜ ገላጮች ነን:: እናንተ (ወደ ክህደታችሁ) በእርግጥ ተመላሾች ናችሁ::

إِنَّا كَاشِفُواْ ٱلْعَذَابِ قَلِيلًاۚ إِنَّكُمْ عَآئِدُونَ ١٥

16. ታላቂቱን ብርቱ አያያዝ በምንይዝበት ቀን፤ እኛ ተበቃዮች ነን::

يَوْمَ نَبْطِشُ ٱلْبَطْشَةَ ٱلْكُبْرَىٰٓ إِنَّا مُنتَقِمُونَ ١٦

17. ከእነርሱም በፊት የፈርዖንን ሕዝቦች በእርግጥ ሞከርን:: ክቡር መልእክተኛም መጣላቸው::

۞وَلَقَدْ فَتَنَّا قَبْلَهُمْ قَوْمَ فِرْعَوْنَ وَجَآءَهُمْ رَسُولٌ كَرِيمٌ ١٧

18. «የአላህን ባሮች ወደኔ አድርሱ:: እኔ ለእናንተ ታማኝ መልክተኛ ነኝና::

أَنْ أَدُّوٓاْ إِلَيَّ عِبَادَ ٱللَّهِۖ إِنِّي لَكُمْ رَسُولٌ أَمِينٌ ١٨

19. «በአላህም ላይ አትኩሩ:: እኔ ግልጽ የኾነን አስረጅ ያመጣሁላችሁ ነኝና (በማለት መጣላቸው)::

وَأَن لَّا تَعْلُواْ عَلَى ٱللَّهِۖ إِنِّيٓ ءَاتِيكُم بِسُلْطَٰنٍ مُّبِينٍ ١٩

20. «እኔም እንዳትወግሩኝ በጌታየና በጌታችሁ ተጠብቂያለሁ::

وَإِنِّي عُذْتُ بِرَبِّي وَرَبِّكُمْ أَن تَرْجُمُونِ ٢٠

21. «በእኔም ባታምኑ ራቁኝ» (ተዉኝ አለ)::

وَإِن لَّمْ تُؤْمِنُواْ لِي فَٱعْتَزِلُونِ ٢١

22. ቀጥሎም (ስለ ዛቱበት) «እነዚህ አመጸኞች ሕዝቦች ናቸው» (አጥፋቸው) ሲል ጌታውን ለመነ::

فَدَعَا رَبَّهُۥٓ أَنَّ هَٰٓؤُلَآءِ قَوْمٌ مُّجْرِمُونَ ٢٢

23. (ጌታው) «ባሮቼንም ይዘህ በሌሊት ኺድ:: እናንተ የሚከተሉዋችሁ ናችሁና::

فَأَسْرِ بِعِبَادِي لَيْلًا إِنَّكُم مُّتَّبَعُونَ ٢٣

24. «ባሕሩንም የተከፈተ ኾኖ ተወው:: እነርሱ የሚሰጥጠሙ ሰራዊት ናቸውና» (አለው)::

وَٱتْرُكِ ٱلْبَحْرَ رَهْوًاۖ إِنَّهُمْ جُندٌ مُّغْرَقُونَ ٢٤

25. ከአትክልቶችና ከምንጮችም ብዙ ነገሮችን ተዉ::

كَمْ تَرَكُواْ مِن جَنَّٰتٍ وَعُيُونٍ ٢٥

26. ከአዝመራዎችም ከመልካም መቀመጫም::

وَزُرُوعٍ وَمَقَامٍ كَرِيمٍ ٢٦

27. በእርሷ ተደሳቾች ከነበሩባትም ድሎት (ብዙን ነገር ተዉ)::

وَنَعْمَةٍ كَانُواْ فِيهَا فَٰكِهِينَ ٢٧

28. (ነገሩ) እንደዚሁ ኾነ:: ሌሎችንም ሕዝቦች አወረስናት::

كَذَٰلِكَۖ وَأَوْرَثْنَٰهَا قَوْمًا ءَاخَرِينَ ٢٨

29. ሰማይና ምድርም በእነርሱ ላይ አላለቀሱም:: የሚቆዩም አልነበሩም::

فَمَا بَكَتْ عَلَيْهِمُ ٱلسَّمَآءُ وَٱلْأَرْضُ وَمَا كَانُواْ مُنظَرِينَ ٢٩

30. የእስራኤልንም ልጆች አዋራጅ ከኾነ ስቃይ በእርግጥ አዳንናቸው፡፡

وَلَقَدۡ نَجَّيۡنَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ مِنَ ٱلۡعَذَابِ ٱلۡمُهِينِ ٣٠

31. ከፈርዖን፤ እርሱ የኮራ ከወሰን አላፊዎቹ ነበርና፡፡

مِن فِرۡعَوۡنَۚ إِنَّهُۥ كَانَ عَالِيٗا مِّنَ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ٣١

32. ከማወቅም ጋር በዓለማት ላይ በእርግጥ መረጥናቸው፡፡

وَلَقَدِ ٱخۡتَرۡنَٰهُمۡ عَلَىٰ عِلۡمٍ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ٣٢

33. ከታምራቶችም በውስጡ ግልጽ የኾነ ፈተና ያለበትን ሰጠናቸው፡፡

وَءَاتَيۡنَٰهُم مِّنَ ٱلۡأٓيَٰتِ مَا فِيهِ بَلَٰٓؤٞاْ مُّبِينٌ ٣٣

34. እነዚህ (የመካ ከሓዲዎች) በእርግጥ ይላሉ፡-

إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ لَيَقُولُونَ ٣٤

35. እርሷ የፊተኛይቱ ሞታችን እንጅ አይደለችም፡፡ እኛም የምንቀሰቀስ አይደለንም፡፡

إِنۡ هِيَ إِلَّا مَوۡتَتُنَا ٱلۡأُولَىٰ وَمَا نَحۡنُ بِمُنشَرِينَ ٣٥

36. እውነተኞችም እንደ ኾናችሁ አባቶቻችንን አምጡልን፡፡

فَأۡتُواْ بِـَٔابَآئِنَآ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٣٦

37. እነርሱ በላጮች ናቸውን ወይስ የቱብበዕ ሕዝቦችና እነዚያ ከእነርሱ በፊት የነበሩት? አጠፋናቸው፡፡ እነርሱ አመጸኞች ነበሩና፡፡

أَهُمۡ خَيۡرٌ أَمۡ قَوۡمُ تُبَّعٖ وَٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ أَهۡلَكۡنَٰهُمۡۚ إِنَّهُمۡ كَانُواْ مُجۡرِمِينَ ٣٧

38. ሰማያትንና ምድርንም በሁለቱ መካከል ያለውንም ሁሉ ቀላጆች ኾነን አልፈጠርንም፡፡

وَمَا خَلَقۡنَا ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَا لَٰعِبِينَ ٣٨

39. ሁለቱንም በምር እንጅ አልፈጠርናቸውም፡፡ ግን አብዛኞቻቸው አያውቁም፡፡

مَا خَلَقۡنَٰهُمَآ إِلَّا بِٱلۡحَقِّ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٣٩

40. የመለያው ቀን ለሁሉም ቀጠሯቸው ነው፡፡

إِنَّ يَوۡمَ ٱلۡفَصۡلِ مِيقَٰتُهُمۡ أَجۡمَعِينَ ٤٠

41. ዘመድ ከዘመዱ ምንንም የማይጠቅምበት እነርሱም የማይርረዱበት ቀን ነው፡፡

يَوۡمَ لَا يُغۡنِي مَوۡلًى عَن مَّوۡلٗى شَيۡـٔٗا وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ٤١

42. አላህ ያዘነለት ሰውና ያመነ ብቻ ሲቀር፡፡ (እርሱስ ይርረዳል)፡፡ እርሱ አሸናፊው አዛኙ ነውና፡፡

إِلَّا مَن رَّحِمَ ٱللَّهُۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ٤٢

43. የዘቁም ዛፍ

إِنَّ شَجَرَتَ ٱلزَّقُّومِ ٤٣

44. የኀጢአተኛው ምግብ ነው፡፡

طَعَامُ ٱلۡأَثِيمِ ٤٤

45. እንደ ዘይት አተላ ነው፡፡ በሆዶች ውስጥ የሚፈላ ሲኾን፡፡

كَٱلۡمُهۡلِ يَغۡلِي فِي ٱلۡبُطُونِ ٤٥

46. እንደ ገነፈለ ውሃ አፈላል (የሚፈላ ሲኾን)፡፡

كَغَلْيِ ٱلْحَمِيمِ ﴿٤٦﴾

47. ያዙት፤ ወደ ገሀነም መካከልም በኀይል ጎትቱት፡፡

خُذُوهُ فَٱعْتِلُوهُ إِلَىٰ سَوَآءِ ٱلْجَحِيمِ ﴿٤٧﴾

48. ከዚያም «ከራሱ በላይ ከፈላ ውሃ ስቃይ አንቧቡበት፡፡»

ثُمَّ صُبُّوا۟ فَوْقَ رَأْسِهِۦ مِنْ عَذَابِ ٱلْحَمِيمِ ﴿٤٨﴾

49. «ቅመስ፤ አንተ አሸናፊው ክብሩ ነህና» (ይባላል)፡፡

ذُقْ إِنَّكَ أَنتَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْكَرِيمُ ﴿٤٩﴾

50. «ይህ ያ በእርሱ ትጠራጠሩበት የነበራችሁት ነው» (ይባላሉ)፡፡

إِنَّ هَٰذَا مَا كُنتُم بِهِۦ تَمْتَرُونَ ﴿٥٠﴾

51. ጥንቁቆቹ በእርግጥ በጸጥተኛ መኖሪያ ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلْمُتَّقِينَ فِى مَقَامٍ أَمِينٍ ﴿٥١﴾

52. በአትክልቶችና በምንጮች ውስጥ ናቸው፡፡

فِى جَنَّٰتٍ وَعُيُونٍ ﴿٥٢﴾

53. ፊት ለፊት የተቅጣጩ ኾነው ከስስ ሐርና ከወፍራም ሐር ይለብሳሉ፡፡

يَلْبَسُونَ مِن سُندُسٍ وَإِسْتَبْرَقٍ مُّتَقَٰبِلِينَ ﴿٥٣﴾

54. (ነገሩ) እንደዚሁ ነው፤ ዓይናማዎች የኾኑን ነጫጭ ሴቶችም እናጠናዳቸዋለን፡፡

كَذَٰلِكَ وَزَوَّجْنَٰهُم بِحُورٍ عِينٍ ﴿٥٤﴾

55. በእርሷም ውስጥ የተማመኑ ኾነው፤ ከፍራፍሬ ሁሉ ያዝዛሉ፡፡

يَدْعُونَ فِيهَا بِكُلِّ فَٰكِهَةٍ ءَامِنِينَ ﴿٥٥﴾

56. የፊተኛይቱን ሞት እንጅ (ዳግመኛ) በእርሷ ውስጥ ሞትን አይቀምሱም፡፡ የገሀነምንም ቅጣት (አላህ) ጠበቃቸው፡፡

لَا يَذُوقُونَ فِيهَا ٱلْمَوْتَ إِلَّا ٱلْمَوْتَةَ ٱلْأُولَىٰ ۖ وَوَقَىٰهُمْ عَذَابَ ٱلْجَحِيمِ ﴿٥٦﴾

57. ከጌታህ በኾነ ችሮታ (ጠበቃቸው)፡፡ ይህ እርሱ ታላቅ ዕድል ነው፡፡

فَضْلًا مِّن رَّبِّكَ ۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلْفَوْزُ ٱلْعَظِيمُ ﴿٥٧﴾

58. (ቁርኣኑን) በቋንቋህም ያገራነው (ሕዝቦችህ) ይገነዘቡ ዘንድ ብቻ ነው፡፡

فَإِنَّمَا يَسَّرْنَٰهُ بِلِسَانِكَ لَعَلَّهُمْ يَتَذَكَّرُونَ ﴿٥٨﴾

59. ተጠባበቅም እነርሱ ተጠባባቂዎች ናቸውና፡፡

فَٱرْتَقِبْ إِنَّهُم مُّرْتَقِبُونَ ﴿٥٩﴾

# ሱረቱ አል ጃሲያህ

# سورة الجاثية

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሓ ሚም)፡፡

حمٓ ١

2. የመጽሐፉ መወረድ አሸናፊ ጥበበኛ ከኾነው አላህ ነው፡፡

تَنزِيلُ ٱلۡكِتَٰبِ مِنَ ٱللَّهِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَكِيمِ ٢

3. በሰማያትና በምድር ውስጥ ለምእምናን ሁሉ (ለችሎታው) እርገጠኛ ምልክቶች አልሉ፡፡

إِنَّ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ لَأٓيَٰتٖ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ ٣

4. እናንተንም በመፍጠር ከተንቀሳቃሽም (በምድር ላይ) የሚበትነውን ሁሉ (በመፍጠሩ) ለሚያረጋግጡ ሕዝቦች ተዓምራቶች አልሉ፡፡

وَفِي خَلۡقِكُمۡ وَمَا يَبُثُّ مِن دَآبَّةٍ ءَايَٰتٞ لِّقَوۡمٖ يُوقِنُونَ ٤

5. በሌሊትና መዓልት መተካካትም፣ ከሲሳይም (ከዝናም) አላህ ከሰማይ ባወረደው በርሱም ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው በማድረጉ፣ ነፋሶችንም (በያቅጣጫቸው) በማዘዋወሩ ለሚያውቁ ሕዝቦች ማስረጃዎች አልሉ፡፡

وَٱخۡتِلَٰفِ ٱلَّيۡلِ وَٱلنَّهَارِ وَمَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ مِن رِّزۡقٖ فَأَحۡيَا بِهِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَا وَتَصۡرِيفِ ٱلرِّيَٰحِ ءَايَٰتٞ لِّقَوۡمٖ يَعۡقِلُونَ ٥

6. እነዚህ ባንተ ላይ በውነት የምናነባቸው ሲኾኑ የአላህ ማስረጃዎች ናቸው፡፡ ከአላህና ከማስረጃዎቹም ወዲያ በየትኛው ንግግር ያምናሉ?

تِلۡكَ ءَايَٰتُ ٱللَّهِ نَتۡلُوهَا عَلَيۡكَ بِٱلۡحَقِّۖ فَبِأَيِّ حَدِيثِۭ بَعۡدَ ٱللَّهِ وَءَايَٰتِهِۦ يُؤۡمِنُونَ ٦

7. ውሸታም ኀጢአተኛ ለኾነ ሁሉ ወዮለት፡፡ (ጥፋት ተገባው)፡፡

وَيۡلٞ لِّكُلِّ أَفَّاكٍ أَثِيمٖ ٧

8. የአላህን አንቀጾች በእርሱ ላይ የሚነበቡለት ሲኾኑ ይሰማል፡፡ ከዚያም የኮራ ሲኾን እንዳልሰማት ኾኖ (በክሕደቱ ላይ) ይዘወትራል፡፡ በአሳማሚም ቅጣት አብስረው፡፡

يَسۡمَعُ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِ ثُمَّ يُصِرُّ مُسۡتَكۡبِرٗا كَأَن لَّمۡ يَسۡمَعۡهَاۖ فَبَشِّرۡهُ بِعَذَابٍ أَلِيمٖ ٨

9. ከአንቀጾቻችንም አንዳችን ባወቀ ጊዜ መሳለቂያ አድርጎ ይይዛታል፡፡ እነዚያ ለእነርሱ አዋራጅ ቅጣት አልላቸው፡፡

وَإِذَا عَلِمَ مِنۡ ءَايَٰتِنَا شَيۡـًٔا ٱتَّخَذَهَا هُزُوًاۚ أُوْلَٰٓئِكَ لَهُمۡ عَذَابٞ مُّهِينٞ ٩

10. ከፊታቸውም ገሀነም አልለች፡፡ የሰበሰቡትም ሀብት ከእነርሱ ላይ ምንንም አይመልስላቸውም፡፡ ከአላህ ሌላም ረዳቶች አድርገው የያዙዋቸው (አይጠቅሟቸውም)፡፡ ለእነርሱም ታላቅ ቅጣት አልላቸው፡፡

مِّن وَرَآئِهِمۡ جَهَنَّمُۖ وَلَا يُغۡنِي عَنۡهُم مَّا كَسَبُواْ شَيۡـٔٗا وَلَا مَا ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَوۡلِيَآءَۖ وَلَهُمۡ عَذَابٌ عَظِيمٌ ١٠

11. ይህ (ቁርኣን) መሪ ነው፡፡ እነዚያም በጌታቸው አንቀጾች የካዱት ለእነርሱ ከብርቱ ቅጣት የኾነ አሳማሚ ስቃይ አልላቸው፡፡

هَٰذَا هُدٗىۖ وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِ رَبِّهِمۡ لَهُمۡ عَذَابٞ مِّن رِّجۡزٍ أَلِيمٌ ١١

12. አላህ ያ ባሕርን በውስጡ ታንኳዎች በፈቃዱ እንዲንሻለሉበት ከችሮታውም እንድትፈልጉበት እንድታመሰግኑትም ለእናንተ የገራላችሁ ነው፡፡

۞ٱللَّهُ ٱلَّذِي سَخَّرَ لَكُمُ ٱلۡبَحۡرَ لِتَجۡرِيَ ٱلۡفُلۡكُ فِيهِ بِأَمۡرِهِۦ وَلِتَبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِهِۦ وَلَعَلَّكُمۡ تَشۡكُرُونَ ١٢

13. ለናንተም በሰማያት ያለውንና በምድርም ያለውን ሁሉ በመላ ከእርሱ ሲኾን የገራላችሁ ነው፡፡ በዚህ ለሚያስተነትኑ ሕዝቦች ተዓምራት አልለበት፡፡

وَسَخَّرَ لَكُم مَّا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا مِّنۡهُۚ إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَأٓيَٰتٖ لِّقَوۡمٖ يَتَفَكَّرُونَ ١٣

14. ለእነዚያ ለአመኑት ሰዎች (ምሕረት አድርጉ) በላቸው፡፡ ለእነዚያ የአላህን ቀኖች ለማይፈሩት ይምራሉና፡፡ ሕዝቦችን ይሠሩት በነበሩት ነገር ይመነዳ ዘንድ (ምሕረት አድርጉ በላቸው)፡፡

قُل لِّلَّذِينَ ءَامَنُواْ يَغۡفِرُواْ لِلَّذِينَ لَا يَرۡجُونَ أَيَّامَ ٱللَّهِ لِيَجۡزِيَ قَوۡمَۢا بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ١٤

15. መልካምን የሠራ ሰው ለነፍሱ ነው፡፡ ያከፋም ሰው በእርሷ ላይ ነው፡፡ ከዚያም ወደ ጌታችሁ ትመለሳላችሁ፡፡

مَنۡ عَمِلَ صَٰلِحٗا فَلِنَفۡسِهِۦۖ وَمَنۡ أَسَآءَ فَعَلَيۡهَاۖ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّكُمۡ تُرۡجَعُونَ ١٥

16. ለእስራኤል ልጆችም መጽሐፍንና ሕግን፣ ነቢይነትንም በእርግጥ ሰጠናቸው፡፡ ከመልካም ሲሳዮችም ለገስንላቸው፡፡ በዓለማት ላይም አበለጥናቸው፡፡

وَلَقَدۡ ءَاتَيۡنَا بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحُكۡمَ وَٱلنُّبُوَّةَ وَرَزَقۡنَٰهُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ وَفَضَّلۡنَٰهُمۡ عَلَى ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٦

17. ከትዕዛዝም ግልጾችን ሰጠናቸው፡፡ ዕውቀቱም ከመጣላቸው በኋላ በመካከላቸው ለምቀኝነት እንጅ ለሌላ አልተለያዩም፡፡ ጌታህ በትንሣኤ ቀን በዚያ በእርሱ ይለያዩበት በነበሩት ነገር በመካከላቸው በእርግጥ ይፈርዳል፡፡

وَءَاتَيۡنَٰهُم بَيِّنَٰتٖ مِّنَ ٱلۡأَمۡرِۖ فَمَا ٱخۡتَلَفُوٓاْ إِلَّا مِنۢ بَعۡدِ مَا جَآءَهُمُ ٱلۡعِلۡمُ بَغۡيَۢا بَيۡنَهُمۡۚ إِنَّ رَبَّكَ يَقۡضِي بَيۡنَهُمۡ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ فِيمَا كَانُواْ فِيهِ يَخۡتَلِفُونَ ١٧

18. ከዚያም ከነገሩ (ከሃይማኖት) በትክክለኛይቱ ሕግ ላይ አደረግንህ፡፡ ስለዚህ ተከተላት፡፡ የእነዚያንም የማያውቁትን ሕዝቦች ዝንባሌዎች አትከተል፡፡

ثُمَّ جَعَلۡنَٰكَ عَلَىٰ شَرِيعَةٖ مِّنَ ٱلۡأَمۡرِ فَٱتَّبِعۡهَا وَلَا تَتَّبِعۡ أَهۡوَآءَ ٱلَّذِينَ لَا يَعۡلَمُونَ ١٨

19. እነርሱ ከአላህ (ቅጣት) ምንንም ከአንተ አይገፈትሩልህምና፡፡ በደለኞም ከፊላቸው የከፊሉ ረዳቶች ናቸው፡፡ አላህም የጥንቁቆቹ ረዳት ነው፡፡

إِنَّهُمْ لَن يُغْنُواْ عَنكَ مِنَ ٱللَّهِ شَيْـًٔاۚ وَإِنَّ ٱلظَّٰلِمِينَ بَعْضُهُمْ أَوْلِيَآءُ بَعْضٍۖ وَٱللَّهُ وَلِيُّ ٱلْمُتَّقِينَ ١٩

20. ይህ (ቁርአን) ለሰዎች የልብ ብርሃኖች ነው፡፡ ለሚያረጋግጡም ሕዝቦች መሪና እዝነት ነው፡፡

هَٰذَا بَصَٰٓئِرُ لِلنَّاسِ وَهُدًى وَرَحْمَةٌ لِّقَوْمٍ يُوقِنُونَ ٢٠

21. እነዚያ ኀጢአቶችን የሠሩ ሕይወታቸውም ሞታቸውም ትክክል ሲኾን እንደእነዚያ እንደ አመኑትና መልካሞችን እንደሠሩት ልናደርጋቸው ይጠረጥራሉን? (አይጠርጥሩ)፡፡ የሚፈርዱት ምንኛ ከፋ!

أَمْ حَسِبَ ٱلَّذِينَ ٱجْتَرَحُواْ ٱلسَّيِّـَٔاتِ أَن نَّجْعَلَهُمْ كَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ سَوَآءً مَّحْيَاهُمْ وَمَمَاتُهُمْۚ سَآءَ مَا يَحْكُمُونَ ٢١

22. አላህም ሰማያትንና ምድርን (ለችሎታው እንደሚያመለክትባቸውና) ነፍስም ሁሉ በሠራችው ሥራ ትምመነዳ ዘንድ በትክክል ፈጠረ፡፡ እነርሱም አይበደሉም፡፡

وَخَلَقَ ٱللَّهُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ بِٱلْحَقِّ وَلِتُجْزَىٰ كُلُّ نَفْسٍۭ بِمَا كَسَبَتْ وَهُمْ لَا يُظْلَمُونَ ٢٢

23. ዝንባሌውን አምላኩ አድርጎ የያዘውን፣ አላህም ከዕውቀት ጋር ያጠመመውን፣ በጆሮውና በልቡ ላይም ያተመበትን፣ በዓይኑም ላይ ሺፋን ያደረገበትን ሰው አየህን! ታዲያ ከአላህ በኋላ የሚያቀናው ማነው? አትገሠጹምን?

أَفَرَءَيْتَ مَنِ ٱتَّخَذَ إِلَٰهَهُۥ هَوَىٰهُ وَأَضَلَّهُ ٱللَّهُ عَلَىٰ عِلْمٍ وَخَتَمَ عَلَىٰ سَمْعِهِۦ وَقَلْبِهِۦ وَجَعَلَ عَلَىٰ بَصَرِهِۦ غِشَٰوَةً فَمَن يَهْدِيهِ مِنۢ بَعْدِ ٱللَّهِۚ أَفَلَا تَذَكَّرُونَ ٢٣

24. እርሷም (ሕይወት) የቅርቢቱ ሕይወታችን እንጅ ሌላ አይደለችም፡፡ «እንሞታለን፤ ሕያውም እንኾናለን፡፡ ከጊዜም (ማለፍ) በስተቀር ሌላ አያጠፋንም» አሉ፡፡ ለእነርሱም በዚህ (በሚሉት) ምንም ዕውቀት የላቸውም፡፡ እነርሱ የሚጠራጠሩ እንጅ ሌላ አይደሉም፡፡

وَقَالُواْ مَا هِىَ إِلَّا حَيَاتُنَا ٱلدُّنْيَا نَمُوتُ وَنَحْيَا وَمَا يُهْلِكُنَآ إِلَّا ٱلدَّهْرُۚ وَمَا لَهُم بِذَٰلِكَ مِنْ عِلْمٍۖ إِنْ هُمْ إِلَّا يَظُنُّونَ ٢٤

25. አንቀጾቻችንም ግልጾች ኾነው በእነርሱ ላይ በተነበቡላቸው ጊዜ ክርክራቸው «እውነተኞች እንደ ኾናችሁ አባቶቻችንን አምጡ» ማለት እንጅ ሌላ አልነበረም፡፡

وَإِذَا تُتْلَىٰ عَلَيْهِمْ ءَايَٰتُنَا بَيِّنَٰتٍ مَّا كَانَ حُجَّتَهُمْ إِلَّآ أَن قَالُواْ ٱئْتُواْ بِـَٔابَآئِنَآ إِن كُنتُمْ صَٰدِقِينَ ٢٥

26. «አላህ ሕያው ያደርጋችኋል፤ ከዚያም ይገድላችኋል፣ ከዚያም ወደ ትንሣኤ ቀን ይሰበስባችኋል፡፡ በእርሱ ጥርጥር የለበትም፡፡ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች አያውቁም» በላቸው፡፡

قُلِ ٱللَّهُ يُحْيِيكُمْ ثُمَّ يُمِيتُكُمْ ثُمَّ يَجْمَعُكُمْ إِلَىٰ يَوْمِ ٱلْقِيَٰمَةِ لَا رَيْبَ فِيهِ وَلَٰكِنَّ أَكْثَرَ ٱلنَّاسِ لَا يَعْلَمُونَ ٢٦

27. የሰማያትና የምድር ግዛት የአላህ ብቻ ነው፡፡ ሰዓቲቱም በምትቆምበት ቀን ያን ጊዜ አጥፊዎች ሁሉ ይከስራሉ፡፡

وَلِلَّهِ مُلْكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِۚ وَيَوْمَ تَقُومُ ٱلسَّاعَةُ يَوْمَئِذٍ يَخْسَرُ ٱلْمُبْطِلُونَ ٢٧

28. ሕዝብንም ሁሉ ተንበርካኪ ኾና ታያታለህ፡፡ ሕዝብ ሁሉ ወደ መጽሐፏ ትጥጠራለች፡፡ «ዛሬ ትሠሩት የነበራችሁትን ነገር ትመነዳላችሁ» (ይባላሉ)፡፡

وَتَرَىٰ كُلَّ أُمَّةٍ جَاثِيَةً ۚ كُلُّ أُمَّةٍ تُدْعَىٰٓ إِلَىٰ كِتَـٰبِهَا ٱلْيَوْمَ تُجْزَوْنَ مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ۝٢٨

29. ይህ መጽሐፋችን ነው፡፡ በእናንተ ላይ በእውነት ይናገራል፡፡ እኛ ያንን ትሠሩት የነበራችሁትን እናስገለብጥ ነበርን (ይባላሉ)፡፡

هَـٰذَا كِتَـٰبُنَا يَنطِقُ عَلَيْكُم بِٱلْحَقِّ ۚ إِنَّا كُنَّا نَسْتَنسِخُ مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ۝٢٩

30. እነዚያ ያመኑትና መልካሞችን የሠሩትማ ጌታቸው በእዝነቱ ውስጥ ያገባቸዋል፡፡ ይህ እርሱ ግልጽ የኾነ ማግኘት ነው፡፡

فَأَمَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَعَمِلُوا۟ ٱلصَّـٰلِحَـٰتِ فَيُدْخِلُهُمْ رَبُّهُمْ فِى رَحْمَتِهِۦ ۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلْفَوْزُ ٱلْمُبِينُ ۝٣٠

31. እነዚያም የካዱትማ (ለእነርሱ ይባላሉ) «አንቀጾቼ በእናንተ ላይ ይነበቡ አልነበሩምን? ኮራችሁም፡፡ ከሓዲዎች ሕዝቦችም ነበራችሁ፡፡»

وَأَمَّا ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ أَفَلَمْ تَكُنْ ءَايَـٰتِى تُتْلَىٰ عَلَيْكُمْ فَٱسْتَكْبَرْتُمْ وَكُنتُمْ قَوْمًا مُّجْرِمِينَ ۝٣١

32. «የአላህ ቀጠሮ እውነት ነው፡፡ ሰዓቲቱም በእርሷ (መምጣት) ጥርጥር የለም፡፡» በተባለ ጊዜም «ሰዓቲቱ ምን እንደ ኾነች አናውቅም፡፡ መጠራጠርን የምንጠራጠር እንጅ ሌላ አይደለንም፡፡ እኛም አረጋጋጮች አይደለንም» አላችሁ፡፡

وَإِذَا قِيلَ إِنَّ وَعْدَ ٱللَّهِ حَقٌّ وَٱلسَّاعَةُ لَا رَيْبَ فِيهَا قُلْتُم مَّا نَدْرِى مَا ٱلسَّاعَةُ إِن نَّظُنُّ إِلَّا ظَنًّا وَمَا نَحْنُ بِمُسْتَيْقِنِينَ ۝٣٢

33. የሠሩዋቸውም ኀጢአቶች ለእነርሱ ይገለጹላቸዋል፡፡ ያም በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩት ቅጣት በእነርሱ ላይ ይወርድባቸዋል፡፡

وَبَدَا لَهُمْ سَيِّـَٔاتُ مَا عَمِلُوا۟ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُوا۟ بِهِۦ يَسْتَهْزِءُونَ ۝٣٣

34. «ይህንንም ቀናችሁን መገናኘትን እንደ ረሳችሁ ዛሬ እንረሳችኋለን፡፡ (እንተዋችኋለን)፡፡ መኖሪያችሁም እሳት ናት፡፡ ለእናንተም ከረዳቶች ምንም የላችሁም» ይባላል፡፡

وَقِيلَ ٱلْيَوْمَ نَنسَىٰكُمْ كَمَا نَسِيتُمْ لِقَآءَ يَوْمِكُمْ هَـٰذَا وَمَأْوَىٰكُمُ ٱلنَّارُ وَمَا لَكُم مِّن نَّـٰصِرِينَ ۝٣٤

35. ይህ እናንተ የአላህን አንቀጾች መቀለጃ አድርጋችሁ በመያዛችሁና ቅርቢቱም ሕይወት ስለአታለለቻችሁ ነው፤ (ይባላሉ)፡፡ ዛሬ ከእርሷ አይወጥጡም፤ እነርሱም በወቀሳ አይታለፉም፡፡

ذَٰلِكُم بِأَنَّكُمُ ٱتَّخَذْتُمْ ءَايَـٰتِ ٱللَّهِ هُزُوًا وَغَرَّتْكُمُ ٱلْحَيَوٰةُ ٱلدُّنْيَا ۚ فَٱلْيَوْمَ لَا يُخْرَجُونَ مِنْهَا وَلَا هُمْ يُسْتَعْتَبُونَ ۝٣٥

36. ምስጋናም ለአላህ ለሰማያት ጌታ ለምድርም ጌታ ለዓለማት ጌታ የተገባው ነው፡፡

فَلِلَّهِ ٱلْحَمْدُ رَبِّ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَرَبِّ ٱلْأَرْضِ رَبِّ ٱلْعَـٰلَمِينَ ۝٣٦

37. ኩራትም በሰማያትም በምድርም ለእርሱ ብቻ ነው፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

وَلَهُ ٱلْكِبْرِيَآءُ فِى ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۖ وَهُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ۝٣٧

# ሱረቱ አል አህቃፍ

# سورة الأحقاف

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ሐ.መ (ሓ ሚም)::

حمٓ ١

2. የመጽሐፉ መወረድ አሸናፊ ጥበበኛ ከኾነው አላህ ነው::

تَنزِيلُ ٱلۡكِتَٰبِ مِنَ ٱللَّهِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَكِيمِ ٢

3. ሰማያትንና ምድርን በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ በምርና የተወሰነ ጊዜንም በመለካት እንጅ (ለቀልድ) አልፈጠርናቸውም:: እነዚያ የካዱትም ከተስፈራሩት ነገር (ትተው) ዘዋሪዎች ናቸው::

مَا خَلَقۡنَا ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَآ إِلَّا بِٱلۡحَقِّ وَأَجَلٖ مُّسَمّٗىۚ وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ عَمَّآ أُنذِرُواْ مُعۡرِضُونَ ٣

4. «ከአላህ ሌላ የምትግገዟቸውን አያችሁን? ከምድር ምንን እንደ ፈጠሩ አሳዩኝ:: ወይም በሰማያት ለእነርሱ (ከአላህ ጋር) መጋራት አላቸውን? (ያማልዱናል በማለታችሁ) እውነተኞች እንደ ኾናችሁ ከዚህ (ቁርኣን) በፊት የኾነን መጽሐፍ ወይም ከዕውቀት የኾነ ቅርስን አምጡልኝ» በላቸው::

قُلۡ أَرَءَيۡتُم مَّا تَدۡعُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ أَرُونِي مَاذَا خَلَقُواْ مِنَ ٱلۡأَرۡضِ أَمۡ لَهُمۡ شِرۡكٞ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِۖ ٱئۡتُونِي بِكِتَٰبٖ مِّن قَبۡلِ هَٰذَآ أَوۡ أَثَٰرَةٖ مِّنۡ عِلۡمٍ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٤

5. እስከ ትንሣኤ ቀን ድረስም ለእርሱ የማይመልስለትን (ጣዖት) ከአላህ ሌላ ከሚጠራ ሰው ይበልጥ የተሳሳተ ማነው? እነርሱም ከጥሪያቸው ዘንጊዎች ናቸው::

وَمَنۡ أَضَلُّ مِمَّن يَدۡعُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ مَن لَّا يَسۡتَجِيبُ لَهُۥٓ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ وَهُمۡ عَن دُعَآئِهِمۡ غَٰفِلُونَ ٥

6. ሰዎችም በተሰበሰቡ ጊዜ (ጣዖቶቹ) ለእነርሱ ጠላቶች ይኾናሉ:: (እነሱን) መገዛታቸውንም ከሓዲዎች ይኾናሉ::

وَإِذَا حُشِرَ ٱلنَّاسُ كَانُواْ لَهُمۡ أَعۡدَآءٗ وَكَانُواْ بِعِبَادَتِهِمۡ كَٰفِرِينَ ٦

7. በእነርሱም ላይ አንቀጾቻችን ግልጾች ኾነው በተነበቡ ጊዜ እነዚያ እውነቱን በመጣላቸው ጊዜ የካዱትን «ይህ ግልጽ ድግምት ነው» አሉ::

وَإِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتُنَا بَيِّنَٰتٖ قَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لِلۡحَقِّ لَمَّا جَآءَهُمۡ هَٰذَا سِحۡرٞ مُّبِينٌ ٧

8. ይልቁንም ቀጠፈው ይላሉን? «ብቀጥፈው ለእኔ ከአላህ (ቅጣት ለማዳን) ምንንም አትችሉም:: እርሱ ያንን በእርሱ የምትቀባዥሩበትን ዐዋቂ ነው:: በእኔና በእናንተ መካከል መስካሪ በእርሱ በቃ:: እርሱም መሓሪው አዛኙ ነው» በላቸው::

أَمۡ يَقُولُونَ ٱفۡتَرَىٰهُۖ قُلۡ إِنِ ٱفۡتَرَيۡتُهُۥ فَلَا تَمۡلِكُونَ لِي مِنَ ٱللَّهِ شَيۡـًٔاۖ هُوَ أَعۡلَمُ بِمَا تُفِيضُونَ فِيهِۚ كَفَىٰ بِهِۦ شَهِيدَۢا بَيۡنِي وَبَيۡنَكُمۡۖ وَهُوَ ٱلۡغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ٨

9. «ከመልክተኞች ብጤ የሌለኝ አይደለሁም፡፡ በእኔም በእናንተም ምን እንደሚሥሠራም አላውቅም፡፡ ወደእኔ የሚወረደውን እንጅ ሌላን አልከተልም፡፡ እኔም ግልጽ አስፈራሪ እንጅ ሌላ አይደለሁም» በላቸው፡፡

قُلْ مَا كُنتُ بِدْعًا مِّنَ ٱلرُّسُلِ وَمَآ أَدْرِى مَا يُفْعَلُ بِى وَلَا بِكُمْۖ إِنْ أَتَّبِعُ إِلَّا مَا يُوحَىٰٓ إِلَىَّ وَمَآ أَنَا۠ إِلَّا نَذِيرٌ مُّبِينٌ ﴿٩﴾

10. (ሙሐመድ ሆይ!) በላቸው «እስቲ ንገሩኝ፤ (ቁርኣኑ) ከአላህ ዘንድ ቢኾን፡፡ በእርሱም ብትክዱ፣ ከእስራኤል ልጆችም መስካሪ በብጤው (በእርሱ) ላይ ቢመሰክር፣ ቢያምንም፣ (ከእምነት) ብትኮሩም፣ (በዳይ አትኾኑምን?)» አላህ በእርግጥ በደለኞችን ሕዝቦች አያቀናም፡፡

قُلْ أَرَءَيْتُمْ إِن كَانَ مِنْ عِندِ ٱللَّهِ وَكَفَرْتُم بِهِۦ وَشَهِدَ شَاهِدٌ مِّنۢ بَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ عَلَىٰ مِثْلِهِۦ فَـَٔامَنَ وَٱسْتَكْبَرْتُمْۖ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿١٠﴾

11. እነዚያንም የካዱት ሰዎች ስለእነዚያ ስለ አመኑት ሰዎች (እምነቱ) «መልካም ነገር በኾነ ኖሮ ወደርሱ ባልቀደሙን ነበር» አሉ፡፡ በእርሱም ባልተመሩ ጊዜ «ይህ (ቁርኣን) ጥንታዊ ቅጥፈት ነው» ይላሉ፡፡

وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ لِلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ لَوْ كَانَ خَيْرًا مَّا سَبَقُونَآ إِلَيْهِۚ وَإِذْ لَمْ يَهْتَدُوا۟ بِهِۦ فَسَيَقُولُونَ هَٰذَآ إِفْكٌ قَدِيمٌ ﴿١١﴾

12. ከበፊቱም የሙሳ መጽሐፍ መሪና ጸጋ ሲኾን አለለ፡ ፡ ይህም እነዚያን የበደሉትን ሊያስፈራራ በዐረብኛ ቋንቋ ሲኾን (የፊቶቹን መጻሕፍት) አረጋጋጭ መጽሐፍ ነው፡፡ ለበጎ አድራጊዎችም ብስራት ነው፡፡

وَمِن قَبْلِهِۦ كِتَٰبُ مُوسَىٰٓ إِمَامًا وَرَحْمَةًۚ وَهَٰذَا كِتَٰبٌ مُّصَدِّقٌ لِّسَانًا عَرَبِيًّا لِّيُنذِرَ ٱلَّذِينَ ظَلَمُوا۟ وَبُشْرَىٰ لِلْمُحْسِنِينَ ﴿١٢﴾

13. እነዚያ «ጌታችን አላህ ነው» ያሉ፣ ከዚያም ቀጥ ያሉ በነርሱ ላይ ፍርሃት የለባቸውም፡፡ እነርሱም አያዝኑም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ قَالُوا۟ رَبُّنَا ٱللَّهُ ثُمَّ ٱسْتَقَٰمُوا۟ فَلَا خَوْفٌ عَلَيْهِمْ وَلَا هُمْ يَحْزَنُونَ ﴿١٣﴾

14. እነዚያ የገነት ጓዶች ናቸው፡፡ በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ሲኾኑ፡፡ በዚያ ይሠሩት በነበሩት ምክንያት ታላቅን ምንዳ (ይምመነዳሉ)፡፡

أُو۟لَٰٓئِكَ أَصْحَٰبُ ٱلْجَنَّةِ خَٰلِدِينَ فِيهَا جَزَآءًۢ بِمَا كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ﴿١٤﴾

15. ሰውንም በወላጆቹ በጎ መዋልን በጥብቅ አዘዝነው፡ ፡ እናቱ በችግር ላይ ኾና አረገዘችው፡፡ በችግርም ወለደችው፡፡ እርግዝናውና ከጡት መለያውም ሰላሳ ወር ነው፡፡ ጥንካሬውንም ወቅት በደረሰ ጊዜ (ከዚያ አልፎ) አርባ ዓመትንም በደረሰ ጊዜ «ጌታዬ ሆይ! ያችን በእኔ ላይና በወላጆቼ ላይ የለገስካትን ጸጋህን እንዳመሰግን የምትወደውንም መልካም ሥራ እንድሠራ ምራኝ፡፡ ዘሮቼንም ለእኔ አብጅልኝ፡፡ እኔ ወዳንተ ተመለስኩ፡፡ እኔም ከሙስሊሞ ነኝ» አለ፡፡

وَوَصَّيْنَا ٱلْإِنسَٰنَ بِوَٰلِدَيْهِ إِحْسَٰنًاۖ حَمَلَتْهُ أُمُّهُۥ كُرْهًا وَوَضَعَتْهُ كُرْهًاۖ وَحَمْلُهُۥ وَفِصَٰلُهُۥ ثَلَٰثُونَ شَهْرًاۚ حَتَّىٰٓ إِذَا بَلَغَ أَشُدَّهُۥ وَبَلَغَ أَرْبَعِينَ سَنَةً قَالَ رَبِّ أَوْزِعْنِىٓ أَنْ أَشْكُرَ نِعْمَتَكَ ٱلَّتِىٓ أَنْعَمْتَ عَلَىَّ وَعَلَىٰ وَٰلِدَىَّ وَأَنْ أَعْمَلَ صَٰلِحًا تَرْضَىٰهُ وَأَصْلِحْ لِى فِى ذُرِّيَّتِىٓۖ إِنِّى تُبْتُ إِلَيْكَ وَإِنِّى مِنَ ٱلْمُسْلِمِينَ ﴿١٥﴾

16. እነዚህ (ይህንን ባዮች) በገነት ጓዶች ውስጥ ሲኾኑ እነዚያ ከሠሩት ሥራ መልካሙን ከነሱ የምንቀበላቸውና ከኀጢአቶቻቸውም የምናልፋቸው ናቸው፡፡ ያንን ተስፋ ይሰሰጡት የነበሩትን እውነተኛ ቀጠሮ (እንሞላላቸዋለን)፡፡

أُو۟لَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ نَتَقَبَّلُ عَنْهُمْ أَحْسَنَ مَا عَمِلُوا۟ وَنَتَجَاوَزُ عَن سَيِّـَٔاتِهِمْ فِىٓ أَصْحَٰبِ ٱلْجَنَّةِۖ وَعْدَ ٱلصِّدْقِ ٱلَّذِى كَانُوا۟ يُوعَدُونَ ﴿١٦﴾

17. ያንንም ለወላጆቹ «ፎህ ለእናንተ ከእኔ በፊት የከፍል ዘመናት ሰዎች (ሳይወጡ) በእርግጥ ያለፉ ሲኾኑ (ከመቃብር) እንድወጥጣ ታስፈራሩኛላችሁን?» ያለውን ሁለቱም (ወላጆቹ) አላህን የሚለምኑ ሲኾኑ (ባታምን) «ወዮልህ፡፡ እመን፡፡ የአላህ ቀጠሮ እርግጠኛ ነው፡፡»(ሲሉት) «ይህ የፊተኞቹ ሰዎች ጽሑፍ ተረቶች እንጅ ሌላ አይደለም» የሚለውንም ሰው (አስታውስ)፡፡

وَٱلَّذِى قَالَ لِوَٰلِدَيۡهِ أُفّٖ لَّكُمَآ أَتَعِدَانِنِيٓ أَنۡ أُخۡرَجَ وَقَدۡ خَلَتِ ٱلۡقُرُونُ مِن قَبۡلِي وَهُمَا يَسۡتَغِيثَانِ ٱللَّهَ وَيۡلَكَ ءَامِنۡ إِنَّ وَعۡدَ ٱللَّهِ حَقّٞ فَيَقُولُ مَا هَٰذَآ إِلَّآ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ﴿١٧﴾

18. እነዚህ እነዚያ ከጋኔንም ከሰውም ከእነርሱ በፊት ካለፉት ሕዝቦች ጋር ቃሉ በእነርሱ ላይ የተረጋገጠባቸው ናቸው፡፡ እነርሱ ከሳሪዎች ነበሩና፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ حَقَّ عَلَيۡهِمُ ٱلۡقَوۡلُ فِيٓ أُمَمٖ قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلِهِم مِّنَ ٱلۡجِنِّ وَٱلۡإِنسِۖ إِنَّهُمۡ كَانُواْ خَٰسِرِينَ ﴿١٨﴾

19. ለሁሉም ከሠሩት ሥራ ደረጃዎች አልሏቸው፡፡ ሥራዎቻቸውንም ይሞላላቸው ዘንድ (ይህንን መነዳቸው) እነርሱም አይበደሉም፡፡

وَلِكُلّٖ دَرَجَٰتٞ مِّمَّا عَمِلُواْۖ وَلِيُوَفِّيَهُمۡ أَعۡمَٰلَهُمۡ وَهُمۡ لَا يُظۡلَمُونَ ﴿١٩﴾

20. እነዚያም የካዱት በእሳት ላይ በሚጋፈጡ ቀን «ጣፋጮቻችሁን በአነስተኛይቱ ሕይወታችሁ አሳለፋችሁ፡፡ በእርሷም ተጣቀማችሁ፡፡ ስለዚህ በምድር ላይ ያለ አግባብ ትኮሩ በነበራችሁትና ታምጹ በነበራችሁት ዛሬ የውርደትን ቅጣት ትምመነዳላችሁ» (ይባላሉ)፡፡

وَيَوۡمَ يُعۡرَضُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ عَلَى ٱلنَّارِ أَذۡهَبۡتُمۡ طَيِّبَٰتِكُمۡ فِي حَيَاتِكُمُ ٱلدُّنۡيَا وَٱسۡتَمۡتَعۡتُم بِهَا فَٱلۡيَوۡمَ تُجۡزَوۡنَ عَذَابَ ٱلۡهُونِ بِمَا كُنتُمۡ تَسۡتَكۡبِرُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ بِغَيۡرِ ٱلۡحَقِّ وَبِمَا كُنتُمۡ تَفۡسُقُونَ ﴿٢٠﴾

21. የዓድንም ወንድም (ሁድን) ሕዝቦቹን በአሕቃፍ ባስጠነቀቀ ጊዜ አውሳለቸው፡፡ በስተፊቱና በስተኋላውም ብዙ አስፈራሪዎች በእርግጥ አልፈዋል፡፡ «ከአላህ በስተቀር አትግገዙ እኔ በእናንተ ላይ የከባድ ቀንን ቅጣት እፈራላችኋለሁና» በማለት (ባሰጠነቀቀ ጊዜ)፡፡

۞وَٱذۡكُرۡ أَخَا عَادٍ إِذۡ أَنذَرَ قَوۡمَهُۥ بِٱلۡأَحۡقَافِ وَقَدۡ خَلَتِ ٱلنُّذُرُ مِنۢ بَيۡنِ يَدَيۡهِ وَمِنۡ خَلۡفِهِۦٓ أَلَّا تَعۡبُدُوٓاْ إِلَّا ٱللَّهَ إِنِّيٓ أَخَافُ عَلَيۡكُمۡ عَذَابَ يَوۡمٍ عَظِيمٖ ﴿٢١﴾

22. «ከአማልክቶቻችን ልታዞረን መጣህብን? ከውነተኞቹም እንደኾንክ የምትዝትብንን (ቅጣት) አምጣው» አሉ፡፡

قَالُوٓاْ أَجِئۡتَنَا لِتَأۡفِكَنَا عَنۡ ءَالِهَتِنَا فَأۡتِنَا بِمَا تَعِدُنَآ إِن كُنتَ مِنَ ٱلصَّٰدِقِينَ ﴿٢٢﴾

23. «ዕውቀቱ አላህ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ ያን በእርሱ የተላክሁበትንም አደርስላችኋለሁ፡፡ ግን እኔ የምትሳሳቱ ሕዝቦች ኾናችሁ አያችኋለሁ» አላቸው፡፡

قَالَ إِنَّمَا ٱلۡعِلۡمُ عِندَ ٱللَّهِ وَأُبَلِّغُكُم مَّآ أُرۡسِلۡتُ بِهِۦ وَلَٰكِنِّيٓ أَرَىٰكُمۡ قَوۡمٗا تَجۡهَلُونَ ﴿٢٣﴾

24. ሸለቆዎቻቸውን ተቅጣጪ አግዳሚ ደመና ኾኖ ባዩትም ጊዜ «ይህ አዝናቢያችን የኾነ ደመና ነው» አሉ፡ ፡ (ሁድም) «አይደለም፤ እርሱ ያ በእርሱ የተቻኮላችሁበት መዐት ነው፡፡ በውስጧ አሳማሚ ስቃይ ያለባት ነፋስ ናት፡፡

فَلَمَّا رَأَوۡهُ عَارِضٗا مُّسۡتَقۡبِلَ أَوۡدِيَتِهِمۡ قَالُواْ هَٰذَا عَارِضٞ مُّمۡطِرُنَاۚ بَلۡ هُوَ مَا ٱسۡتَعۡجَلۡتُم بِهِۦۖ رِيحٞ فِيهَا عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿٢٤﴾

25. በጌታዋ ትዕዛዝ አንዳቹን ሁሉ ታጠፋለች» (አላቸው)፡፡ ከመኖሪያዎቻቸውም በስተቀር ምንም የማይታዩ ኾኑ፡፡ እንደዚሁ አመጸኞችን ሕዝቦች ሁሉ እንቀጣለን፡፡

تُدَمِّرُ كُلَّ شَيۡءِۭ بِأَمۡرِ رَبِّهَا فَأَصۡبَحُواْ لَا يُرَىٰٓ إِلَّا مَسَٰكِنُهُمۡۚ كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡمُجۡرِمِينَ ٢٥

26. በዚያም እናንተን በእርሱ ባላስመቸንበት (ድሎት) በእርግጥ አስመቸናቸው፡፡ ለእነርሱም መስሚያንና ማያዎችን፣ ልቦችንም አደረግንላቸው፡፡ ግን መስሚያቸውና ማያዎቻቸው፣ ልቦቻቸውም ከእነሱ ምንም አልጠቀሟቸውም፡፡ በአላህ አንቀጾች ይክዱ ነበሩና፡፡ በእነርሱም ላይ ያ በእርሱ ይሳለቁበት የነበሩት ቅጣት ወረደባቸው፡፡

وَلَقَدۡ مَكَّنَّٰهُمۡ فِيمَآ إِن مَّكَّنَّٰكُمۡ فِيهِ وَجَعَلۡنَا لَهُمۡ سَمۡعٗا وَأَبۡصَٰرٗا وَأَفۡـِٔدَةٗ فَمَآ أَغۡنَىٰ عَنۡهُمۡ سَمۡعُهُمۡ وَلَآ أَبۡصَٰرُهُمۡ وَلَآ أَفۡـِٔدَتُهُم مِّن شَيۡءٍ إِذۡ كَانُواْ يَجۡحَدُونَ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِ وَحَاقَ بِهِم مَّا كَانُواْ بِهِۦ يَسۡتَهۡزِءُونَ ٢٦

27. ከከተሞችም እነዚያን በአካባቢያችሁ የነበሩትን በእርግጥ አጠፉን (ከክሕደታቸው) ይመለሱም ዘንድ አስረጂዎችን መላለስን፡፡

وَلَقَدۡ أَهۡلَكۡنَا مَا حَوۡلَكُم مِّنَ ٱلۡقُرَىٰ وَصَرَّفۡنَا ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّهُمۡ يَرۡجِعُونَ ٢٧

28. እነዚያም መቃረቢያ ይኾኑ ዘንድ ከአላህ ሌላ አማልክት አድርገው የያዙዋቸው አይረዷቸውም ኖሯልን? በእርግጥ ከነሱ ራቁ፡፡ ይህም ውሸታቸውና (በልማድ) ይቀጥፉት የነበሩት ነው፡፡

فَلَوۡلَا نَصَرَهُمُ ٱلَّذِينَ ٱتَّخَذُواْ مِن دُونِ ٱللَّهِ قُرۡبَانًا ءَالِهَةَۢۖ بَلۡ ضَلُّواْ عَنۡهُمۡۚ وَذَٰلِكَ إِفۡكُهُمۡ وَمَا كَانُواْ يَفۡتَرُونَ ٢٨

29. ከጋኔን የኾኑን ጭፍሮች ቁርኣንን የሚያዳምጡ ሲኾኑ ወዳንተ ባዞርን ጊዜም (አስታውስ)፡፡ በተጣዱትም ጊዜ ዝም ብላችሁ አዳምጡ ተባባሉ፡፡ በተጨረሰም ጊዜ አስጠንቃቂዎች ኾነው ወደ ሕዝቦቻቸው ተመለሱ፡፡

وَإِذۡ صَرَفۡنَآ إِلَيۡكَ نَفَرٗا مِّنَ ٱلۡجِنِّ يَسۡتَمِعُونَ ٱلۡقُرۡءَانَ فَلَمَّا حَضَرُوهُ قَالُوٓاْ أَنصِتُواْۖ فَلَمَّا قُضِيَ وَلَّوۡاْ إِلَىٰ قَوۡمِهِم مُّنذِرِينَ ٢٩

30. አሉም «ሕዝቦቻችን ሆይ! እኛ ከሙሳ በኋላ የተወረደን መጽሐፍ በፊቱ ያለውን (መጽሐፍ) የሚያረጋግጥ ወደ እውነትና ወደ ቀጥተኛ መንገድ የሚመራ የኾነን ሰማን፡፡

قَالُواْ يَٰقَوۡمَنَآ إِنَّا سَمِعۡنَا كِتَٰبًا أُنزِلَ مِنۢ بَعۡدِ مُوسَىٰ مُصَدِّقٗا لِّمَا بَيۡنَ يَدَيۡهِ يَهۡدِيٓ إِلَى ٱلۡحَقِّ وَإِلَىٰ طَرِيقٖ مُّسۡتَقِيمٖ ٣٠

31. ወገኖቻችን ሆይ! የአላህን ጠሪ ተቀበሉ፡፡ በእርሱም እመኑ፡፡ (አላህ) ከኀጢአቶቻችሁ ለእናንተ ይምራልና፡፡ ከአሳማሚ ቅጣትም ያድናችኋልና፡፡

يَٰقَوۡمَنَآ أَجِيبُواْ دَاعِيَ ٱللَّهِ وَءَامِنُواْ بِهِۦ يَغۡفِرۡ لَكُم مِّن ذُنُوبِكُمۡ وَيُجِرۡكُم مِّنۡ عَذَابٍ أَلِيمٖ ٣١

32. የአላህንም ጠሪ የማይቀበል ሰው በምድር ውስጥ የሚያመልጥ አይደለም፡፡ ከእርሱም ሌላ ለእርሱ ረዳቶች የሉትም፡፡ እነዚያ በግልጽ ስሕተት ውስጥ ናቸው» (አሉ)፡፡

وَمَن لَّا يُجِبۡ دَاعِيَ ٱللَّهِ فَلَيۡسَ بِمُعۡجِزٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَيۡسَ لَهُۥ مِن دُونِهِۦٓ أَوۡلِيَآءُۚ أُوْلَٰٓئِكَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٍ ٣٢

أَوَ لَمۡ يَرَوۡاْ أَنَّ ٱللَّهَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَلَمۡ يَعۡيَ بِخَلۡقِهِنَّ بِقَٰدِرٍ عَلَىٰٓ أَن يُحۡـِۧيَ ٱلۡمَوۡتَىٰۚ بَلَىٰٓۚ إِنَّهُۥ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٣٣

33. ያ ሰማያትንና ምድርን የፈጠረ እነርሱንም በመፍጠሩ ያልደከመው አላህ ሙታንን ሕያው በማድረግ ላይ ቻይ መኾኑን አላስተዋሉምን? (በማስነሳት) ቻይ ነው፡፡ እርሱ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡

وَيَوۡمَ يُعۡرَضُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ عَلَى ٱلنَّارِ أَلَيۡسَ هَٰذَا بِٱلۡحَقِّۖ قَالُواْ بَلَىٰ وَرَبِّنَاۚ قَالَ فَذُوقُواْ ٱلۡعَذَابَ بِمَا كُنتُمۡ تَكۡفُرُونَ ٣٤

34. እነዚያም የካዱት ሰዎች በእሳት ላይ በሚቀረቡ ቀን «ይህ እውነት አይደለምን?» (ይባላሉ)፡፡ «እውነት ነው፤ በጌታችን ይኹንብን» ይላሉ፡፡ (አላህም) «ትክዱ በነበራችሁት ምክንያት ቅጣቱን ቅመሱ» ይላቸዋል፡፡

فَٱصۡبِرۡ كَمَا صَبَرَ أُوْلُواْ ٱلۡعَزۡمِ مِنَ ٱلرُّسُلِ وَلَا تَسۡتَعۡجِل لَّهُمۡۚ كَأَنَّهُمۡ يَوۡمَ يَرَوۡنَ مَا يُوعَدُونَ لَمۡ يَلۡبَثُوٓاْ إِلَّا سَاعَةٗ مِّن نَّهَارِۭۚ بَلَٰغٞۚ فَهَلۡ يُهۡلَكُ إِلَّا ٱلۡقَوۡمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ٣٥

35. ከመልክተኞችም የቆራጥነት ባለቤቶች የኾኑት እንደ ታገሱ ሁሉ ታገስ፡፡ ለእነርሱም (ለሕዝቦችህ ቅጣት) አትቻኮል፡፡ ያንን የሚስፈራሩበትን ቅጣት በሚያዩ ቀን እነርሱ ከቀን አንዲትን ሰዓት አንጅ እንዳልቆዩ ይኾናሉ፡፡ (ይህ ቁርኣን) በቂ ግሳጼ ነው አመጸኞችም ሕዝቦች እንጅ (ሌሎች) ይጥጠፋሉን?

## سورة محمّد

## ሱረቱ ሙሀመድ

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ أَضَلَّ أَعۡمَٰلَهُمۡ ١

1. እነዚያ የካዱ ከአላህ መንገድም የከለከሉ (አላህ) ሥራዎቻቸውን አጠፋባቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ وَءَامَنُواْ بِمَا نُزِّلَ عَلَىٰ مُحَمَّدٖ وَهُوَ ٱلۡحَقُّ مِن رَّبِّهِمۡ كَفَّرَ عَنۡهُمۡ سَيِّـَٔاتِهِمۡ وَأَصۡلَحَ بَالَهُمۡ ٢

2. እነዚያም ያመኑ፣ በጎዎችንም የሠሩ፣ በሙሐመድ ላይም የወረደው እርሱ ከጌታቸው ሲኾን እውነት ስለ ኾነ ያመኑ ከእነርሱ ላይ ኃጢአቶቻቸውን ያባብሳል፡፡ ኹኔታቸውንም ሁሉ ያበጃል፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ ٱتَّبَعُواْ ٱلۡبَٰطِلَ وَأَنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّبَعُواْ ٱلۡحَقَّ مِن رَّبِّهِمۡۚ كَذَٰلِكَ يَضۡرِبُ ٱللَّهُ لِلنَّاسِ أَمۡثَٰلَهُمۡ ٣

3. ይህ እነዚያ የካዱት ውሸትን የተከተሉ በመኾናቸውና እነዚያም ያመኑት ከጌታቸው የኾነን እውነት ስለተከተሉ ነው፡፡ እንደዚሁ አላህ ለሰዎች ምሳሌዎቻቸውን ያብራራል፡፡

4. እነዚያንም የካዱትን (በጦር ላይ) ባገኛችሁ ጊዜ ጫንቃዎችን በኀይል ምቱ፡፡ ባደካማችኋቸውም ጊዜ (አትግደሏቸው ማርኳቸው)፡፡ ማሰሪያውንም አጥብቁ፡ ፡ በኋላም ወይም በነጻ ትለቋቸዋላችሁ፤ ወይም ትበዧቸዋላችሁ፡፡ (ይህም) ጦሪቱ መሳሪያዋን እስከምትጥል ድረስ ነው፡፡ (ነገሩ) ይህ ነው፡፡ አላህም ቢሻ ከእነርሱ (ያለጦር) በተበቀለ ነበር፡፡ ግን ከፊላችሁን በከፊሉ ሊሞክር (በዚህ አዘዛችሁ)፡፡ እነዚያንም በአላህ መንገድ ላይ የተገደሉትን ሥራዎቻቸውን ፈጽሞ አያጠፋባቸውም፡፡

فَإِذَا لَقِيتُمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَضَرْبَ ٱلرِّقَابِ حَتَّىٰٓ إِذَآ أَثْخَنتُمُوهُمْ فَشُدُّواْ ٱلْوَثَاقَ فَإِمَّا مَنَّۢا بَعْدُ وَإِمَّا فِدَآءً حَتَّىٰ تَضَعَ ٱلْحَرْبُ أَوْزَارَهَاۚ ذَٰلِكَۖ وَلَوْ يَشَآءُ ٱللَّهُ لَٱنتَصَرَ مِنْهُمْ وَلَٰكِن لِّيَبْلُوَاْ بَعْضَكُم بِبَعْضٍۗ وَٱلَّذِينَ قُتِلُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ فَلَن يُضِلَّ أَعْمَٰلَهُمْ ٤

5. በእርግጥ ይመራቸዋል፡፡ ኹኔታቸውንም ሁሉ ያበጃል፡፡

سَيَهْدِيهِمْ وَيُصْلِحُ بَالَهُمْ ٥

6. ገነትንም ያገባቸዋል፡፡ ለእነርሱ አስታውቋታል፡፡

وَيُدْخِلُهُمُ ٱلْجَنَّةَ عَرَّفَهَا لَهُمْ ٦

7. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን (ሃይማኖቱን) ብትረዱ፤ ይረዳችኋል፡፡ ጫማዎቻችሁንም ያደላድላል፡ ፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِن تَنصُرُواْ ٱللَّهَ يَنصُرْكُمْ وَيُثَبِّتْ أَقْدَامَكُمْ ٧

8. እነዚያም የካዱት ለእነርሱ ጥፋት ተገባቸው፡፡ ሥራዎቻቸውንም አጠፋባቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فَتَعْسًا لَّهُمْ وَأَضَلَّ أَعْمَٰلَهُمْ ٨

9. ይህ እነርሱ አላህ ያወረደውን ስለጠሉ ነው፡፡ ስለዚህ ሥራዎቻቸውን አበላሸባቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمْ كَرِهُواْ مَآ أَنزَلَ ٱللَّهُ فَأَحْبَطَ أَعْمَٰلَهُمْ ٩

10. የእነዚያ ከእነርሱ በፊት የነበሩት (ከሓዲዎች) መጨረሻ እንዴት እንደ ነበረ ያዩ ዘንድ በምድር ላይ አልኼዱምን? አላህ በእነርሱ ላይ (ያላቸውን ሁሉ) አጠፋባቸው፡፡ ለከሐዲዎችም ሁሉ ብጤዎችዋ አልሏቸው፡፡

۞أَفَلَمْ يَسِيرُواْ فِي ٱلْأَرْضِ فَيَنظُرُواْ كَيْفَ كَانَ عَٰقِبَةُ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْۖ دَمَّرَ ٱللَّهُ عَلَيْهِمْۖ وَلِلْكَٰفِرِينَ أَمْثَٰلُهَا ١٠

11. ይህ አላህ የእነዚያ ያመኑት ሰዎች ረዳት ስለኾነና ከሓዲዎችም ለእነርሱ ረዳት ስለሌላቸው ነው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّ ٱللَّهَ مَوْلَى ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَأَنَّ ٱلْكَٰفِرِينَ لَا مَوْلَىٰ لَهُمْ ١١

12. አላህ እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች ያገባቸዋል፡፡ እነዚያም የካዱት (በቅርቢቱ ዓለም) ይጣቀማሉ፡፡ እንስሳዎችም እንደሚበሉ ይበላሉ፡፡ እሳትም ለእነርሱ መኖሪያቸው ናት፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ يُدْخِلُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ جَنَّٰتٍ تَجْرِي مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُۖ وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يَتَمَتَّعُونَ وَيَأْكُلُونَ كَمَا تَأْكُلُ ٱلْأَنْعَٰمُ وَٱلنَّارُ مَثْوًى لَّهُمْ ١٢

13. ከከተማም እርሷ ከዚያች ካወጣችህ ከተማህ ይበልጥ በኀይል ጠንካራ የኾነች (ባለቤቶችዋን) ያጠፋናቸው ብዙ ናት፡፡ ለእነርሱም ረዳት አልነበራቸውም፡፡

وَكَأَيِّن مِّن قَرْيَةٍ هِيَ أَشَدُّ قُوَّةً مِّن قَرْيَتِكَ ٱلَّتِيٓ أَخْرَجَتْكَ أَهْلَكْنَٰهُمْ فَلَا نَاصِرَ لَهُمْ ١٣

14. ከጌታው በኾነች አስረጅ ላይ የኾነ ምእመን ክፉ ሥራቸው ለእነርሱ እንደ ተሸለመላቸውና ዝንባሌዎቻቸውን እንደ ተከተሉት ነውን?

أَفَمَن كَانَ عَلَىٰ بَيِّنَةٖ مِّن رَّبِّهِۦ كَمَن زُيِّنَ لَهُۥ سُوٓءُ عَمَلِهِۦ وَٱتَّبَعُوٓاْ أَهۡوَآءَهُم ١٤

15. የዚያች ጥንቁቆቹ ተስፋ የተሰጡት ገነት ምስል በውስጧ ሺታው ከማይለውጥ ውሃ ወንዞች፣ ጣዕሙ ከማይለወጥ ወተትም ወንዞች፣ ለጠጪዎች ሁሉ ጣፋጭ ከኾነች የወይን ጠጅም ወንዞች ከተነጠረ ማርም ወንዞች አልሉባት፡፡ ለእነርሱም በውስጧ ከፍሬዎች ሁሉ (በያይነቱ) ከጌታቸው ምሕረትም አልላቸው፡፡ (በዚች ገነት ውስጥ ዘውታሪ የኾነ ሰው) እርሱ በእሳት ውስጥ ዘውታሪ እንደኾነ ሰው፣ ሞቃትንም ውሃ እንደተጋቱ፣ አንጀቶቻቸውንም ወዲያውኑ እንደቆራረጠው ነውን? (አይደለም)፡፡

مَّثَلُ ٱلۡجَنَّةِ ٱلَّتِي وُعِدَ ٱلۡمُتَّقُونَۖ فِيهَآ أَنۡهَٰرٞ مِّن مَّآءٍ غَيۡرِ ءَاسِنٖ وَأَنۡهَٰرٞ مِّن لَّبَنٖ لَّمۡ يَتَغَيَّرۡ طَعۡمُهُۥ وَأَنۡهَٰرٞ مِّنۡ خَمۡرٖ لَّذَّةٖ لِّلشَّٰرِبِينَ وَأَنۡهَٰرٞ مِّنۡ عَسَلٖ مُّصَفّٗىۖ وَلَهُمۡ فِيهَا مِن كُلِّ ٱلثَّمَرَٰتِ وَمَغۡفِرَةٞ مِّن رَّبِّهِمۡۖ كَمَنۡ هُوَ خَٰلِدٞ فِي ٱلنَّارِ وَسُقُواْ مَآءً حَمِيمٗا فَقَطَّعَ أَمۡعَآءَهُمۡ ١٥

16. ከእነርሱም ወዳንተ የሚያዳምጡ አልሉ፡፡ ከአንተም ዘንድ በወጡ ጊዜ ለእነዚያ ዕውቀት ለተሰጡት «አሁን ምን አለ?» ይላሉ፡፡ እነዚህ እነዚያ በልቦቻቸው ላይ አላህ ያተመባቸው ዝንባሌዎቻቸውንም የተከተሉ ናቸው፡፡

وَمِنۡهُم مَّن يَسۡتَمِعُ إِلَيۡكَ حَتَّىٰٓ إِذَا خَرَجُواْ مِنۡ عِندِكَ قَالُواْ لِلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡعِلۡمَ مَاذَا قَالَ ءَانِفًاۚ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ طَبَعَ ٱللَّهُ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ وَٱتَّبَعُوٓاْ أَهۡوَآءَهُمۡ ١٦

17. እነዚያም የተመሩት (አላህ) መመራትን ጨመረላቸው፡፡ (ከእሳት) መጥጠበቂያቸውንም ሰጣቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ٱهۡتَدَوۡاْ زَادَهُمۡ هُدٗى وَءَاتَىٰهُمۡ تَقۡوَىٰهُمۡ ١٧

18. ሰዓቲቱንም ድንገት የምትመጣባቸው መኾንዋን እንጅ ይጠባበቃሉን? ምልክቶችዋም በእርግጥ መጥተዋል፡፡ በመጣቻቸውም ጊዜ ማስታወሳቸው ለእነርሱ እንዴት ይጠቅማቸዋል?

فَهَلۡ يَنظُرُونَ إِلَّا ٱلسَّاعَةَ أَن تَأۡتِيَهُم بَغۡتَةٗۖ فَقَدۡ جَآءَ أَشۡرَاطُهَاۚ فَأَنَّىٰ لَهُمۡ إِذَا جَآءَتۡهُمۡ ذِكۡرَىٰهُمۡ ١٨

19. እነሆ ከአላህ ሌላ አምላክ አለመኖሩንም ዕወቅ፡፡ ስለ ስህተትህም ለምእመናንም ምሕረትን ለምን፡፡ አላህም መዘዋወሪያችሁን፣ መርጊያችሁንም ያውቃል፡፡

فَٱعۡلَمۡ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا ٱللَّهُ وَٱسۡتَغۡفِرۡ لِذَنۢبِكَ وَلِلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِۗ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ مُتَقَلَّبَكُمۡ وَمَثۡوَىٰكُمۡ ١٩

20. እነዚያም ያመኑት ሰዎች (መታገል ያለባት) «ሱራ አትወርድም ኖሮአልን?» ይላሉ፡፡ የጠነከረችም ሱራ በተወረደችና በውስጧም መጋደል በተወሳ ጊዜ እነዚያን በልቦቻቸው ውስጥ (የንፍቅና) በሺታ ያለባቸውን ሰዎች ከሞት የኾነ መከራ በርሱ ላይ እንደ ወደቀበት ሰው አስተያየት ወዳንተ ሲመለከቱ ታያቸዋለህ፡፡ ለእነሱም ወዮላቸው፡፡

وَيَقُولُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَوۡلَا نُزِّلَتۡ سُورَةٞۖ فَإِذَآ أُنزِلَتۡ سُورَةٞ مُّحۡكَمَةٞ وَذُكِرَ فِيهَا ٱلۡقِتَالُ رَأَيۡتَ ٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ يَنظُرُونَ إِلَيۡكَ نَظَرَ ٱلۡمَغۡشِيِّ عَلَيۡهِ مِنَ ٱلۡمَوۡتِۖ فَأَوۡلَىٰ لَهُمۡ ٢٠

21. ታዛዥነትና መልካም ንግግር (ይሻላቸዋል) ትዕዛዙም ቁርጥ በኾነ ጊዜ ለአላህ (ትዕዛዝ) እውነተኞች በኾኑ ኖሮ ለእነርሱ የተሻለ በኾነ ነበር፡፡

طَاعَةٞ وَقَوۡلٞ مَّعۡرُوفٞۚ فَإِذَا عَزَمَ ٱلۡأَمۡرُ فَلَوۡ صَدَقُواْ ٱللَّهَ لَكَانَ خَيۡرٗا لَّهُمۡ ٢١

22. ብትሸሾሙም በምድር ላይ ማበላሸትን ዝምድናችሁንም መቁረጥን ከጀላችሁን?

فَهَلۡ عَسَيۡتُمۡ إِن تَوَلَّيۡتُمۡ أَن تُفۡسِدُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَتُقَطِّعُوٓاْ أَرۡحَامَكُمۡ ٢٢

23. እነዚህ እነዚያ አላህ የረገማቸው፣ ያደነቆራቸውም፣ ዓይኖቻቸውንም ያወራቸው ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ لَعَنَهُمُ ٱللَّهُ فَأَصَمَّهُمۡ وَأَعۡمَىٰٓ أَبۡصَٰرَهُمۡ ٢٣

24. ቁርአንንም አያስተነትኑምን? በእውነቱ በልቦቻቸው ላይ ቁልፎቿ አልሉባትን?

أَفَلَا يَتَدَبَّرُونَ ٱلۡقُرۡءَانَ أَمۡ عَلَىٰ قُلُوبٍ أَقۡفَالُهَآ ٢٤

25. እነዚያ ለእነርሱ ቅኑ መንገድ ከተብራራላቸው በኋላ ወደ ኋላቸው የተመለሱት ሰይጣን ለእነርሱ መመለሳቸውን ሸለመላቸው፡፡ ለእነርሱም አዝዘናጋቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ٱرۡتَدُّواْ عَلَىٰٓ أَدۡبَٰرِهِم مِّنۢ بَعۡدِ مَا تَبَيَّنَ لَهُمُ ٱلۡهُدَى ٱلشَّيۡطَٰنُ سَوَّلَ لَهُمۡ وَأَمۡلَىٰ لَهُمۡ ٢٥

26. ይህ እነርሱ ለእነዚያ አላህ ያወረደውን ለጠሉት «በነገሩ ከፊል እንታዘዛችኋለን» ያሉ በመኾናቸው ነው፡፡ አላህም መደበቃቸውን ያውቃል፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَالُواْ لِلَّذِينَ كَرِهُواْ مَا نَزَّلَ ٱللَّهُ سَنُطِيعُكُمۡ فِي بَعۡضِ ٱلۡأَمۡرِۖ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ إِسۡرَارَهُمۡ ٢٦

27. መላእክትም ፊቶቻቸውንና ጀርባዎቻቸውን የሚመቱ ሲኾኑ በገደሉዋቸው ጊዜ (ኹኔታቸው) እንዴት ይኾናል?

فَكَيۡفَ إِذَا تَوَفَّتۡهُمُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ يَضۡرِبُونَ وُجُوهَهُمۡ وَأَدۡبَٰرَهُمۡ ٢٧

28. ይህ እነርሱ አላህን ያስቆጣውን ነገር ስለ ተከተሉ ውዴታውንም ስለ ጠሉ ነው፡፡ ስለዚህ ሥራዎቻቸውን አበላሸባቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمُ ٱتَّبَعُواْ مَآ أَسۡخَطَ ٱللَّهَ وَكَرِهُواْ رِضۡوَٰنَهُۥ فَأَحۡبَطَ أَعۡمَٰلَهُمۡ ٢٨

29. እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ በሽታ ያለባቸው አላህ ቂሞቻቸውን አለማውጣቱን ጠረጠሩን?

أَمۡ حَسِبَ ٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٌ أَن لَّن يُخۡرِجَ ٱللَّهُ أَضۡغَٰنَهُمۡ ٢٩

30. በሻንም ኖሮ እነርሱን ባሳየንህና በምልክታቸውም በእርግጥ ባወቅሃቸው ነበር፡፡ ንግግርንም በማሸሞራቸው በእርግጥ ታውቃቸዋለህ፡፡ አላህም ሥራዎቻችሁን ያውቃል፡፡

وَلَوۡ نَشَآءُ لَأَرَيۡنَٰكَهُمۡ فَلَعَرَفۡتَهُم بِسِيمَٰهُمۡۚ وَلَتَعۡرِفَنَّهُمۡ فِي لَحۡنِ ٱلۡقَوۡلِۚ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ أَعۡمَٰلَكُمۡ ٣٠

31. ከእናንተም ታጋዮቹንና ታጋሾቹን እስከምናውቅ፣ ወሬዎቻችሁንም እስከምንገልጽ ድረስ በእርግጥ እንሞክራችኋለን፡፡

وَلَنَبۡلُوَنَّكُمۡ حَتَّىٰ نَعۡلَمَ ٱلۡمُجَٰهِدِينَ مِنكُمۡ وَٱلصَّٰبِرِينَ وَنَبۡلُوَاْ أَخۡبَارَكُمۡ ٣١

32. እነዚያ የካዱና ከአላህም መንገድ ያገዱ ለእነርሱም ቅኑ መንገድ ከተገለጸላቸው በኋላ መልክተኛውን የተከራከሩ አላህን በምንም አይጎዱትም፡፡ ሥራዎቻቸውንም በእርግጥ ያበላሻል፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ وَشَآقُّواْ ٱلرَّسُولَ مِنۢ بَعۡدِ مَا تَبَيَّنَ لَهُمُ ٱلۡهُدَىٰ لَن يَضُرُّواْ ٱللَّهَ شَيۡـٔٗا وَسَيُحۡبِطُ أَعۡمَٰلَهُمۡ ٣٢

33. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገዙ፡፡ መልክተኛውንም ታዘዙ፡፡ ሥራዎቻችሁንም አታበላሹ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُواْ ٱلرَّسُولَ وَلَا تُبۡطِلُوٓاْ أَعۡمَٰلَكُمۡ ٣٣

34. እነዚያ የካዱ፣ ከአላህም መንገድ ያገዱ፣ ከዚያም እነርሱ ከሓዲዎች ኾነው የሞቱ አላህ ለእነርሱ በፍጹም አይምርም፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ ثُمَّ مَاتُواْ وَهُمۡ كُفَّارٞ فَلَن يَغۡفِرَ ٱللَّهُ لَهُمۡ ٣٤

35. እናንተም አሸናፊዎቹ ስትኾኑ አላህ ከእናንተ ጋር ሲሆን አትድከሙ፡፡ ወደ ዕርቅም አትጥሩ፡፡ ሥራዎቻችሁንም ፈጽሞ አያጎድልባችሁም፡፡

فَلَا تَهِنُواْ وَتَدۡعُوٓاْ إِلَى ٱلسَّلۡمِ وَأَنتُمُ ٱلۡأَعۡلَوۡنَ وَٱللَّهُ مَعَكُمۡ وَلَن يَتِرَكُمۡ أَعۡمَٰلَكُمۡ ٣٥

36. ቅርቢቱ ሕይወት ጫወታና ዛዛታ ብቻ ናት፡፡ ብታምኑም ብትጠነቀቁም ምንዳዎቻችሁን ይሰጣችኋል፡፡ ገንዘቦቻችሁንም (ሁሉ) አይጠይቃችሁም፡፡

إِنَّمَا ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا لَعِبٞ وَلَهۡوٞۚ وَإِن تُؤۡمِنُواْ وَتَتَّقُواْ يُؤۡتِكُمۡ أُجُورَكُمۡ وَلَا يَسۡـَٔلۡكُمۡ أَمۡوَٰلَكُمۡ ٣٦

37. እርሷን ቢጠይቃችሁና ችክ ቢልባችሁ ትሰስታላችሁ፡፡ ቂሞቻችሁንም ያወጣል፡፡

إِن يَسۡـَٔلۡكُمُوهَا فَيُحۡفِكُمۡ تَبۡخَلُواْ وَيُخۡرِجۡ أَضۡغَٰنَكُمۡ ٣٧

38. ንቁ! እናንተ እነዚያ በአላህ መንገድ ትለግሱ ዘንድ የምትጥጠሩ ናችሁ፡፡ ከእናንተም ውስጥ የሚሰስት ሰው አልለ፡፡ የሚሰስትም ሰው የሚሰስተው በራሱ ላይ ብቻ ነው፡፡ አላህም ከበርቴ ነው፡፡ እናንተም ድኾች ናችሁ፡፡ ብትሸሹም ሌሎችን ሕዝቦች ይለውጣል፡፡ ከዚያም (ባለመታዘዝ) ብጤዎቻችሁ አይኾኑም፡፡

هَٰٓأَنتُمۡ هَٰٓؤُلَآءِ تُدۡعَوۡنَ لِتُنفِقُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ فَمِنكُم مَّن يَبۡخَلُۖ وَمَن يَبۡخَلۡ فَإِنَّمَا يَبۡخَلُ عَن نَّفۡسِهِۦۚ وَٱللَّهُ ٱلۡغَنِيُّ وَأَنتُمُ ٱلۡفُقَرَآءُۚ وَإِن تَتَوَلَّوۡاْ يَسۡتَبۡدِلۡ قَوۡمًا غَيۡرَكُمۡ ثُمَّ لَا يَكُونُوٓاْ أَمۡثَٰلَكُم ٣٨

# ሱረቱ አል ፈትህ

# سورة الفتح

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. እኛ ላንተ ግልጽ የኾነን መክፈት ከፈትንልህ፡፡

إِنَّا فَتَحۡنَا لَكَ فَتۡحٗا مُّبِينٗا ١

2. አላህ ከኃጢአትህ ያለፈውንና የሚመጣውን ላንተ ሊምር ጸጋውንም ባንተ ላይ ሊሞላ ቀጥተኛውንም መንገድ ሊመራህ (ከፈተልህ)፡፡

لِّيَغۡفِرَ لَكَ ٱللَّهُ مَا تَقَدَّمَ مِن ذَنۢبِكَ وَمَا تَأَخَّرَ وَيُتِمَّ نِعۡمَتَهُۥ عَلَيۡكَ وَيَهۡدِيَكَ صِرَٰطٗا مُّسۡتَقِيمٗا ﴿٢﴾

3. አላህ ብርቱን እርዳታ ሊረዳህም (ከፈተልህ)፡፡

وَيَنصُرَكَ ٱللَّهُ نَصۡرًا عَزِيزًا ﴿٣﴾

4. እርሱ ያ በምእምናን ልቦች ውስጥ ከእምነታቸው ጋር እምነትን ይጨምሩ ዘንድ እርጋታን ያወረደ ነው፡፡ ለአላህም የሰማያትና የምድር ሰራዊቶች አልሉት፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِيٓ أَنزَلَ ٱلسَّكِينَةَ فِي قُلُوبِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ لِيَزۡدَادُوٓاْ إِيمَٰنٗا مَّعَ إِيمَٰنِهِمۡۗ وَلِلَّهِ جُنُودُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلِيمًا حَكِيمٗا ﴿٤﴾

5. ምእምናንንና ምእምናትን ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ ሊያገባቸው ከነርሱም ኃጢአቶቻቸውን ሊያብስላቸው (በትግል አዘዛቸው)፡፡ ይህም ከአላህ ዘንድ የኾነ ታላቅ ማግኘት ነው፡፡

لِّيُدۡخِلَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا وَيُكَفِّرَ عَنۡهُمۡ سَيِّـَٔاتِهِمۡۚ وَكَانَ ذَٰلِكَ عِندَ ٱللَّهِ فَوۡزًا عَظِيمٗا ﴿٥﴾

6. በአላህም ክፉ ጥርጣሬን ተጠራጣሪዎቹን መናፍቃንና መናፍቃትን፣ ወንዶች አጋሪዎቻችንና ሴቶች አጋሪዎችንም ያሰቃይ ዘንድ (በትግል አዘዘ)፡፡ በእነርሱ ላይ ክፉ ከባቢ አለባቸው፡፡ በእነርሱም ላይ አላህ ተቆጣባቸው፡፡ ረገማቸውም፡፡ ለእነርሱም ገሀነምን አዘጋጀላቸው፡፡ መመለሻነትዋም ከፋች፡፡

وَيُعَذِّبَ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ وَٱلۡمُنَٰفِقَٰتِ وَٱلۡمُشۡرِكِينَ وَٱلۡمُشۡرِكَٰتِ ٱلظَّآنِّينَ بِٱللَّهِ ظَنَّ ٱلسَّوۡءِۚ عَلَيۡهِمۡ دَآئِرَةُ ٱلسَّوۡءِۖ وَغَضِبَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمۡ وَلَعَنَهُمۡ وَأَعَدَّ لَهُمۡ جَهَنَّمَۖ وَسَآءَتۡ مَصِيرٗا ﴿٦﴾

7. ለአላህም የሰማያትና የምድር ሰራዊቶች አልሉት፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَلِلَّهِ جُنُودُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَزِيزًا حَكِيمًا ﴿٧﴾

8. እኛ መስካሪ አብሳሪና አስፈራሪም አድርገን በእርግጥ ላክንህ፡፡

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَٰكَ شَٰهِدٗا وَمُبَشِّرٗا وَنَذِيرٗا ﴿٨﴾

9. በአላህ ልታምኑ፣ በመልክተኛውም (ልታምኑ)፣ ልትረዱትም፣ ልታከብሩትም፣ (አላህን) በጧትና ከቀትር በኋላ ልታወድሱትም (ላክነው)፡፡

لِّتُؤۡمِنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَتُعَزِّرُوهُ وَتُوَقِّرُوهُۚ وَتُسَبِّحُوهُ بُكۡرَةٗ وَأَصِيلًا ﴿٩﴾

10. እነዚያ ቃል ኪዳን የሚጋቡህ ቃል ኪዳን የሚጋቡት አላህን ብቻ ነው፡፡ የአላህ እጅ (ኀይሉ) ከእጆቻቸው በላይ ነው፡፡ ያፈረሰም ሰው የሚያፈርሰው በነፍሱ ላይ ብቻ ነው፡፡ በእርሱ ላይ አላህን ቃል ኪዳን የተጋባበትን የሞላም ሰው ታላቅ ምንዳን በእርግጥ ይሰጠዋል፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُبَايِعُونَكَ إِنَّمَا يُبَايِعُونَ ٱللَّهَ يَدُ ٱللَّهِ فَوۡقَ أَيۡدِيهِمۡۚ فَمَن نَّكَثَ فَإِنَّمَا يَنكُثُ عَلَىٰ نَفۡسِهِۦۖ وَمَنۡ أَوۡفَىٰ بِمَا عَٰهَدَ عَلَيۡهُ ٱللَّهَ فَسَيُؤۡتِيهِ أَجۡرًا عَظِيمٗا ﴿١٠﴾

11. ከአዕራብ ሰዎች እነዚያ (ከዘመቻ) ወደ ኋላ የቀሩት ለአንተ «ገንዘቦቻችንና ቤተሰቦቻችን አስቸገሩን፤ ስለዚህ ምሕረትን ለምንልን፤» ይሉሃል፡፡ በልቦቻቸው ውስጥ የሌለውን ነገር በምላሶቻቸው ይናገራሉ፡፡ (አላህ) «በእናንተ ላይ ጉዳትን ቢሻ ወይም በእናንተ መጥቀምን ቢሻ ከአላህ (ለማገድ) ለእናንተ አንዳችን የሚችል ማነው? በእውነቱ አላህ፤በምትሠሩት ሁሉ ውስጥ ዐዋቂ ነው» በላቸው፡፡

سَيَقُولُ لَكَ ٱلْمُخَلَّفُونَ مِنَ ٱلْأَعْرَابِ شَغَلَتْنَآ أَمْوَٰلُنَا وَأَهْلُونَا فَٱسْتَغْفِرْ لَنَا ۚ يَقُولُونَ بِأَلْسِنَتِهِم مَّا لَيْسَ فِى قُلُوبِهِمْ ۚ قُلْ فَمَن يَمْلِكُ لَكُم مِّنَ ٱللَّهِ شَيْـًٔا إِنْ أَرَادَ بِكُمْ ضَرًّا أَوْ أَرَادَ بِكُمْ نَفْعًۢا ۚ بَلْ كَانَ ٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرًۢا ﴿١١﴾

12. ይልቁንም መልክተኛውና ምእመናኖቹ ወደ ቤተሰቦቻቸው ፈጽሞ አለመመለሳቸውን ጠረጠራችሁ፡፡ ይህም በልቦቻችሁ ውስጥ ተሸለመላችሁ፡፡ መጥፎንም መጠርጠር ጠረጠራችሁ፡፡ ጠፊዎች ሕዝቦችም ኾናችሁ፡፡

بَلْ ظَنَنتُمْ أَن لَّن يَنقَلِبَ ٱلرَّسُولُ وَٱلْمُؤْمِنُونَ إِلَىٰٓ أَهْلِيهِمْ أَبَدًا وَزُيِّنَ ذَٰلِكَ فِى قُلُوبِكُمْ وَظَنَنتُمْ ظَنَّ ٱلسَّوْءِ وَكُنتُمْ قَوْمًۢا بُورًا ﴿١٢﴾

13. በአላህና በመልክተኛው ያላመነም ሰው እኛ ላከሓዲዎች እሳትን አዘጋጅተናል፡፡

وَمَن لَّمْ يُؤْمِنۢ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ فَإِنَّآ أَعْتَدْنَا لِلْكَٰفِرِينَ سَعِيرًا ﴿١٣﴾

14. የሰማያትና የምድር ንግሥናም የአላህ ነው፡፡ ለሚሻው ሰው ይምራል፤ የሚሻውንም ይቀጣል፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

وَلِلَّهِ مُلْكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۚ يَغْفِرُ لِمَن يَشَآءُ وَيُعَذِّبُ مَن يَشَآءُ ۚ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورًا رَّحِيمًا ﴿١٤﴾

15. ወደ ዘረፋዎች ልትይዟት በኼዳችሁ ጊዜ እነዚያ ወደ ኋላ የቀሩት ሰዎች «ተዉን እንከተላችሁ» ይሏችኋል፡፡ (በዚህም) የአላህን ቃል ሊለውጡ ይፈልጋሉ፡፡ «ፈጽሞ አትከተሉንም፡፡ ይህን (ቃል) ከዚህ በፊት አላህ ብሏል» በላቸው፡፡ ይልቁንም «ትመቀኙናላችሁ» ይላሉም፡፡ በእውነት እነርሱ ጥቂትን እንጅ የማያውቁ ነበሩ፡፡

سَيَقُولُ ٱلْمُخَلَّفُونَ إِذَا ٱنطَلَقْتُمْ إِلَىٰ مَغَانِمَ لِتَأْخُذُوهَا ذَرُونَا نَتَّبِعْكُمْ ۖ يُرِيدُونَ أَن يُبَدِّلُوا۟ كَلَٰمَ ٱللَّهِ ۚ قُل لَّن تَتَّبِعُونَا كَذَٰلِكُمْ قَالَ ٱللَّهُ مِن قَبْلُ ۖ فَسَيَقُولُونَ بَلْ تَحْسُدُونَنَا ۚ بَلْ كَانُوا۟ لَا يَفْقَهُونَ إِلَّا قَلِيلًا ﴿١٥﴾

16. ከአዕራቦች ወደ ኋላ ለቀሩት በላቸው፡- «የብርቱ ጭካኔ ባለቤት ወደ ኾኑ ሕዝቦች (ውጊያ) ወደ ፊት ትጥጠራላችሁ፡፡ ትጋደሏቸዋላችሁ፤ ወይም ይሰልማሉ፡፡ ብትታዘዙም አላህ መልካም ምንዳን ይሰጣችኋል፡፡ ከአሁን በፊት እንደ ሸሻችሁ ብትሸሹም አሳማሚን ቅጣት ይቀጣችኋል፡፡»

قُل لِّلْمُخَلَّفِينَ مِنَ ٱلْأَعْرَابِ سَتُدْعَوْنَ إِلَىٰ قَوْمٍ أُو۟لِى بَأْسٍ شَدِيدٍ تُقَٰتِلُونَهُمْ أَوْ يُسْلِمُونَ ۖ فَإِن تُطِيعُوا۟ يُؤْتِكُمُ ٱللَّهُ أَجْرًا حَسَنًا ۖ وَإِن تَتَوَلَّوْا۟ كَمَا تَوَلَّيْتُم مِّن قَبْلُ يُعَذِّبْكُمْ عَذَابًا أَلِيمًا ﴿١٦﴾

17. በዕውር ላይ (ከዘመቻ በመቅቱ) ኃጢአት የለበትም፡፡ በአንካሳም ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ በበሽተኛም ላይ ኃጢአት የለበትም፡፡ አላህንና መልክተኛውንም የሚታዘዝ ሰው ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች ያገባዋል፡፡ የሚሸሸውንም ሰው አሳማሚውን ቅጣት ይቀጣዋል፡፡

لَّيۡسَ عَلَى ٱلۡأَعۡمَىٰ حَرَجٞ وَلَا عَلَى ٱلۡأَعۡرَجِ حَرَجٞ وَلَا عَلَى ٱلۡمَرِيضِ حَرَجٞۗ وَمَن يُطِعِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ يُدۡخِلۡهُ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۖ وَمَن يَتَوَلَّ يُعَذِّبۡهُ عَذَابًا أَلِيمٗا ١٧

18. ከምእምናኖቹ በዛፊቱ ሥር ቃል ኪዳን በሚጋቡህ ጊዜ አላህ በእርግጥ ወደደ፡፡ በልቦቻቸውም ውስጥ ያለውን ዐወቀ፡፡ በእነርሱም ላይ እርጋታን አወረደ፡፡ ቅርብ የኾነንም መከፈት መነዳቸው፡፡

۞لَّقَدۡ رَضِيَ ٱللَّهُ عَنِ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ إِذۡ يُبَايِعُونَكَ تَحۡتَ ٱلشَّجَرَةِ فَعَلِمَ مَا فِي قُلُوبِهِمۡ فَأَنزَلَ ٱلسَّكِينَةَ عَلَيۡهِمۡ وَأَثَٰبَهُمۡ فَتۡحٗا قَرِيبٗا ١٨

19. ብዙዎች ዘረፋዎችንም የሚወስዷቸው የኾኑን (መነዳቸው)፡፡ አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው፡፡

وَمَغَانِمَ كَثِيرَةٗ يَأۡخُذُونَهَاۗ وَكَانَ ٱللَّهُ عَزِيزًا حَكِيمٗا ١٩

20. አላህ ብዙዎችን ዘረፋዎች የምትወስዷቸው የኾኑን ተስፋ አደረገላችሁ፡፡ ይህችንም ለእናንተ አስቸኮለላችሁ፡፡ ከእናንተም የሰዎችን እጆች ከለከለላችሁ፡፡ (ልታመሰግኑትና) ለምእምናንም ምልክት እንድትኾን ቀጥተኛውን መንገድ ይመራችሁም ዘንድ (ይህንን ሠራላችሁ)፡፡

وَعَدَكُمُ ٱللَّهُ مَغَانِمَ كَثِيرَةٗ تَأۡخُذُونَهَا فَعَجَّلَ لَكُمۡ هَٰذِهِۦ وَكَفَّ أَيۡدِيَ ٱلنَّاسِ عَنكُمۡ وَلِتَكُونَ ءَايَةٗ لِّلۡمُؤۡمِنِينَ وَيَهۡدِيَكُمۡ صِرَٰطٗا مُّسۡتَقِيمٗا ٢٠

21. ሌላይቱንም በእርሷ ላይ ገና ያልቻላችኋትን አላህ ያወቃትን (ለእናንተ አዘጋጃት)፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

وَأُخۡرَىٰ لَمۡ تَقۡدِرُواْ عَلَيۡهَا قَدۡ أَحَاطَ ٱللَّهُ بِهَاۚ وَكَانَ ٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٗا ٢١

22. እነዚያም የካዱት (የመካ ሰዎች በሑደይቢያ) በተወጉችሁ ኖሮ ( ለሺሺት) ጀርባዎችን ባዞሩ ነበር፡፡ ከዚያም ዘመድም ረዳትም አያገኙም፡፡

وَلَوۡ قَٰتَلَكُمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَوَلَّوُاْ ٱلۡأَدۡبَٰرَ ثُمَّ لَا يَجِدُونَ وَلِيّٗا وَلَا نَصِيرٗا ٢٢

23. አላህ ያችን ከዚህ በፊት በእርግጥ ያለፈችውን ልማድ ደነገገ፡፡ ለአላህም ልማድ ለውጥን አታገኝም፡፡

سُنَّةَ ٱللَّهِ ٱلَّتِي قَدۡ خَلَتۡ مِن قَبۡلُۖ وَلَن تَجِدَ لِسُنَّةِ ٱللَّهِ تَبۡدِيلٗا ٢٣

24. እርሱም ያ በመካ ውስጥ በእነርሱ ላይ ካስቻለችሁ በኋላ እጆቻቸውን ከእናንተ ላይ እጆቻችሁንም ከእነርሱ ላይ የከለከለ ነው፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

وَهُوَ ٱلَّذِي كَفَّ أَيۡدِيَهُمۡ عَنكُمۡ وَأَيۡدِيَكُمۡ عَنۡهُم بِبَطۡنِ مَكَّةَ مِنۢ بَعۡدِ أَنۡ أَظۡفَرَكُمۡ عَلَيۡهِمۡۚ وَكَانَ ٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرًا ٢٤

25. እነርሱ እነዚያ የካዱ፣ ከተከበረው መስጊድም የከለከሏችሁ፣ መስዋእቱንም የታሰረ ሲኾን በስፍራው እንዳይደርስ (የከለከሉ) ናቸው፡፡ የማታውቋቸው የኾኑ ምእመናን ወንዶችና ምእምናት ሴቶች (ከከሓዲዎቹ ጋር) ባልነበሩ ያለ ዕውቀት እነርሱን መርገጣችሁና ከእነረሱ (በኩል) መከፋት የሚነካችሁ ባልኾነ ኖሮ (እጆቻችሁን ባላገድን ነበር) አላህ የሚሻውን ሰው በእዝነቱ ውስጥ ያገባ ዘንድ (እጆቻችሁን አገደ)፡፡ በተለዩ ኖሮ እነዚያን ከእነርሱ ውስጥ የካዱትን አሳማሚን ቅጣት በቀጣናቸው ነበር፡፡

هُمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَصَدُّوكُمْ عَنِ ٱلْمَسْجِدِ ٱلْحَرَامِ وَٱلْهَدْىَ مَعْكُوفًا أَن يَبْلُغَ مَحِلَّهُۥ ۚ وَلَوْلَا رِجَالٌ مُّؤْمِنُونَ وَنِسَآءٌ مُّؤْمِنَٰتٌ لَّمْ تَعْلَمُوهُمْ أَن تَطَـُٔوهُمْ فَتُصِيبَكُم مِّنْهُم مَّعَرَّةٌۢ بِغَيْرِ عِلْمٍ ۖ لِّيُدْخِلَ ٱللَّهُ فِى رَحْمَتِهِۦ مَن يَشَآءُ ۚ لَوْ تَزَيَّلُواْ لَعَذَّبْنَا ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنْهُمْ عَذَابًا أَلِيمًا ﴿٢٥﴾

26. እነዚያ የካዱት ደራይቱን የመሀይምነቲቱን ደራ በልቦቻቸው ውስጥ ባደረጉ ጊዜ (በቀጣናቸው ነበር)፡፡ አላህም በመልክተኛው ላይና በምእምናኖቹ ላይ እርጋታውን አወረደ፡፡ መጥጠበቂያይቱንም ቃል አስያዛቸው፡፡ በእርሷም ተገቢዎች ባለቤቶችዋም ነበሩ፡ ፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

إِذْ جَعَلَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فِى قُلُوبِهِمُ ٱلْحَمِيَّةَ حَمِيَّةَ ٱلْجَٰهِلِيَّةِ فَأَنزَلَ ٱللَّهُ سَكِينَتَهُۥ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ وَعَلَى ٱلْمُؤْمِنِينَ وَأَلْزَمَهُمْ كَلِمَةَ ٱلتَّقْوَىٰ وَكَانُوٓاْ أَحَقَّ بِهَا وَأَهْلَهَا ۚ وَكَانَ ٱللَّهُ بِكُلِّ شَىْءٍ عَلِيمًا ﴿٢٦﴾

27. አላህ ለመልክተኛው ሕልሙን እውነተኛ ሲኾን አላህ የሻ እንደ ኾነ ጸጥተኞች ኾናችሁ ራሶቻችሁን ላጭታችሁ፣ አሳጥራችሁም የማትፈሩ ስትኾኑ የተከበረውን መስጊድ በእርግጥ ትገባላችሁ፤ ያለውን በእርግጥ እውነት አደረገለት፡፡ (ከእርቁ) ያላወቃችሁትንም ነገር ዐወቀ፡፡ ከዚህም በፊት ቅርብን መክፈት አደረገ፡፡

لَّقَدْ صَدَقَ ٱللَّهُ رَسُولَهُ ٱلرُّءْيَا بِٱلْحَقِّ ۖ لَتَدْخُلُنَّ ٱلْمَسْجِدَ ٱلْحَرَامَ إِن شَآءَ ٱللَّهُ ءَامِنِينَ مُحَلِّقِينَ رُءُوسَكُمْ وَمُقَصِّرِينَ لَا تَخَافُونَ ۖ فَعَلِمَ مَا لَمْ تَعْلَمُواْ فَجَعَلَ مِن دُونِ ذَٰلِكَ فَتْحًا قَرِيبًا ﴿٢٧﴾

28. እርሱ ያ መልክተኛውን በመሪ መጽሐፍና በእውነተኛ ሃይማኖት በሃይማኖት ሁሉ ላይ ሊያልቀው የላከ ነው፡፡ መስካሪም በአላህ በቃ፡፡

هُوَ ٱلَّذِىٓ أَرْسَلَ رَسُولَهُۥ بِٱلْهُدَىٰ وَدِينِ ٱلْحَقِّ لِيُظْهِرَهُۥ عَلَى ٱلدِّينِ كُلِّهِۦ ۚ وَكَفَىٰ بِٱللَّهِ شَهِيدًا ﴿٢٨﴾

29. የአላህ መልክተኛ ሙሐመድ እነዚያም ከእርሱ ጋር ያሉት (ወዳጆቹ) በከሓዲዎቹ ላይ ብርቱዎች በመካከላቸው አዛኞች ናቸው፡፡ አጎንባሾች፣ ሰጋጆች ኾነው ታያቸዋለህ፡፡ ከአላህ ችሮታንና ውዴታን ይፈልጋሉ፡፡ ምልክታቸው ከስግደታቸው ፈለግ ስትኾን በፊቶቻቸው ላይ ናት፡፡ ይህ በተውራት (የተነገረው) ጠባያቸው ነው፡፡ በኢንጂልም ውስጥ ምሳሌያቸው ቀንዘሉን እንደአወጣ አዝመራና፣ (ቀንዘሉ) እንዳበረታው፣ እንደወፈረምና፣ ገበሬዎቹን የሚያስደንቅ ኾኖ በአገዳዎቹ ላይ ተስተካክሎ እንደ ቆመ (አዝመራ) ነው፡፡ (ያበረታቸውና ያበዛቸው) ከሓዲዎችን በእነርሱ ሊያስቆጭ ነው፡፡ አላህም እነዚያን ያመኑትንና ከእነርሱ በጎዎችን የሠሩትን ምሕረትንና ታላቅ ምንዳን ተስፋ አድርጎላቸዋል፡፡

مُّحَمَّدٌ رَّسُولُ ٱللَّهِ ۚ وَٱلَّذِينَ مَعَهُۥٓ أَشِدَّآءُ عَلَى ٱلْكُفَّارِ رُحَمَآءُ بَيْنَهُمْ ۖ تَرَىٰهُمْ رُكَّعًا سُجَّدًا يَبْتَغُونَ فَضْلًا مِّنَ ٱللَّهِ وَرِضْوَٰنًا ۖ سِيمَاهُمْ فِى وُجُوهِهِم مِّنْ أَثَرِ ٱلسُّجُودِ ۚ ذَٰلِكَ مَثَلُهُمْ فِى ٱلتَّوْرَىٰةِ ۚ وَمَثَلُهُمْ فِى ٱلْإِنجِيلِ كَزَرْعٍ أَخْرَجَ شَطْـَٔهُۥ فَـَٔازَرَهُۥ فَٱسْتَغْلَظَ فَٱسْتَوَىٰ عَلَىٰ سُوقِهِۦ يُعْجِبُ ٱلزُّرَّاعَ لِيَغِيظَ بِهِمُ ٱلْكُفَّارَ ۗ وَعَدَ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ مِنْهُم مَّغْفِرَةً وَأَجْرًا عَظِيمًۢا ﴿٢٩﴾

# سورةالحُجُرات

# ሱረቱ አል ሑጅራት

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُقَدِّمُواْ بَيۡنَ يَدَيِ ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌ عَلِيمٞ ١

1. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በአላህና በመልክተኛው ፊት (ነፍሶቻችሁን) አታስቀድሙ:: አላህንም ፍሩ:: አላህ ሰሚ ዐዋቂ ነውና::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَرۡفَعُوٓاْ أَصۡوَٰتَكُمۡ فَوۡقَ صَوۡتِ ٱلنَّبِيِّ وَلَا تَجۡهَرُواْ لَهُۥ بِٱلۡقَوۡلِ كَجَهۡرِ بَعۡضِكُمۡ لِبَعۡضٍ أَن تَحۡبَطَ أَعۡمَٰلُكُمۡ وَأَنتُمۡ لَا تَشۡعُرُونَ ٢

2. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ድምጾቻችሁን ከነቢዩ ድምጽ በላይ ከፍ አታድርጉ:: ከፊላችሁም ለከፊሉ እንደሚጮህ በንግግር ለርሱ አትጩሁ:: እናንተ የማታውቁ ስትኾኑ ሥራዎቻችሁ እንዳይበላሹ (ተከልከሉ)::

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَغُضُّونَ أَصۡوَٰتَهُمۡ عِندَ رَسُولِ ٱللَّهِ أُوْلَٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ ٱمۡتَحَنَ ٱللَّهُ قُلُوبَهُمۡ لِلتَّقۡوَىٰۚ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَأَجۡرٌ عَظِيمٌ ٣

3. እነዚያ በአላህ መልክተኛ ዘንድ ድምጾቻቸውን ዝቅ የሚያደርጉ እነዚህ እነዚያ አላህ ልቦቻቸውን ለፍርሃት የፈተናቸው ናቸው:: ለእነርሱም ምሕረትና ታላቅ ምንዳ አላቸው::

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُنَادُونَكَ مِن وَرَآءِ ٱلۡحُجُرَٰتِ أَكۡثَرُهُمۡ لَا يَعۡقِلُونَ ٤

4. እነዚያ ከክፍሎቹ ውጭ ኾነው የሚጠሩህ አብዛኞቻቸው አያውቁም::

وَلَوۡ أَنَّهُمۡ صَبَرُواْ حَتَّىٰ تَخۡرُجَ إِلَيۡهِمۡ لَكَانَ خَيۡرٗا لَّهُمۡۚ وَٱللَّهُ غَفُورٞ رَّحِيمٞ ٥

5. ወደእነርሱም እስክትወጣ ድረስ እነርሱ በታገሡ ኖሮ ለእነርሱ በላጭ በኾነ ነበር:: አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِن جَآءَكُمۡ فَاسِقُۢ بِنَبَإٖ فَتَبَيَّنُوٓاْ أَن تُصِيبُواْ قَوۡمَۢا بِجَهَٰلَةٖ فَتُصۡبِحُواْ عَلَىٰ مَا فَعَلۡتُمۡ نَٰدِمِينَ ٦

6. እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ነገረኛ ወሬን ቢያመጣላችሁ በስህተት ላይ ኾናችሁ ሕዝቦችን እንዳትጎዱና በሠራችሁት ነገር ላይ ተጸጸኞች እንዳትኾኑ አረጋግጡ::

وَٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ فِيكُمۡ رَسُولَ ٱللَّهِۚ لَوۡ يُطِيعُكُمۡ فِي كَثِيرٖ مِّنَ ٱلۡأَمۡرِ لَعَنِتُّمۡ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ حَبَّبَ إِلَيۡكُمُ ٱلۡإِيمَٰنَ وَزَيَّنَهُۥ فِي قُلُوبِكُمۡ وَكَرَّهَ إِلَيۡكُمُ ٱلۡكُفۡرَ وَٱلۡفُسُوقَ وَٱلۡعِصۡيَانَۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلرَّٰشِدُونَ ٧

7. በውስጣችሁም የአላህ መልክተኛ መኖሩን ዕወቁ:: ከነገሩ በብዙው ቢከተላችሁ ኖሮ በእርግጥ በተቸገራችሁ ነበር:: ግን አላህ እምነትን ወደናንተ አስወደደ:: በልቦቻችሁም ውሰጥ አጌጠው:: ክህደትንና አመጽንም እንቢተኛነትንም ወደናንተ የተጠላ አደረገ:: እነዚያ (እምነትን የወደዱና ክሕደተን የጠሉ) እነርሱ ቅኖቹ ናቸው::

فَضۡلٗا مِّنَ ٱللَّهِ وَنِعۡمَةٗۚ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٞ ٨

8. ከአላህ በኾነው ችሮታና ጸጋ (ቅኖች ናቸው)፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

وَإِن طَآئِفَتَانِ مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٱقۡتَتَلُواْ فَأَصۡلِحُواْ بَيۡنَهُمَاۖ فَإِنۢ بَغَتۡ إِحۡدَىٰهُمَا عَلَى ٱلۡأُخۡرَىٰ فَقَٰتِلُواْ ٱلَّتِي تَبۡغِي حَتَّىٰ تَفِيٓءَ إِلَىٰٓ أَمۡرِ ٱللَّهِۚ فَإِن فَآءَتۡ فَأَصۡلِحُواْ بَيۡنَهُمَا بِٱلۡعَدۡلِ وَأَقۡسِطُوٓاْۖ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلۡمُقۡسِطِينَ ٩

9. ከምዕምናንም የኾኑ ሁለት ጭፍሮች ቢጋደሉ በመካከላቸው አስታርቁ፡፡ ከሁለቱ አንደኛይቱም በሌላይቱ ላይ ወሰን ብታልፍ ያችን ወሰን የምታልፈውን ወደ አላህ ትዕዛዝ እስከምትመለስ ድረስ ተጋደሉ፡፡ ብትመለስም በመካከላቸው በትክክል አስታርቁ፡፡ በነገሩ ሁሉ አስተካክሉም፡፡ አላህ አስተካካዮችን ይወዳልና፡፡

إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ إِخۡوَةٞ فَأَصۡلِحُواْ بَيۡنَ أَخَوَيۡكُمۡۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ لَعَلَّكُمۡ تُرۡحَمُونَ ١٠

10. ምእመናኖች ወንድማማቾች ናቸው፡፡ በሁለት ወንድሞቻችሁም መካከል አስታርቁ፡፡ ይታዘንላችሁም ዘንድ አላህን ፍሩ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا يَسۡخَرۡ قَوۡمٞ مِّن قَوۡمٍ عَسَىٰٓ أَن يَكُونُواْ خَيۡرٗا مِّنۡهُمۡ وَلَا نِسَآءٞ مِّن نِّسَآءٍ عَسَىٰٓ أَن يَكُنَّ خَيۡرٗا مِّنۡهُنَّۖ وَلَا تَلۡمِزُوٓاْ أَنفُسَكُمۡ وَلَا تَنَابَزُواْ بِٱلۡأَلۡقَٰبِۖ بِئۡسَ ٱلِٱسۡمُ ٱلۡفُسُوقُ بَعۡدَ ٱلۡإِيمَٰنِۚ وَمَن لَّمۡ يَتُبۡ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ١١

11. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ወንዶች ከወንዶች አይቀልዱ፡፡ ከእነርሱ የበለጡ ሊኾኑ ይከጀላልና፡፡ ሴቶችም ከሴቶች (አይሳለቁ)፡፡ ከእነርሱ የበለጡ ሊኾኑ ይከጀላልና፡፡ ነፍሶቻችሁንም አታነውሩ፡፡ በመጥፎ ስሞችም አትጠራሩ፡፡ ከእምነት በኋላ የማመጽ ስም ከፋ፡፡ ያልተጸጸተም ሰው እነዚያ እነርሱ በዳዮቹ ናቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱجۡتَنِبُواْ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلظَّنِّ إِنَّ بَعۡضَ ٱلظَّنِّ إِثۡمٞۖ وَلَا تَجَسَّسُواْ وَلَا يَغۡتَب بَّعۡضُكُم بَعۡضًاۚ أَيُحِبُّ أَحَدُكُمۡ أَن يَأۡكُلَ لَحۡمَ أَخِيهِ مَيۡتٗا فَكَرِهۡتُمُوهُۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ تَوَّابٞ رَّحِيمٞ ١٢

12. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከጥርጣሬ ብዙውን ራቁ፤ ከጥርጣሬ ከፊሉ ኃጢአት ነውና፡፡ ነውርንም አትከታተሉ፡፡ ከፊላችሁም ከፊሉን አይማ፡፡ አንደኛችሁ የወንድሙን ስጋ የሞተ ኾኖ ሊበላው ይወዳልን? (መብላቱን) ጠላችሁትም፤ (ሐሜቱንም ጥሉት)፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ አላህ ጸጸትን ተቀባይ አዛኝ ነውና፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِنَّا خَلَقۡنَٰكُم مِّن ذَكَرٖ وَأُنثَىٰ وَجَعَلۡنَٰكُمۡ شُعُوبٗا وَقَبَآئِلَ لِتَعَارَفُوٓاْۚ إِنَّ أَكۡرَمَكُمۡ عِندَ ٱللَّهِ أَتۡقَىٰكُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلِيمٌ خَبِيرٞ ١٣

13. እናንተ ሰዎች ሆይ! እኛ ከወንድና ከሴት ፈጠርናችሁ፡፡ እንድትተዋወቁም ጎሳዎችና ነገዶች አደረግናችሁ፡፡ አላህ ዘንድ በላጫችሁ በጣም አላህን ፈሪያችሁ ነው፡፡ አላህ ግልጽን ዐዋቂ ውስጥንም ዐዋቂ ነው፡፡

۞قَالَتِ ٱلۡأَعۡرَابُ ءَامَنَّاۖ قُل لَّمۡ تُؤۡمِنُواْ وَلَٰكِن قُولُوٓاْ أَسۡلَمۡنَا وَلَمَّا يَدۡخُلِ ٱلۡإِيمَٰنُ فِي قُلُوبِكُمۡۖ وَإِن تُطِيعُواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ لَا يَلِتۡكُم مِّنۡ أَعۡمَٰلِكُمۡ شَيۡـًٔاۚ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ١٤

14. የዐረብ ዘላኖች «አምነናል» አሉ፡፡ «አላመናችሁም፤ ግን ሰልመናል በሉ፡፡ «እምነቱም በልቦቻችሁ ውስጥ ገና (ጠልቆ) አልገባም፡፡ አላህንና መልክተኛውንም ብትታዘዙ ከሥራዎቻችሁ ምንንም አያጎድልባችሁም፡፡ አላህ መሓሪ አዛኝ ነውና» በላቸው፡፡

15. (እውነተኛዎቹ) ምእምናን እነዚያ በአላህና በመልእክተኛው ያመኑት ከዚያም ያልተጠራጠሩት በገንዘቦቻቸውና በነፍሶ ቻቸውም በአላህ መንገድ የታገሉት ብቻ ናቸው:: እነዚያ እነሱ እውነተኞቹ ናቸው::

إِنَّمَا ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ ثُمَّ لَمۡ يَرۡتَابُواْ وَجَٰهَدُواْ بِأَمۡوَٰلِهِمۡ وَأَنفُسِهِمۡ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلصَّٰدِقُونَ ١٥

16. «አላህ በሰማያት ውስጥ ያለውንና በምድር ውስጥ ያለውን ሁሉ የሚያውቅ ሲኾን አላህን በሃይማኖታችሁ ታስታውቁ ታላችሁን?» በላቸው:: አላህም በነገሩ ሁሉ ዐዋቂ ነው::

قُلۡ أَتُعَلِّمُونَ ٱللَّهَ بِدِينِكُمۡ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۚ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ١٦

17. በመስለማቸው በአንተ ላይ ይመጻደቃሉ «በስልምናችሁ በኔ ላይ አትመጻደቁ፤ ይልቁንም አላህ ወደ እምነት ስለ መራችሁ ይመጻደቅባችኋል፤ እውነተኞች ብትኾኑ» (መመጻደቅ ለአላህ ነው) በላቸው::

يَمُنُّونَ عَلَيۡكَ أَنۡ أَسۡلَمُواْۖ قُل لَّا تَمُنُّواْ عَلَيَّ إِسۡلَٰمَكُمۖ بَلِ ٱللَّهُ يَمُنُّ عَلَيۡكُمۡ أَنۡ هَدَىٰكُمۡ لِلۡإِيمَٰنِ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ١٧

18. አላህ የሰማያትንና የምድርን ሩቅ ምስጢር ያውቃል፤ አላህም የምትሰሩትን ሁሉ ተመልካች ነው::

إِنَّ ٱللَّهَ يَعۡلَمُ غَيۡبَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَٱللَّهُ بَصِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١٨




በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ቀ (ቃፍ) በተከበረው ቁርአን እምላለሁ (በሙሐመድ አላመኑም)::

قٓۚ وَٱلۡقُرۡءَانِ ٱلۡمَجِيدِ ١

2. ይልቁንም ከነሱ ጎሳ የኾነ አስፈራሪ ስለ መጣላቸው ተደነቁ:: ከሓዲዎቹም «ይህ አስደናቂ ነገር ነው» አሉ::

بَلۡ عَجِبُوٓاْ أَن جَآءَهُم مُّنذِرٞ مِّنۡهُمۡ فَقَالَ ٱلۡكَٰفِرُونَ هَٰذَا شَيۡءٌ عَجِيبٌ ٢

3. «በሞትንና ዐፈር በኾን ጊዜ (እንመለሳለን?) ይህ ሩቅ የኾነ መመለስ ነው፤» (አሉ)::

أَءِذَا مِتۡنَا وَكُنَّا تُرَابٗاۖ ذَٰلِكَ رَجۡعُۢ بَعِيدٞ ٣

4. ከእነርሱ (አካል) ምድር የምታጎድለውን በእርግጥ ዐውቀናል:: እኛም ዘንድ ጠባቂ መጽሐፍ አልለ::

قَدۡ عَلِمۡنَا مَا تَنقُصُ ٱلۡأَرۡضُ مِنۡهُمۡۖ وَعِندَنَا كِتَٰبٌ حَفِيظُۢ ٤

5. (አልተመለከቱም):: ይልቁንም በቁርአን በመጣላቸው ጊዜ አስተባበሉ:: እነርሱም በተማታ ነገር ውስጥ ናቸው::

بَلۡ كَذَّبُواْ بِٱلۡحَقِّ لَمَّا جَآءَهُمۡ فَهُمۡ فِيٓ أَمۡرٖ مَّرِيجٍ ٥

6. ወደ ሰማይም ከበላያቸው ስትኾን ለእርሷ ምንም ቀዳዳዎች የሌሏት ኾና እንዴት እንደ ገነባናትና (በከዋክብት) እንዳጌጥናት አልተመለከቱምን?

أَفَلَمۡ يَنظُرُوٓاْ إِلَى ٱلسَّمَآءِ فَوۡقَهُمۡ كَيۡفَ بَنَيۡنَٰهَا وَزَيَّنَّٰهَا وَمَا لَهَا مِن فُرُوجٖ ٦

7. ምድርንም ዘረጋናት፡፡ በእርሷም ውስጥ ጋራዎችን ጣልንባት፡፡ በውስጧም ከሚያስደስት ዓይነት ሁሉ አበቀልን፡፡

وَٱلۡأَرۡضَ مَدَدۡنَٰهَا وَأَلۡقَيۡنَا فِيهَا رَوَٰسِيَ وَأَنۢبَتۡنَا فِيهَا مِن كُلِّ زَوۡجِۭ بَهِيجٖ ٧

8. (ይህንን ያደረግነው) ተመላሽ ለኾነ ባሪያ ሁሉ ለማሳየትና ለማስገንዘብ ነው፡፡

تَبۡصِرَةٗ وَذِكۡرَىٰ لِكُلِّ عَبۡدٖ مُّنِيبٖ ٨

9. ከሰማይም ብሩክን ውሃ አወረድን፡፡ በእርሱም አትክልቶችንና የሚታጨድን (አዝመራ) ፍሬ አበቀልን፡፡

وَنَزَّلۡنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءٗ مُّبَٰرَكٗا فَأَنۢبَتۡنَا بِهِۦ جَنَّٰتٖ وَحَبَّ ٱلۡحَصِيدِ ٩

10. ዘምባባንም ረዣዢም ለእርሷ የተደራረበ እንቡጥ ያላት ስትኾን (አበቀልን)፡፡

وَٱلنَّخۡلَ بَاسِقَٰتٖ لَّهَا طَلۡعٞ نَّضِيدٞ ١٠

11. ለባሮቹ ሲሳይ ትኾን ዘንድ (አዘጋጀናት)፡፡ በእርሱም የሞተችን አገር ሕያው አደረግንበት፡፡ (ከመቃብር) መውጣትም እንደዚሁ ነው፡፡

رِّزۡقٗا لِّلۡعِبَادِۖ وَأَحۡيَيۡنَا بِهِۦ بَلۡدَةٗ مَّيۡتٗاۚ كَذَٰلِكَ ٱلۡخُرُوجُ ١١

12. ከእነርሱ በፊት የኑሕ ሕዝቦችና የረሰስ ሰዎች፣ ሰሙድም አስተባበሉ፡፡

كَذَّبَتۡ قَبۡلَهُمۡ قَوۡمُ نُوحٖ وَأَصۡحَٰبُ ٱلرَّسِّ وَثَمُودُ ١٢

13. ዓድም ፈርዖንም፣ የሉጥ ወንድሞችም፣

وَعَادٞ وَفِرۡعَوۡنُ وَإِخۡوَٰنُ لُوطٖ ١٣

14. የአይከት ሰዎችም የቱብበዕ ሕዝቦችም ሁሉም መልክተኞቹን አስተባበሉ፡፡ ዛቻዬም ተረጋገጠባቸው፡፡

وَأَصۡحَٰبُ ٱلۡأَيۡكَةِ وَقَوۡمُ تُبَّعٖۚ كُلّٞ كَذَّبَ ٱلرُّسُلَ فَحَقَّ وَعِيدِ ١٤

15. በፊተኛው መፍጠር ደከምን? በእውነቱ እነርሱ ከአዲስ መፍጠር በመጠራጠር ውስጥ ናቸው፡፡

أَفَعَيِينَا بِٱلۡخَلۡقِ ٱلۡأَوَّلِۚ بَلۡ هُمۡ فِي لَبۡسٖ مِّنۡ خَلۡقٖ جَدِيدٖ ١٥

16. ሰውንም ነፍሱ (በሐሳቡ) የምታጫውተውን የምናውቅ ስንኾን በእርግጥ ፈጠርነው፣ እኛም ከደም ጋኑ ጅማት ይበልጥ ወደርሱ ቅርብ ነን፡፡

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ وَنَعۡلَمُ مَا تُوَسۡوِسُ بِهِۦ نَفۡسُهُۥۖ وَنَحۡنُ أَقۡرَبُ إِلَيۡهِ مِنۡ حَبۡلِ ٱلۡوَرِيدِ ١٦

17. ሁለቱ ቃል ተቀባዮች (መላእክት) ከቀኝና ከግራ ተቀማጮች ኾነው በሚቀበሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡

إِذۡ يَتَلَقَّى ٱلۡمُتَلَقِّيَانِ عَنِ ٱلۡيَمِينِ وَعَنِ ٱلشِّمَالِ قَعِيدٞ ١٧

18. ከቃል ምንም አይናገርም በአጠገቡ ተጠባባቂና ዝግጁ የኾኑ (መላእክት) ያሉበት ቢኾን እንጅ፡፡

مَّا يَلۡفِظُ مِن قَوۡلٍ إِلَّا لَدَيۡهِ رَقِيبٌ عَتِيدٞ ١٨

| | |
|---|---|
| 19. የሞትም መከራ እውነቱን ነገር ታመጣለች፡፡ (ሰው ሆይ)፡- «ይህ ያ ከርሱ ትሸሸው የነበርከው ነው» (ይባላል)፡፡ | وَجَآءَتۡ سَكۡرَةُ ٱلۡمَوۡتِ بِٱلۡحَقِّۖ ذَٰلِكَ مَا كُنتَ مِنۡهُ تَحِيدُ ١٩ |
| 20. በቀንዱም ውስጥ ይንነፋል፡፡ ያ (ቀን) የዛቻው (መፈጸሚያ) ቀን ነው፡፡ | وَنُفِخَ فِي ٱلصُّورِۚ ذَٰلِكَ يَوۡمُ ٱلۡوَعِيدِ ٢٠ |
| 21. ነፍስም ሁሉ ከእርሷ ጋር ነጂና መስካሪ ያለባት ኾና ትመጣለች፡፡ | وَجَآءَتۡ كُلُّ نَفۡسٖ مَّعَهَا سَآئِقٞ وَشَهِيدٞ ٢١ |
| 22. «ከዚህ ነገር በእርግጥ በዝንጋቴ ውስጥ ነበርክ፡፡ ሺፋንህንም ካንተ ላይ ገለጥንልህ፡፡ ስለዚህ ዛሬ ዓይንህ ስለታም ነው» (ይባላል)፡፡ | لَّقَدۡ كُنتَ فِي غَفۡلَةٖ مِّنۡ هَٰذَا فَكَشَفۡنَا عَنكَ غِطَآءَكَ فَبَصَرُكَ ٱلۡيَوۡمَ حَدِيدٞ ٢٢ |
| 23. ቁራኛውም (መልአክ) «ይህ ያ እኔ ዘንድ ያለው ቀራቢ ነው» ይላል፡፡ | وَقَالَ قَرِينُهُۥ هَٰذَا مَا لَدَيَّ عَتِيدٌ ٢٣ |
| 24. «ሞገደኛ ከሓዲን ሁሉ በገሀነም ውስጥ ጣሉ፡፡» | أَلۡقِيَا فِي جَهَنَّمَ كُلَّ كَفَّارٍ عَنِيدٖ ٢٤ |
| 25. «ለበጎ ሥራ ከልካይ፣ በዳይ፣ ተጠራጣሪ የኾነን ሁሉ፤» (ጣሉ)፡፡ | مَّنَّاعٖ لِّلۡخَيۡرِ مُعۡتَدٖ مُّرِيبٍ ٢٥ |
| 26. «ያንን ከአላህ ጋር ሌላን አምላክ ያደረገውን በብርቱ ቅጣት ውስጥ ጣሉት፤» (ይባላል)፡፡ | ٱلَّذِي جَعَلَ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَ فَأَلۡقِيَاهُ فِي ٱلۡعَذَابِ ٱلشَّدِيدِ ٢٦ |
| 27. ቁራኛው (ሰይጣን) «ጌታችን ሆይ! እኔ አላሳሳትኩትም፡፡ ግን (ራሱ) በሩቅ ስሕተት ውስጥ ነበር» ይላል፡፡ | ۞قَالَ قَرِينُهُۥ رَبَّنَا مَآ أَطۡغَيۡتُهُۥ وَلَٰكِن كَانَ فِي ضَلَٰلِۭ بَعِيدٖ ٢٧ |
| 28. (አላህ) «ወደእናንተ ዛቻን በእርግጥ ያስቀደምኩ ስኾን እኔ ዘንድ አትጨቃጨቁ» ይላቸዋል፡፡ | قَالَ لَا تَخۡتَصِمُواْ لَدَيَّ وَقَدۡ قَدَّمۡتُ إِلَيۡكُم بِٱلۡوَعِيدِ ٢٨ |
| 29. «ቃሉ እኔ ዘንድ አይለወጥም፡፡ እኔም ለባሮቼ ፈጽሞ በዳይ አይደለሁም» (ይላቸዋል)፡፡ | مَا يُبَدَّلُ ٱلۡقَوۡلُ لَدَيَّ وَمَآ أَنَا۠ بِظَلَّٰمٖ لِّلۡعَبِيدِ ٢٩ |
| 30. ለገሀነም «ሞላሽን? የምንልበትንና ጭማሪ አለን? የምትልበትን ቀን» (አስጠንቅቃቸው)፡፡ | يَوۡمَ نَقُولُ لِجَهَنَّمَ هَلِ ٱمۡتَلَأۡتِ وَتَقُولُ هَلۡ مِن مَّزِيدٖ ٣٠ |
| 31. ገነትም አላህን ለፈሩት እሩቅ ባልኾነ ስፍራ ትቀቀረባለች፡፡ | وَأُزۡلِفَتِ ٱلۡجَنَّةُ لِلۡمُتَّقِينَ غَيۡرَ بَعِيدٍ ٣١ |
| 32. «ይህ ወደ አላህ ተመላሽና (ሕግጋቱን) ጠባቂ ለኾነ ሁሉ የተቀጠራችሁት ነው» (ይባላሉ)፡፡ | هَٰذَا مَا تُوعَدُونَ لِكُلِّ أَوَّابٍ حَفِيظٖ ٣٢ |
| 33. «አልረሕማንን በሩቁ ኾኖ ለፈራና በንጹሕ ልብ ለመጣ» (ትቀቀረባለች)፡፡ | مَّنۡ خَشِيَ ٱلرَّحۡمَٰنَ بِٱلۡغَيۡبِ وَجَآءَ بِقَلۡبٖ مُّنِيبٍ ٣٣ |

34. «በሰላም ግቧት ይህ የመዘውተሪያ ቀን ነው» (ይባላሉ)::

ٱدۡخُلُوهَا بِسَلَٰمٖۖ ذَٰلِكَ يَوۡمُ ٱلۡخُلُودِ ٣٤

35. ለነርሱ በውስጧ ሲኾኑ የሚሹት ሁሉ አልላቸው:: እኛም ዘንድ ጭማሪ አልለ::

لَهُم مَّا يَشَآءُونَ فِيهَا وَلَدَيۡنَا مَزِيدٞ ٣٥

36. ከእነርሱም (ከቁረይሾች) በፊት ከክፍለ ዘመናት ሕዝቦች ብዙዎችን እነርሱ በኀያልነት ከእነርሱ ይበልጥ የበረቱ የኾኑትን (ማምለጫ ፍለጋ) በየአገሮቹም የመረመሩትን አጥፍተናል:: ማምለጫ አለን?

وَكَمۡ أَهۡلَكۡنَا قَبۡلَهُم مِّن قَرۡنٍ هُمۡ أَشَدُّ مِنۡهُم بَطۡشٗا فَنَقَّبُواْ فِي ٱلۡبِلَٰدِ هَلۡ مِن مَّحِيصٍ ٣٦

37. በዚህ ውሰጥ ለእርሱ ልብ ላለው ወይም እርሱ (በልቡ) የተጣደ ኾኖ (ወደሚነበብለት) ጆሮውን ለጣለ ሰው ግሳጼ አለበት::

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَذِكۡرَىٰ لِمَن كَانَ لَهُۥ قَلۡبٌ أَوۡ أَلۡقَى ٱلسَّمۡعَ وَهُوَ شَهِيدٞ ٣٧

38. ሰማያትንና ምድርን በመካከላቸው ያለውንም ሁሉ በስድስት ቀናት ውስጥ በእርግጥ ፈጠርን:: ድካምም ምንም አልነካንም::

وَلَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ وَمَا بَيۡنَهُمَا فِي سِتَّةِ أَيَّامٖ وَمَا مَسَّنَا مِن لُّغُوبٖ ٣٨

39. በሚሉትም ላይ ታገሥ፤ ጌታህንም ከማመስገን ጋር ፀሐይ ከመውጣቷ በፊት ከመግባቷም በፊት አወድሰው::

فَٱصۡبِرۡ عَلَىٰ مَا يَقُولُونَ وَسَبِّحۡ بِحَمۡدِ رَبِّكَ قَبۡلَ طُلُوعِ ٱلشَّمۡسِ وَقَبۡلَ ٱلۡغُرُوبِ ٣٩

40. ከሌሊቱም አወድሰው ከስግደቶችም በኋላዎች (አወድሰው)::

وَمِنَ ٱلَّيۡلِ فَسَبِّحۡهُ وَأَدۡبَٰرَ ٱلسُّجُودِ ٤٠

41. (የሚነገርህን) አዳምጥም:: ጠሪው ከቅርብ ስፍራ በሚጠራበት ቀን (ከመቃብራቸው ይወጣሉ)::

وَٱسۡتَمِعۡ يَوۡمَ يُنَادِ ٱلۡمُنَادِ مِن مَّكَانٖ قَرِيبٖ ٤١

42. ጩኸቲቱን በእውነት የሚሰሙበት ቀን ያ (ከመቃብር) የመውጫው ቀን ነው::

يَوۡمَ يَسۡمَعُونَ ٱلصَّيۡحَةَ بِٱلۡحَقِّۚ ذَٰلِكَ يَوۡمُ ٱلۡخُرُوجِ ٤٢

43. እኛ እኛው ሕያው እናደርጋለን:: እንገድላለንም:: መመለሻም ወደእኛ ብቻ ነው::

إِنَّا نَحۡنُ نُحۡيِۦ وَنُمِيتُ وَإِلَيۡنَا ٱلۡمَصِيرُ ٤٣

44. የሚፈጥኑ ኾነው ምድር ከእነርሱ ላይ የምትሰነጣጠቅበት ቀን (የመውጫው ቀን ነው):: ይህ በእኛ ላይ ገር የኾነ መሰብሰብ ነው::

يَوۡمَ تَشَقَّقُ ٱلۡأَرۡضُ عَنۡهُمۡ سِرَاعٗاۚ ذَٰلِكَ حَشۡرٌ عَلَيۡنَا يَسِيرٞ ٤٤

45. እኛ የሚሉትን ሁሉ ዐዋቂ ነን:: አንተም በእነርሱ ላይ አስገዳጅ አይደለህም:: ስለዚህ ዛቻየን የሚፈራን ሰው በቁርኣን አስታውስ::

نَّحۡنُ أَعۡلَمُ بِمَا يَقُولُونَۖ وَمَآ أَنتَ عَلَيۡهِم بِجَبَّارٖۖ فَذَكِّرۡ بِٱلۡقُرۡءَانِ مَن يَخَافُ وَعِيدِ ٤٥

# ሱረቱ አል ዛሪያት

# سورة الذاريات

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. መበተንን በታኞች በኾኑት (ነፋሶች)::

وَٱلذَّٰرِيَٰتِ ذَرۡوٗا ﴿١﴾

2. ከባድ (ዝናምን) ተሸካሚዎች በኾኑትም (ደመናዎች)::

فَٱلۡحَٰمِلَٰتِ وِقۡرٗا ﴿٢﴾

3. ገር (መንሻለልን) ተንሻላዮች በኾኑትም (መርከቦች)::

فَٱلۡجَٰرِيَٰتِ يُسۡرٗا ﴿٣﴾

4. ነገርን ሁሉ አከፋፋዮች በኾኑትም (መላእክት) እምላለሁ::

فَٱلۡمُقَسِّمَٰتِ أَمۡرًا ﴿٤﴾

5. የምትቀጠሩት (ትንሣኤ) እውነት ነው::

إِنَّمَا تُوعَدُونَ لَصَادِقٞ ﴿٥﴾

6. (እንደየሥራው) ዋጋን ማግኘትም፤ ኋኝ ነው፤ (የማይቀር ነው)::

وَإِنَّ ٱلدِّينَ لَوَٰقِعٞ ﴿٦﴾

7. የ(ከዋክብት) መንገዶች ባለቤት በኾነችው ሰማይ እምላለሁ::

وَٱلسَّمَآءِ ذَاتِ ٱلۡحُبُكِ ﴿٧﴾

8. እናንተ (የመካ ሰዎች) በተለያየ ቃል ውስጥ ናችሁ::

إِنَّكُمۡ لَفِي قَوۡلٖ مُّخۡتَلِفٖ ﴿٨﴾

9. ከርሱ የሚዝዞር ሰው ይዝዞራል::

يُؤۡفَكُ عَنۡهُ مَنۡ أُفِكَ ﴿٩﴾

10. በግምት የሚናገሩ ውሸታሞች ተረገሙ::

قُتِلَ ٱلۡخَرَّٰصُونَ ﴿١٠﴾

11. እነዚያ እነርሱ በሚሸፍን ስሕተተ ውስጥ ዘንጊዎች የኾኑት::

ٱلَّذِينَ هُمۡ فِي غَمۡرَةٖ سَاهُونَ ﴿١١﴾

12. የዋጋ መስጫው ቀን መቼ እንደ ኾነ ይጠይቃሉ::

يَسۡـَٔلُونَ أَيَّانَ يَوۡمُ ٱلدِّينِ ﴿١٢﴾

13. (እነርሱ) በእሳት ላይ በሚፈተኑበት ቀን ነው::

يَوۡمَ هُمۡ عَلَى ٱلنَّارِ يُفۡتَنُونَ ﴿١٣﴾

14. «መከራችሁን ቅመሱ፤ ይህ ያ በእርሱ ትቻኮሉበት የነበራችሁት ነው» (ይባላሉ)::

ذُوقُواْ فِتۡنَتَكُمۡ هَٰذَا ٱلَّذِي كُنتُم بِهِۦ تَسۡتَعۡجِلُونَ ﴿١٤﴾

15. አላህን ፈሪዎቹ በአትክልቶችና በምንጮች ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُتَّقِينَ فِي جَنَّٰتٖ وَعُيُونٍ ١٥

16. ያንን ጌታቸው የሰጣቸውን ተቀባዮች ኾነው፤ (በገነት ውስጥ ይኾናሉ)፡፡ እነርሱ ከዚህ በፊት መልካም ሰሪዎች ነበሩና፡፡

ءَاخِذِينَ مَآ ءَاتَىٰهُمۡ رَبُّهُمۡۚ إِنَّهُمۡ كَانُواْ قَبۡلَ ذَٰلِكَ مُحۡسِنِينَ ١٦

17. ከሌሊቱ ጥቂትን ብቻ ይተኙ ነበሩ፡፡

كَانُواْ قَلِيلٗا مِّنَ ٱلَّيۡلِ مَا يَهۡجَعُونَ ١٧

18. በሌሊቱ መጨረሻዎችም እነርሱ ምሕረትን ይለምናሉ፡፡

وَبِٱلۡأَسۡحَارِ هُمۡ يَسۡتَغۡفِرُونَ ١٨

19. በገንዘቦቻቸውም ውስጥ ለለማኝና (ከልመና) ለተከለከለም (በችሮታቸው) መብት አለለ፡፡

وَفِيٓ أَمۡوَٰلِهِمۡ حَقّٞ لِّلسَّآئِلِ وَٱلۡمَحۡرُومِ ١٩

20. በምድርም ውስጥ ለሚያረጋግጡ ሰዎች ምልክቶች አልሉ፡፡

وَفِي ٱلۡأَرۡضِ ءَايَٰتٞ لِّلۡمُوقِنِينَ ٢٠

21. በነፍሶቻችሁም ውስጥ (ምልክቶች አልሉ)፤ ታዲያ አትመለከቱምን?›

وَفِيٓ أَنفُسِكُمۡۚ أَفَلَا تُبۡصِرُونَ ٢١

22. ሲሳያችሁም የምትቀጠሩትም (ፍዳና ምንዳ) በሰማይ ውስጥ ነው፡፡

وَفِي ٱلسَّمَآءِ رِزۡقُكُمۡ وَمَا تُوعَدُونَ ٢٢

23. በሰማይና በምድር ጌታም እምላለሁ፡፡ እርሱ እናንተ እንደምትናገሩት ብጤ እርግጠኛ ነው፡፡

فَوَرَبِّ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِ إِنَّهُۥ لَحَقّٞ مِّثۡلَ مَآ أَنَّكُمۡ تَنطِقُونَ ٢٣

24. የተከበሩት የኢብራሂም እንግዶች ወሬ መጥቶሃልን?

هَلۡ أَتَىٰكَ حَدِيثُ ضَيۡفِ إِبۡرَٰهِيمَ ٱلۡمُكۡرَمِينَ ٢٤

25. በእርሱ ላይ በገቡና «ሰለም» ባሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ «ሰላም ያልታወቃችሁ ሕዝቦች ናችሁ፤» አላቸው፡፡

إِذۡ دَخَلُواْ عَلَيۡهِ فَقَالُواْ سَلَٰمٗاۖ قَالَ سَلَٰمٞ قَوۡمٞ مُّنكَرُونَ ٢٥

26. ወደ ቤተሰቡም ተዘነበለ፤» ወዲያውም የሰባ ወይፈንን አመጣ፡፡

فَرَاغَ إِلَىٰٓ أَهۡلِهِۦ فَجَآءَ بِعِجۡلٖ سَمِينٖ ٢٦

27. ወደእነርሱም (አርዶና ጠብሶ) አቀረበው፡፡ «አትበሉም ወይ?» አላቸው፡፡

فَقَرَّبَهُۥٓ إِلَيۡهِمۡ قَالَ أَلَا تَأۡكُلُونَ ٢٧

28. ከእነርሱ መፍራትንም በልቡ አሳደረ፡፡ «አትፍራ» አሉት፡፡ በዐዋቂ ወጣት ልጅም አበሰሩት፡፡

فَأَوۡجَسَ مِنۡهُمۡ خِيفَةٗۖ قَالُواْ لَا تَخَفۡۖ وَبَشَّرُوهُ بِغُلَٰمٍ عَلِيمٖ ٢٨

29. ሚስቱም እየጮኸች መጣች፡፡ ፊቷንም መታች፡፡ «መካን አሮጊት ነኝ» አለችም፡፡

فَأَقۡبَلَتِ ٱمۡرَأَتُهُۥ فِي صَرَّةٖ فَصَكَّتۡ وَجۡهَهَا وَقَالَتۡ عَجُوزٌ عَقِيمٞ ٢٩

30. እንደዚህ ጌታሽ ብሏል፡፡ «እነሆ እርሱ ጥበባ ዐዋቂ ነውና» አሏት፡፡

قَالُواْ كَذَٰلِكِ قَالَ رَبُّكِۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡحَكِيمُ ٱلۡعَلِيمُ ٣٠

31. «እናንተ መልክተኞች ሆይ! ታዲያ ነገራችሁ ምንድን ነው?» አላቸው፡፡

۞قَالَ فَمَا خَطۡبُكُمۡ أَيُّهَا ٱلۡمُرۡسَلُونَ ٣١

32. (እነርሱም) አሉ፡- «እኛ ወደ አመጸኞች ሕዝቦች ተልከናል፡፡»

قَالُوٓاْ إِنَّآ أُرۡسِلۡنَآ إِلَىٰ قَوۡمٖ مُّجۡرِمِينَ ٣٢

33. በእነርሱ ላይ ከጭቃ የኾኑን ድንጋዮች ልንለቅባቸው (ተላክን)፡፡

لِنُرۡسِلَ عَلَيۡهِمۡ حِجَارَةٗ مِّن طِينٖ ٣٣

34. በጌታህ ዘንድ ለድንበር አላፊዎቹ (በየስማቸው) ምልክት የተደረገባት ስትኾን፡፡

مُّسَوَّمَةً عِندَ رَبِّكَ لِلۡمُسۡرِفِينَ ٣٤

35. ከምእምናንም፤ በእርሷ (በከተማቸው) ውስጥ የነበሩትን አወጣን፡፡

فَأَخۡرَجۡنَا مَن كَانَ فِيهَا مِنَ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٣٥

36. በውስጧም ከሙስሊሞች ከአንድ ቤት (ቤተሰቦች) በስተቀር አላገኘንም፡፡

فَمَا وَجَدۡنَا فِيهَا غَيۡرَ بَيۡتٖ مِّنَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ٣٦

37. በውስጧም ለእነዚያ አሳማሚውን ቅጣት ለሚፈሩት ምልክትን አስቀረን፡፡

وَتَرَكۡنَا فِيهَآ ءَايَةٗ لِّلَّذِينَ يَخَافُونَ ٱلۡعَذَابَ ٱلۡأَلِيمَ ٣٧

38. በሙሳም (ወሬ) ውስጥ ወደ ፈርዖን በግልጽ ማስረጃ በላክነው ጊዜ (ምልክትን አደረግን)፡፡

وَفِي مُوسَىٰٓ إِذۡ أَرۡسَلۡنَٰهُ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ بِسُلۡطَٰنٖ مُّبِينٖ ٣٨

39. ከድጋፉ (ከሰራዊቱ) ጋርም (ከእምነት) ዞረ፡፡ (እርሱ) «ድግምተኛ ወይም ዕብድ ነው» አለም፡፡

فَتَوَلَّىٰ بِرُكۡنِهِۦ وَقَالَ سَٰحِرٌ أَوۡ مَجۡنُونٞ ٣٩

40. እርሱንም ሰራዊቱንም ያዝናቸው፡፡ እርሱ ተወቃሽ ሲኾን በባሕር ውስጥም ጣልናቸው፡፡

فَأَخَذۡنَٰهُ وَجُنُودَهُۥ فَنَبَذۡنَٰهُمۡ فِي ٱلۡيَمِّ وَهُوَ مُلِيمٞ ٤٠

41. በዓድም በእነርሱ ላይ መካንን ነፋስ በላክን ጊዜ (ምልክት አልለ)፡፡

وَفِي عَادٍ إِذۡ أَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمُ ٱلرِّيحَ ٱلۡعَقِيمَ ٤١

42. በላዩ ላይ የመጣችበትን ማንኛውንም ነገር እንደ በሰበሰ አጥንት ያደረገችው ብትኾን እንጂ አትተወውም፡፡

مَا تَذَرُ مِن شَيۡءٍ أَتَتۡ عَلَيۡهِ إِلَّا جَعَلَتۡهُ كَٱلرَّمِيمِ ٤٢

43. በሰሙድም ለእነርሱ «እስከ ጊዜ (ሞታችሁ) ድረስ ተጣቀሙ» በተባሉ ጊዜ (ምልክት አልለ)፡፡

وَفِي ثَمُودَ إِذۡ قِيلَ لَهُمۡ تَمَتَّعُواْ حَتَّىٰ حِينٖ ٤٣

44. ከጌታቸው ትዕዛዝም ኮሩ፡፡ እነርሱም እያዩ ጩኸት ያዘቻቸው፡፡

فَعَتَوۡاْ عَنۡ أَمۡرِ رَبِّهِمۡ فَأَخَذَتۡهُمُ ٱلصَّٰعِقَةُ وَهُمۡ يَنظُرُونَ ٤٤

45. መቆምንም ምንም አልቻሉም፡፡ የሚርረዱም አልነበሩም፡፡

فَمَا ٱسۡتَطَٰعُواْ مِن قِيَامٖ وَمَا كَانُواْ مُنتَصِرِينَ ٤٥

46. የኑሕንም ሕዝቦች ከዚህ በፊት (አጠፋን)፡፡ እነርሱ አመጸኞች ሕዝቦች ነበሩና፡፡

وَقَوۡمَ نُوحٖ مِّن قَبۡلُۖ إِنَّهُمۡ كَانُواْ قَوۡمٗا فَٰسِقِينَ ٤٦

47. ሰማይንም በኀይል ገነባናት፡፡ እኛም በእርግጥ ቻዮች ነን፡፡

وَٱلسَّمَآءَ بَنَيۡنَٰهَا بِأَيۡيْدٖ وَإِنَّا لَمُوسِعُونَ ٤٧

48. ምድርንም ዘረጋናት፡፡ ምን ያማርንም ዘርጊዎች (ነን!)

وَٱلۡأَرۡضَ فَرَشۡنَٰهَا فَنِعۡمَ ٱلۡمَٰهِدُونَ ٤٨

49. ትገነዘቡም ዘንድ ከነገሩ ሁሉ ሁለት (ተቃራኒ) ዓይነትን ፈጠርን፡፡

وَمِن كُلِّ شَيۡءٍ خَلَقۡنَا زَوۡجَيۡنِ لَعَلَّكُمۡ تَذَكَّرُونَ ٤٩

50. «ወደ አላህም ሽሹ፤ እኔ ለእናንተ ከርሱ ግልጽ አስጠንቃቂ ነኝና» (በላቸው)፡፡

فَفِرُّوٓاْ إِلَى ٱللَّهِۖ إِنِّي لَكُم مِّنۡهُ نَذِيرٞ مُّبِينٞ ٥٠

51. ከአላህም ጋር ሌላን አምላክ አታድርጉ፡፡ እኔ ለእናንተ ከእርሱ (የተላክሁ) ግልጽ አስፈራሪ ነኝና፡፡

وَلَا تَجۡعَلُواْ مَعَ ٱللَّهِ إِلَٰهًا ءَاخَرَۖ إِنِّي لَكُم مِّنۡهُ نَذِيرٞ مُّبِينٞ ٥١

52. (ነገሩ) እንደዚሁ ነው፡፡ እነዚያን ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ከመልክተኛ ማንም አልመጣቸውም፡፡ (እርሱ) «ድግምተኛ ወይም ዕብድ ነው» ያሉ ቢኾኑ እንጂ፡፡

كَذَٰلِكَ مَآ أَتَى ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِم مِّن رَّسُولٍ إِلَّا قَالُواْ سَاحِرٌ أَوۡ مَجۡنُونٌ ٥٢

53. በእርሱ (በዚህ ቃል) አደራ ተባብለዋልን? አይደለም፤ እነርሱ ጥጋበኞች ሕዝቦች ናቸው፡፡

أَتَوَاصَوۡاْ بِهِۦۚ بَلۡ هُمۡ قَوۡمٞ طَاغُونَ ٥٣

54. ከእነርሱም (ክርክር) ዘወር በል፤ (ተዋቸው)፡፡ አንተ ምንም ተወቃሽ አይደለህምና፡፡

فَتَوَلَّ عَنۡهُمۡ فَمَآ أَنتَ بِمَلُومٖ ٥٤

55. ገሥጽም፤ ግሣጼ ምእመናንን ትጠቅማለችና፡፡

وَذَكِّرۡ فَإِنَّ ٱلذِّكۡرَىٰ تَنفَعُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ ٥٥

56. ጋኔንንና ሰውንም ሊግገዙኝ እንጅ ለሌላ አልፈጠርኳቸውም፡፡

وَمَا خَلَقۡتُ ٱلۡجِنَّ وَٱلۡإِنسَ إِلَّا لِيَعۡبُدُونِ ٥٦

57. ከነርሱም ምንም ሲሳይ አልፈልግም፡፡ ሊመግቡኝም አልሻም፡፡

مَآ أُرِيدُ مِنۡهُم مِّن رِّزۡقٖ وَمَآ أُرِيدُ أَن يُطۡعِمُونِ ٥٧

58. አላህ እርሱ ሲሳይን ሰጪ የብርቱ ኀይል ባለቤት ነው፡፡

إِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلرَّزَّاقُ ذُو ٱلۡقُوَّةِ ٱلۡمَتِينُ ٥٨

59. ለእነዚያም ለበደሉት እንደ ጓደኞቻቸው ፋንታ ብጤ (የቅጣት) ፋንታ አልላቸው፡፡ ስለዚህ አያስቸኩሉኝ፡፡

فَإِنَّ لِلَّذِينَ ظَلَمُواْ ذَنُوبٗا مِّثۡلَ ذَنُوبِ أَصۡحَٰبِهِمۡ فَلَا يَسۡتَعۡجِلُونِ ٥٩

60. ለነዚያም ለካዱት ከዚያ ከሚቀጠሩት ቀናቸው ወዮላቸው፡

فَوَيۡلٞ لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن يَوۡمِهِمُ ٱلَّذِي يُوعَدُونَ ٦٠

# ሱረቱ አል ጡር

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

1. በጡር (ጋራ) እምላለሁ፡፡

2. በተጻፈው መጽሐፍም፡፡

3. በተዘረጋ ብራና ላይ፤ (በተጻፈው)፡፡

4. በደመቀው ቤትም፡፡

5. ከፍ በተደረገው ጣራም፡፡

6. በተመላው ባሕርም እምላለሁ፡፡

7. የጌታህ ቅጣት በእርግጥ ወዳቂ ነው፤ (የማይቀር ነው)፡፡

8. ለእርሱ ምንም ገፍታሪ የለውም፡፡

9. ሰማይ ብርቱ መዞርን በምትዞርበት ቀን (ይኾናል)፡፡

10. ተራራዎችም መኼድን በሚኼዱበት (ቀን)፡፡

11. ለአስተባባዮችም ያን ጊዜ ወዮላቸው፡፡

12. ለእነዚያ እነርሱ በውሸት ውስጥ የሚጫወቱ ለኾኑት፡፡

13. ወደ ገሀነም እሳት በኀይል መግገፍተርን በሚግገፈተሩበት ቀን፡፡

14. ይህቺ ያቺ በእርሷ ታስተባብሉባት የነበራችሁት እሳት ናት፡፡

# سورة الطور

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

وَٱلطُّورِ ١

وَكِتَٰبٖ مَّسۡطُورٖ ٢

فِي رَقّٖ مَّنشُورٖ ٣

وَٱلۡبَيۡتِ ٱلۡمَعۡمُورِ ٤

وَٱلسَّقۡفِ ٱلۡمَرۡفُوعِ ٥

وَٱلۡبَحۡرِ ٱلۡمَسۡجُورِ ٦

إِنَّ عَذَابَ رَبِّكَ لَوَٰقِعٞ ٧

مَّا لَهُۥ مِن دَافِعٖ ٨

يَوۡمَ تَمُورُ ٱلسَّمَآءُ مَوۡرٗا ٩

وَتَسِيرُ ٱلۡجِبَالُ سَيۡرٗا ١٠

فَوَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ١١

ٱلَّذِينَ هُمۡ فِي خَوۡضٖ يَلۡعَبُونَ ١٢

يَوۡمَ يُدَعُّونَ إِلَىٰ نَارِ جَهَنَّمَ دَعًّا ١٣

هَٰذِهِ ٱلنَّارُ ٱلَّتِي كُنتُم بِهَا تُكَذِّبُونَ ١٤

15. ይህ (ፊት ትሉ እንደነበራችሁት) ድግምት ነውን? ወይስ እናንተ አታዩምን?

أَفَسِحۡرٌ هَٰذَآ أَمۡ أَنتُمۡ لَا تُبۡصِرُونَ ١٥

16. ግቧት ታገሱም ወይም አትታገሡ በእናንተ ላይ እኩል ነው፡፡ የምትምመነዱት ትሠሩት የነበራችሁትን (ፍዳ) ብቻ ነው (ይባላሉ)፡፡

ٱصۡلَوۡهَا فَٱصۡبِرُوٓاْ أَوۡ لَا تَصۡبِرُواْ سَوَآءٌ عَلَيۡكُمۡۖ إِنَّمَا تُجۡزَوۡنَ مَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ١٦

17. አላህን ፈሪዎቹ በእርግጥ በገነቶችና በጸጋ ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُتَّقِينَ فِي جَنَّٰتٖ وَنَعِيمٖ ١٧

18. ጌታቸው በሰጣቸው ጸጋ ተደሳቾች ኾነው (በገነት ውስጥ ናቸው)፡፡ የገሀነምንም ስቃይ ጌታቸው ጠበቃቸው፡፡

فَٰكِهِينَ بِمَآ ءَاتَىٰهُمۡ رَبُّهُمۡ وَوَقَىٰهُمۡ رَبُّهُمۡ عَذَابَ ٱلۡجَحِيمِ ١٨

19. «ትሠሩት በነበራችሁት ምክንያት ተደሳቾች ኾናችሁ ብሉ፤ ጠጡም፤» (ይባላሉ)፡፡

كُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ هَنِيٓـَٔۢا بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ١٩

20. በተደረደሩ አልጋዎች ላይ ተደጋፊዎች ኾነው (በገነት ይኖራሉ)፡፡ ዓይናማዎች በኾኑ ነጫጭ ሴቶችም እናጠናዳቸዋለን፡፡

مُتَّكِـِٔينَ عَلَىٰ سُرُرٖ مَّصۡفُوفَةٖۖ وَزَوَّجۡنَٰهُم بِحُورٍ عِينٖ ٢٠

21. እነዚያም ያመኑትና ዝርያቸውም በእምነት የተከተለቻቸው ዝርያቸውን በእነርሱ እናስጠጋለን፡፡ ከሥራቸውም ምንም አናጎድልባቸውም፡፡ ሰው ሁሉ በሠራው ሥራ ተያዢ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَٱتَّبَعَتۡهُمۡ ذُرِّيَّتُهُم بِإِيمَٰنٍ أَلۡحَقۡنَا بِهِمۡ ذُرِّيَّتَهُمۡ وَمَآ أَلَتۡنَٰهُم مِّنۡ عَمَلِهِم مِّن شَيۡءٖۚ كُلُّ ٱمۡرِيِٕۭ بِمَا كَسَبَ رَهِينٞ ٢١

22. ከሚሹትም ሁሉ እሸትንና ስጋን እንጨምርላቸዋለን፡፡

وَأَمۡدَدۡنَٰهُم بِفَٰكِهَةٖ وَلَحۡمٖ مِّمَّا يَشۡتَهُونَ ٢٢

23. በውስጧ መጠጥን ይሰጣጣሉ፡፡ በውስጧ ውድቅ ንግግርና መውወንጀልም የለም፡፡

يَتَنَٰزَعُونَ فِيهَا كَأۡسٗا لَّا لَغۡوٞ فِيهَا وَلَا تَأۡثِيمٞ ٢٣

24. ለነርሱም የኾኑ ወጣቶች ልክ የተሸፈነ ሉል መስለው በእነርሱ ላይ (ለማሳለፍ) ይዘዋወራሉ፡፡

۞وَيَطُوفُ عَلَيۡهِمۡ غِلۡمَانٞ لَّهُمۡ كَأَنَّهُمۡ لُؤۡلُؤٞ مَّكۡنُونٞ ٢٤

25. የሚጠያየቁ ኾነውም ከፊላቸው በከፊሉ ላይ ይዞራል፡፡

وَأَقۡبَلَ بَعۡضُهُمۡ عَلَىٰ بَعۡضٖ يَتَسَآءَلُونَ ٢٥

26. «እኛ ፊት በቤተሰቦቻችን ውስጥ (ከቅጣት) ፈሪዎች ነበርን» ይላሉ፡፡

قَالُوٓاْ إِنَّا كُنَّا قَبۡلُ فِيٓ أَهۡلِنَا مُشۡفِقِينَ ٢٦

27. «አላህም በእኛ ላይ ለገሰ፡፡ የመርዛም እሳት ቅጣትንም ጠበቀን፡፡

فَمَنَّ ٱللَّهُ عَلَيۡنَا وَوَقَىٰنَا عَذَابَ ٱلسَّمُومِ ٢٧

28. «እኛ ከዚህ በፊት እንለምነው ነበርን፡፡ እነሆ እርሱ በጎ ዋይ አዛኝ ነውና» (ይላሉ)፡፡

إِنَّا كُنَّا مِن قَبۡلُ نَدۡعُوهُۖ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلۡبَرُّ ٱلرَّحِيمُ ٢٨

29. (ሰዎችን) አስታውስም፡፡ አንተም በጌታህ ጸጋ ምክንያት ጠንቋይም ዕብድም አይደለህም፡፡

فَذَكِّرۡ فَمَآ أَنتَ بِنِعۡمَتِ رَبِّكَ بِكَاهِنٖ وَلَا مَجۡنُونٍ ٢٩

30. ይልቁንም የሞትን አደጋ በእርሱ የምንጠባበቅበት የኾነ ባለ ቅኔ ነው ይላሉን?

أَمۡ يَقُولُونَ شَاعِرٞ نَّتَرَبَّصُ بِهِۦ رَيۡبَ ٱلۡمَنُونِ ٣٠

31. «ተጠባበቁ፤ እኔም ከእናንተ ጋር ከሚጠባበቁት ነኝ» በላቸው፡፡

قُلۡ تَرَبَّصُواْ فَإِنِّي مَعَكُم مِّنَ ٱلۡمُتَرَبِّصِينَ ٣١

32. አእምሮዎቻቸው በዚህ ያዟቸዋልን? አይደለም በእውነቱ እነርሱ ወሰን አላፊዎች ሕዝቦች ናቸው፡፡

أَمۡ تَأۡمُرُهُمۡ أَحۡلَٰمُهُم بِهَٰذَآۚ أَمۡ هُمۡ قَوۡمٞ طَاغُونَ ٣٢

33. ወይም «ቀጠፈው ይላሉን?» አይደለም፤ በእውነቱ አያምኑም፡፡

أَمۡ يَقُولُونَ تَقَوَّلَهُۥۚ بَل لَّا يُؤۡمِنُونَ ٣٣

34. እውነተኞችም ቢኾኑ መሰሉ የኾነን ንግግር ያምጡ፡፡

فَلۡيَأۡتُواْ بِحَدِيثٖ مِّثۡلِهِۦٓ إِن كَانُواْ صَٰدِقِينَ ٣٤

35. ወይስ ያለ አንዳች (ፈጣሪ) ተፈጠሩን? ወይስ እነርሱ ፈጣሪዎች ናቸውን?

أَمۡ خُلِقُواْ مِنۡ غَيۡرِ شَيۡءٍ أَمۡ هُمُ ٱلۡخَٰلِقُونَ ٣٥

36. ወይስ ሰማያትንና ምድርን ፈጠሩን? አይደለም አያረጋግጡም፡፡

أَمۡ خَلَقُواْ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَۚ بَل لَّا يُوقِنُونَ ٣٦

37. ወይስ የጌታህ ግምጃ ቤቶች እነርሱ ዘንድ ናቸውን? ወይስ እነርሱ አሸናፊዎች ናቸውን?

أَمۡ عِندَهُمۡ خَزَآئِنُ رَبِّكَ أَمۡ هُمُ ٱلۡمُصَيۡطِرُونَ ٣٧

38. ወይስ ለእነርሱ በእርሱ ላይ (ከሰማይ) የሚያዳምጡበት መሰላል አላቸውን? አድማጫቸውም (ሰማሁ ቢል) ግልጽን አስረጅ ያምጣ፡፡

أَمۡ لَهُمۡ سُلَّمٞ يَسۡتَمِعُونَ فِيهِۖ فَلۡيَأۡتِ مُسۡتَمِعُهُم بِسُلۡطَٰنٖ مُّبِينٍ ٣٨

39. ወይስ ለእርሱ ሴቶች ልጆች አሉትን? ለእናንተም ወንዶች ልጆች አሏችሁን?

أَمۡ لَهُ ٱلۡبَنَٰتُ وَلَكُمُ ٱلۡبَنُونَ ٣٩

40. ወይስ ዋጋን ትጠይቃቸዋለህን? ስለዚህ እነርሱ ከዕዳው የተከበዱ ናቸውን?

أَمۡ تَسۡـَٔلُهُمۡ أَجۡرٗا فَهُم مِّن مَّغۡرَمٖ مُّثۡقَلُونَ ٤٠

41. ወይስ ሩቁ ምስጢር እነርሱ ዘንድ ነውን? ስለዚህ እነርሱ ይጽፋሉን?

أَمۡ عِندَهُمُ ٱلۡغَيۡبُ فَهُمۡ يَكۡتُبُونَ ٤١

42. ወይስ ተንኮልን (ባንተ) ይሻሉን? እነዚያም የካዱት እነርሱ በተንኮል ተሸናፊዎች ናቸው፡፡

أَمۡ يُرِيدُونَ كَيۡدٗاۖ فَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ هُمُ ٱلۡمَكِيدُونَ ٤٢

43. ወይስ ለእነርሱ ከአላህ ሌላ አምላክ አላቸውን? አላህ ከሚያጋሩት ሁሉ ጠራ፡፡

أَمۡ لَهُمۡ إِلَٰهٌ غَيۡرُ ٱللَّهِۚ سُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ٤٣

44. ከሰማይም ቁራጭን (በእነርሱ ላይ) ወዳቂ ኾኖ ቢያዩ ኖሮ «ይህ የተደራረበ ደመና ነው» ይሉ ነበር፡፡

وَإِن يَرَوۡاْ كِسۡفٗا مِّنَ ٱلسَّمَآءِ سَاقِطٗا يَقُولُواْ سَحَابٞ مَّرۡكُومٞ ٤٤

45. ያንንም በእርሱ የሚግገደሉበትን ቀናቸውን እስከሚገናኙ ድረስ ተዋቸው፡፡

فَذَرۡهُمۡ حَتَّىٰ يُلَٰقُواْ يَوۡمَهُمُ ٱلَّذِي فِيهِ يُصۡعَقُونَ ٤٥

46. ተንኮላቸው ከእነርሱ ምንንም የማይጠቅማቸውንና እነርሱም የማይርረዱበትን ቀን (እስከ ሚገናኙ ተዋቸው)፡፡

يَوۡمَ لَا يُغۡنِي عَنۡهُمۡ كَيۡدُهُمۡ شَيۡـٔٗا وَلَا هُمۡ يُنصَرُونَ ٤٦

47. ለእነዚያ ለበደሉትም ከዚህ ሌላ ቅርብ ቅጣት አልላቸው፡፡ ግን አብዛኞዎቻቸው አያውቁም፡፡

وَإِنَّ لِلَّذِينَ ظَلَمُواْ عَذَابٗا دُونَ ذَٰلِكَ وَلَٰكِنَّ أَكۡثَرَهُمۡ لَا يَعۡلَمُونَ ٤٧

48. ለጌታህ ፍርድም ታገሥ፡፡ አንተ በጥበቃችን ውስጥ ነህና፡፡ ጌታህንም በምትነሳ ጊዜ ከማመስገን ጋር አወድሰው፡፡

وَٱصۡبِرۡ لِحُكۡمِ رَبِّكَ فَإِنَّكَ بِأَعۡيُنِنَاۖ وَسَبِّحۡ بِحَمۡدِ رَبِّكَ حِينَ تَقُومُ ٤٨

49. ከሌሊቱም አወድሰው፡፡ በከዋክብት መዳበቂያ ጊዜም (ንጋት ላይ አወድሰው)፡፡

وَمِنَ ٱلَّيۡلِ فَسَبِّحۡهُ وَإِدۡبَٰرَ ٱلنُّجُومِ ٤٩

## ሱረቱ አን-ነጅም

## سورةالنحم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በኮከብ እምላለሁ በወደቀ (በገባ) ጊዜ፡፡

وَٱلنَّجۡمِ إِذَا هَوَىٰ ١

2. ነቢያችሁ (ሙሐመድ) አልተሳሳተም፤ አልጠመመምም፡፡

مَا ضَلَّ صَاحِبُكُمۡ وَمَا غَوَىٰ ٢

3. ከልብ ወለድም አይናገርም፡፡

وَمَا يَنطِقُ عَنِ ٱلۡهَوَىٰٓ ٣

4. እርሱ (ንግግሩ) የሚወርረድ ራእይ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

إِنۡ هُوَ إِلَّا وَحۡيٞ يُوحَىٰ ٤

5. ኀይሎቹ ብርቱው (መልአክ) አስተማረው፡፡

عَلَّمَهُۥ شَدِيدُ ٱلۡقُوَىٰ ٥

6. የዕውቀት ባለቤት የኾነው (አስተማረው፤ በተፈጥሮ ቅርጹ ኾኖ በአየር ላይ) ተደላደለም፡፡

ذُو مِرَّةٖ فَٱسۡتَوَىٰ ٦

7. እርሱ በላይኛው አድማስ ኾኖ፡፡

وَهُوَ بِٱلۡأُفُقِ ٱلۡأَعۡلَىٰ ٧

8. ከዚያም ቀረበ፤ ወረደም፡፡

ثُمَّ دَنَا فَتَدَلَّىٰ ٨

9. (ከእርሱ) የሁለት ደጋኖች ጫፍ ያህል ወይም (ከዚህ) ይበልጥ የቀረበ ኾነም፡፡

فَكَانَ قَابَ قَوۡسَيۡنِ أَوۡ أَدۡنَىٰ ٩

10. ወደ ባሪያውም (አላህ) ያወረደውን አወረደ፡፡

فَأَوۡحَىٰٓ إِلَىٰ عَبۡدِهِۦ مَآ أَوۡحَىٰ ١٠

11. (ነቢዩም በዓይኑ) ያየውን ልቡ አልዋሸም፡፡

مَا كَذَبَ ٱلۡفُؤَادُ مَا رَأَىٰٓ ١١

12. ታዲያ በሚያየው ላይ ትከራከሩታላችሁን?

أَفَتُمَٰرُونَهُۥ عَلَىٰ مَا يَرَىٰ ١٢

13. በሌላይቱም መውረድ ጊዜ በእርግጥ አይቶታል፡፡

وَلَقَدۡ رَءَاهُ نَزۡلَةً أُخۡرَىٰ ١٣

14. በመጨረሻይቱ ቁርቁራ አጠገብ፤

عِندَ سِدۡرَةِ ٱلۡمُنتَهَىٰ ١٤

15. እርሷ ዘንድ መኖሪያይቱ ገነት ያለች ስትኾን፡፡

عِندَهَا جَنَّةُ ٱلۡمَأۡوَىٰٓ ١٥

16. ቁርቁራይቱን የሚሸፍን ነገር በሚሸፍናት ጊዜ (አየው)፡፡

إِذۡ يَغۡشَى ٱلسِّدۡرَةَ مَا يَغۡشَىٰ ١٦

17. ዓይኑ (ካየው) አልተዘነበለም፡፡ ወሰንም አላለፈም፡፡

مَا زَاغَ ٱلۡبَصَرُ وَمَا طَغَىٰ ١٧

18. ከጌታው ታምራቶች ታላላቆቹን በእርግጥ አየ፡፡

لَقَدۡ رَأَىٰ مِنۡ ءَايَٰتِ رَبِّهِ ٱلۡكُبۡرَىٰٓ ١٨

19. አል-ላትንና አል-ዑዛን አያችሁን?

أَفَرَءَيۡتُمُ ٱللَّٰتَ وَٱلۡعُزَّىٰ ١٩

20. ሦስተኛይቱንም አነስተኛዋን መናትን (አያችሁን? የምትግገዟቸው ኃይል አላቸውን?)

وَمَنَوٰةَ ٱلثَّالِثَةَ ٱلۡأُخۡرَىٰٓ ٢٠

21. ለእናንተ ወንድ ለእርሱም ሴት (ልጅ) ይኖራልን?

أَلَكُمُ ٱلذَّكَرُ وَلَهُ ٱلۡأُنثَىٰ ٢١

22. ይህቺ ያን ጊዜ አድላዊ ክፍያ ናት፡፡

تِلۡكَ إِذٗا قِسۡمَةٞ ضِيزَىٰٓ ٢٢

23. እነርሱ እናንተና አባቶቻችሁ (አማልክት ብላችሁ) የጠራችኋቸው ስሞች ብቻ እንጅ ምንም አይደሉም፡፡ አላህ በእርሷ (መግገዛት) ምንም ማስረጃ አላወረደም፡፡ ከጌታቸውም መምሪያ የመጣላቸው ሲኾኑ ጥርጣሬንና ነፍሶች የሚዘነበሉበትን እንጅ ሌላ አይከተሉም፡፡

إِنۡ هِيَ إِلَّآ أَسۡمَآءٞ سَمَّيۡتُمُوهَآ أَنتُمۡ وَءَابَآؤُكُم مَّآ أَنزَلَ ٱللَّهُ بِهَا مِن سُلۡطَٰنٍۚ إِن يَتَّبِعُونَ إِلَّا ٱلظَّنَّ وَمَا تَهۡوَى ٱلۡأَنفُسُۖ وَلَقَدۡ جَآءَهُم مِّن رَّبِّهِمُ ٱلۡهُدَىٰٓ ٢٣

24. ለሰው የተመኘው ሁሉ አለውን?

أَمۡ لِلۡإِنسَٰنِ مَا تَمَنَّىٰ ٢٤

25. መጨረሻይቱም መጀመሪያይቱም (ዓለም) የአላህ ብቻ ናቸው፡፡

فَلِلَّهِ ٱلۡأٓخِرَةُ وَٱلۡأُولَىٰ ٢٥

26. በሰማያት ውስጥ ካለ መልአክም ብዙዎች (ሊማለዱለት) ለሚሻውና ለሚወደው ሰው ከፈቀደ በኋላ ቢኾን እንጅ ምልጃቸው ምንም አትጠቅምም፡፡

۞وَكَم مِّن مَّلَكٖ فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ لَا تُغۡنِي شَفَٰعَتُهُمۡ شَيۡـًٔا إِلَّا مِنۢ بَعۡدِ أَن يَأۡذَنَ ٱللَّهُ لِمَن يَشَآءُ وَيَرۡضَىٰٓ ﴿٢٦﴾

27. እነዚያ በመጨረሻይቱ ዓለም የማያምኑት መላእክትን በሴት አጠራር ይጠራሉ፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يُؤۡمِنُونَ بِٱلۡأٓخِرَةِ لَيُسَمُّونَ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةَ تَسۡمِيَةَ ٱلۡأُنثَىٰ ﴿٢٧﴾

28. ለእነርሱም በእርሱ ምንም ዕውቀት የላቸውም፡፡ ጥርጣሬን እንጅ ሌላን አይከተሉም፡፡ ጥርጣሬም ከእውነት ምንም አያብቃቃም፡፡

وَمَا لَهُم بِهِۦ مِنۡ عِلۡمٍۖ إِن يَتَّبِعُونَ إِلَّا ٱلظَّنَّۖ وَإِنَّ ٱلظَّنَّ لَا يُغۡنِي مِنَ ٱلۡحَقِّ شَيۡـٔٗا ﴿٢٨﴾

29. ከግሣጼያችንም (ከቁርኣን) ከሸሸና አነስተኛይቱን ሕይወት እንጅ ሌላን ከማይሻ ሰው ዞር (ተወው)፡፡

فَأَعۡرِضۡ عَن مَّن تَوَلَّىٰ عَن ذِكۡرِنَا وَلَمۡ يُرِدۡ إِلَّا ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا ﴿٢٩﴾

30. ይህ (አነስተኛይቱን ሕይወት መምረጥ) ከዕውቀት ድካቸው ነው፡፡ ጌታህ እርሱ ከመንገዱ የተሳሳተውን በእርግጥ ዐዋቂ ነው፡፡ እርሱም የቀናውን ሰው ዐዋቂ ነው፡፡

ذَٰلِكَ مَبۡلَغُهُم مِّنَ ٱلۡعِلۡمِۚ إِنَّ رَبَّكَ هُوَ أَعۡلَمُ بِمَن ضَلَّ عَن سَبِيلِهِۦ وَهُوَ أَعۡلَمُ بِمَنِ ٱهۡتَدَىٰ ﴿٣٠﴾

31. በሰማያት ያለውና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነው፡፡ እነዚያን ያጠፉትን በሠሩት ሊቀጣ እነዚያን ያሳመሩትንም በመልካሚቱ (ገነት) ሊመነዳ (የጠመመውንና የቀናውን ያውቃል)፡፡

وَلِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ لِيَجۡزِيَ ٱلَّذِينَ أَسَٰٓـُٔواْ بِمَا عَمِلُواْ وَيَجۡزِيَ ٱلَّذِينَ أَحۡسَنُواْ بِٱلۡحُسۡنَى ﴿٣١﴾

32. (እነርሱ) እነዚያ የኃጢአትን ታላለቆችና አስጸያፊዎቹን የሚርቁ ናቸው፡፡ ግን ትናንሾቹ የሚማሩ ናቸው፡፡ ጌታህ ምሕረተ ሰፊ ነውና፡፡ ከምድር በፈጠራችሁ ጊዜ እናንተም በእናቶቻችሁ ሆዶች ውስጥ ሽሎች በኾናችሁ ጊዜ እርሱ በናንተ (ኹነታ) ዐዋቂ ነው፡ ፡ ነፍሶቻችሁንም አታወድሱ እርሱ የሚፈራውን ሰው ዐዋቂ ነው፡፡

ٱلَّذِينَ يَجۡتَنِبُونَ كَبَٰٓئِرَ ٱلۡإِثۡمِ وَٱلۡفَوَٰحِشَ إِلَّا ٱللَّمَمَۚ إِنَّ رَبَّكَ وَٰسِعُ ٱلۡمَغۡفِرَةِۚ هُوَ أَعۡلَمُ بِكُمۡ إِذۡ أَنشَأَكُم مِّنَ ٱلۡأَرۡضِ وَإِذۡ أَنتُمۡ أَجِنَّةٞ فِي بُطُونِ أُمَّهَٰتِكُمۡۖ فَلَا تُزَكُّوٓاْ أَنفُسَكُمۡۖ هُوَ أَعۡلَمُ بِمَنِ ٱتَّقَىٰٓ ﴿٣٢﴾

33. ያንን (ከእምነት) የዞረውን አየህን?

أَفَرَءَيۡتَ ٱلَّذِي تَوَلَّىٰ ﴿٣٣﴾

34. ጥቂትን የሰጠውንና ያቋረጠውንም (አየህን?)

وَأَعۡطَىٰ قَلِيلٗا وَأَكۡدَىٰٓ ﴿٣٤﴾

35. የሩቁ ምስጢር ዕውቀት እርሱ ዘንድ አልለን? ስለዚህ እርሱ ያያልን?

أَعِندَهُۥ عِلۡمُ ٱلۡغَيۡبِ فَهُوَ يَرَىٰٓ ﴿٣٥﴾

36. ይልቁንም በዚያ በሙሳ ጽሑፎች ውስጥ ባለው ነገር አልተነገረምን?

أَمۡ لَمۡ يُنَبَّأۡ بِمَا فِي صُحُفِ مُوسَىٰ ﴿٣٦﴾

37. በዚያም (የታዘዘውን) በፈጸመው በኢብራሂም (ጽሑፎች ውስጥ ባለው አልተነገረምን?)

وَإِبۡرَٰهِيمَ ٱلَّذِي وَفَّىٰٓ ﴿٣٧﴾

38. (እርሱም ኃጢያት) ተሸካሚ ነፍስ የሌላይቱን ነፍስ ኃጢአት አትሸከምም፡፡

أَلَّا تَزِرُ وَازِرَةٞ وِزۡرَ أُخۡرَىٰ ٣٨

39. ለሰውም ሁሉ የሠራው እንጅ ሌላ የለውም፡፡

وَأَن لَّيۡسَ لِلۡإِنسَٰنِ إِلَّا مَا سَعَىٰ ٣٩

40. ሥራውም ሁሉ ወደ ፊት ይታያል፡፡

وَأَنَّ سَعۡيَهُۥ سَوۡفَ يُرَىٰ ٤٠

41. ከዚያም ሙሉውን ምንዳ ይመነዳዋል፡፡

ثُمَّ يُجۡزَىٰهُ ٱلۡجَزَآءَ ٱلۡأَوۡفَىٰ ٤١

42. መጨረሻውም ወደ ጌታህ ብቻ ነው፡፡

وَأَنَّ إِلَىٰ رَبِّكَ ٱلۡمُنتَهَىٰ ٤٢

43. እነሆ እርሱም አስሳቀ፣ አስለቀሰም፡፡

وَأَنَّهُۥ هُوَ أَضۡحَكَ وَأَبۡكَىٰ ٤٣

44. እነሆ እርሱም ገደለ፣ አስነሳም፡፡

وَأَنَّهُۥ هُوَ أَمَاتَ وَأَحۡيَا ٤٤

45. እርሱም ሁለቱን ዓይነቶች ወንድንና ሴትን ፈጠረ፡፡

وَأَنَّهُۥ خَلَقَ ٱلزَّوۡجَيۡنِ ٱلذَّكَرَ وَٱلۡأُنثَىٰ ٤٥

46. ከፍትወት ጠብታ (በማህጸን ውስጥ) በምትፈሰስ ጊዜ፡፡

مِن نُّطۡفَةٍ إِذَا تُمۡنَىٰ ٤٦

47. የኋለኛይቱም ማስነሳት በእርሱ ላይ ነው፡፡

وَأَنَّ عَلَيۡهِ ٱلنَّشۡأَةَ ٱلۡأُخۡرَىٰ ٤٧

48. እነሆ እርሱም አከበረ፣ ጥሪተኛም አደረገ፡፡

وَأَنَّهُۥ هُوَ أَغۡنَىٰ وَأَقۡنَىٰ ٤٨

49. እነሆ እርሱም የሺዕራ ጌታ ነው፡፡

وَأَنَّهُۥ هُوَ رَبُّ ٱلشِّعۡرَىٰ ٤٩

50. እነሆ እርሱም የፊተኛይቱን ዓድ አጥፍቷል፡፡

وَأَنَّهُۥٓ أَهۡلَكَ عَادًا ٱلۡأُولَىٰ ٥٠

51. ሰሙድንም (አጥፍቷል)፤ አላስቀረምም፡፡

وَثَمُودَاْ فَمَآ أَبۡقَىٰ ٥١

52. በፊትም የኑሕን ሕዝቦች (አጥፍቷል)፡፡ እነርሱ በጣም በደለኞችና እጅግ የጠመሙ እነርሱ ነበሩና፡፡

وَقَوۡمَ نُوحٖ مِّن قَبۡلُۖ إِنَّهُمۡ كَانُواْ هُمۡ أَظۡلَمَ وَأَطۡغَىٰ ٥٢

53. የተገለበጠችውንም ከተማ ደፋ፡፡

وَٱلۡمُؤۡتَفِكَةَ أَهۡوَىٰ ٥٣

54. ያለበሳትንም አለበሳት፡፡

فَغَشَّىٰهَا مَا غَشَّىٰ ٥٤

55. ከጌታህም ጸጋዎች በየትኛው ትጠራጠራለህ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكَ تَتَمَارَىٰ ٥٥

هَٰذَا نَذِيرٞ مِّنَ ٱلنُّذُرِ ٱلۡأُولَىٰٓ ٥٦

56. ይህ ከፊተኞቹ አስፈራሪዎች (ጎሳ) የኾነ አስፈራሪ ነው::

أَزِفَتِ ٱلۡأٓزِفَةُ ٥٧

57. ቀራቢይቱ (ኅልፈተ ዓለም) ቀረበች::

لَيۡسَ لَهَا مِن دُونِ ٱللَّهِ كَاشِفَةٌ ٥٨

58. ለእርሷ ከአላህ ሌላ ገላጭ የላትም::

أَفَمِنۡ هَٰذَا ٱلۡحَدِيثِ تَعۡجَبُونَ ٥٩

59. ከዚህ ንግግር ትደነቃላችሁን?

وَتَضۡحَكُونَ وَلَا تَبۡكُونَ ٦٠

60. ትስቃላችሁምን? አታለቅሱምን?

وَأَنتُمۡ سَٰمِدُونَ ٦١

61. እናንተም ዘንጊዎች ናችሁ::

فَٱسۡجُدُواْۤ لِلَّهِۤ وَٱعۡبُدُواْ۩ ٦٢

62. ለአላህም ስገዱ ተገዙትም::

## ሱረቱ አል ቀመር

## سورة القمر

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

ٱقۡتَرَبَتِ ٱلسَّاعَةُ وَٱنشَقَّ ٱلۡقَمَرُ ١

1. ሰዓቲቱ (የትንሣኤ ቀን) ተቃረበች፤ ጨረቃም ተገመሰ::

وَإِن يَرَوۡاْ ءَايَةٗ يُعۡرِضُواْ وَيَقُولُواْ سِحۡرٞ مُّسۡتَمِرّٞ ٢

2. ተዓምርንም ቢያዩ (ከእምነት) ይዞራሉ:: (ይህ) «ዘውታሪ ድግምት ነውም» ይላሉ::

وَكَذَّبُواْ وَٱتَّبَعُوٓاْ أَهۡوَآءَهُمۡۚ وَكُلُّ أَمۡرٖ مُّسۡتَقِرّٞ ٣

3. አስተባበሉም:: ዝንባሌዎቻቸውንም ተከተሉ:: ነገርም ሁሉ (ወሰን አለው)፤ ረጊ ነው::

وَلَقَدۡ جَآءَهُم مِّنَ ٱلۡأَنۢبَآءِ مَا فِيهِ مُزۡدَجَرٌ ٤

4. ከዜናዎችም በእርሱ ውስጥ መገሰጥ ያለበት ነገር በእርግጥ መጣላቸው::

حِكۡمَةُۢ بَٰلِغَةٞۖ فَمَا تُغۡنِ ٱلنُّذُرُ ٥

5. ሙሉ የኾነች ጥበብ (መጣቻቸው) ግን አስፈራሪዎቹ አያብቃቁም::

فَتَوَلَّ عَنۡهُمۡۘ يَوۡمَ يَدۡعُ ٱلدَّاعِ إِلَىٰ شَيۡءٖ نُّكُرٍ ٦

6. ከነርሱም ዙር:: ጠሪው (መልአክ) ወደ አስደንጋጭ ነገር የሚጠራበትን ቀን (አስታውስ)::

خُشَّعًا أَبۡصَٰرُهُمۡ يَخۡرُجُونَ مِنَ ٱلۡأَجۡدَاثِ كَأَنَّهُمۡ جَرَادٞ

7. ዓይኖቻቸው ያቀረቀሩ ኾነው፤ ፍጹም የተበተነ አንበጣ መስለው ከመቃብሮቹ ይወጣሉ::

مُّنتَشِرٌ ۝٧

مُّهۡطِعِينَ إِلَى ٱلدَّاعِۖ يَقُولُ ٱلۡكَٰفِرُونَ هَٰذَا يَوۡمٌ عَسِرٞ ۝٨

8. ወደ ጠሪው አንገቶቻቸውን ሳቢዎች ቸኳዮች ኾነው (ይወጣሉ)፡፡ ከሓዲዎቹ (ያን ጊዜ ምን ይላሉ?) «ይህ ብርቱ ቀን ነው» ይላሉ፡፡

۞ كَذَّبَتۡ قَبۡلَهُمۡ قَوۡمُ نُوحٖ فَكَذَّبُواْ عَبۡدَنَا وَقَالُواْ مَجۡنُونٞ وَٱزۡدُجِرَ ۝٩

9. ከእነርሱ በፊት የኑሕ ነገድ አስተባበለች፡፡ ባሪያችንንም (ኑሕን) አስተባበሉ፡፡ «ዕብድ ነውም» አሉ፡፡ ተገላመጠም፡፡

فَدَعَا رَبَّهُۥٓ أَنِّي مَغۡلُوبٞ فَٱنتَصِرۡ ۝١٠

10. ጌታውንም «እኔ የተሸነፍኩ ነኝና እርዳኝ» ሲል ጠራ፡፡

فَفَتَحۡنَآ أَبۡوَٰبَ ٱلسَّمَآءِ بِمَآءٖ مُّنۡهَمِرٖ ۝١١

11. ወዲያውም የሰማይን ደጃፎች በሚንቧቧ ውሃ ከፈትን፡፡

وَفَجَّرۡنَا ٱلۡأَرۡضَ عُيُونٗا فَٱلۡتَقَى ٱلۡمَآءُ عَلَىٰٓ أَمۡرٖ قَدۡ قُدِرَ ۝١٢

12. የምድርንም ምንጮች አፈነዳን፡፡ ውሃውም (የሰማዩና የምድሩ) በእርግጥ በተወሰነ ኹነታ ላይ ተገናኘ፡፡

وَحَمَلۡنَٰهُ عَلَىٰ ذَاتِ أَلۡوَٰحٖ وَدُسُرٖ ۝١٣

13. ባለ ሳንቃዎችና ባለሚስማሮች በኾነችም ታንኳ ላይ ጫንነው፡፡

تَجۡرِي بِأَعۡيُنِنَا جَزَآءٗ لِّمَن كَانَ كُفِرَ ۝١٤

14. በጥበቃችን ስር ኾና ትንሻለላለች፡፡ ተክዶ ለነበረው ሰው ምንዳ (ይህንን ሠራን)፡፡

وَلَقَد تَّرَكۡنَٰهَآ ءَايَةٗ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ۝١٥

15. ተዓምር አድርገንም በእርግጥ ተውናት፡፡ ከተገሳጭም አልለን?

فَكَيۡفَ كَانَ عَذَابِي وَنُذُرِ ۝١٦

16. ቅጣቴና ማስጠንቀቂያዎቼም እንዴት ነበሩ?

وَلَقَدۡ يَسَّرۡنَا ٱلۡقُرۡءَانَ لِلذِّكۡرِ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ۝١٧

17. ቁርአንንም ለመገንዘብ በእርግጥ አገራነው፡፡ ተገንዛቢም አልለን?

كَذَّبَتۡ عَادٞ فَكَيۡفَ كَانَ عَذَابِي وَنُذُرِ ۝١٨

18. ዓድ አስተባበለች፡፡ ቅጣቴና ማስጠንቀቂያዎቼም እንዴት ነበሩ!

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ رِيحٗا صَرۡصَرٗا فِي يَوۡمِ نَحۡسٖ مُّسۡتَمِرّٖ ۝١٩

19. እኛ በእነርሱ ላይ ዘወትር መናጢ በኾነ ቀን በኀይል የምትንሻሻ ነፋስን ላክንባቸው፡፡

تَنزِعُ ٱلنَّاسَ كَأَنَّهُمۡ أَعۡجَازُ نَخۡلٖ مُّنقَعِرٖ ۝٢٠

20. ሰዎቹን ልክ ከሥሮቻቸው የተገለሰሱ የዘንባባ ግንዶች መስለው (ከተደበቁበት) ትነቅላቸዋለች፡፡

فَكَيۡفَ كَانَ عَذَابِي وَنُذُرِ ۝٢١

21. ቅጣቴና ማስጠንቀቂያዎቼም እንዴት ነበሩ?

وَلَقَدۡ يَسَّرۡنَا ٱلۡقُرۡءَانَ لِلذِّكۡرِ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ۝٢٢

22. ቁርአንንም ለማስታወስ በእርግጥ አገራነው፡፡ ተገሳጭም አልለን?

23. ሰሙድ በአስፈራሪዎቹ አስተባበለች፡፡

كَذَّبَتۡ ثَمُودُ بِٱلنُّذُرِ ٢٣

24. «ከእኛ የኾነን አንድን ሰው እንከተለዋለን? እኛ ያን ጊዜ በስህተትና በዕብደት ውስጥ ነን» አሉ፡፡

فَقَالُوٓاْ أَبَشَرٗا مِّنَّا وَٰحِدٗا نَّتَّبِعُهُۥٓ إِنَّآ إِذٗا لَّفِي ضَلَٰلٖ وَسُعُرٍ ٢٤

25. «ከኛ መካከል በእርሱ ላይ (ብቻ) ማስገንዘቢያ (ራእይ) ተጣለለትን? አይደለም እርሱ ውሸታም ኩሩ ነው» (አሉ)፡፡

أَءُلۡقِيَ ٱلذِّكۡرُ عَلَيۡهِ مِنۢ بَيۡنِنَا بَلۡ هُوَ كَذَّابٌ أَشِرٞ ٢٥

26. ውሸታሙ ኩሩው ማን እንደኾነ ነገ በእርግጥ ያውቃሉ፡፡

سَيَعۡلَمُونَ غَدٗا مَّنِ ٱلۡكَذَّابُ ٱلۡأَشِرُ ٢٦

27. እኛ ሴት ግመልን ለእነርሱ መፈተኛ ትኾን ዘንድ ላኪዎች ነን፡፡ ተጠባበቃቸውም፡፡ ታገስም፡፡

إِنَّا مُرۡسِلُواْ ٱلنَّاقَةِ فِتۡنَةٗ لَّهُمۡ فَٱرۡتَقِبۡهُمۡ وَٱصۡطَبِرۡ ٢٧

28. ውሃውንም በመካከላቸው የተከፈለ መኾኑን ንገራቸው፡፡ ከውሃ የኾነ ፋንታ ሁሉ (ተረኞቹ) የሚጣዱት ነው፡፡

وَنَبِّئۡهُمۡ أَنَّ ٱلۡمَآءَ قِسۡمَةُۢ بَيۡنَهُمۡۖ كُلُّ شِرۡبٖ مُّحۡتَضَرٞ ٢٨

29. ጓደኛቸውንም ጠሩ፡፡ ወዲያውም (ሰይፍን) ተቀበለ፡፡ ወጋትም፡፡

فَنَادَوۡاْ صَاحِبَهُمۡ فَتَعَاطَىٰ فَعَقَرَ ٢٩

30. ቅጣቴና ማስጠንቀቂያዎቼም እንዴት ነበሩ?

فَكَيۡفَ كَانَ عَذَابِي وَنُذُرِ ٣٠

31. እኛ በእነርሱ ላይ አንዲትን ጩኸት ላክንባቸው፡፡ ወዲያውም ከበረት አጣሪ (አጥር) እንደ ተሰባበረ ርግጋፊ ኾኑ፡፡

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ صَيۡحَةٗ وَٰحِدَةٗ فَكَانُواْ كَهَشِيمِ ٱلۡمُحۡتَظِرِ ٣١

32. ቁርአንንም ለመገንዘብ አገራነው፡፡ ተገሳጭም አልለን?

وَلَقَدۡ يَسَّرۡنَا ٱلۡقُرۡءَانَ لِلذِّكۡرِ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ٣٢

33. የሉጥ ሕዝብ በአስፈራሪዎቹ አስተባበለች፡፡

كَذَّبَتۡ قَوۡمُ لُوطِۭ بِٱلنُّذُرِ ٣٣

34. እኛ በእነርሱ ላይ ጠጠርን ያዘለች ነፋስን ላክን፡፡ የሉጥ ቤተሰቦች ብቻ ሲቀሩ (እነርሱንስ) በሌሊት መጨረሻ ላይ አዳንናቸው፡፡

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَا عَلَيۡهِمۡ حَاصِبًا إِلَّآ ءَالَ لُوطٖۖ نَّجَّيۡنَٰهُم بِسَحَرٖ ٣٤

35. ከእኛ በኾነ ጸጋ (አዳንናቸው)፡፡ እንደዚሁ ያመሰገነን ሰው እንመነዳለን፡፡

نِّعۡمَةٗ مِّنۡ عِندِنَاۚ كَذَٰلِكَ نَجۡزِي مَن شَكَرَ ٣٥

36. ብርቱይቱን አያያዛችንንም በእርግጥ አስጠነቀቃቸው፡፡ በማስጠንቀቂያዎቹም ተከራከሩ፡፡

وَلَقَدۡ أَنذَرَهُم بَطۡشَتَنَا فَتَمَارَوۡاْ بِٱلنُّذُرِ ٣٦

37. ከእንግዶቹም እንዲያስመቻቸው ደጋገመው ፈለጉት፡፡ ወዲያውም ዓይኖቻቸውን አበስን፡፡ «ቅጣቴንና ማስጠንቀቂያዎቼንም ቅመሱ» (አልናቸው)፡፡

وَلَقَدۡ رَٰوَدُوهُ عَن ضَيۡفِهِۦ فَطَمَسۡنَآ أَعۡيُنَهُمۡ فَذُوقُواْ عَذَابِي وَنُذُرِ ٣٧

38. በማለዳም ዘውታሪ የኾነ ቅጣት በእርግጥ ማለደባቸው፡፡

وَلَقَدۡ صَبَّحَهُم بُكۡرَةً عَذَابٌ مُّسۡتَقِرٌّ ٣٨

39. «ቅጣቴንና ማስጠንቀቂያዎቼንም ቅመሱ» (ተባሉ)፡፡

فَذُوقُواْ عَذَابِي وَنُذُرِ ٣٩

40. ቁርኣንንም ለመገንዘብ በእርግጥ አገራነው፡፡ ተገሳጭም አልለን?

وَلَقَدۡ يَسَّرۡنَا ٱلۡقُرۡءَانَ لِلذِّكۡرِ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ٤٠

41. የፈርዖንንም ቤተሰቦች ማስጠንቀቂያዎች በእርግጥ መጡዋቸው፡፡

وَلَقَدۡ جَآءَ ءَالَ فِرۡعَوۡنَ ٱلنُّذُرُ ٤١

42. በተዓምራቶቻችን በሁሏም አስተባበሉ፡፡ የብርቱ ቻይንም አያያዝ ያዝናቸው፡፡

كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا كُلِّهَا فَأَخَذۡنَٰهُمۡ أَخۡذَ عَزِيزٖ مُّقۡتَدِرٍ ٤٢

43. ከሓዲዎቻችሁ ከእነዚህ በላጮች ናቸውን? ወይስ ለናንተ በመጽሐፎች ውስጥ (የተነገረ) ነፃነት አላችሁን?

أَكُفَّارُكُمۡ خَيۡرٞ مِّنۡ أُوْلَٰٓئِكُمۡ أَمۡ لَكُم بَرَآءَةٞ فِي ٱلزُّبُرِ ٤٣

44. ወይስ «እኛ የተረዳን ከምቹዎች ነን» ይላሉን?

أَمۡ يَقُولُونَ نَحۡنُ جَمِيعٞ مُّنتَصِرٞ ٤٤

45. ከምቹዎቹ በእርግጥ ድል ይምመታሉ፡፡ ጀርባዎችንም ያዞራሉ፡፡

سَيُهۡزَمُ ٱلۡجَمۡعُ وَيُوَلُّونَ ٱلدُّبُرَ ٤٥

46. ይልቁንም ሰዓቲቱ (ትንሣኤ) ቀጠሮዋቸው ናት፡፡ ሰዓቲቱም በጣም የከበደችና የመረረች ናት፡፡

بَلِ ٱلسَّاعَةُ مَوۡعِدُهُمۡ وَٱلسَّاعَةُ أَدۡهَىٰ وَأَمَرُّ ٤٦

47. አመጸኞች በስህተትና በእሳቶች ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُجۡرِمِينَ فِي ضَلَٰلٖ وَسُعُرٖ ٤٧

48. በእሳት ውስጥ በፊቶቻቸው በሚጎተቱበት ቀን «የሰቀርን መንካት ቅመሱ» (ይባላሉ)፡፡

يَوۡمَ يُسۡحَبُونَ فِي ٱلنَّارِ عَلَىٰ وُجُوهِهِمۡ ذُوقُواْ مَسَّ سَقَرَ ٤٨

49. እኛ ሁሉን ነገር በልክ ፈጠርነው፡፡

إِنَّا كُلَّ شَيۡءٍ خَلَقۡنَٰهُ بِقَدَرٖ ٤٩

50. ትእዛዛችንም እንደ ዓይን ቅጽበት አንዲት (ቃል) እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

وَمَآ أَمۡرُنَآ إِلَّا وَٰحِدَةٞ كَلَمۡحِۭ بِٱلۡبَصَرِ ٥٠

51. ብጤዎቻችሁንም በእርግጥ አጠፋን፡፡ ተገሳጭም አልለን?

وَلَقَدۡ أَهۡلَكۡنَآ أَشۡيَاعَكُمۡ فَهَلۡ مِن مُّدَّكِرٖ ٥١

52. የሠሩትም ነገር ሁሉ በመጽሐፎች ውስጥ ነው፡፡

وَكُلُّ شَيۡءٖ فَعَلُوهُ فِي ٱلزُّبُرِ ﴿٥٢﴾

53. ትንሹም ትልቁም ሁሉ የተጻፈ ነው፡፡

وَكُلُّ صَغِيرٖ وَكَبِيرٖ مُّسۡتَطَرٌ ﴿٥٣﴾

54. አላህን ፈሪዎቹ በአትክልቶችና በወንዞች ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُتَّقِينَ فِي جَنَّٰتٖ وَنَهَرٖ ﴿٥٤﴾

55. (እነርሱም ውድቅ ቃልና መውወንጀል በሌለበት) በእውነት መቀመጫ ውስጥ ቻይ የሆነው ንጉሥ ዘንድ ናቸው፡፡

فِي مَقۡعَدِ صِدۡقٍ عِندَ مَلِيكٖ مُّقۡتَدِرِۭ ﴿٥٥﴾

## ሱረቱ አል ረሕማን

## سورة الحديد

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አል-ረሕማን፤

ٱلرَّحۡمَٰنُ ﴿١﴾

2. ቁርኣንን አስተማረ፡፡

عَلَّمَ ٱلۡقُرۡءَانَ ﴿٢﴾

3. ሰውን ፈጠረ፡፡

خَلَقَ ٱلۡإِنسَٰنَ ﴿٣﴾

4. መናገርን አስተማረው፡፡

عَلَّمَهُ ٱلۡبَيَانَ ﴿٤﴾

5. ፀሐይና ጨረቃ በተወሰነ ልክ (ይኼዳሉ)፡፡

ٱلشَّمۡسُ وَٱلۡقَمَرُ بِحُسۡبَانٖ ﴿٥﴾

6. ሐረግና ዛፍም (ለእርሱ) ይሰግዳሉ፡፡

وَٱلنَّجۡمُ وَٱلشَّجَرُ يَسۡجُدَانِ ﴿٦﴾

7. ሰማይንም አጓናት፡፡ ትክክለኛነትንም ደነገገ፡፡

وَٱلسَّمَآءَ رَفَعَهَا وَوَضَعَ ٱلۡمِيزَانَ ﴿٧﴾

8. በሚዛን (ስትመዝኑ) እንዳትበድሉ፡፡

أَلَّا تَطۡغَوۡاْ فِي ٱلۡمِيزَانِ ﴿٨﴾

9. መመዘንንም በትክክል መዝኑ፡፡ ተመዛኙንም አታጉድሉ፡፡

وَأَقِيمُواْ ٱلۡوَزۡنَ بِٱلۡقِسۡطِ وَلَا تُخۡسِرُواْ ٱلۡمِيزَانَ ﴿٩﴾

10. ምድርንም ለፍጡሩ አደላደላት፡፡

وَٱلۡأَرۡضَ وَضَعَهَا لِلۡأَنَامِ ﴿١٠﴾

فِيهَا فَٰكِهَةٞ وَٱلنَّخۡلُ ذَاتُ ٱلۡأَكۡمَامِ ١١

11. በውስጧ እሸት ባለ ሺፋኖች የኾኑ ዘንባባዎችም ያሉባት ስትኾን፡፡

وَٱلۡحَبُّ ذُو ٱلۡعَصۡفِ وَٱلرَّيۡحَانُ ١٢

12. የገለባ ባለቤት የኾነ ቅንጣትም፡፡ ባለ መልካም መዐዛ ቅጠሎችም (ያሉባት ስትኾን)፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ١٣

13. (ሰዎችና ጋኔኖች ሆይ!) ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

خَلَقَ ٱلۡإِنسَٰنَ مِن صَلۡصَٰلٖ كَٱلۡفَخَّارِ ١٤

14. ሰውን እንደ ሸክላ ከሚቅጨለጨል ደረቅ ጭቃ ፈጠረው፡፡

وَخَلَقَ ٱلۡجَآنَّ مِن مَّارِجٖ مِّن نَّارٖ ١٥

15. ጃንንም ከእሳት ከኾነ ነበልባል ፈጠረው፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ١٦

16. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

رَبُّ ٱلۡمَشۡرِقَيۡنِ وَرَبُّ ٱلۡمَغۡرِبَيۡنِ ١٧

17. የሁለቱ ምሥራቆች ጌታ፤ የሁለቱ ምዕራቦችም ጌታ ነው፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ١٨

18. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

مَرَجَ ٱلۡبَحۡرَيۡنِ يَلۡتَقِيَانِ ١٩

19. ሁለቱን ባሕሮች የሚገናኙ ሲኾኑ ለቀቃቸው፡፡

بَيۡنَهُمَا بَرۡزَخٞ لَّا يَبۡغِيَانِ ٢٠

20. (እንዳይዋሐዱ) በመካከላቸው ጋራጅ አለለ፡፡ (አንዱ ባንዱ ላይ) ወሰን አያልፉም፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٢١

21. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?›

يَخۡرُجُ مِنۡهُمَا ٱللُّؤۡلُؤُ وَٱلۡمَرۡجَانُ ٢٢

22. ሉልና መርጃን ከሁለቱ ይወጣል፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٢٣

23. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

وَلَهُ ٱلۡجَوَارِ ٱلۡمُنشَـَٔاتُ فِي ٱلۡبَحۡرِ كَٱلۡأَعۡلَٰمِ ٢٤

24. እንደ ጋራዎች ኾነው በባሕር ውስጥ የተሠሩት ተንሻለዮቹም (ታንኳዎች) የእርሱ ናቸው፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٢٥

25. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

كُلُّ مَنۡ عَلَيۡهَا فَانٖ ٢٦

26. በእርሷ (በምድር) ላይ ያለው ሁሉ ጠፊ ነው፡፡

وَيَبۡقَىٰ وَجۡهُ رَبِّكَ ذُو ٱلۡجَلَٰلِ وَٱلۡإِكۡرَامِ ٢٧

27. የልቅናና የልግሥና ባለቤት የኾነው የጌታህ ፊትም ይቀራል፡፡ (አይጠፋም)፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٢٨

28. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

29. በሰማያትና በምድር ውስጥ ያሉት ሁሉ ይለምኑታል፡፡ በየቀኑ ሁሉ እርሱ በሥራ ላይ ነው፡፡

يَسْـَٔلُهُۥ مَن فِى ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۚ كُلَّ يَوْمٍ هُوَ فِى شَأْنٍ ﴿٢٩﴾

30. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?›

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٣٠﴾

31. እናንተ ሁለት ከባዶች (ሰዎችና ጋኔኖች) ሆይ! ለእናንተ (መቆጣጠር) በእርግጥ እናስባለን፡፡

سَنَفْرُغُ لَكُمْ أَيُّهَ ٱلثَّقَلَانِ ﴿٣١﴾

32. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٣٢﴾

33. የጋኔንና የሰው ጭፍሮች ሆይ! ከሰማያትና ከምድር ቀበሌዎች መውጣትን ብትችሉ ውጡ፡፡ በስልጣን እንጅ አትወጡም፡፡ (ግን ስልጣን የላችሁም)

يَـٰمَعْشَرَ ٱلْجِنِّ وَٱلْإِنسِ إِنِ ٱسْتَطَعْتُمْ أَن تَنفُذُوا۟ مِنْ أَقْطَارِ ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ فَٱنفُذُوا۟ ۚ لَا تَنفُذُونَ إِلَّا بِسُلْطَـٰنٍ ﴿٣٣﴾

34. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٣٤﴾

35. በሁለታችሁም ላይ ከእሳት ነበልባል፣ ጭስም ይላከባችኋል፡፡ (ሁለታችሁም) አትርረዱምም፡፡

يُرْسَلُ عَلَيْكُمَا شُوَاظٌ مِّن نَّارٍ وَنُحَاسٌ فَلَا تَنتَصِرَانِ ﴿٣٥﴾

36. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٣٦﴾

37. ሰማይም በተሰነጠቀችና እንደ ጽጌረዳ፣ እንደታረበ ቆዳ በኾነች ጊዜ፤ (ጭንቁን ምን አበረታው)፡፡

فَإِذَا ٱنشَقَّتِ ٱلسَّمَآءُ فَكَانَتْ وَرْدَةً كَٱلدِّهَانِ ﴿٣٧﴾

38. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٣٨﴾

39. በዚያም ቀን ሰውም ጃንም ከኃጢአቱ ገና አይጠየቅም፡፡

فَيَوْمَئِذٍ لَّا يُسْـَٔلُ عَن ذَنۢبِهِۦٓ إِنسٌ وَلَا جَآنٌّ ﴿٣٩﴾

40. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٤٠﴾

41. ከሓዲዎች በምልክታቸው ይታወቃሉ፡፡ አናቶቻቸውንና ጫማዎቻቸውንም ይያዛሉ፡፡

يُعْرَفُ ٱلْمُجْرِمُونَ بِسِيمَـٰهُمْ فَيُؤْخَذُ بِٱلنَّوَٰصِى وَٱلْأَقْدَامِ ﴿٤١﴾

42. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ፡፡

فَبِأَىِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٤٢﴾

43. ይህቺ ያቺ አመጸኞች በእርሷ ያስተባብሉባት የነበረችው ገሀነም ናት (ይባላሉ)፡፡

هَـٰذِهِۦ جَهَنَّمُ ٱلَّتِى يُكَذِّبُ بِهَا ٱلْمُجْرِمُونَ ﴿٤٣﴾

44. በእርሷና በጣም ሞቃት በኾነ ፍል ውሃ መካከል ይመላለሳሉ፡፡

يَطُوفُونَ بَيْنَهَا وَبَيْنَ حَمِيمٍ ءَانٍ ﴿٤٤﴾

45. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٤٥﴾

46. በጌታውም ፊት መቆምን ለፈራ ሰው ሁለት ገነቶች አልሉት፡፡

وَلِمَنْ خَافَ مَقَامَ رَبِّهِۦ جَنَّتَانِ ﴿٤٦﴾

47. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٤٧﴾

48. የቀንዘሎች ባለ ቤቶች የኾኑ (ገነቶች አልሉት)፡፡

ذَوَاتَآ أَفْنَانٍ ﴿٤٨﴾

49. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٤٩﴾

50. በሁለቱ ውስጥ የሚፈስሱ ሁለት ምንጮች አልሉ፡፡

فِيهِمَا عَيْنَانِ تَجْرِيَانِ ﴿٥٠﴾

51. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٥١﴾

52. በሁለቱ ውስጥ ከፍራፍሬዎች ሁሉ ሁለት ዓይነቶች (እርጥብና ደረቅ) አልሉ፡፡

فِيهِمَا مِن كُلِّ فَٰكِهَةٍ زَوْجَانِ ﴿٥٢﴾

53. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٥٣﴾

54. የውስጥ ጉስጉሳቸው ከወፍራም ሐር በኾኑ ምንጣፎች ላይ የተመቻቹ ሲኾኑ (ይንፈላሰሳሉ)፡፡ የሁለቱም ገነቶች ፍሬ (ለለቃሚ) ቅርብ ነው፡፡

مُتَّكِـِٔينَ عَلَىٰ فُرُشٍۭ بَطَآئِنُهَا مِنْ إِسْتَبْرَقٍۚ وَجَنَى ٱلْجَنَّتَيْنِ دَانٍ ﴿٥٤﴾

55. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٥٥﴾

56. በውስጣቸው ከበፊታቸው (ከባሎቻቸው በፊት) ሰውም ጃንም ያልገሰሳቸው ዓይኖቻቸውን (በባሎቻቸው ላይ) አሳጣሪዎች (ሴቶች) አልሉ፡፡

فِيهِنَّ قَٰصِرَٰتُ ٱلطَّرْفِ لَمْ يَطْمِثْهُنَّ إِنسٌ قَبْلَهُمْ وَلَا جَآنٌّ ﴿٥٦﴾

57. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٥٧﴾

58. ልክ ያቁትና መርጃን ይመስላሉ፡፡

كَأَنَّهُنَّ ٱلْيَاقُوتُ وَٱلْمَرْجَانُ ﴿٥٨﴾

59. ከጌታችሁም ጸጋዎቸ በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٥٩﴾

60. የበጎ ሥራ ዋጋ በጎ እንጅ ሌላ ነውን?

هَلْ جَزَآءُ ٱلْإِحْسَٰنِ إِلَّا ٱلْإِحْسَٰنُ ﴿٦٠﴾

61. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ﴿٦١﴾

62. ከሁለቱ ገነቶችም ሌላ ሁለት ገነቶች አልሉ፡፡

وَمِن دُونِهِمَا جَنَّتَانِ ﴿٦٢﴾

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٦٣

63. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?›

مُدۡهَآمَّتَانِ ٦٤

64. ከልምላሜያቸው የተነሳ ወደ ጥቁረት ያዘነበሉ ናቸው፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٦٥

65. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فِيهِمَا عَيۡنَانِ نَضَّاخَتَانِ ٦٦

66. በውስጣቸው ሁለት የሚንፏፉ ምንጮች አልሉ፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٦٧

67. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فِيهِمَا فَٰكِهَةٞ وَنَخۡلٞ وَرُمَّانٞ ٦٨

68. በውስጣቸው ፍራፍሬ፣ ዘምባባም፣ ሩማንም አልለ፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٦٩

69. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

فِيهِنَّ خَيۡرَٰتٌ حِسَانٞ ٧٠

70. በውስጣቸው ጠባየ መልካሞች መልከ ውቦች (ሴቶች) አልሉ፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٧١

71. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

حُورٞ مَّقۡصُورَٰتٞ فِي ٱلۡخِيَامِ ٧٢

72. በድንኳኖች ውስጥ የተጨጎሉ የዓይኖቻቸው ጥቁረትና ንጣት ደማቅ የኾኑ ናቸው፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٧٣

73. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

لَمۡ يَطۡمِثۡهُنَّ إِنسٞ قَبۡلَهُمۡ وَلَا جَآنّٞ ٧٤

74. ከነርሱ በፊት ሰውም ጃንም አልገሰሳቸውም፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٧٥

75. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባበላላችሁ?

مُتَّكِـِٔينَ عَلَىٰ رَفۡرَفٍ خُضۡرٖ وَعَبۡقَرِيٍّ حِسَانٖ ٧٦

76. በሚያረገርጉ አረንጓዴ ምንጣፎችና በሚያማምሩ ስጋጃዎች ላይ የተደላደሉ ሲኾኑ (ይቀመጣሉ)፡፡

فَبِأَيِّ ءَالَآءِ رَبِّكُمَا تُكَذِّبَانِ ٧٧

77. ከጌታችሁም ጸጋዎች በየትኛው ታስተባብላላችሁ?

تَبَٰرَكَ ٱسۡمُ رَبِّكَ ذِي ٱلۡجَلَٰلِ وَٱلۡإِكۡرَامِ ٧٨

78. የግርማና የመክበር ባለቤት የኾነው ጌታህ ስም ተባረከ፡፡

# ሱረቱ አል ዋቂዓህ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

1. መከራይቱ በወደቀች ጊዜ፡፡

2. ለመውደቋ አስተባባይ (ነፍስ) የለችም፡፡

3. ዝቅ አድራጊና ከፍ አድራጊ ናት፡፡

4. ምድር መናወጥን በተናወጠች ጊዜ፡፡

5. ተራራዎችም መፍፈርፈርን በተፈረፈሩ ጊዜ (እንደተፈጨ ዱቄት በኾኑ ጊዜ)፡፡

6. የተበተነ ብናኝ በኾኑም ጊዜ

7. ሦስት ዓይነቶችም በኾናችሁ ጊዜ (ታዋርዳለች፤ ታነሳለችም)፡፡

8. የቀኝ ጓዶችም ምን (የተከበሩ) የቀኝ ጓዶች ናቸው፡፡

9. የግራ ጓዶችም ምን (የተዋረዱ) የግራ ጓዶች ናቸው፡፡

10. (ለበጎ ሥራ) ቀዳሚዎቹም (ለገነት) ቀዳሚዎች ናቸው፡፡

11. እነዚያ ባለሟሎቹ ናቸው፡፡

12. በመጠቀሚያ ገነቶች ውስጥ ሲኾኑ፡፡

13. ከፊተኞቹ ብዙ ጭፍሮች ናቸው፡፡

14. ከኋለኞቹም ጥቂቶች ናቸው፡፡

15. በተታቱ አልጋዎች ላይ ይኾናሉ፡፡

16. በእርሷ ላይ የተመቻቹና ፊት ለፊት የተቅጣጩ ሲኾኑ፡፡

# سورة الواقيـة

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

إِذَا وَقَعَتِ ٱلۡوَاقِعَةُ ١

لَيۡسَ لِوَقۡعَتِهَا كَاذِبَةٌ ٢

خَافِضَةٞ رَّافِعَةٌ ٣

إِذَا رُجَّتِ ٱلۡأَرۡضُ رَجّٗا ٤

وَبُسَّتِ ٱلۡجِبَالُ بَسّٗا ٥

فَكَانَتۡ هَبَآءٗ مُّنۢبَثّٗا ٦

وَكُنتُمۡ أَزۡوَٰجٗا ثَلَٰثَةٗ ٧

فَأَصۡحَٰبُ ٱلۡمَيۡمَنَةِ مَآ أَصۡحَٰبُ ٱلۡمَيۡمَنَةِ ٨

وَأَصۡحَٰبُ ٱلۡمَشۡـَٔمَةِ مَآ أَصۡحَٰبُ ٱلۡمَشۡـَٔمَةِ ٩

وَٱلسَّٰبِقُونَ ٱلسَّٰبِقُونَ ١٠

أُوْلَٰٓئِكَ ٱلۡمُقَرَّبُونَ ١١

فِي جَنَّٰتِ ٱلنَّعِيمِ ١٢

ثُلَّةٞ مِّنَ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٣

وَقَلِيلٞ مِّنَ ٱلۡأٓخِرِينَ ١٤

عَلَىٰ سُرُرٖ مَّوۡضُونَةٖ ١٥

مُّتَّكِـِٔينَ عَلَيۡهَا مُتَقَٰبِلِينَ ١٦

17. በእነርሱ ላይ ሁል ጊዜ የማያረጁ ወጣቶች ልጆች ይዘዋወራሉ፡፡

يَطُوفُ عَلَيۡهِمۡ وِلۡدَٰنٞ مُّخَلَّدُونَ ١٧

18. ከጠጅ ምንጭም በብርጭቆዎችና በኩስኩስቶች በጽዋም (በእነርሱ ላይ ይዝዞራሉ)፡፡

بِأَكۡوَابٖ وَأَبَارِيقَ وَكَأۡسٖ مِّن مَّعِينٖ ١٨

19. ከእርሷ የራስ ምታት አያገኛቸውም፤ አይሰክሩምም፡፡

لَّا يُصَدَّعُونَ عَنۡهَا وَلَا يُنزِفُونَ ١٩

20. ከሚመርጡትም ዓይነት በእሸቶች፡፡

وَفَٰكِهَةٖ مِّمَّا يَتَخَيَّرُونَ ٢٠

21. ከሚሹትም በኾነ የበራሪ ሥጋ (ይዞሩባቸዋል)፡፡

وَلَحۡمِ طَيۡرٖ مِّمَّا يَشۡتَهُونَ ٢١

22. ዓይናማዎች የኾኑ ነጫጭ ቆንጆዎችም አሏቸው፡፡

وَحُورٌ عِينٞ ٢٢

23. ልክ እንደተሸፈነ ሉል መሰሎች የኾኑ፡፡

كَأَمۡثَٰلِ ٱللُّؤۡلُوِ ٱلۡمَكۡنُونِ ٢٣

24. በዚያ ይሠሩት በነበሩት ምክንያት ዋጋ ይኾን ዘንድ (ይህንን አደረግንላቸው)፡፡

جَزَآءَۢ بِمَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٢٤

25. በውስጥዋ ውድቅ ንግግርንና መውወንጀልን አይሰሙም፡፡

لَا يَسۡمَعُونَ فِيهَا لَغۡوٗا وَلَا تَأۡثِيمًا ٢٥

26. ግን ሰላም መባባልን (ይሰማሉ)፡፡

إِلَّا قِيلٗا سَلَٰمٗا سَلَٰمٗا ٢٦

27. የቀኝም ጓዶች ምንኛ (የከበሩ) የቀኝ ጓዶች!

وَأَصۡحَٰبُ ٱلۡيَمِينِ مَآ أَصۡحَٰبُ ٱلۡيَمِينِ ٢٧

28. በተቀፈቀፈ (እሾህ በሌለው) ቁርቁራ ውስጥ ናቸው፡፡

فِي سِدۡرٖ مَّخۡضُودٖ ٢٨

29. (ፍሬው) በተነባበረ በሙዝ ዛፍም፡፡

وَطَلۡحٖ مَّنضُودٖ ٢٩

30. በተዘረጋ ጥላ ሥርም፡፡

وَظِلّٖ مَّمۡدُودٖ ٣٠

31. በሚንቧቧ ውሃ አጠገብም፡፡

وَمَآءٖ مَّسۡكُوبٖ ٣١

32. ብዙ (ዓይነት) በኾኑ ፍራፍሬዎችም፡፡

وَفَٰكِهَةٖ كَثِيرَةٖ ٣٢

33. የማትቋረጥም የማትከለከልም የኾነች፡፡

لَّا مَقۡطُوعَةٖ وَلَا مَمۡنُوعَةٖ ٣٣

34. ከፍ በተደረጉ ምንጣፎችም (ሴቶችም መካከል)፡፡

وَفُرُشٖ مَّرۡفُوعَةٍ ٣٤

35. እኛ አዲስ ፍጥረት አድርገን (ለእነርሱ) ፈጠርናቸው፡፡

إِنَّآ أَنشَأۡنَٰهُنَّ إِنشَآءٗ ٣٥

36. ደናግሎችም አደረግናቸው፡፡

فَجَعَلۡنَٰهُنَّ أَبۡكَارًا ٣٦

37. ለባሎቻቸው ተሽሞርሟሪዎች እኩያዎች (አደረግናቸው)፡፡

عُرُبًا أَتۡرَابٗا ٣٧

38. ለቀኝ ጓዶች (አዘጋጀናቸው)፡፡

لِّأَصۡحَٰبِ ٱلۡيَمِينِ ٣٨

39. ከፊተኞቹ ብዙ ጭፍሮች ናቸው፡፡

ثُلَّةٞ مِّنَ ٱلۡأَوَّلِينَ ٣٩

40. ከኋለኞቹም ብዙ ጭፍሮች ናቸው፡፡

وَثُلَّةٞ مِّنَ ٱلۡأٓخِرِينَ ٤٠

41. የግራ ጓደኞችም ምንኛ (የተዋረዱ) የግራ ጓዶች! ናቸው፡፡

وَأَصۡحَٰبُ ٱلشِّمَالِ مَآ أَصۡحَٰبُ ٱلشِّمَالِ ٤١

42. በመርዛም ነፋስ በጣም በፈላ ውሃም ውስጥ ናቸው፡፡

فِي سَمُومٖ وَحَمِيمٖ ٤٢

43. ከጥቁር ጭስም በኾነ ጥላ ውስጥ፡፡

وَظِلّٖ مِّن يَحۡمُومٖ ٤٣

44. ቀዝቃዛም መልካምም ያልኾነ፡፡

لَّا بَارِدٖ وَلَا كَرِيمٍ ٤٤

45. እነርሱ ከዚህ በፊት ቅምጥሎች ነበሩና፡፡

إِنَّهُمۡ كَانُواْ قَبۡلَ ذَٰلِكَ مُتۡرَفِينَ ٤٥

46. በታላቅ ኀጢአትም ላይ ይዘወትሩ ነበሩና፡፡

وَكَانُواْ يُصِرُّونَ عَلَى ٱلۡحِنثِ ٱلۡعَظِيمِ ٤٦

47. ይሉም ነበሩ፡- «በሞትንና ዐፈር፣ ዐጥንቶችም በኾን ጊዜ እኛ በእርግጥ የምንቀሰቀስ ነን?

وَكَانُواْ يَقُولُونَ أَئِذَا مِتۡنَا وَكُنَّا تُرَابٗا وَعِظَٰمًا أَءِنَّا لَمَبۡعُوثُونَ ٤٧

48. «የፊተኞቹ አባቶቻችንም?»

أَوَ ءَابَآؤُنَا ٱلۡأَوَّلُونَ ٤٨

49. በላቸው፡- «ፊተኞቹም ኋለኞቹም፡፡

قُلۡ إِنَّ ٱلۡأَوَّلِينَ وَٱلۡأٓخِرِينَ ٤٩

50. «በተወሰነ ቀን ቀጠሮ በእርግጥ ተሰብሳቢዎች ናቸው፡፡

لَمَجۡمُوعُونَ إِلَىٰ مِيقَٰتِ يَوۡمٖ مَّعۡلُومٖ ٥٠

51. «ከዚያም እናንተ ጠማሞች አስተባባዮች ሆይ!

ثُمَّ إِنَّكُمۡ أَيُّهَا ٱلضَّآلُّونَ ٱلۡمُكَذِّبُونَ ٥١

52. « ከዘቁም ዛፍ በእርግጥ በይዎች ናችሁ፡፡

لَأٓكِلُونَ مِن شَجَرٖ مِّن زَقُّومٖ ٥٢

53. «ከእርሷም ሆዶቻችሁን ሞይዎች ናችሁ፡፡

فَمَالِـُٔونَ مِنْهَا ٱلْبُطُونَ ٥٣

54. «በእርሱ ላይም ከፈላ ውሃ ጠጪዎች ናችሁ፡፡

فَشَٰرِبُونَ عَلَيْهِ مِنَ ٱلْحَمِيمِ ٥٤

55. «የተጠሙንም ግመሎች አጠጣጥ ብጤ ጠጪዎች ናችሁ፡፡»

فَشَٰرِبُونَ شُرْبَ ٱلْهِيمِ ٥٥

56. ይህ በፍርዱ ቀን መስተንግዷቸው ነው፡፡

هَٰذَا نُزُلُهُمْ يَوْمَ ٱلدِّينِ ٥٦

57. እኛ ፈጠርናችሁ አታምኑምን?

نَحْنُ خَلَقْنَٰكُمْ فَلَوْلَا تُصَدِّقُونَ ٥٧

58. (በማኅፀኖች) የምታፈሱትን አያችሁን?

أَفَرَءَيْتُم مَّا تُمْنُونَ ٥٨

59. እናንተ ትፈጥሩታላችሁን? ወይስ እኛ ፈጣሪዎቹ ነን?

ءَأَنتُمْ تَخْلُقُونَهُۥٓ أَمْ نَحْنُ ٱلْخَٰلِقُونَ ٥٩

60. እኛ ሞትን (ጊዜውን) በመካከላችሁ ወሰንን፡፡ እኛም ተሸናፊዎች አይደለንም፡፡

نَحْنُ قَدَّرْنَا بَيْنَكُمُ ٱلْمَوْتَ وَمَا نَحْنُ بِمَسْبُوقِينَ ٦٠

61. ብጤዎቻችሁን በመለወጥና በዚያ በማታውቁትም (ቅርጽ) እናንተን በመፍጠር ላይ (አንሸነፍም)፡፡

عَلَىٰٓ أَن نُّبَدِّلَ أَمْثَٰلَكُمْ وَنُنشِئَكُمْ فِى مَا لَا تَعْلَمُونَ ٦١

62. የፊተኛይቱንም አፈጣጠር በእርግጥ ዐውቃችኋል፡፡ አትገነዘቡምን?

وَلَقَدْ عَلِمْتُمُ ٱلنَّشْأَةَ ٱلْأُولَىٰ فَلَوْلَا تَذَكَّرُونَ ٦٢

63. የምትዘሩትንም አያችሁን?

أَفَرَءَيْتُم مَّا تَحْرُثُونَ ٦٣

64. እናንተ ታበቅሉታላችሁን? ወይስ እኛ አብቃዮቹ ነን?

ءَأَنتُمْ تَزْرَعُونَهُۥٓ أَمْ نَحْنُ ٱلزَّٰرِعُونَ ٦٤

65. ብነሻ ኖሮ ደረቅ ስብርብር ባደረግነውና የምትደነቁም በኾናችሁ ነበር፡፡

لَوْ نَشَآءُ لَجَعَلْنَٰهُ حُطَٰمًا فَظَلْتُمْ تَفَكَّهُونَ ٦٥

66. «እኛ በዕዳ ተያዦች ነን፡፡

إِنَّا لَمُغْرَمُونَ ٦٦

67. «በእርግጥም እኛ (ከመጠቀም) የተከለከልን ነን» (ትሉ ነበር)፡፡

بَلْ نَحْنُ مَحْرُومُونَ ٦٧

68. ያንንም የምትጠጡትን ውሃ አየችሁን?

أَفَرَءَيْتُمُ ٱلْمَآءَ ٱلَّذِى تَشْرَبُونَ ٦٨

69. እናንተ ከደመናው አወረዳችሁትን? ወይስ እኛ አውራጆቹ ነን?

ءَأَنتُمْ أَنزَلْتُمُوهُ مِنَ ٱلْمُزْنِ أَمْ نَحْنُ ٱلْمُنزِلُونَ ٦٩

70. ብንሻ ኖሮ መርጋጋ ባደረግነው ነበር፡፡ አታመሰግኑምን?

لَوْ نَشَآءُ جَعَلْنَٰهُ أُجَاجًا فَلَوْلَا تَشْكُرُونَ ٧٠

71. ያቺንም የምትሰብቋትን እሳት አያችሁን?

أَفَرَءَيۡتُمُ ٱلنَّارَ ٱلَّتِي تُورُونَ ٧١

72. እናንተ ዛፏን ፈጠራችሁን? ወይስ እኛ ፈጣሪዎችዋ ነን?

ءَأَنتُمۡ أَنشَأۡتُمۡ شَجَرَتَهَآ أَمۡ نَحۡنُ ٱلۡمُنشِـُٔونَ ٧٢

73. እኛ (ለገሀናም) ማስታወሻ ለመንገደኞችም መጠቀሚያ አደረግናት፡፡

نَحۡنُ جَعَلۡنَٰهَا تَذۡكِرَةٗ وَمَتَٰعٗا لِّلۡمُقۡوِينَ ٧٣

74. የታላቁን ጌታህንም ስም አወድስ፡፡

فَسَبِّحۡ بِٱسۡمِ رَبِّكَ ٱلۡعَظِيمِ ٧٤

75. በከዋክብትም መጥለቂያዎች እምላለሁ፡፡

۞فَلَآ أُقۡسِمُ بِمَوَٰقِعِ ٱلنُّجُومِ ٧٥

76. እርሱም ብታወቁ ታላቅ መሐላ ነው፡፡

وَإِنَّهُۥ لَقَسَمٞ لَّوۡ تَعۡلَمُونَ عَظِيمٌ ٧٦

77. እርሱ የከበረ ቁርኣን ነው፡፡

إِنَّهُۥ لَقُرۡءَانٞ كَرِيمٞ ٧٧

78. በተጠበቀ መጽሐፍ ውስጥ ነው፡፡

فِي كِتَٰبٖ مَّكۡنُونٖ ٧٨

79. የተጥራሩት እንጅ ሌላ አይነካውም፡፡

لَّا يَمَسُّهُۥٓ إِلَّا ٱلۡمُطَهَّرُونَ ٧٩

80. ከዓለማት ጌታ የተወረደ ነው፡፡

تَنزِيلٞ مِّن رَّبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ٨٠

81. በዚህ ንግግር እናንተ ቸልተኞች ናችሁን?

أَفَبِهَٰذَا ٱلۡحَدِيثِ أَنتُم مُّدۡهِنُونَ ٨١

82. ሲሳያችሁንም (ዝናምን) እናንተ የምታስተባብሉት ታደርጋላችሁን?

وَتَجۡعَلُونَ رِزۡقَكُمۡ أَنَّكُمۡ تُكَذِّبُونَ ٨٢

83. (ነፍስ) ጉረሮንም በደረሰች ጊዜ፡፡

فَلَوۡلَآ إِذَا بَلَغَتِ ٱلۡحُلۡقُومَ ٨٣

84. እናንተ ያን ጊዜ የምታዩ ስትኾኑ፡፡

وَأَنتُمۡ حِينَئِذٖ تَنظُرُونَ ٨٤

85. እኛም ግን አታዩም እንጅ ከእናንተ ይልቅ ወደእርሱ የቀረብን ስንኾን፡፡

وَنَحۡنُ أَقۡرَبُ إِلَيۡهِ مِنكُمۡ وَلَٰكِن لَّا تُبۡصِرُونَ ٨٥

86. የማትዳኙም ከኾናችሁ፡፡

فَلَوۡلَآ إِن كُنتُمۡ غَيۡرَ مَدِينِينَ ٨٦

87. እውነተኞች እንደ ኾናችሁ (ነፍሲቱን ወደ አካሉ) ለምን አትመልሷትም፡፡

تَرۡجِعُونَهَآ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٨٧

88. (ሟቹ) ከባለሟሎቹ ቢኾንማ፡፡

فَأَمَّآ إِن كَانَ مِنَ ٱلۡمُقَرَّبِينَ ٨٨

89. (ለእርሱ) ዕረፍት፣ መልካም ሲሳይም፣ የመጠቀሚያ ገነትም አልለው፡፡

فَرَوۡحٞ وَرَيۡحَانٞ وَجَنَّتُ نَعِيمٖ ﴿٨٩﴾

90. ከቀኝ ጓዶችም ቢኾንማ፡፡

وَأَمَّآ إِن كَانَ مِنۡ أَصۡحَٰبِ ٱلۡيَمِينِ ﴿٩٠﴾

91. ከቀኝ ጓዶች ስለ ኾንክ ላንተ ሰላም አልለህ (ይባላል)፡፡

فَسَلَٰمٞ لَّكَ مِنۡ أَصۡحَٰبِ ٱلۡيَمِينِ ﴿٩١﴾

92. ከሚያስዋሹት ጠማማዎችም ቢኾንማ፡፡

وَأَمَّآ إِن كَانَ مِنَ ٱلۡمُكَذِّبِينَ ٱلضَّآلِّينَ ﴿٩٢﴾

93. ከፈላ ውሃ የኾነ መስተንግዶ አልለው፡፡

فَنُزُلٞ مِّنۡ حَمِيمٖ ﴿٩٣﴾

94. በገሀነም መቃጠልም (አልለው)፡፡

وَتَصۡلِيَةُ جَحِيمٍ ﴿٩٤﴾

95. ይህ እርሱ እርግጠኛ እውነት ነው፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَهُوَ حَقُّ ٱلۡيَقِينِ ﴿٩٥﴾

96. የታላቁንም ጌታህን ስም አወድስ፡፡

فَسَبِّحۡ بِٱسۡمِ رَبِّكَ ٱلۡعَظِيمِ ﴿٩٦﴾

# ሱረቱ አል ሐዲድ

# سورة الحديد

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሰማያትና በምድር ያለው ሁሉ ለአላህ አሞገሰ፡፡ እርሱም ሁሉን አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

سَبَّحَ لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ﴿١﴾

2. የሰማያትና የምድር ንግሥና የእርሱ ብቻ ነው፡፡ ሕያው ያደርጋል፤ ይገድላልም፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ يُحۡيِۦ وَيُمِيتُۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ﴿٢﴾

3. እርሱ ፊትም ያለ፣ ኋላም ቀሪ፣ ግልጽም፣ ስውርም ነው፡፡ እርሱም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

هُوَ ٱلۡأَوَّلُ وَٱلۡأٓخِرُ وَٱلظَّٰهِرُ وَٱلۡبَاطِنُۖ وَهُوَ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٌ ﴿٣﴾

4. እርሱ ያ ሰማያትንና ምድርን በስድስት ቀናት ውስጥ የፈጠረ፤ ከዚያም በዙፋኑ ላይ (ስልጣኑ) የተደላደለ ነው፡፡ በምድር ውስጥ የሚገባውን፣ ከእርሷም የሚወጣውን፣ ከሰማይም የሚወርደውን በእርሷም ውስጥ የሚያርገውን ያውቃል፡፡ እርሱም የትም ብትኾኑ ከእናንተ ጋር ነው፡፡ አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ فِي سِتَّةِ أَيَّامٖ ثُمَّ ٱسۡتَوَىٰ عَلَى ٱلۡعَرۡشِۖ يَعۡلَمُ مَا يَلِجُ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا يَخۡرُجُ مِنۡهَا وَمَا يَنزِلُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ وَمَا يَعۡرُجُ فِيهَاۖ وَهُوَ مَعَكُمۡ أَيۡنَ مَا كُنتُمۡۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ﴿٤﴾

| | |
|---|---|
| 5. የሰማያትና የምድር ንግሥና የእርሱ ብቻ ነው፡፡ ነገሮችም (ሁሉ) ወደ አላህ ብቻ ይመለሳሉ፡፡ | لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَإِلَى ٱللَّهِ تُرۡجَعُ ٱلۡأُمُورُ ٥ |
| 6. ሌሊትን በቀን ውስጥ ያስገባል፡፡ ቀንንም በሌሊት ውስጥ ያስገባል፡፡ እርሱም በልቦች ውስጥ የተደበቁትን ዐዋቂ ነው፡፡ | يُولِجُ ٱلَّيۡلَ فِي ٱلنَّهَارِ وَيُولِجُ ٱلنَّهَارَ فِي ٱلَّيۡلِۚ وَهُوَ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ٦ |
| 7. በአላህና በመልክተኛው እመኑ፡፡ (አላህ) በእርሱ ተተኪዎች ባደረጋችሁም ገንዘብ ለግሱ፡፡ እነዚያም ከእናንተ ውስጥ ያመኑትና የለገሱት ለእነርሱ ታላቅ ምንዳ አልላቸው፡፡ | ءَامِنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَأَنفِقُواْ مِمَّا جَعَلَكُم مُّسۡتَخۡلَفِينَ فِيهِۖ فَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مِنكُمۡ وَأَنفَقُواْ لَهُمۡ أَجۡرٞ كَبِيرٞ ٧ |
| 8. መልክተኛው በጌታችሁ እንድታምኑ የሚጠራችሁ ሲኾን (ጌታችሁ) ኪዳናችሁንም የያዘባችሁ ሲኾን በአላህ የማታምኑት ለእናንተ ምን አልላችሁ? የምታምኑ ብትኾኑ (ወደ እምነት ቸኩሉ)፡፡ | وَمَا لَكُمۡ لَا تُؤۡمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلرَّسُولُ يَدۡعُوكُمۡ لِتُؤۡمِنُواْ بِرَبِّكُمۡ وَقَدۡ أَخَذَ مِيثَٰقَكُمۡ إِن كُنتُم مُّؤۡمِنِينَ ٨ |
| 9. እርሱ ከጨለማዎች ወደ ብርሃን ሊያወጣችሁ ያ ግልጾች የኾኑን አንቀጾች በበሪያው ላይ የሚያወርድ ነው፡፡ አላህም ለእናንተ በእርግጥ ርኅሩህ አዛኝ ነው፡፡ | هُوَ ٱلَّذِي يُنَزِّلُ عَلَىٰ عَبۡدِهِۦٓ ءَايَٰتِۭ بَيِّنَٰتٖ لِّيُخۡرِجَكُم مِّنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ بِكُمۡ لَرَءُوفٞ رَّحِيمٞ ٩ |
| 10. የሰማያትና የምድር ውርስ ለአላህ ሲኾን በአላህ መንገድ የማትለግሱትም ለእናንተ ምን አልላችሁ? ከእናንተ ውስጥ (መካን) ከመከፈት በፊት የለገሰና የተጋደለ ሰው (ከተከፈተች በኋላ ከለገሰና ከተጋደለ ጋር) አይስተካከልም፡፡ ከእነዚያ በኋላ ከለገሱትና ከተጋደሉት እነዚህ በደረጃ በጣም የላቁ ናቸው፡፡ ሁሉንም አላህ መልካሚቱን ተስፋ ቃል ገብቶላቸዋል፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡ | وَمَا لَكُمۡ أَلَّا تُنفِقُواْ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِ وَلِلَّهِ مِيرَٰثُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ لَا يَسۡتَوِي مِنكُم مَّنۡ أَنفَقَ مِن قَبۡلِ ٱلۡفَتۡحِ وَقَٰتَلَۚ أُوْلَٰٓئِكَ أَعۡظَمُ دَرَجَةٗ مِّنَ ٱلَّذِينَ أَنفَقُواْ مِنۢ بَعۡدُ وَقَٰتَلُواْۚ وَكُلّٗا وَعَدَ ٱللَّهُ ٱلۡحُسۡنَىٰۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ خَبِيرٞ ١٠ |
| 11. ያ ለአላህ መልካም ብድርን የሚያበድር ለእርሱም (አላህ) የሚያነባብርለት ሰው ማነው? ለእርሱም መልካም ምንዳ አልለው፡፡ | مَّن ذَا ٱلَّذِي يُقۡرِضُ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنٗا فَيُضَٰعِفَهُۥ لَهُۥ وَلَهُۥٓ أَجۡرٞ كَرِيمٞ ١١ |
| 12. ምእመናንንና ምእምናትን በስተፊቶቻቸው፣ በቀኞቻቸውም ብርሃናቸው የሚሮጥ ሲኾን በምታያቸው ቀን (ምንዳ አልላቸው)፡፡ ዛሬ ብስራታችሁ በውስጦቻቸው ዘውታሪዎች ስትኾኑ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈስሱባቸው ገነቶች ናቸው (ይባላሉ)፡፡ ይህ እርሱ ታላቁ ዕድል ነው፡፡ | يَوۡمَ تَرَى ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ يَسۡعَىٰ نُورُهُم بَيۡنَ أَيۡدِيهِمۡ وَبِأَيۡمَٰنِهِمۖ بُشۡرَىٰكُمُ ٱلۡيَوۡمَ جَنَّٰتٞ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَاۚ ذَٰلِكَ هُوَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ١٢ |

يَوۡمَ يَقُولُ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ وَٱلۡمُنَٰفِقَٰتُ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱنظُرُونَا نَقۡتَبِسۡ مِن نُّورِكُمۡ قِيلَ ٱرۡجِعُواْ وَرَآءَكُمۡ فَٱلۡتَمِسُواْ نُورٗاۖ فَضُرِبَ بَيۡنَهُم بِسُورٖ لَّهُۥ بَابُۢ بَاطِنُهُۥ فِيهِ ٱلرَّحۡمَةُ وَظَٰهِرُهُۥ مِن قِبَلِهِ ٱلۡعَذَابُ ١٣

13. መናፍቃንና መናፍቃት ለእነዚያ ለአመኑት «ተመልከቱን፤ ከብርሃናችሁ እናበራለንና» የሚሉበትን ቀን (አስታውስ)፡፡ «ወደ ኋላችሁ ተመለሱ፡፡ ብርሃንንም ፈልጉ» ይባላሉ፡፡ ግቢው በውስጡ ችሮታ (ገነት) ያለበት ውጭውም ከበኩሉ ስቃይ (እሳት) ያለበት የኾነ (ደጃፍ ባለው አጥር)፡፡

يُنَادُونَهُمۡ أَلَمۡ نَكُن مَّعَكُمۡۖ قَالُواْ بَلَىٰ وَلَٰكِنَّكُمۡ فَتَنتُمۡ أَنفُسَكُمۡ وَتَرَبَّصۡتُمۡ وَٱرۡتَبۡتُمۡ وَغَرَّتۡكُمُ ٱلۡأَمَانِيُّ حَتَّىٰ جَآءَ أَمۡرُ ٱللَّهِ وَغَرَّكُم بِٱللَّهِ ٱلۡغَرُورُ ١٤

14. «ከእናንተ ጋር አልነበርንምን?» በማለት ይጠሩዋቸዋል፡፡ «እውነት ነው፡፡ ግን እናንተ ነፍሶቻችሁን አጠፋችሁ፡፡ (በነቢዩ አደጋዎችን) ተጠባበቃችሁም፡፡ ተጠራጠራችሁም፡፡ የአላህም ትዕዛዝ እስከ መጣ ድረስ ከንቱ ምኞቶች አታለሏችሁ፡፡ አታላዩም (ሰይጣን) በአላህ (መታገስ) ሸነገላችሁ፤» ይሏቸዋል፡፡

فَٱلۡيَوۡمَ لَا يُؤۡخَذُ مِنكُمۡ فِدۡيَةٞ وَلَا مِنَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْۚ مَأۡوَىٰكُمُ ٱلنَّارُۖ هِيَ مَوۡلَىٰكُمۡۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ١٥

15. «ዛሬም ከእናንተ ቤዛ አይወሰድም፡፡ ከእነዚያ ከካዱትም፡፡ መኖሪያችሁ እሳት ናት፡፡ እርሷ ተገቢያችሁ ናት፡፡ ምን ትከፋም መመለሻ!» (ይሏቸዋል)፡፡

۞أَلَمۡ يَأۡنِ لِلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ أَن تَخۡشَعَ قُلُوبُهُمۡ لِذِكۡرِ ٱللَّهِ وَمَا نَزَلَ مِنَ ٱلۡحَقِّ وَلَا يَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ مِن قَبۡلُ فَطَالَ عَلَيۡهِمُ ٱلۡأَمَدُ فَقَسَتۡ قُلُوبُهُمۡۖ وَكَثِيرٞ مِّنۡهُمۡ فَٰسِقُونَ ١٦

16. ለነዚያ ለአመኑት ለአላህ ተግሳጽና ከቁርኣንም ለወረደው ልቦቻቸው ሊፈሩ እንደእነዚያም በፊት መጽሐፍን እንደ ተሰጡትና በእነርሱ ላይ ጊዜ እንደረዘመባቸው ልቦቻቸውም እንደ ደረቁት ላይኾኑ (ጊዜው) አልቀረበምን? ከእነርሱም ብዙዎቹ አመጸኞች ናቸው፡፡

ٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ يُحۡيِ ٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ مَوۡتِهَاۚ قَدۡ بَيَّنَّا لَكُمُ ٱلۡأٓيَٰتِ لَعَلَّكُمۡ تَعۡقِلُونَ ١٧

17. አላህ ምድርን ከሞተች በኋላ ሕያው የሚያደርጋት መኾኑን ዕወቁ፡፡ ታውቁ ዘንድ አንቀጾችን ለእናንተ በእርግጥ አብራራንላችሁ፡፡

إِنَّ ٱلۡمُصَّدِّقِينَ وَٱلۡمُصَّدِّقَٰتِ وَأَقۡرَضُواْ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنٗا يُضَٰعَفُ لَهُمۡ وَلَهُمۡ أَجۡرٞ كَرِيمٞ ١٨

18. የመጸወቱ ወንዶችና፣ የመጸወቱ ሴቶች፣ ለአላህም መልካምን ብድር ያበደሩ ለእነርሱ መልካም ምንዳ አልላቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦٓ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلصِّدِّيقُونَۖ وَٱلشُّهَدَآءُ عِندَ رَبِّهِمۡ لَهُمۡ أَجۡرُهُمۡ وَنُورُهُمۡۖ وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَحِيمِ ١٩

19. እነዚያም በአላህና በመልክተኞቹ ያመኑት እነዚያ እነርሱ በጣም እውነተኞቹ በጌታቸውም ዘንድ መስካሪዎቹ ናቸው፡፡ ለእነርሱ ምንዳቸው ብርሃናቸውም አልላቸው፡፡ እነዚያም የካዱት በአንቀጾቻችንም ያስተባበሉት እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡

20. ቅርቢቱ ሕይወት ጨዋታና ዛዛታ፣ ማጌጫም፣ በመካከላችሁም መፎካከሪያ፣ በገንዘቦችና በልጆችም ብዛት መበላለጫ ብቻ መኾንዋን ዕወቁ፡፡ (እርሷ) በቃዩ ገበሬዎችን እንደሚያስደስት ዝናም፣ ከዚያም በቃዩ እንደሚደርቅና ገርጥቶ እንደምታየው፣ ከዚያም የተሰባበረ እንደሚኾን ብጤ ናት፣ በመጨረሻይቱም ዓለም ብርቱ ቅጣት ከአላህም ምሕረትና ውዴታ አልለ፡ ፡ የቅርቢቱም ሕይወት የመታለያ ጥቅም እንጅ ሌላ አይደለችም፡፡

ٱعۡلَمُوٓاْ أَنَّمَا ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَا لَعِبٞ وَلَهۡوٞ وَزِينَةٞ وَتَفَاخُرُۢ بَيۡنَكُمۡ وَتَكَاثُرٞ فِي ٱلۡأَمۡوَٰلِ وَٱلۡأَوۡلَٰدِۖ كَمَثَلِ غَيۡثٍ أَعۡجَبَ ٱلۡكُفَّارَ نَبَاتُهُۥ ثُمَّ يَهِيجُ فَتَرَىٰهُ مُصۡفَرّٗا ثُمَّ يَكُونُ حُطَٰمٗاۖ وَفِي ٱلۡأٓخِرَةِ عَذَابٞ شَدِيدٞ وَمَغۡفِرَةٞ مِّنَ ٱللَّهِ وَرِضۡوَٰنٞۚ وَمَا ٱلۡحَيَوٰةُ ٱلدُّنۡيَآ إِلَّا مَتَٰعُ ٱلۡغُرُورِ ۝٢٠

21. ከጌታችሁ ወደ ኾነች ምሕረት፣ ወርዷ እደ ሰማይና ምድር ወርድ ወደ ሆነችም ገነት ተሽቀዳደሙ፡፡ ለእነዚያ በአላህና በመልክተኞቹ ላመኑት ተዘጋጅታለች፡፡ ይህ የአላህ ችሮታ ነው፡፡ ለሚሻው ሰው ይሰጠዋል፡፡ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

سَابِقُوٓاْ إِلَىٰ مَغۡفِرَةٖ مِّن رَّبِّكُمۡ وَجَنَّةٍ عَرۡضُهَا كَعَرۡضِ ٱلسَّمَآءِ وَٱلۡأَرۡضِ أُعِدَّتۡ لِلَّذِينَ ءَامَنُواْ بِٱللَّهِ وَرُسُلِهِۦۚ ذَٰلِكَ فَضۡلُ ٱللَّهِ يُؤۡتِيهِ مَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ ذُو ٱلۡفَضۡلِ ٱلۡعَظِيمِ ۝٢١

22. በምድርም በነፍሶቻችሁም መከራ (ማንንም) አትነካም ሳንፈጥራት በፊት በመጽሐፍ የተመዘገበች ብትኾን እንጅ፡፡ ይህ በአላህ ላይ ገር ነው፡፡

مَآ أَصَابَ مِن مُّصِيبَةٖ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَا فِيٓ أَنفُسِكُمۡ إِلَّا فِي كِتَٰبٖ مِّن قَبۡلِ أَن نَّبۡرَأَهَآۚ إِنَّ ذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٞ ۝٢٢

23. (ይህ ማሳወቃችን) ባመለጣችሁ ጸጋ ላይ እንዳታዝኑ አላህም በሰጣችሁ ነገር (በትዕቢት) እንዳትደሰቱ ነው፡፡ አላህም ኩራተኛን ጉረኛን ሁሉ አይወድም፡፡

لِّكَيۡلَا تَأۡسَوۡاْ عَلَىٰ مَا فَاتَكُمۡ وَلَا تَفۡرَحُواْ بِمَآ ءَاتَىٰكُمۡۗ وَٱللَّهُ لَا يُحِبُّ كُلَّ مُخۡتَالٖ فَخُورٍ ۝٢٣

24. (እነርሱም) እነዚያ የሚሰስቱና ሰዎችንም በስስት የሚያዝዙ ናቸው፡፡ (ከእውነት) የሚሸሽም ሰው (ጥፋቱ በራሱ ላይ ነው)፡፡ አላህም እርሱ ተብቃቂ ምስጉን ነው፡ ፡

ٱلَّذِينَ يَبۡخَلُونَ وَيَأۡمُرُونَ ٱلنَّاسَ بِٱلۡبُخۡلِۗ وَمَن يَتَوَلَّ فَإِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلۡغَنِيُّ ٱلۡحَمِيدُ ۝٢٤

25. መልክተኞቻችንን በግልጽ ማስረጃዎች በእርግጥ ላክን፡፡ ሰዎችም በትክክል ቀጥ እንዲሉ መጽሐፎችንና ሚዛንን ወደእነርሱ አወረድን፤ ብረትንም በውስጡ ብርቱ ኀይልና ለሰዎችም መጠቀቀሚያዎች ያልሉበት ሲኾን አወረድን፡፡ (እንዲጠቀሙበት) አላህም ሃይማኖቱንና መልክተኞቹን በሩቅ ኾኖ የሚረዳውን ሰው ሊያውቅ (ሊገልጽ አወረደው)፡፡ አላህ ብርቱ አሸናፊ ነውና፡፡

لَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا رُسُلَنَا بِٱلۡبَيِّنَٰتِ وَأَنزَلۡنَا مَعَهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡمِيزَانَ لِيَقُومَ ٱلنَّاسُ بِٱلۡقِسۡطِۖ وَأَنزَلۡنَا ٱلۡحَدِيدَ فِيهِ بَأۡسٞ شَدِيدٞ وَمَنَٰفِعُ لِلنَّاسِ وَلِيَعۡلَمَ ٱللَّهُ مَن يَنصُرُهُۥ وَرُسُلَهُۥ بِٱلۡغَيۡبِۚ إِنَّ ٱللَّهَ قَوِيٌّ عَزِيزٞ ۝٢٥

26. ኑሕን፣ ኢብራሂምንም በእርግጥ ላክን፡፡ በዘሮቻቸውም ውስጥ ነቢይነትንና መጽሐፎችን አደረግን፡፡ ከእነርሱም ቅን አልለ፡፡ ከእነርሱም ብዙዎቹ አመጸኞች ናቸው፡፡

وَلَقَدۡ أَرۡسَلۡنَا نُوحٗا وَإِبۡرَٰهِيمَ وَجَعَلۡنَا فِي ذُرِّيَّتِهِمَا ٱلنُّبُوَّةَ وَٱلۡكِتَٰبَۖ فَمِنۡهُم مُّهۡتَدٖۖ وَكَثِيرٞ مِّنۡهُمۡ فَٰسِقُونَ ۝٢٦

27. ከዚያም በዱካዎቻቸው ላይ መልክተኞቻችንን አስከታተልን፡፡ የመርየምን ልጅ ዒሳንም አስከተልን፡፡ ኢንጂልንም ሰጠነው፡፡ በእነዚያም በተከተሉት (ሰዎች) ልቦች ውስጥ መለዘብንና እዝነትን፣ አዲስ የፈጠሩዋትንም ምንኩስና አደረግን፡፡ በእነርሱ ላይ (ምንኩስናን) አልጻፍናትም፡፡ ግን የአላህን ውዴታ ለመፈለግ ሲሉ (ፈጠሩዋት)፡፡ ተገቢ አጠባበቋንም፤ አልጠበቋትም፡፡ ከእነርሱም ለእነዚያ ላመኑት ምንዳቸውን ሰጠናቸው፡፡ ከእነርሱም ብዙዎቹ አመጸኞች ናቸው፡፡

ثُمَّ قَفَّيْنَا عَلَىٰٓ ءَاثَٰرِهِم بِرُسُلِنَا وَقَفَّيْنَا بِعِيسَى ٱبْنِ مَرْيَمَ وَءَاتَيْنَٰهُ ٱلْإِنجِيلَ ۖ وَجَعَلْنَا فِى قُلُوبِ ٱلَّذِينَ ٱتَّبَعُوهُ رَأْفَةً وَرَحْمَةً ۚ وَرَهْبَانِيَّةً ٱبْتَدَعُوهَا مَا كَتَبْنَٰهَا عَلَيْهِمْ إِلَّا ٱبْتِغَآءَ رِضْوَٰنِ ٱللَّهِ فَمَا رَعَوْهَا حَقَّ رِعَايَتِهَا ۖ فَـَٔاتَيْنَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ مِنْهُمْ أَجْرَهُمْ ۖ وَكَثِيرٌ مِّنْهُمْ فَٰسِقُونَ ﴿٢٧﴾

28. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ በመልእክተኛውም እመኑ፡፡ ከችሮታው ሁለትን ክፍሎች ይሰጣችኋልና፡፡ ለእናንተም በእርሱ የምትኼዱበት የኾነ ብርሃንን ያደርግላችኋል፡፡ ለእናንተም ይምራል፡፡ አላህም መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ وَءَامِنُوا۟ بِرَسُولِهِۦ يُؤْتِكُمْ كِفْلَيْنِ مِن رَّحْمَتِهِۦ وَيَجْعَل لَّكُمْ نُورًا تَمْشُونَ بِهِۦ وَيَغْفِرْ لَكُمْ ۚ وَٱللَّهُ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿٢٨﴾

29. (ይህም) የመጽሐፉ ሰዎች ከአላህ ችሮታ በምንም ላይ የማይችሉ መኾናቸውን ችሮታም በአላህ እጅ ነው፡ ፡ ለሚሻው ሰው ይሰጠዋል ማለትን እንዲያውቁ ነው፤ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

لِّئَلَّا يَعْلَمَ أَهْلُ ٱلْكِتَٰبِ أَلَّا يَقْدِرُونَ عَلَىٰ شَىْءٍ مِّن فَضْلِ ٱللَّهِ ۙ وَأَنَّ ٱلْفَضْلَ بِيَدِ ٱللَّهِ يُؤْتِيهِ مَن يَشَآءُ ۚ وَٱللَّهُ ذُو ٱلْفَضْلِ ٱلْعَظِيمِ ﴿٢٩﴾

# ሱረቱ አል ሙጃደላ

# سورة المجادلة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አላህ የዚያችን በባሏ (ነገር) የምትከራከርህንና ወደ አላህ የምታሰሙተውን (ሴት) ቃል በእርግጥ ሰማ፡፡ አላህም (በንግግር) መመላለሳችሁን ይሰማል፡፡ አላህ ሰሚ ተመልካች ነውና፡፡

قَدْ سَمِعَ ٱللَّهُ قَوْلَ ٱلَّتِى تُجَٰدِلُكَ فِى زَوْجِهَا وَتَشْتَكِىٓ إِلَى ٱللَّهِ وَٱللَّهُ يَسْمَعُ تَحَاوُرَكُمَآ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعٌۢ بَصِيرٌ ﴿١﴾

2. እነዚያ ከእናንተ ውስጥ ከሚስቶቻቸው እንደናቶቻችን ጀርባዎች ይኹኑብን በማለት የሚምሉ እነርሱ እናቶቻቸው አይደሉም፡፡ እናቶቻቸው እኒያ የወለዱዋቸው ብቻ ናቸው፡፡ እነርሱም (በዚህ ቃል) ከንግግር የተጠላንና ውሸትን በእርግጥ ይናገራሉ፡፡ አላህም (ለሚጸጸት) ይቅር ባይ መሓሪ ነው፡፡

ٱلَّذِينَ يُظَٰهِرُونَ مِنكُم مِّن نِّسَآئِهِم مَّا هُنَّ أُمَّهَٰتِهِمْ ۖ إِنْ أُمَّهَٰتُهُمْ إِلَّا ٱلَّٰٓـِٔى وَلَدْنَهُمْ ۚ وَإِنَّهُمْ لَيَقُولُونَ مُنكَرًا مِّنَ ٱلْقَوْلِ وَزُورًا ۚ وَإِنَّ ٱللَّهَ لَعَفُوٌّ غَفُورٌ ﴿٢﴾

3. እነዚያም ከሚስቶቻቸው እንደናቶቻችን ጀርባዎች ኹኑብን በማለት የሚምሉ ከዚያም ወደ ተናገሩት የሚመለሱ ሳይነካኩ በፊት ጫንቃን ነጻ ማውጣት በነርሱ ላይ አለባቸው፡፡ እነሆ በእርሱ ትገሰጹበታላችሁ፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጥ ዓዋቂ ነው፡፡

وَٱلَّذِينَ يُظَٰهِرُونَ مِن نِّسَآئِهِمْ ثُمَّ يَعُودُونَ لِمَا قَالُوا۟ فَتَحْرِيرُ رَقَبَةٍ مِّن قَبْلِ أَن يَتَمَآسَّا ۚ ذَٰلِكُمْ تُوعَظُونَ بِهِۦ ۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرٌ ﴿٣﴾

4. ያላገኘም ሰው ከመነካካታቸው በፊት ሁለት የተከታተሉ ወሮችን መጾም አለበት፡፡ ያልቻለም ሰው ስድሳ ድኾችን ማብላት (አለበት)፡፡ ይህ በአላህና በመልክተኛው እንድታምኑ ነው፡፡ ይህችም የአላህ ሕግጋት ናት፡፡ ለከሓዲዎችም አሳማሚ ቅጣት አልላቸው፡፡

فَمَن لَّمْ يَجِدْ فَصِيَامُ شَهْرَيْنِ مُتَتَابِعَيْنِ مِن قَبْلِ أَن يَتَمَآسَّا ۖ فَمَن لَّمْ يَسْتَطِعْ فَإِطْعَامُ سِتِّينَ مِسْكِينًا ۚ ذَٰلِكَ لِتُؤْمِنُوا۟ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ ۚ وَتِلْكَ حُدُودُ ٱللَّهِ ۗ وَلِلْكَٰفِرِينَ عَذَابٌ أَلِيمٌ ﴿٤﴾

5. ግልጾች ማስረጃዎችን ያወረድን ስንኾን እነዚያ አላህንና መልክተኛውን የሚከራከሩ እነዚያ ከእነርሱ በፊት የነበሩት እንደተዋረዱ ይዋረዳሉ፡፡ ለከሓዲዎችም አዋራጅ ቅጣት አልላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُحَآدُّونَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ كُبِتُوا۟ كَمَا كُبِتَ ٱلَّذِينَ مِن قَبْلِهِمْ ۚ وَقَدْ أَنزَلْنَآ ءَايَٰتٍۭ بَيِّنَٰتٍ ۚ وَلِلْكَٰفِرِينَ عَذَابٌ مُّهِينٌ ﴿٥﴾

6. አላህ ሁላቸውንም በሚቀስቅሳቸው ቀን (ይቀጣቸዋል)፡፡ የሠሩትንም ሁሉ ይነግራቸዋል፡፡ የረሱት ሲኾኑ አላህ ዐውቆታል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ዐዋቂ ነው፡፡

يَوْمَ يَبْعَثُهُمُ ٱللَّهُ جَمِيعًا فَيُنَبِّئُهُم بِمَا عَمِلُوٓا۟ ۚ أَحْصَىٰهُ ٱللَّهُ وَنَسُوهُ ۚ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ شَهِيدٌ ﴿٦﴾

7. አላህ በሰማያት ውስጥ ያለውን በምድርም ውስጥ ያለውን ሁሉ የሚያውቅ መኾኑን አታይምን? ከሦስት ሰዎች መሾካሾክ አይኖርም እርሱ አራተኛቸው ቢኾን እንጅ፡፡ ከአምስትም (አይኖርም) እርሱ ስድስተኛቸው ቢኾን እንጅ፡፡ ከዚያ ያነሰም የበዛም (አይኖርም) እርሱ የትም ቢኾኑ እንጂ፡፡ ከዚያም በትንሣኤ ቀን የሠሩትን ሁሉ ይነግራቸዋል፡፡ አላህ ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَمْ تَرَ أَنَّ ٱللَّهَ يَعْلَمُ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۖ مَا يَكُونُ مِن نَّجْوَىٰ ثَلَٰثَةٍ إِلَّا هُوَ رَابِعُهُمْ وَلَا خَمْسَةٍ إِلَّا هُوَ سَادِسُهُمْ وَلَآ أَدْنَىٰ مِن ذَٰلِكَ وَلَآ أَكْثَرَ إِلَّا هُوَ مَعَهُمْ أَيْنَ مَا كَانُوا۟ ۖ ثُمَّ يُنَبِّئُهُم بِمَا عَمِلُوا۟ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ بِكُلِّ شَىْءٍ عَلِيمٌ ﴿٧﴾

8. ወደእነዚያ (በመጥፎ) ከመሾካሾክ ወደ ተከለከሉት፣ ከዚያም ከእርሱ ወደ ተከለከሉት ነገር ወደሚመለሱት፣ በኃጢአትና ድንበር በማለፍ መልክተኛውን በመቃወም ወደሚንሾካሾኩት አላየህምን? (ሰላም ሲሉ) በመጡህም ጊዜ አላህ በእርሱ ባላናገረህ ቃል ያናግሩሃል፡፡ በነፍሶቻቸውም ውስጥ (ነቢይ ከኾንክ) «በምንለው ነገር አላህ አይቀጣንም ኖሮአልን?» ይላሉ፡፡ ገሀነም የሚገቧት ሲኾኑ በቂያቸው ናት፡፡ ምን ትከፋም መመለሻ!

أَلَمْ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ نُهُوا۟ عَنِ ٱلنَّجْوَىٰ ثُمَّ يَعُودُونَ لِمَا نُهُوا۟ عَنْهُ وَيَتَنَٰجَوْنَ بِٱلْإِثْمِ وَٱلْعُدْوَٰنِ وَمَعْصِيَتِ ٱلرَّسُولِ ۖ وَإِذَا جَآءُوكَ حَيَّوْكَ بِمَا لَمْ يُحَيِّكَ بِهِ ٱللَّهُ وَيَقُولُونَ فِىٓ أَنفُسِهِمْ لَوْلَا يُعَذِّبُنَا ٱللَّهُ بِمَا نَقُولُ ۚ حَسْبُهُمْ جَهَنَّمُ يَصْلَوْنَهَا ۖ فَبِئْسَ ٱلْمَصِيرُ ﴿٨﴾

9. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በተንሾካሾካችሁ ጊዜ በኃጢአትና ወሰንን በማለፍ፣ መልክተኛውንም በመቃወም አትንሾካሾኩ፡፡ ግን በበጎ ሥራና አላህን በመፍራት ተወያዩ፡፡ ያንንም ወደእርሱ የምትሰበሰቡበትን አላህን ፍሩ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ إِذَا تَنَٰجَيْتُمْ فَلَا تَتَنَٰجَوْا۟ بِٱلْإِثْمِ وَٱلْعُدْوَٰنِ وَمَعْصِيَتِ ٱلرَّسُولِ وَتَنَٰجَوْا۟ بِٱلْبِرِّ وَٱلتَّقْوَىٰ ۖ وَٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ ٱلَّذِىٓ إِلَيْهِ تُحْشَرُونَ ﴿٩﴾

10. (በመጥፎ) መንሾካሾክ ከሰይጣን ብቻ ነው፡፡ እነዚያ ያመኑት ያዝኑ ዘንድ (ይቀሰቅሰዋል)፡፡ በአላህ ፈቃድ ካልኾነ በቀር በምንም አይጎዳቸውም፡፡ በአላህ ላይም አማኞች ይጠጉ፡፡

إِنَّمَا ٱلنَّجْوَىٰ مِنَ ٱلشَّيْطَٰنِ لِيَحْزُنَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ وَلَيْسَ بِضَآرِّهِمْ شَيْـًٔا إِلَّا بِإِذْنِ ٱللَّهِ ۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلْيَتَوَكَّلِ ٱلْمُؤْمِنُونَ ﴿١٠﴾

11. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ለእናንተ በመቀመጫዎች ስፍራ ተስፋፉ በተባላችሁ ጊዜ (ስፍራን) አስፉ፡፡ አላህ ያሰፋላችኋልና፡፡ ተነሱ በተባላችሁም ጊዜ ተነሱ፡፡ አላህ ከናንተ እነዚያን ያመኑትንና እነዚያንም ዕውቀትን የተሰጡትን በደረጃዎች ከፍ ያደርጋል፡፡ አላህም በምትሰሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ إِذَا قِيلَ لَكُمْ تَفَسَّحُوا۟ فِى ٱلْمَجَٰلِسِ فَٱفْسَحُوا۟ يَفْسَحِ ٱللَّهُ لَكُمْ ۖ وَإِذَا قِيلَ ٱنشُزُوا۟ فَٱنشُزُوا۟ يَرْفَعِ ٱللَّهُ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ مِنكُمْ وَٱلَّذِينَ أُوتُوا۟ ٱلْعِلْمَ دَرَجَٰتٍ ۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرٌ ﴿١١﴾

12. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! መልክተኛውን በተወያያችሁ ጊዜ ከመወያየታችሁ በፊት ምጽዋትን አስቀድሙ፡፡ ይህ ለእናንተ መልካም ነው፡፡ አጥሪም ነው፡፡ ባታገኙም አላህ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓا۟ إِذَا نَٰجَيْتُمُ ٱلرَّسُولَ فَقَدِّمُوا۟ بَيْنَ يَدَىْ نَجْوَىٰكُمْ صَدَقَةً ۚ ذَٰلِكَ خَيْرٌ لَّكُمْ وَأَطْهَرُ ۚ فَإِن لَّمْ تَجِدُوا۟ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١٢﴾

13. ከውይይታችሁ በፊት ምጽዋቶችን ከማስቀደም (ድህነትን) ፈራችሁን? ባልሠራችሁም ጊዜ አላህ ከእናንተ ጸጸትን የተቀበለ ሲኾን ሶላትን ስገዱ፡፡ ዘካንም ስጡ፡፡ አላህንና መልክተኛውንም ታዘዙ፡፡ አላህም ውስጥ ዐዋቂ ነው፡፡

ءَأَشْفَقْتُمْ أَن تُقَدِّمُوا۟ بَيْنَ يَدَىْ نَجْوَىٰكُمْ صَدَقَٰتٍ ۚ فَإِذْ لَمْ تَفْعَلُوا۟ وَتَابَ ٱللَّهُ عَلَيْكُمْ فَأَقِيمُوا۟ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُوا۟ ٱلزَّكَوٰةَ وَأَطِيعُوا۟ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ ۚ وَٱللَّهُ خَبِيرٌۢ بِمَا تَعْمَلُونَ ﴿١٣﴾

14. ወደእነዚያ አላህ በእነርሱ ላይ የተቆጣባቸውን ሕዝቦች ወደ ተወዳጁት (መናፍቃን) አላየኽምን? እነርሱ ከእናንተ አይደሉም፡፡ ከእነርሱም አይደሉም፡፡ እነርሱም የሚያውቁ ሲኾኑ በውሸት ላይ ይምላሉ፡፡

۞ أَلَمْ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ تَوَلَّوْا۟ قَوْمًا غَضِبَ ٱللَّهُ عَلَيْهِم مَّا هُم مِّنكُمْ وَلَا مِنْهُمْ وَيَحْلِفُونَ عَلَى ٱلْكَذِبِ وَهُمْ يَعْلَمُونَ ﴿١٤﴾

15. አላህ ለእነርሱ ብርቱን ቅጣት አዘጋጀ፡፡ እነርሱ ይሠሩት የነበሩት ሥራ ምንኛ ከፋ!

أَعَدَّ ٱللَّهُ لَهُمْ عَذَابًا شَدِيدًا ۖ إِنَّهُمْ سَآءَ مَا كَانُوا۟ يَعْمَلُونَ ﴿١٥﴾

16. መሓሎቻቸውን ጋሻ አድርገው ያዙ፡፡ ከአላህም መንገድ አገዱ፡፡ ስለዚህ ለእነርሱ አዋራጅ ቅጣት አልላቸው፡፡

ٱتَّخَذُوٓا۟ أَيْمَٰنَهُمْ جُنَّةً فَصَدُّوا۟ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِ فَلَهُمْ عَذَابٌ مُّهِينٌ ﴿١٦﴾

17. ገንዘቦቻቸውና ልጆቻቸው ከአላህ (ቅጣት) ምንንም ከእነርሱ አያድኗቸውም፡፡ እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በእርሷ ውስጥ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡

لَّن تُغْنِىَ عَنْهُمْ أَمْوَٰلُهُمْ وَلَآ أَوْلَٰدُهُم مِّنَ ٱللَّهِ شَيْـًٔا ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ أَصْحَٰبُ ٱلنَّارِ ۖ هُمْ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿١٧﴾

18. አላህ የተሰበሰቡ ኾነው በሚያስነሳቸው ቀን ለእናንተ እንደሚምሉላችሁም እነርሱ (በሚጠቅም) ነገር ላይ መኾናቸውን የሚያስቡ ኾነው ለእርሱ በሚምሉበት ቀን (አዋራጅ ቅጣት አልላቸው)፡፡ ንቁ! እነርሱ ውሸታሞቹ እነርሱ ናቸው፡፡

يَوْمَ يَبْعَثُهُمُ ٱللَّهُ جَمِيعًا فَيَحْلِفُونَ لَهُۥ كَمَا يَحْلِفُونَ لَكُمْ ۖ وَيَحْسَبُونَ أَنَّهُمْ عَلَىٰ شَىْءٍ ۚ أَلَآ إِنَّهُمْ هُمُ ٱلْكَٰذِبُونَ ﴿١٨﴾

19. በእነርሱ ላይ ሰይጣን ተሾመባቸው፡፡ አላህንም ማስታወስን አስረሳቸው፡፡ እነዚያ የሰይጣን ጭፍሮች ናቸው፡፡ ንቁ! የሰይጣን ጭፍሮች ከሳሪዎቹ እነርሱ ናቸው፡፡

ٱسْتَحْوَذَ عَلَيْهِمُ ٱلشَّيْطَٰنُ فَأَنسَىٰهُمْ ذِكْرَ ٱللَّهِ ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ حِزْبُ ٱلشَّيْطَٰنِ ۚ أَلَآ إِنَّ حِزْبَ ٱلشَّيْطَٰنِ هُمُ ٱلْخَٰسِرُونَ ﴿١٩﴾

20. እነዚያ አላህንና መልክተኛውን የሚከራከሩት እነዚያ በጣም በወራዶቹ ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يُحَآدُّونَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥٓ أُو۟لَٰٓئِكَ فِى ٱلْأَذَلِّينَ ﴿٢٠﴾

21. አላህ፡- «እኔ በእርግጥ አሸንፋለሁ፣ መልክተኞቼም (ያሸንፋሉ)» ሲል፤ ጽፏል፡፡ አላህ ብርቱ አሸናፊ ነውና፡፡

كَتَبَ ٱللَّهُ لَأَغْلِبَنَّ أَنَا۠ وَرُسُلِىٓ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ قَوِىٌّ عَزِيزٌ ﴿٢١﴾

22. በአላህና በመጨረሻው ቀን የሚያምኑትን ሕዝቦች አላህንና መልክተኛውን የሚከራከሩትን ሰዎች፤ አባቶቻቸው፣ ወይም ልጆቻቸው፣ ወይም ወንድሞቻቸው፣ ወይም ዘመዶቻቸው ቢኾኑም እንኳ የሚወዳጁ ኾነው አታገኛቸውም፡፡ እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ እምነትን ጽፏል፡፡ ከእርሱም በኾነ መንፈስ ደግፏቸዋል፡፡ ከሥሮቻቸውም ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪዎች ሲኾኑ ያገባቸዋል፡፡ አላህ ከእነርሱ ወዷል፡፡ ከእርሱም ወደዋል፡፡ እነዚያ የአላህ ሕዝቦች ናቸው፡፡ ንቁ! የአላህ ሕዝቦች እነርሱ ምኞታቸውን የሚያገኙ ናቸው፡፡

لَّا تَجِدُ قَوْمًا يُؤْمِنُونَ بِٱللَّهِ وَٱلْيَوْمِ ٱلْءَاخِرِ يُوَآدُّونَ مَنْ حَآدَّ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ وَلَوْ كَانُوٓا۟ ءَابَآءَهُمْ أَوْ أَبْنَآءَهُمْ أَوْ إِخْوَٰنَهُمْ أَوْ عَشِيرَتَهُمْ ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ كَتَبَ فِى قُلُوبِهِمُ ٱلْإِيمَٰنَ وَأَيَّدَهُم بِرُوحٍ مِّنْهُ ۖ وَيُدْخِلُهُمْ جَنَّٰتٍ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَا ۚ رَضِىَ ٱللَّهُ عَنْهُمْ وَرَضُوا۟ عَنْهُ ۚ أُو۟لَٰٓئِكَ حِزْبُ ٱللَّهِ ۚ أَلَآ إِنَّ حِزْبَ ٱللَّهِ هُمُ ٱلْمُفْلِحُونَ ﴿٢٢﴾

# ሱረቱ አል ሐሽር

# سورة الحشر

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሰማያትና በምድር ውስጥ ያለው ሁሉ ለአላህ አሞገሰ፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

سَبَّحَ لِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۖ وَهُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ﴿١﴾

هُوَ ٱلَّذِيٓ أَخۡرَجَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ مِن دِيَٰرِهِمۡ لِأَوَّلِ ٱلۡحَشۡرِۚ مَا ظَنَنتُمۡ أَن يَخۡرُجُواْۖ وَظَنُّوٓاْ أَنَّهُم مَّانِعَتُهُمۡ حُصُونُهُم مِّنَ ٱللَّهِ فَأَتَىٰهُمُ ٱللَّهُ مِنۡ حَيۡثُ لَمۡ يَحۡتَسِبُواْۖ وَقَذَفَ فِي قُلُوبِهِمُ ٱلرُّعۡبَۚ يُخۡرِبُونَ بُيُوتَهُم بِأَيۡدِيهِمۡ وَأَيۡدِي ٱلۡمُؤۡمِنِينَ فَٱعۡتَبِرُواْ يَٰٓأُوْلِي ٱلۡأَبۡصَٰرِ ٢

2. እርሱ ያ ከመጽሐፉ ሰዎች እነዚያን የካዱትን ከቤቶቻቸው ለመጀመሪያው ማውጣት ያወጣቸው ነው፡፡ መውጣታቸውን አላሰባችሁም፡፡ እነርሱም ምሽጎቻቸው ከአላህ (ኀይል) የሚከላከሉላቸው መኾናቸውን አሰቡ፡፡ አላህም ካላሰቡት ስፍራ መጣባቸው፡፡ በልቦቻቸውም ውስጥ መርበድበድን ጣለባቸው፡፡ ቤቶቻቸውን በእጆቻቸውና በምእምናኖቹ እጆች ያፈርሳሉ፡፡ አስተውሉም የአእምሮ ባለቤቶች ሆይ!

وَلَوۡلَآ أَن كَتَبَ ٱللَّهُ عَلَيۡهِمُ ٱلۡجَلَآءَ لَعَذَّبَهُمۡ فِي ٱلدُّنۡيَاۖ وَلَهُمۡ فِي ٱلۡأٓخِرَةِ عَذَابُ ٱلنَّارِ ٣

3. በእነርሱም ላይ አላህ ከአገር መውጣትን ባልጻፈ ኖሮ በቅርቢቱ ዓለም በቀጣቸው ነበር፡፡ ለእነርሱም በመጨረሻይቱ (ዓለም) የእሳት ቅጣት አልላቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ شَآقُّواْ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥۖ وَمَن يُشَآقِّ ٱللَّهَ فَإِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٤

4. ይህ እነርሱ አላህንና መልክተኛውን በመከራከራቸው ነው፡፡ አላህንም የሚከራከር ሰው (ይቀጣዋል)፡፡ አላህ ቅጣተ ብርቱ ነውና፡፡

مَا قَطَعۡتُم مِّن لِّينَةٍ أَوۡ تَرَكۡتُمُوهَا قَآئِمَةً عَلَىٰٓ أُصُولِهَا فَبِإِذۡنِ ٱللَّهِ وَلِيُخۡزِيَ ٱلۡفَٰسِقِينَ ٥

5. ከዘንባባ (ከተምር ዛፍ) ማንኛዋም የቆረጣችኋት ወይም በግንዶቿ ላይ የቆመች ኾና የተዋችኋት በአላህ ፈቃድ ነው፡፡ አመጸኞቹንም ያዋርድ ዘንድ (በመቁረጥ ፈቀደ)፡፡

وَمَآ أَفَآءَ ٱللَّهُ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ مِنۡهُمۡ فَمَآ أَوۡجَفۡتُمۡ عَلَيۡهِ مِنۡ خَيۡلٖ وَلَا رِكَابٖ وَلَٰكِنَّ ٱللَّهَ يُسَلِّطُ رُسُلَهُۥ عَلَىٰ مَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٞ ٦

6. ከእነርሱም (ገንዘብ) በመልእክተኛው ላይ አላህ የመለሰው በእርሱ ላይ ፈረሶችንና ግመሎችን አላስጋለባችሁበትም፡፡ ግን አላህ መልክተኞቹን በሚሻው ሰው ላይ ይሾማል፡፡ አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

مَّآ أَفَآءَ ٱللَّهُ عَلَىٰ رَسُولِهِۦ مِنۡ أَهۡلِ ٱلۡقُرَىٰ فَلِلَّهِ وَلِلرَّسُولِ وَلِذِي ٱلۡقُرۡبَىٰ وَٱلۡيَتَٰمَىٰ وَٱلۡمَسَٰكِينِ وَٱبۡنِ ٱلسَّبِيلِ كَيۡ لَا يَكُونَ دُولَةَۢ بَيۡنَ ٱلۡأَغۡنِيَآءِ مِنكُمۡۚ وَمَآ ءَاتَىٰكُمُ ٱلرَّسُولُ فَخُذُوهُ وَمَا نَهَىٰكُمۡ عَنۡهُ فَٱنتَهُواْۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۖ إِنَّ ٱللَّهَ شَدِيدُ ٱلۡعِقَابِ ٧

7. አላህ ከከተሞቹ ሰዎች (ሀብት) በመልክተኛው ላይ የመለሰው (ሀብት) ከእናንተ ውስጥ በሀብታሞቹ መካከል ተዘዋዋሪ እንዳይኾን፡፡ ለአላህና ለመልክተኛው፣ ለዝምድና ባለቤትም፣ አባት ለሌላቸው ልጆችም፣ ለድኾችም፣ ለመንገደኛም (የሚሰሰጥ) ነው፡፡ መልክተኛውም የሰጣችሁን (ማንኛውንም) ነገር ያዙት፡፡ ከእርሱም የከለከላችሁን ነገር ተከልከሉ፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ አላህ ቅጣተ ብርቱ ነውና፡፡

لِلۡفُقَرَآءِ ٱلۡمُهَٰجِرِينَ ٱلَّذِينَ أُخۡرِجُواْ مِن دِيَٰرِهِمۡ وَأَمۡوَٰلِهِمۡ يَبۡتَغُونَ فَضۡلٗا مِّنَ ٱللَّهِ وَرِضۡوَٰنٗا وَيَنصُرُونَ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥٓۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلصَّٰدِقُونَ ٨

8. ለእነዚያ የአላህን ችሮታና ውዴታውን የሚፈልጉ፣ አላህንና መልክተኛውንም የሚረዱ ኾነው ከአገሮቻቸውና ከገንዘቦቻቸው ለተወጡት ስደተኞች ድኾች (ይሰሰጣል)፡፡ እነዚያ እነርሱ እውነተኞቹ ናቸው፡፡

9. እነዚያም ከበፊታቸው አገሪቱን መኖሪያ ያደረጉት እምነትንም የለመዱት ወደእነርሱ የተሰደዱትን ሰዎች ይወዳሉ። (ስደተኞቹ) ከተሰጡትም ነገር በልቦቻቸው ውስጥ ቅሬታን አያገኙም። በእነርሱ ላይ ችግር ቢኖርባቸውም በነፍሶቻቸው ላይ ሌላውን ይመርጣሉ። የነፍሱንም ንፍገት የሚጠበቅ ሰው እነዚያ እነሱ ምኞታቸውን አግኚዎች ናቸው።

وَٱلَّذِينَ تَبَوَّءُو ٱلدَّارَ وَٱلۡإِيمَٰنَ مِن قَبۡلِهِمۡ يُحِبُّونَ مَنۡ هَاجَرَ إِلَيۡهِمۡ وَلَا يَجِدُونَ فِي صُدُورِهِمۡ حَاجَةٗ مِّمَّآ أُوتُواْ وَيُؤۡثِرُونَ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمۡ وَلَوۡ كَانَ بِهِمۡ خَصَاصَةٞۚ وَمَن يُوقَ شُحَّ نَفۡسِهِۦ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ٩

10. እነዚያም ከበኋላቸው የመጡት «ጌታችን ሆይ! ለእኛም ለእነዚያም በእምነት ለቀደሙን ወንድሞቻችን ምሕረት አድርግ። በልቦቻችንም ውስጥ ለእነዚያ ለአመኑት (ሰዎች) ጥላቻን አታድርግ። ጌታችን ሆይ! አንተ ርኅሩህ አዛኝ ነህና» ይላሉ።

وَٱلَّذِينَ جَآءُو مِنۢ بَعۡدِهِمۡ يَقُولُونَ رَبَّنَا ٱغۡفِرۡ لَنَا وَلِإِخۡوَٰنِنَا ٱلَّذِينَ سَبَقُونَا بِٱلۡإِيمَٰنِ وَلَا تَجۡعَلۡ فِي قُلُوبِنَا غِلّٗا لِّلَّذِينَ ءَامَنُواْ رَبَّنَآ إِنَّكَ رَءُوفٞ رَّحِيمٌ ١٠

11. ወደእነዚያ ወደ ነፈቁት አላየህምን? ከመጽሐፉ ሰዎች ውስጥ ለእነዚያ ለካዱት ወንድሞቻቸው (ከአገር) «ብትባረሩ አብረናችሁ እንወጣለን። በእናንተም (ጉዳይ) አንድንም በፍጹም አንታዘዝም። ብትገደሉም በእርግጥ እንረዳችኋለን» ይሏቸዋል። አላህም እነርሱ ውሸታሞች መኾናቸውን ይመሰክራል።

۞أَلَمۡ تَرَ إِلَى ٱلَّذِينَ نَافَقُواْ يَقُولُونَ لِإِخۡوَٰنِهِمُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِنۡ أَهۡلِ ٱلۡكِتَٰبِ لَئِنۡ أُخۡرِجۡتُمۡ لَنَخۡرُجَنَّ مَعَكُمۡ وَلَا نُطِيعُ فِيكُمۡ أَحَدًا أَبَدٗا وَإِن قُوتِلۡتُمۡ لَنَنصُرَنَّكُمۡ وَٱللَّهُ يَشۡهَدُ إِنَّهُمۡ لَكَٰذِبُونَ ١١

12. ቢወጥጡ አብረዋቸው አይወጡም፤ ቢገደሉም አይረዱዋቸውም። ቢረዷቸውም (ለሽሽት) ጀርባቸውን ያዞራሉ። ከዚያም እርዳታን አያገኙም።

لَئِنۡ أُخۡرِجُواْ لَا يَخۡرُجُونَ مَعَهُمۡ وَلَئِن قُوتِلُواْ لَا يَنصُرُونَهُمۡ وَلَئِن نَّصَرُوهُمۡ لَيُوَلُّنَّ ٱلۡأَدۡبَٰرَ ثُمَّ لَا يُنصَرُونَ ١٢

13. እናንተ በልቦቻቸው ውስጥ በማስፈራት ከአላህ ይልቅ የበረታችሁ ናችሁ። ይህ እነርሱ የማያውቁ ሕዝቦች በመኾናቸው ነው።

لَأَنتُمۡ أَشَدُّ رَهۡبَةٗ فِي صُدُورِهِم مِّنَ ٱللَّهِۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَوۡمٞ لَّا يَفۡقَهُونَ ١٣

14. በተመሸጉ ከተሞች ውስጥ ወይም ከአጥሮች ጀርባ ኾነው እንጅ፤ የተሰበሰቡ ኾነው አይዋጉዋችሁም። ኃይላቸው በመካከላቸው ብርቱ ነው። ልቦቻቸው የተበታተኑ ሲኾኑ የተሰበሰቡ ናቸው ብለህ ትጠረጥራቸዋለህ። ይህ እነሱ አእምሮ የሌላቸው ሕዝቦች በመኾናቸው ነው።

لَا يُقَٰتِلُونَكُمۡ جَمِيعًا إِلَّا فِي قُرٗى مُّحَصَّنَةٍ أَوۡ مِن وَرَآءِ جُدُرِۭۚ بَأۡسُهُم بَيۡنَهُمۡ شَدِيدٞۚ تَحۡسَبُهُمۡ جَمِيعٗا وَقُلُوبُهُمۡ شَتَّىٰۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ قَوۡمٞ لَّا يَعۡقِلُونَ ١٤

15. (ብጤያቸው) እንደእነዚያ ከእነሱ በፊት በቅርብ ጊዜ የነገራቸውን ቅጣት እንደቀመሱት ብጤ ነው። ለእነርሱም አሳማሚ ቅጣት አላቸው።

كَمَثَلِ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ قَرِيبٗاۖ ذَاقُواْ وَبَالَ أَمۡرِهِمۡ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ١٥

16. እንደ ሰይጣን ብጤ ለሰውየው «ካድ» ባለው ጊዜና በካደም ጊዜ «እኔ ከአንተ ንጹሕ ነኝ እኔ አላህን የዓለማትን ጌታ እፈራለሁ» እንዳለው ነው።

كَمَثَلِ ٱلشَّيۡطَٰنِ إِذۡ قَالَ لِلۡإِنسَٰنِ ٱكۡفُرۡ فَلَمَّا كَفَرَ قَالَ إِنِّي بَرِيٓءٞ مِّنكَ إِنِّيٓ أَخَافُ ٱللَّهَ رَبَّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ١٦

17. መጨረሻቸውም እነርሱ በውስጡ ዘውታሪዎች ሲኾኑ በእሳት ውስጥ መኾን ነው። ይህም የበዳዮች ዋጋ ነው።

فَكَانَ عَٰقِبَتَهُمَآ أَنَّهُمَا فِي ٱلنَّارِ خَٰلِدَيۡنِ فِيهَاۚ وَذَٰلِكَ جَزَٰٓؤُاْ ٱلظَّٰلِمِينَ ١٧

18. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ ማንኛይቱም ነፍስ ለነገ ያስቀደመችውን ትመልከት፡፡ አላህንም ፍሩ፡ ፡ አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَلۡتَنظُرۡ نَفۡسٞ مَّا قَدَّمَتۡ لِغَدٖۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١٨

19. እንደነዚያም አላህን እንደረሱትና ነፍሶቻቸውን እንዳስረሳቸው (ሰዎች) አትኹኑ፡፡ እነዚያ እነርሱ አመጸኞቹ ናቸው፡፡

وَلَا تَكُونُواْ كَٱلَّذِينَ نَسُواْ ٱللَّهَ فَأَنسَىٰهُمۡ أَنفُسَهُمۡۚ أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡفَٰسِقُونَ ١٩

20. የእሳት ጓዶችና የገነት ጓዶች አይተካከሉም፡፡ የገነት ጓዶች እነርሱ ምኞታቸውን አግኚዎች ናቸው፡፡

لَا يَسۡتَوِيٓ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِ وَأَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِۚ أَصۡحَٰبُ ٱلۡجَنَّةِ هُمُ ٱلۡفَآئِزُونَ ٢٠

21. ይህንን ቁርኣን በተራራ ላይ ባወረድነው ኖሮ ከአላህ ፍራቻ (የተነሳ) ተዋራጅ ተሰንጣቂ ኾኖ ባየኸው ነበር፡፡ ይህችንም ምሳሌ ይገመግሙ ዘንድ ለሰዎች እንገልፃለን፡፡

لَوۡ أَنزَلۡنَا هَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانَ عَلَىٰ جَبَلٖ لَّرَأَيۡتَهُۥ خَٰشِعٗا مُّتَصَدِّعٗا مِّنۡ خَشۡيَةِ ٱللَّهِۚ وَتِلۡكَ ٱلۡأَمۡثَٰلُ نَضۡرِبُهَا لِلنَّاسِ لَعَلَّهُمۡ يَتَفَكَّرُونَ ٢١

22. እርሱ አላህ ነው፤ ያ ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ የሌለ፣ ሩቁንና ቅርቡን ዐዋቂ የኾነ ነው፡፡ እርሱ እጅግ በጣም ርኅሩህ በጣም አዛኝ ነው፡፡

هُوَ ٱللَّهُ ٱلَّذِي لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۖ عَٰلِمُ ٱلۡغَيۡبِ وَٱلشَّهَٰدَةِۖ هُوَ ٱلرَّحۡمَٰنُ ٱلرَّحِيمُ ٢٢

23. እርሱ አላህ ነው፡፡ ያ ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ የሌለ፣ ንጉሡ ከጉድለት ሁሉ የጠራው፣ የሰላም ባለቤቱ፣ ጸጥታን ሰጪው፣ ባሮቹን ጠባቂው፣ አሸናፊው፣ ኀያሉ፣ ኩሩው ነው፡፡ አላህ ከሚያጋሩት ሁሉ ጠራ፡፡

هُوَ ٱللَّهُ ٱلَّذِي لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ ٱلۡمَلِكُ ٱلۡقُدُّوسُ ٱلسَّلَٰمُ ٱلۡمُؤۡمِنُ ٱلۡمُهَيۡمِنُ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡجَبَّارُ ٱلۡمُتَكَبِّرُۚ سُبۡحَٰنَ ٱللَّهِ عَمَّا يُشۡرِكُونَ ٢٣

24. እርሱ አላህ ፈጣሪው (ከኢምንት) አስገኚው፣ ቅርጽን አሳማሪው ነው፡፡ ለእርሱ መልካሞች ስሞች አልሉት፡፡ በሰማያትና በምድርም ያለው ሁሉ ለእርሱ ያሞግሳል፡፡ እርሱም

هُوَ ٱللَّهُ ٱلۡخَٰلِقُ ٱلۡبَارِئُ ٱلۡمُصَوِّرُۖ لَهُ ٱلۡأَسۡمَآءُ ٱلۡحُسۡنَىٰۚ يُسَبِّحُ لَهُۥ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٢٤

# ሱረቱ አል ሙምተሒናህ

# سورة الممتحنة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

1. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ጠላቶቼንና ጠላቶቻችሁን ወዳጆች አድርገችሁ አትያዙ:: ከእውነቱ የመጣላችሁን ሃይማኖት በእርግጥ የካዱ ሲኾኑ ውዴታን ወደእነርሱ ታደርሳላችሁ:: መልክተኛውንና እናንተን በአላህ በጌታችሁ ስላመናችሁ (ከመካ) ያወጣሉ:: በመንገዴ ለመታገልና ውዴታዬን ለመፈለግ የወጣችሁ እንደኾናችሁ (ወዳጆች አድርጋችሁ አትያዙዋቸው):: እኔ የምትደብቁትንና የምትገልጹትን ሁሉ የማውቅ ስኾን ወደእነርሱ በፍቅር ትመሳጠራላችሁ:: ከእናንተም (ይህንን) የሚሠራ ሰው ቀጥተኛውን መንገድ በእርግጥ ተሳሳተ::

2. ቢያሸንፏችሁ ለእናንተ ጠላቶች ይኾናሉ:: እጆቻቸውንና ምላሶቻቸውንም ወደእናንተ በክፉ ይዘረጋሉ:: ብትክዱም ተመኙ::

3. ዘመዶቻችሁም፣ ልጆቻችሁም በትንሣኤ ቀን አይጠቅሟችሁም፤ (አላህ) በመካከላችሁ ይለያል:: አላህም የምትሠሩትን ሁሉ ተመልካች ነው::

4. በኢብራሂምና በእነዚያ ከእርሱ ጋር በነበሩት (ምእምናን) መልካም መከተል አለቻችሁ:: ለሕዝቦቻቸው «እኛ ከእናንተ ከአላህ ሌላ ከምትግገዙትም ንጹሖች ነን:: በእናንተ ካድን:: በአላህ አንድ ብቻ ሲኾን እስከምታምኑ ድረስ በእኛና በእናንተ መካከል ጠብና ጥላቻ ዘወትር ተገለጸ::» ባሉ ጊዜ (መልካም መከተል አለቻችሁ):: ኢብራሂም ለአባቱ «እኔ ለአንተ ከአላህ (ቅጣት) ምንም የማልጠቅም ስኾን ለአንተ በእርግጥ ምሕረትን እለምንልሻለሁ» ማለቱ ብቻ ሲቀር:: «ጌታችን ሆይ! በአንተ ላይ ተመካን:: ወደ አንተም ተመለስን መመለሻም ወደ አንተ ብቻ ነው፤» (ባለው ተከተሉት)::

5. ጌታችን ሆይ! ለእነዚያ ለካዱት ሰዎች መሞከሪያ አታድርገን:: ለእኛም ምሕረት አድርግልን:: ጌታችን ሆይ! አንተ አሸናፊው ጥበበኛው አንተ ብቻ ነህ::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تَتَّخِذُواْ عَدُوِّي وَعَدُوَّكُمۡ أَوۡلِيَآءَ تُلۡقُونَ إِلَيۡهِم بِٱلۡمَوَدَّةِ وَقَدۡ كَفَرُواْ بِمَا جَآءَكُم مِّنَ ٱلۡحَقِّ يُخۡرِجُونَ ٱلرَّسُولَ وَإِيَّاكُمۡ أَن تُؤۡمِنُواْ بِٱللَّهِ رَبِّكُمۡ إِن كُنتُمۡ خَرَجۡتُمۡ جِهَٰدٗا فِي سَبِيلِي وَٱبۡتِغَآءَ مَرۡضَاتِيۚ تُسِرُّونَ إِلَيۡهِم بِٱلۡمَوَدَّةِ وَأَنَا۠ أَعۡلَمُ بِمَآ أَخۡفَيۡتُمۡ وَمَآ أَعۡلَنتُمۡۚ وَمَن يَفۡعَلۡهُ مِنكُمۡ فَقَدۡ ضَلَّ سَوَآءَ ٱلسَّبِيلِ ١

إِن يَثۡقَفُوكُمۡ يَكُونُواْ لَكُمۡ أَعۡدَآءٗ وَيَبۡسُطُوٓاْ إِلَيۡكُمۡ أَيۡدِيَهُمۡ وَأَلۡسِنَتَهُم بِٱلسُّوٓءِ وَوَدُّواْ لَوۡ تَكۡفُرُونَ ٢

لَن تَنفَعَكُمۡ أَرۡحَامُكُمۡ وَلَآ أَوۡلَٰدُكُمۡۚ يَوۡمَ ٱلۡقِيَٰمَةِ يَفۡصِلُ بَيۡنَكُمۡۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٞ ٣

قَدۡ كَانَتۡ لَكُمۡ أُسۡوَةٌ حَسَنَةٞ فِيٓ إِبۡرَٰهِيمَ وَٱلَّذِينَ مَعَهُۥٓ إِذۡ قَالُواْ لِقَوۡمِهِمۡ إِنَّا بُرَءَٰٓؤُاْ مِنكُمۡ وَمِمَّا تَعۡبُدُونَ مِن دُونِ ٱللَّهِ كَفَرۡنَا بِكُمۡ وَبَدَا بَيۡنَنَا وَبَيۡنَكُمُ ٱلۡعَدَٰوَةُ وَٱلۡبَغۡضَآءُ أَبَدًا حَتَّىٰ تُؤۡمِنُواْ بِٱللَّهِ وَحۡدَهُۥٓ إِلَّا قَوۡلَ إِبۡرَٰهِيمَ لِأَبِيهِ لَأَسۡتَغۡفِرَنَّ لَكَ وَمَآ أَمۡلِكُ لَكَ مِنَ ٱللَّهِ مِن شَيۡءٖۖ رَّبَّنَا عَلَيۡكَ تَوَكَّلۡنَا وَإِلَيۡكَ أَنَبۡنَا وَإِلَيۡكَ ٱلۡمَصِيرُ ٤

رَبَّنَا لَا تَجۡعَلۡنَا فِتۡنَةٗ لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ وَٱغۡفِرۡ لَنَا رَبَّنَآۖ إِنَّكَ أَنتَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٥

6. ለእናንተ አላህንና የመጨረሻውን ቀን ለሚፈራ ሰው በእነርሱ መልካም መከተል አልላችሁ፡፡ የሚዞርም ሰው (ራሱን ይጎዳል)፡፡ አላህ ተብቃቂው ምስጉኑ እርሱ ብቻ ነውና፡፡

لَقَدْ كَانَ لَكُمْ فِيهِمْ أُسْوَةٌ حَسَنَةٌ لِّمَن كَانَ يَرْجُواْ ٱللَّهَ وَٱلْيَوْمَ ٱلْأٓخِرَۚ وَمَن يَتَوَلَّ فَإِنَّ ٱللَّهَ هُوَ ٱلْغَنِيُّ ٱلْحَمِيدُ ٦

7. በናንተና በእነዚያ ከእነርሱ ጋር በተጣላችሁት ሰዎች መካከል አላህ መፋቀርን ሊያደርግ ይቻላል፡፡ አላህም ቻይ ነው፡፡ አላህም በጣም አዛኝ ነው፡፡

۞عَسَى ٱللَّهُ أَن يَجْعَلَ بَيْنَكُمْ وَبَيْنَ ٱلَّذِينَ عَادَيْتُم مِّنْهُم مَّوَدَّةًۚ وَٱللَّهُ قَدِيرٌۚ وَٱللَّهُ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ٧

8. ከእነዚያ በሃይማኖት ካልተጋደሏችሁ ከአገሮቻችሁም ካላወጡዋችሁ (ከሓዲዎች) መልካም ብትውሉላቸውና ወደእነርሱ ብታስተካክሉ አላህ አይከለክላችሁም፡፡ አላህ ትክክለኞችን ይወዳልና፡፡

لَّا يَنْهَىٰكُمُ ٱللَّهُ عَنِ ٱلَّذِينَ لَمْ يُقَٰتِلُوكُمْ فِي ٱلدِّينِ وَلَمْ يُخْرِجُوكُم مِّن دِيَٰرِكُمْ أَن تَبَرُّوهُمْ وَتُقْسِطُوٓاْ إِلَيْهِمْۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلْمُقْسِطِينَ ٨

9. አላህ የሚከለክላችሁ ከእነዚያ በሃይማኖት ከተጋደሉዋችሁ፣ ከቤቶቻችሁም ካወጡዋችሁ፣ እናንተም በማውጣት ላይ ከረዱት (ከሓዲዎች) እንዳትወዳጁዋቸው ብቻ ነው፡፡ ወዳጅ የሚያደርጓቸውም ሰዎች እነዚያ እነርሱ በዳዮቹ ናቸው፡፡

إِنَّمَا يَنْهَىٰكُمُ ٱللَّهُ عَنِ ٱلَّذِينَ قَٰتَلُوكُمْ فِي ٱلدِّينِ وَأَخْرَجُوكُم مِّن دِيَٰرِكُمْ وَظَٰهَرُواْ عَلَىٰٓ إِخْرَاجِكُمْ أَن تَوَلَّوْهُمْۚ وَمَن يَتَوَلَّهُمْ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلظَّٰلِمُونَ ٩

10. እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ምእምናት ስደተኞች ኾነው በመጧችሁ ጊዜ (ለሃይማኖት መሰደዳቸውን) ፈትኑዋቸው፡፡ አላህ በእምነታቸው ይበልጥ ዐዋቂ ነው፡፡ አማኞችም መኾናቸውን ብትውቁ ወደ ከሓዲዎቹ አትመልሱዋቸው፡፡ እነርሱ (ሴቶቹ) ለእነርሱ የተፈቀዱ አይደሉምና፡፡ እነርሱም (ወንዶቹ) ለእነርሱ አይፈቀዱምና፡፡ ያወጡትንም ገንዘብ ስጧቸው፡፡ መህራቸውንም በሰጣችኋቸው ጊዜ ብታገቡዋቸው በእናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፡፡ የከሓዲዎቹንም ሴቶች የጋብቻ ቃል ኪዳኖች አትያዙ፤ ያወጣችሁትንም ገንዘብ ጠይቁ፡፡ ያወጡትንም ይጠይቁ፡፡ ይህ የአላህ ፍርድ ነው፡፡ በመካከላችሁ ይፈርዳል፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا جَآءَكُمُ ٱلْمُؤْمِنَٰتُ مُهَٰجِرَٰتٍ فَٱمْتَحِنُوهُنَّۖ ٱللَّهُ أَعْلَمُ بِإِيمَٰنِهِنَّۖ فَإِنْ عَلِمْتُمُوهُنَّ مُؤْمِنَٰتٍ فَلَا تَرْجِعُوهُنَّ إِلَى ٱلْكُفَّارِۖ لَا هُنَّ حِلٌّ لَّهُمْ وَلَا هُمْ يَحِلُّونَ لَهُنَّۖ وَءَاتُوهُم مَّآ أَنفَقُواْۚ وَلَا جُنَاحَ عَلَيْكُمْ أَن تَنكِحُوهُنَّ إِذَآ ءَاتَيْتُمُوهُنَّ أُجُورَهُنَّۚ وَلَا تُمْسِكُواْ بِعِصَمِ ٱلْكَوَافِرِ وَسْـَٔلُواْ مَآ أَنفَقْتُمْ وَلْيَسْـَٔلُواْ مَآ أَنفَقُواْۚ ذَٰلِكُمْ حُكْمُ ٱللَّهِ يَحْكُمُ بَيْنَكُمْۖ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ١٠

11. ከሚስቶቻችሁም ወደ ከሓዲዎቹ አንዳቸው ቢያመልጧችሁ ቀጥሎም ብትዘምቱባቸው ለእነዚያ ሚስቶቻቸው ለኼዱባቸው (ሰዎች) ያወጡትን ብጤ ስጧቸው፡፡ ያንንም እናንተ በርሱ ያመናችሁበትን አላህን ፍሩ፡፡

وَإِن فَاتَكُمْ شَيْءٌ مِّنْ أَزْوَٰجِكُمْ إِلَى ٱلْكُفَّارِ فَعَاقَبْتُمْ فَـَٔاتُواْ ٱلَّذِينَ ذَهَبَتْ أَزْوَٰجُهُم مِّثْلَ مَآ أَنفَقُواْۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ ٱلَّذِيٓ أَنتُم بِهِۦ مُؤْمِنُونَ ١١

12. አንተ ነቢዩ ሆይ! ምእምናቶቹ በአላህ ምንንም ላያጋሩ፣ ላይሰርቁም ላያመነዝሩም፣ ልጆቻቸውን ላይገድሉም፣ በእጆቻቸውና በእግሮቻቸው መካከልም የሚቀጣጥፉት የኾነን ኃጢአት ላያመጡ (ላይሠሩ) በበጎም ሥራ ትዕዛዝህን ላይጥሱ ቃል ኪዳን ሊገቡልህ በመጡህ ጊዜ ኪዳን ተጋባቸው:: ለእነርሱም አላህን ምሕረት ለምንላቸው:: አላህ በጣም መሓሪ አዛኝ ነውና::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِىُّ إِذَا جَآءَكَ ٱلْمُؤْمِنَـٰتُ يُبَايِعْنَكَ عَلَىٰٓ أَن لَّا يُشْرِكْنَ بِٱللَّهِ شَيْـًٔا وَلَا يَسْرِقْنَ وَلَا يَزْنِينَ وَلَا يَقْتُلْنَ أَوْلَـٰدَهُنَّ وَلَا يَأْتِينَ بِبُهْتَـٰنٍ يَفْتَرِينَهُۥ بَيْنَ أَيْدِيهِنَّ وَأَرْجُلِهِنَّ وَلَا يَعْصِينَكَ فِى مَعْرُوفٍ فَبَايِعْهُنَّ وَٱسْتَغْفِرْ لَهُنَّ ٱللَّهَ ۖ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١٢﴾

13. እላንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህ በእነርሱ ላይ የተቆጣባቸውን ሕዝቦች አትወዳጁ:: ከሓዲዎች ከመቃብር ሰዎች ተስፋ እንደቆረጡ ከመጨረሻይቱ ዓለም (ምንዳ) በእርግጥ ተስፋ ቆርጠዋል::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ لَا تَتَوَلَّوْا۟ قَوْمًا غَضِبَ ٱللَّهُ عَلَيْهِمْ قَدْ يَئِسُوا۟ مِنَ ٱلْـَٔاخِرَةِ كَمَا يَئِسَ ٱلْكُفَّارُ مِنْ أَصْحَـٰبِ ٱلْقُبُورِ ﴿١٣﴾

# ሱረቱ አል ሶፍ

# سورة الصّف

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَـٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሰማያት ውስጥ ያለው በምድርም ውስጥ ያለው ሁሉ ለአላህ አሞገሠ:: እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው::

سَبَّحَ لِلَّهِ مَا فِى ٱلسَّمَـٰوَٰتِ وَمَا فِى ٱلْأَرْضِ ۖ وَهُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْحَكِيمُ ﴿١﴾

2. እላንተ ያመናችሁ ሆይ! የማትሠሩትን ነገር ለምን ትናገራላችሁ?

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ لِمَ تَقُولُونَ مَا لَا تَفْعَلُونَ ﴿٢﴾

3. የማትሠሩን ነገር መናገራችሁ አላህ ዘንድ መጠላቱ ተለቀ::

كَبُرَ مَقْتًا عِندَ ٱللَّهِ أَن تَقُولُوا۟ مَا لَا تَفْعَلُونَ ﴿٣﴾

4. አላህ እነዚያን እነርሱ ልክ እንደ ተናሰ ግንብ የተሰለፉ ኾነው በመንገዱ (በሃይማኖቱ) የሚጋደሉትን ይወዳል::

إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلَّذِينَ يُقَـٰتِلُونَ فِى سَبِيلِهِۦ صَفًّا كَأَنَّهُم بُنْيَـٰنٌ مَّرْصُوصٌ ﴿٤﴾

5. ሙሳም ለሕዝቦቹ «ሕዝቦቼ ሆይ! እኔ ወደእናንተ የአላህ መልክተኛ መኾኔን በእርግጥ የምታውቁ ስትኾኑ ለምን ታሰቃዩኛላችሁ?» ባለ ጊዜ (አስታውስ:: ከእውነት) በተዘነበሉም ጊዜ አላህ ልቦቻቸውን አዘነበላቸው:: አላህም አመጸኞችን ሕዝቦች አያቀናም::

وَإِذْ قَالَ مُوسَىٰ لِقَوْمِهِۦ يَـٰقَوْمِ لِمَ تُؤْذُونَنِى وَقَد تَّعْلَمُونَ أَنِّى رَسُولُ ٱللَّهِ إِلَيْكُمْ ۖ فَلَمَّا زَاغُوٓا۟ أَزَاغَ ٱللَّهُ قُلُوبَهُمْ ۚ وَٱللَّهُ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلْفَـٰسِقِينَ ﴿٥﴾

6. የመርየም ልጅ ዒሳም፡- «የእስራኤል ልጆች ሆይ! እኔ ከተውራት በፊቴ ያለውን የማረጋግጥና ከእኔ በኋላ በሚመጣው መልክተኛ ስሙ አሕመድ በኾነው የማበስር ስኾን ወደእናንተ (የተላክሁ) የአላህ መልክተኛ ነኝ» ባለ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ በግልጽ ተዓምራቶች በመጣቸውም ጊዜ «ይህ ግልጽ ድግምት ነው» አሉ፡፡

وَإِذْ قَالَ عِيسَى ٱبْنُ مَرْيَمَ يَٰبَنِىٓ إِسْرَٰٓءِيلَ إِنِّى رَسُولُ ٱللَّهِ إِلَيْكُم مُّصَدِّقًا لِّمَا بَيْنَ يَدَىَّ مِنَ ٱلتَّوْرَىٰةِ وَمُبَشِّرًۢا بِرَسُولٍ يَأْتِى مِنۢ بَعْدِى ٱسْمُهُۥٓ أَحْمَدُ ۖ فَلَمَّا جَآءَهُم بِٱلْبَيِّنَٰتِ قَالُوا۟ هَٰذَا سِحْرٌ مُّبِينٌ ﴿٦﴾

7. እርሱ ወደ ኢስላም የሚጥጠራ ሲኾን በአላህ ላይ ውሸትን ከቀጣጠፈ ሰውም ይበልጥ በደለኛ ማን ነው? አላህም በዳዮችን ሕዝቦች አይመራም፡፡

وَمَنْ أَظْلَمُ مِمَّنِ ٱفْتَرَىٰ عَلَى ٱللَّهِ ٱلْكَذِبَ وَهُوَ يُدْعَىٰٓ إِلَى ٱلْإِسْلَٰمِ ۚ وَٱللَّهُ لَا يَهْدِى ٱلْقَوْمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ﴿٧﴾

8. የአላህን ብርሃን በአፎቻቸው ሊያጠፉ ይሻሉ፡፡ አላህም ከሓዲዎቹ ቢጠሉም እንኳ ብርሃኑን ገላጭ ነው፡፡

يُرِيدُونَ لِيُطْفِـُٔوا۟ نُورَ ٱللَّهِ بِأَفْوَٰهِهِمْ وَٱللَّهُ مُتِمُّ نُورِهِۦ وَلَوْ كَرِهَ ٱلْكَٰفِرُونَ ﴿٨﴾

9. እርሱ ያ አጋሪዎቹ ቢጠሉም መልክተኛውን በመምሪያ (መጽሐፍ) በእውነተኛው ሃይማኖትም (በኢስላም) ከሃይማኖት ሁሉ በላይ ይፋ ሊያደርገው የላከ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِىٓ أَرْسَلَ رَسُولَهُۥ بِٱلْهُدَىٰ وَدِينِ ٱلْحَقِّ لِيُظْهِرَهُۥ عَلَى ٱلدِّينِ كُلِّهِۦ وَلَوْ كَرِهَ ٱلْمُشْرِكُونَ ﴿٩﴾

10. «እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከአሳማሚ ቅጣት የምታድናችሁ የኾነችን ንግድ ላመላክታችሁን?» (በላቸው)፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ هَلْ أَدُلُّكُمْ عَلَىٰ تِجَٰرَةٍ تُنجِيكُم مِّنْ عَذَابٍ أَلِيمٍ ﴿١٠﴾

11. (እርሷም) በአላህና በመልክተኛው ታምናላችሁ፣ በአላህ መንገድም በገንዘቦቻችሁ በነፍሶቻችሁም ትታገላላችሁ፣ ይህ የምታውቁ ብትኾኑ ለእናንተ የተሻለ ነው፡፡

تُؤْمِنُونَ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَتُجَٰهِدُونَ فِى سَبِيلِ ٱللَّهِ بِأَمْوَٰلِكُمْ وَأَنفُسِكُمْ ۚ ذَٰلِكُمْ خَيْرٌ لَّكُمْ إِن كُنتُمْ تَعْلَمُونَ ﴿١١﴾

12. ኃጢአቶቻችሁን ለእናንተ ይምራል፡፡ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውንም ገነቶች ያገባችኋል፡፡ በመኖሪያ ገነቶችም በሚያማምሩ ቤቶች ውስጥ (ያስቀምጣችኋል)፡፡ ይህ ታላቅ ዕድል ነው፡፡

يَغْفِرْ لَكُمْ ذُنُوبَكُمْ وَيُدْخِلْكُمْ جَنَّٰتٍ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَٰرُ وَمَسَٰكِنَ طَيِّبَةً فِى جَنَّٰتِ عَدْنٍ ۚ ذَٰلِكَ ٱلْفَوْزُ ٱلْعَظِيمُ ﴿١٢﴾

13. ሌላይቱንም የምትወዷትን (ጸጋ ይሰጣችኋል)፡፡ ከአላህ የኾነ እርዳታና ቅርብ የኾነ የአገር መክፈት ነው፡፡ ምእምናንንም አብስር፡፡

وَأُخْرَىٰ تُحِبُّونَهَا ۖ نَصْرٌ مِّنَ ٱللَّهِ وَفَتْحٌ قَرِيبٌ ۗ وَبَشِّرِ ٱلْمُؤْمِنِينَ ﴿١٣﴾

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُونُوٓاْ أَنصَارَ ٱللَّهِ كَمَا قَالَ عِيسَى ٱبۡنُ مَرۡيَمَ لِلۡحَوَارِيِّـۧنَ مَنۡ أَنصَارِيٓ إِلَى ٱللَّهِۖ قَالَ ٱلۡحَوَارِيُّونَ نَحۡنُ أَنصَارُ ٱللَّهِۖ فَـَٔامَنَت طَّآئِفَةٞ مِّنۢ بَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَكَفَرَت طَّآئِفَةٞۖ فَأَيَّدۡنَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ عَلَىٰ عَدُوِّهِمۡ فَأَصۡبَحُواْ ظَٰهِرِينَ ١٤

14. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! የመርየም ልጅ ዒሳ ለሐዋርያቶቹ «ወደ አላህ ረዳቴ ማነው?» እንዳለ ሐወርያቶቹም «እኛ የአላህ ረዳቶች ነን» እንዳሉት የአላህ ረዳቶች ኹኑ፡፡ ከእስራኤልም ልጆች አንደኛዋ ጭፍራ አመነች፡፡ ሌላይቱም ጭፍራ ካደች፡፡ እነዚያን ያመኑትንም በጠላታቸው ላይ አበረታናቸው፤ አሸናፊዎችም ኾኑ፡፡

## سورة الجمعة

## ሱረቱ አል ጁሙዓህ

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

يُسَبِّحُ لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِ ٱلۡمَلِكِ ٱلۡقُدُّوسِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَكِيمِ ١

1. በሰማያት ያለው በምድርም ያለው ሁሉ ለአላህ ንጉሥ፣ ቅዱስ፣ አሸናፊ፣ ጥበበኛ ለኾነው ያሞግሳል፡፡

هُوَ ٱلَّذِي بَعَثَ فِي ٱلۡأُمِّيِّـۧنَ رَسُولٗا مِّنۡهُمۡ يَتۡلُواْ عَلَيۡهِمۡ ءَايَٰتِهِۦ وَيُزَكِّيهِمۡ وَيُعَلِّمُهُمُ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡحِكۡمَةَ وَإِن كَانُواْ مِن قَبۡلُ لَفِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ٢

2. እርሱ ያ በመሃይሞቹ ውስጥ አንቀጾቹን (ቁርኣንን) በእነርሱ ላይ የሚያነብላቸው፣ (ከማጋራት) የሚያጠራቸውም፣ መጽሐፍንና ጥበብን የሚያስተምራቸውም የኾነን መልክተኛ (ሙሐመድን) ከእነርሱው ውስጥ የላከ ነው፡፡ እነርሱም ከእርሱ በፊት በግልጽ ስሕተት ውስጥ ነበሩ፡፡

وَءَاخَرِينَ مِنۡهُمۡ لَمَّا يَلۡحَقُواْ بِهِمۡۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ٣

3. ከነሱም ሌሎች ገና ያልተጠጉዋቸው በኾኑት ላይ (የላከው ነው)፡፡ እርሱም አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

ذَٰلِكَ فَضۡلُ ٱللَّهِ يُؤۡتِيهِ مَن يَشَآءُۚ وَٱللَّهُ ذُو ٱلۡفَضۡلِ ٱلۡعَظِيمِ ٤

4. ይህ የአላህ ችሮታ ነው፡፡ ለሚሻው ሰው ይሰጠዋል፡፡ አላህም የታላቅ ችሮታ ባለቤት ነው፡፡

مَثَلُ ٱلَّذِينَ حُمِّلُواْ ٱلتَّوۡرَىٰةَ ثُمَّ لَمۡ يَحۡمِلُوهَا كَمَثَلِ ٱلۡحِمَارِ يَحۡمِلُ أَسۡفَارَۢاۚ بِئۡسَ مَثَلُ ٱلۡقَوۡمِ ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِ ٱللَّهِۚ وَٱللَّهُ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلظَّٰلِمِينَ ٥

5. የእነዚያ ተውራትን የተጫኑትና ከዚያም ያልተሸከሟት (ያልሠሩባት) ሰዎች ምሳሌ መጽሐፎችን እንደሚሸከም አህያ ብጤ ነው፡፡ የእነዚያ በአላህ አንቀጾች ያስተባበሉት ሕዝቦች ምሳሌ ከፋ፡፡ አላህም በዳዮችን ሕዝቦች አይመራም፡፡

قُلۡ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ هَادُوٓاْ إِن زَعَمۡتُمۡ أَنَّكُمۡ أَوۡلِيَآءُ لِلَّهِ مِن دُونِ ٱلنَّاسِ فَتَمَنَّوُاْ ٱلۡمَوۡتَ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ٦

6. «እናንተ አይሁዳውያን የኾናችሁ ሆይ! ከሰው ሁሉ በስተቀር እናንተ ብቻ ለአላህ ወዳጆች ነን ብትሉ እውነተኞች እንደኾናችሁ ሞትን ተመኙ» በላቸው፡፡

وَلَا يَتَمَنَّوۡنَهُۥٓ أَبَدَۢا بِمَا قَدَّمَتۡ أَيۡدِيهِمۡۚ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِٱلظَّٰلِمِينَ ٧

7. እጆቻቸውም ባስቀደሙት ኃጢአት ምክንያት በፍጹም አይመኙትም፡፡ አላህም በዳዮቹን ዐዋቂ ነው፡፡

قُلۡ إِنَّ ٱلۡمَوۡتَ ٱلَّذِي تَفِرُّونَ مِنۡهُ فَإِنَّهُۥ مُلَٰقِيكُمۡۖ ثُمَّ تُرَدُّونَ إِلَىٰ عَٰلِمِ ٱلۡغَيۡبِ وَٱلشَّهَٰدَةِ فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ٨

8. «ያ ከእርሱ የምትሸሹት ሞት እርሱ በእርግጥ አግኛችሁ ነው፡፡ ከዚያም ሩቁንና ቅርቡን ዐዋቂ ወደ ኾነው ጌታ ትመለሳላችሁ፡፡ ትሠሩትም የነበራችሁትን ሁሉ ይነግራችኋል» በላቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِذَا نُودِيَ لِلصَّلَوٰةِ مِن يَوۡمِ ٱلۡجُمُعَةِ فَٱسۡعَوۡاْ إِلَىٰ ذِكۡرِ ٱللَّهِ وَذَرُواْ ٱلۡبَيۡعَۚ ذَٰلِكُمۡ خَيۡرٞ لَّكُمۡ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٩

9. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በዐርብ ቀን ለስግደት ጥሪ በተደረገ ጊዜ ወደ አላህ ማውሳት ኺዱ፡፡ መሸጥንም ተዉ፡፡ ይህ የምታውቁ ብትኾኑ ለእናንተ በጣም የተሻለ ነው፡፡

فَإِذَا قُضِيَتِ ٱلصَّلَوٰةُ فَٱنتَشِرُواْ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَٱبۡتَغُواْ مِن فَضۡلِ ٱللَّهِ وَٱذۡكُرُواْ ٱللَّهَ كَثِيرٗا لَّعَلَّكُمۡ تُفۡلِحُونَ ١٠

10. ሶለቲቱም በተፈጸመች ጊዜ በምድር ላይ ተበተኑ፡፡ ከአላህም ችሮታ ፈልጉ፡፡ አላህንም በብዙ አውሱ፡፡ ልትድኑ ይከጀላልና፡፡

وَإِذَا رَأَوۡاْ تِجَٰرَةً أَوۡ لَهۡوًا ٱنفَضُّوٓاْ إِلَيۡهَا وَتَرَكُوكَ قَآئِمٗاۚ قُلۡ مَا عِندَ ٱللَّهِ خَيۡرٞ مِّنَ ٱللَّهۡوِ وَمِنَ ٱلتِّجَٰرَةِۚ وَٱللَّهُ خَيۡرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ١١

11. ንግድን ወይም ዛዛታን ባዩ ጊዜም ቆመህ የተዉህ ሲኾኑ ወደእርሷ ይበተናሉ፡፡ አላህ ዘንድ ያለው ዋጋ ከዛዛታም ከንግድም በላጭ ነው፡፡ «አላህም ከሰጪዎቹ ሁሉ ይበልጥ ሲሳይን ሰጭ ነው» በላቸው፡፡

## سورة المنافقون

## ሱረቱ አል ሙናፊቁን

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

إِذَا جَآءَكَ ٱلۡمُنَٰفِقُونَ قَالُواْ نَشۡهَدُ إِنَّكَ لَرَسُولُ ٱللَّهِۗ وَٱللَّهُ يَعۡلَمُ إِنَّكَ لَرَسُولُهُۥ وَٱللَّهُ يَشۡهَدُ إِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ لَكَٰذِبُونَ ١

1. መናፍቃን በመጡህ ጊዜ «አንተ የአላህ መልክተኛ መኾንህን በእርግጥ (ምለን) እንመሰክራለን» ይላሉ፡፡ አላህም አንተ በእርግጥ መልክተኛው መኾንህን ያውቃል፡፡ አላህም መናፍቃን (ከልብ እንመሰክራለን በማለታቸው) ውሸታሞች መኾናቸውን ይመሰክራል፡፡

ٱتَّخَذُوٓاْ أَيۡمَٰنَهُمۡ جُنَّةٗ فَصَدُّواْ عَن سَبِيلِ ٱللَّهِۚ إِنَّهُمۡ سَآءَ مَا كَانُواْ يَعۡمَلُونَ ٢

2. መሓሎቻቸውን ጋሻ አድርገው ያዙ፡፡ ከአላህም መንገድ ከለከሉ፡፡ እነርሱ ይሠሩት የነበሩት ነገር ከፋ፡፡

3. ይህ እነርሱ (በምላስ) ያመኑ ከዚያም (በልብ) የካዱ በመኾናቸው ነው፡፡ በልቦቻቸውም ላይ ታተመባቸው፤ ስለዚህ እነርሱ አያውቁም፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمۡ ءَامَنُواْ ثُمَّ كَفَرُواْ فَطُبِعَ عَلَىٰ قُلُوبِهِمۡ فَهُمۡ لَا يَفۡقَهُونَ ٣

4. ባየሃቸውም ጊዜ አካሎቻቸው (ግዙፍነታቸው) ያስደንቁሃል፡፡ ቢናገሩም ለንግግራቸው ታዳምጣለህ፤ (ከዕውቀት ባዶ በመኾን)፡፡ እነርሱ ልክ በግድግዳ የተጠጉ ግንዶችን ይመስላሉ፡፡ ጩኸትን ሁሉ በእነርሱ ላይ ነው ብለው ያስባሉ፡፡ እነርሱ ጠላቶች ናቸውና ተጠንቀቃቸው፡፡ አላህ ይጋደላቸው፤ (ከእምነት) እንዴት ይመለሳሉ!

۞وَإِذَا رَأَيۡتَهُمۡ تُعۡجِبُكَ أَجۡسَامُهُمۡۖ وَإِن يَقُولُواْ تَسۡمَعۡ لِقَوۡلِهِمۡۖ كَأَنَّهُمۡ خُشُبٞ مُّسَنَّدَةٞۖ يَحۡسَبُونَ كُلَّ صَيۡحَةٍ عَلَيۡهِمۡۚ هُمُ ٱلۡعَدُوُّ فَٱحۡذَرۡهُمۡۚ قَٰتَلَهُمُ ٱللَّهُۖ أَنَّىٰ يُؤۡفَكُونَ ٤

5. ለእነሱም ፡- «ኑ የአላህ መልክተኛ ለእናንተ ምሕረትን ይለምንላችኋል፤» በተባሉ ጊዜ ራሶቻቸውን ያዞራሉ፡፡ እነርሱም ትዕቢተኞች ኾነው ሲሸሹ ታያቸዋለህ፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمۡ تَعَالَوۡاْ يَسۡتَغۡفِرۡ لَكُمۡ رَسُولُ ٱللَّهِ لَوَّوۡاْ رُءُوسَهُمۡ وَرَأَيۡتَهُمۡ يَصُدُّونَ وَهُم مُّسۡتَكۡبِرُونَ ٥

6. ምሕረትን ብትለምንላቸው ወይም ምሕረትን ባትለምንላቸው በእነርሱ ላይ እኩል ነው፡፡ አላህ ለእነርሱ በፍጹም አይምርም፡፡ አላህ አመጸኞችን ሕዝቦች አየመራምና፡፡

سَوَآءٌ عَلَيۡهِمۡ أَسۡتَغۡفَرۡتَ لَهُمۡ أَمۡ لَمۡ تَسۡتَغۡفِرۡ لَهُمۡ لَن يَغۡفِرَ ٱللَّهُ لَهُمۡۚ إِنَّ ٱللَّهَ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡفَٰسِقِينَ ٦

7. እነርሱ እነዚያ ፡- «አላህ መልክተኛ ዘንድ ላሉት ሰዎች እስከሚበታተኑ ድረስ አትቀልቡ» የሚሉ ናቸው፡፡ የሰማያትና የምድር ድልቦችም የአላህ ናቸው፡፡ ግን መናፍቃን አያውቁም፡፡

هُمُ ٱلَّذِينَ يَقُولُونَ لَا تُنفِقُواْ عَلَىٰ مَنۡ عِندَ رَسُولِ ٱللَّهِ حَتَّىٰ يَنفَضُّواْۗ وَلِلَّهِ خَزَآئِنُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَلَٰكِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ لَا يَفۡقَهُونَ ٧

8. «ወደ መዲና ብንመለስ አሸናፊው ወራዳውን በእርግጥ ከእርሷ ያወጣል» ይላሉ፡፡ አሸናፊነትም ለአላህ፣ ለመልክተኛውና ለምእምናን ነው፡፡ ግን መናፍቃን አያውቁም፡፡

يَقُولُونَ لَئِن رَّجَعۡنَآ إِلَى ٱلۡمَدِينَةِ لَيُخۡرِجَنَّ ٱلۡأَعَزُّ مِنۡهَا ٱلۡأَذَلَّۚ وَلِلَّهِ ٱلۡعِزَّةُ وَلِرَسُولِهِۦ وَلِلۡمُؤۡمِنِينَ وَلَٰكِنَّ ٱلۡمُنَٰفِقِينَ لَا يَعۡلَمُونَ ٨

9. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ገንዘቦቻችሁና ልጆቻችሁ አላህን ከማስታወስ አያታሉዋችሁ፡፡ ይህንንም የሚሠሩ ሰዎች እነዚያ እነርሱ ከሳሪዎች ናቸው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُلۡهِكُمۡ أَمۡوَٰلُكُمۡ وَلَآ أَوۡلَٰدُكُمۡ عَن ذِكۡرِ ٱللَّهِۚ وَمَن يَفۡعَلۡ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡخَٰسِرُونَ ٩

10. አንዳችሁንም ሞት ሳይመጣውና ጌታዬ ሆይ! እንድመጸውትና ከደጋጌቹም ሰዎች እንድኾን ወደ ጥቂት ጊዜ ብታቆየኝ ኖሮ እመኛለሁ ከማለቱ በፊት ከሰጠናችሁ ሲሳይ ለግሱ፡፡

وَأَنفِقُواْ مِن مَّا رَزَقۡنَٰكُم مِّن قَبۡلِ أَن يَأۡتِيَ أَحَدَكُمُ ٱلۡمَوۡتُ فَيَقُولَ رَبِّ لَوۡلَآ أَخَّرۡتَنِيٓ إِلَىٰٓ أَجَلٖ قَرِيبٖ فَأَصَّدَّقَ وَأَكُن مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ١٠

وَلَن يُؤَخِّرَ ٱللَّهُ نَفۡسًا إِذَا جَآءَ أَجَلُهَاۚ وَٱللَّهُ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ﴿١١﴾

11. ማንኛይቱም ነፍስ የሞት ጊዜዋ በመጣበት ጊዜ አላህ በፍጹም አያቆያትም፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡

# سورة التغابن

# ሱረቱ አል ተጋቡን

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

يُسَبِّحُ لِلَّهِ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَمَا فِي ٱلۡأَرۡضِۖ لَهُ ٱلۡمُلۡكُ وَلَهُ ٱلۡحَمۡدُۖ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ﴿١﴾

1. በሰማያት ውስጥ ያለው በምድርም ውስጥ ያለው ሁሉ ለአላህ ያሞግሳል፡፡ ንግሥናው የእርሱ ብቻ ነው፡፡ ምስጋናም ለእርሱ ነው፡፡ እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡

هُوَ ٱلَّذِي خَلَقَكُمۡ فَمِنكُمۡ كَافِرٞ وَمِنكُم مُّؤۡمِنٞۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ بَصِيرٌ ﴿٢﴾

2. እርሱ ያ የፈጠራችሁ ነው፡፡ ከእናንተም ከሓዲ አልለ፡፡ ከእናንተም አማኝ አልለ፡፡ አላህም በምትሠሩት ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

خَلَقَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضَ بِٱلۡحَقِّ وَصَوَّرَكُمۡ فَأَحۡسَنَ صُوَرَكُمۡۖ وَإِلَيۡهِ ٱلۡمَصِيرُ ﴿٣﴾

3. ሰማያትንና ምድርን በእውነት ፈጠረ፡፡ ቀረጻችሁም ቅርጻችሁንም አሳመረ፡፡ መመለሻችሁም ወደእርሱ ነው፡፡

يَعۡلَمُ مَا فِي ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَيَعۡلَمُ مَا تُسِرُّونَ وَمَا تُعۡلِنُونَۚ وَٱللَّهُ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ﴿٤﴾

4. በሰማያትና በምድር ውስጥ ያለውን ሁሉ ያውቃል፡፡ የምትደብቁትንም የምትገልጡትንም ያውቃል፡፡ አላህም በልቦች ውስጥ ያለውን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَمۡ يَأۡتِكُمۡ نَبَؤُاْ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ مِن قَبۡلُ فَذَاقُواْ وَبَالَ أَمۡرِهِمۡ وَلَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ﴿٥﴾

5. የእነዚያ ከአሁን በፊት የካዱትና የክሕደታቸውን ቅጣት ቅመሱ የተባሉት ሕዝቦች ወሬ አልመጣላችሁምን? ለእነሱም አሳማሚ ቅጣት አልላቸው፡፡

ذَٰلِكَ بِأَنَّهُۥ كَانَت تَّأۡتِيهِمۡ رُسُلُهُم بِٱلۡبَيِّنَٰتِ فَقَالُوٓاْ أَبَشَرٞ يَهۡدُونَنَا فَكَفَرُواْ وَتَوَلَّواْۖ وَّٱسۡتَغۡنَى ٱللَّهُۚ وَٱللَّهُ غَنِيٌّ حَمِيدٞ ﴿٦﴾

6. ይህ (ቅጣት) እርሱ መልክተኞቻቸው በአስረጂዎች ይመጡባቸው ስለ ነበሩ «ሰዎችም ይመሩናልን?» ስላሉና ስለካዱ (ከእምነት) ስለ ዞሩም ነው፡፡ አላህም (ከእነሱ እምነት) ተብቃቃ፡፡ አላህም ተብቃቂ ምስጉን ነው፡፡

زَعَمَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓاْ أَن لَّن يُبۡعَثُواْۚ قُلۡ بَلَىٰ وَرَبِّي لَتُبۡعَثُنَّ ثُمَّ لَتُنَبَّؤُنَّ بِمَا عَمِلۡتُمۡۚ وَذَٰلِكَ عَلَى ٱللَّهِ يَسِيرٞ ٧

7. እነዚያ የካዱትን በፍጹም የማይቀሰሱ መኾናቸውን አሰቡ:: «አይደለም በጌታዬ እምላለሁ:: በእርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ:: ከዚያም በሠራችሁት ሁሉ ትነገራላችሁ:: ይህም በአላህ ላይ ቀላል ነው::» በላቸው::

فَـَٔامِنُواْ بِٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَٱلنُّورِ ٱلَّذِيٓ أَنزَلۡنَاۚ وَٱللَّهُ بِمَا تَعۡمَلُونَ خَبِيرٞ ٨

8. በአላህና በመልክተኛውም:: በዚያም ባወረድነው ብርሃን እመኑ:: «አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው» (በላቸው)::

يَوۡمَ يَجۡمَعُكُمۡ لِيَوۡمِ ٱلۡجَمۡعِۖ ذَٰلِكَ يَوۡمُ ٱلتَّغَابُنِۗ وَمَن يُؤۡمِنۢ بِٱللَّهِ وَيَعۡمَلۡ صَٰلِحٗا يُكَفِّرۡ عَنۡهُ سَيِّـَٔاتِهِۦ وَيُدۡخِلۡهُ جَنَّٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۚ ذَٰلِكَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡعَظِيمُ ٩

9. ለመሰብሰቢያ ቀን የሚሰበስብባችሁን ቀን (አስታውሱ)፤ ይህ የመጎዳዳት (መግለጫ) ቀን ነው:: በአላህም የሚያምን ሰው መልካምንም የሚሠራ ከርሱ ኃጢአቶቹን ይሰርይለታል፤ (ይፍቅለታል)፤ ከሥሮቻቸውም ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘለዓለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ ያገባዋል፤ ይህ ታላቅ ማግኘት ነው::

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَآ أُوْلَـٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلنَّارِ خَٰلِدِينَ فِيهَاۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ١٠

10. እነዚያም የካዱና በአንቀጾቻችን ያስተባበሉ እነዚያ በውስጡ ዘውታሪዎች ሲኾኑ የእሳት ጓዶች ናቸው፤ መመለሻቸውም ከፋ!

مَآ أَصَابَ مِن مُّصِيبَةٍ إِلَّا بِإِذۡنِ ٱللَّهِۗ وَمَن يُؤۡمِنۢ بِٱللَّهِ يَهۡدِ قَلۡبَهُۥۚ وَٱللَّهُ بِكُلِّ شَيۡءٍ عَلِيمٞ ١١

11. ከመከራም (ማንንም) አይነካም በአላህ ፈቃድ ቢኾን እንጅ፤ በአላህም የሚያምን ሰው ልቡን (ለትዕግስት) ይመራዋል፤ አላህም ነገሩን ሁሉ ዐዋቂ ነው::

وَأَطِيعُواْ ٱللَّهَ وَأَطِيعُواْ ٱلرَّسُولَۚ فَإِن تَوَلَّيۡتُمۡ فَإِنَّمَا عَلَىٰ رَسُولِنَا ٱلۡبَلَٰغُ ٱلۡمُبِينُ ١٢

12. አላህንም ተገዙ፤ መልክተኛውንም ታዘዙ፤ ብትዞሩም (መልክተኛውን አትጎዱም)፤ በመልክተኛውም ላይ ያለበት ግልጽ ማድረስ ብቻ ነው::

ٱللَّهُ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَۚ وَعَلَى ٱللَّهِ فَلۡيَتَوَكَّلِ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ١٣

13. አላህ ከርሱ በቀር አምላክ የለም፤ በአላህም ላይ አማኞቹ ይመኩ::

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِنَّ مِنۡ أَزۡوَٰجِكُمۡ وَأَوۡلَٰدِكُمۡ عَدُوّٗا لَّكُمۡ فَٱحۡذَرُوهُمۡۚ وَإِن تَعۡفُواْ وَتَصۡفَحُواْ وَتَغۡفِرُواْ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمٌ ١٤

14. እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ከሚስቶቻችሁና ከልጆቻችሁ (ከአላህ መንገድ በማስተጓጎል) ለናንተ ጠላቶች የኾኑ አልሉ፤ ስለዚህ ተጠንቀቋቸው፤ ይቅርታ ብታደርጉ ብታልፏቸውም ብተምሩዋቸውም አላህ በጣም መሓሪ አዛኝ ነው::

إِنَّمَآ أَمۡوَٰلُكُمۡ وَأَوۡلَٰدُكُمۡ فِتۡنَةٞۚ وَٱللَّهُ عِندَهُۥٓ أَجۡرٌ عَظِيمٞ ١٥

15. ገንዘቦቻችሁና ልጆቻችሁ ለናንተ መፈተኛ ብቻ ናቸው፤ አላህም እርሱ ዘንድ ታላቅ ምንዳ አልለ::

16. አላህንም የቻላችሁትን የክል ፍሩት፤ ትዕዛዙን ስሙም፤ ታዘዙም፤ ለግሱም፤ ለነፍሶቻችሁ መልካምን (ይሰጣችኋልና)፤ የነፍሱንም ንፍገት የሚጠበቅ ሰው እነዚያ እነሱ ፍላጎታቸውን የሚያገኙ ናቸው፡፡

فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ مَا ٱسۡتَطَعۡتُمۡ وَٱسۡمَعُواْ وَأَطِيعُواْ وَأَنفِقُواْ خَيۡرٗا لِّأَنفُسِكُمۡۗ وَمَن يُوقَ شُحَّ نَفۡسِهِۦ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡمُفۡلِحُونَ ١٦

17. ለአላህ መልካም ብድርን ብታበድሩ (ምንዳውን) ለናንተ ይደራርበዋል፤ ለናንተም ይምራል፤ አላህም አመስጋኝ ታጋሽ ነው፡፡

إِن تُقۡرِضُواْ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنٗا يُضَٰعِفۡهُ لَكُمۡ وَيَغۡفِرۡ لَكُمۡۚ وَٱللَّهُ شَكُورٌ حَلِيمٌ ١٧

18. ሩቁን ምስጢር ግልጹንም ሁሉ ዐዋቂው አሸናፊው ጥበበኛው ነው፡፡

عَٰلِمُ ٱلۡغَيۡبِ وَٱلشَّهَٰدَةِ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡحَكِيمُ ١٨

## ሱረቱ አል ጠላቅ

## سورة الطلاق

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አንተ ነቢዩ ሆይ! ሴቶችን መፍታት ባሰባችሁ ጊዜ፤ ለዒዳቸው ፍቱዋቸው፡፡ ዒዳንም ቁጠሩ፡፡ አላህንም ጌታችሁን ፍሩ፡፡ ግልጽ የኾነችን ጠያፍ ካልሠሩ በስተቀር ከቤቶቻቸው አታውጡዋቸው፤ አይውጡም፡፡ ይህችም የአላህ ሕግጋት ናት፡፡ የአላህንም ሕግጋት የተላለፈ ሰው በእርግጥ ነፍሱን በደለ፡፡ ከዚህ (ፍች) በኋላ አላህ (የመግለስ) ነገርን ምናልባት ያመጣ እንደኾነ አታውቅም፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِيُّ إِذَا طَلَّقۡتُمُ ٱلنِّسَآءَ فَطَلِّقُوهُنَّ لِعِدَّتِهِنَّ وَأَحۡصُواْ ٱلۡعِدَّةَۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ رَبَّكُمۡۖ لَا تُخۡرِجُوهُنَّ مِنۢ بُيُوتِهِنَّ وَلَا يَخۡرُجۡنَ إِلَّآ أَن يَأۡتِينَ بِفَٰحِشَةٖ مُّبَيِّنَةٖۚ وَتِلۡكَ حُدُودُ ٱللَّهِۚ وَمَن يَتَعَدَّ حُدُودَ ٱللَّهِ فَقَدۡ ظَلَمَ نَفۡسَهُۥۚ لَا تَدۡرِي لَعَلَّ ٱللَّهَ يُحۡدِثُ بَعۡدَ ذَٰلِكَ أَمۡرٗا ١

2. ጊዜያቸውንም ለመዳረስ በተቃረቡ ጊዜ በመልካም ያዙዋቸው፡፡ ወይም በመልካም ተለያዩዋቸው፡፡ ከእናንተም ውስጥ ሁለት የትክክለኛነት ባለቤቶችን አስመስክሩ፡፡ ምስክርነትንም ለአላህ አስተካክሉ፡፡ ይህ በአላህና በመጨረሻው ቀን የሚያምን የኾነ ሰው ሁሉ በእርሱ ይገሰጽበታል፡፡ አላህንም የሚፈራ ሰው ለእርሱ መውጫን ያደርግለታል፡፡

فَإِذَا بَلَغۡنَ أَجَلَهُنَّ فَأَمۡسِكُوهُنَّ بِمَعۡرُوفٍ أَوۡ فَارِقُوهُنَّ بِمَعۡرُوفٖ وَأَشۡهِدُواْ ذَوَيۡ عَدۡلٖ مِّنكُمۡ وَأَقِيمُواْ ٱلشَّهَٰدَةَ لِلَّهِۚ ذَٰلِكُمۡ يُوعَظُ بِهِۦ مَن كَانَ يُؤۡمِنُ بِٱللَّهِ وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡأٓخِرِۚ وَمَن يَتَّقِ ٱللَّهَ يَجۡعَل لَّهُۥ مَخۡرَجٗا ٢

3. ከማያስበውም በኩል ሲሳየን ይሰጠዋል፡፡ በአላህም ላይ የሚጠጋ ሰው እርሱ በቂው ነው፡፡ አላህ ፈቃዱን አድራሽ ነው፡፡ አላህ ለነገሩ ሁሉ የተወሰነ ጊዜን በእርግጥ አድርጓል፡፡

وَيَرۡزُقۡهُ مِنۡ حَيۡثُ لَا يَحۡتَسِبُۚ وَمَن يَتَوَكَّلۡ عَلَى ٱللَّهِ فَهُوَ حَسۡبُهُۥٓۚ إِنَّ ٱللَّهَ بَٰلِغُ أَمۡرِهِۦۚ قَدۡ جَعَلَ ٱللَّهُ لِكُلِّ شَيۡءٖ قَدۡرٗا ٣

4. እኒያም ከሴቶቻቸው ከአደፍ ያቋረጡት (በዒዳቸው ሕግ) ብትጠራጠሩ ዒዳቸው ሦስት ወር ነው፡፡ እኒያም ገና አደፍን ያላዩት (ዒዳቸው እንደዚሁ ነው)፡፡ የእርግዝና ባለቤቶችም ጊዜያቸው እርጉዛቸውን መውለድ ነው፡፡ አላህንም የሚፈራ ሰው ከነገሩ ሁሉ ለርሱ መግራትን ያደርግለታል፡፡

وَٱلَّـٰٓـِٔي يَئِسۡنَ مِنَ ٱلۡمَحِيضِ مِن نِّسَآئِكُمۡ إِنِ ٱرۡتَبۡتُمۡ فَعِدَّتُهُنَّ ثَلَٰثَةُ أَشۡهُرٖ وَٱلَّـٰٓـِٔي لَمۡ يَحِضۡنَۚ وَأُوْلَٰتُ ٱلۡأَحۡمَالِ أَجَلُهُنَّ أَن يَضَعۡنَ حَمۡلَهُنَّۚ وَمَن يَتَّقِ ٱللَّهَ يَجۡعَل لَّهُۥ مِنۡ أَمۡرِهِۦ يُسۡرٗا ٤

5. ይህ የአላህ ፍርድ ነው፡፡ ወደእናንተ አወረደው፡፡ አላህንም የሚፈራ ሰው ኀጢአቶቹን ከእርሱ ይሰርይለታል፡፡ ምንዳንም ለእርሱ ያተልቅለታል፡፡

ذَٰلِكَ أَمۡرُ ٱللَّهِ أَنزَلَهُۥٓ إِلَيۡكُمۡۚ وَمَن يَتَّقِ ٱللَّهَ يُكَفِّرۡ عَنۡهُ سَيِّـَٔاتِهِۦ وَيُعۡظِمۡ لَهُۥٓ أَجۡرًا ٥

6. ከችሎታችሁ ከተቀመጣችሁበት ስፍራ አስቀምጧቸው፡፡ በእነርሱም ላይ ልታጣብቡ አትጉዷቸው፡፡ የእርግዝና ባለቤቶችም ቢኾኑ እርጉዛቸውን እስኪወልዱ ድረስ በእነርሱ ላይ ቀልቡ፡፡ ለእናንተም (ልጆቻችሁን) ቢያጠቡላችሁ ምንዳዎቻቸውን ስጧቸው፡፡ በመካከላችሁም በመልካም ነገር ተመካከሩ፡፡ ብትቸጋገሩም ለእርሱ ሌላ (ሴት) ታጠባለታለች፡፡

أَسۡكِنُوهُنَّ مِنۡ حَيۡثُ سَكَنتُم مِّن وُجۡدِكُمۡ وَلَا تُضَآرُّوهُنَّ لِتُضَيِّقُواْ عَلَيۡهِنَّۚ وَإِن كُنَّ أُوْلَٰتِ حَمۡلٖ فَأَنفِقُواْ عَلَيۡهِنَّ حَتَّىٰ يَضَعۡنَ حَمۡلَهُنَّۚ فَإِنۡ أَرۡضَعۡنَ لَكُمۡ فَـَٔاتُوهُنَّ أُجُورَهُنَّ وَأۡتَمِرُواْ بَيۡنَكُم بِمَعۡرُوفٖۖ وَإِن تَعَاسَرۡتُمۡ فَسَتُرۡضِعُ لَهُۥٓ أُخۡرَىٰ ٦

7. የችሎታ ባለቤት ከችሎታው ይቀልብ፡፡ በእርሱም ላይ ሲሳዩ የተጠበበበት ሰው አላህ ከሰጠው ይቀልብ አላህ ነፍስን የሰጣትን እንጅ አያስገድድም፡፡ አላህ ከችግር በኋላ ምቾትን በእርግጥ ያደርጋል፡፡

لِيُنفِقۡ ذُو سَعَةٖ مِّن سَعَتِهِۦۖ وَمَن قُدِرَ عَلَيۡهِ رِزۡقُهُۥ فَلۡيُنفِقۡ مِمَّآ ءَاتَىٰهُ ٱللَّهُۚ لَا يُكَلِّفُ ٱللَّهُ نَفۡسًا إِلَّا مَآ ءَاتَىٰهَاۚ سَيَجۡعَلُ ٱللَّهُ بَعۡدَ عُسۡرٖ يُسۡرٗا ٧

8. ከከተማም ከጌታዋ ትዕዛዝ ከመልክተኞቹም ያመጸች፣ ብርቱንም ቁጥጥር የተቆጣጠርናት፣ መጥፎንም ቅጣት የቀጣናት ብዙ ናት፡፡

وَكَأَيِّن مِّن قَرۡيَةٍ عَتَتۡ عَنۡ أَمۡرِ رَبِّهَا وَرُسُلِهِۦ فَحَاسَبۡنَٰهَا حِسَابٗا شَدِيدٗا وَعَذَّبۡنَٰهَا عَذَابٗا نُّكۡرٗا ٨

9. የነገርዋንም ቅጣት ቀመሰች፡፡ የነገርዋም መጨረሻ ከሳራ ኾነ፡፡

فَذَاقَتۡ وَبَالَ أَمۡرِهَا وَكَانَ عَٰقِبَةُ أَمۡرِهَا خُسۡرًا ٩

10. አላህ ለእነርሱ ብርቱን ቅጣት አዘጋጀ፡፡ እናንተም የአእምሮ ባለቤቶች ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ እነዚያ ያመኑ (ሆይ)! አላህ ወደናንተ ግሳጼን በእርግጥ አወረደ፡፡ መልክተኛን (ላከ)፡፡

أَعَدَّ ٱللَّهُ لَهُمۡ عَذَابٗا شَدِيدٗاۖ فَٱتَّقُواْ ٱللَّهَ يَـٰٓأُوْلِي ٱلۡأَلۡبَٰبِ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْۚ قَدۡ أَنزَلَ ٱللَّهُ إِلَيۡكُمۡ ذِكۡرٗا ١٠

11. እነዚያን ያመኑትንና መልካሞችን የሠሩትን ከጨለማዎች ወደ ብርሃን ያወጣ ዘንድ የአላህን አንቀጾች ገላጮች ሲኾኑ በእናንተ ላይ የሚያነብላችሁን (ላከ)፡፡ በአላህም አንቀጾች የሚያምን፣ መልካምን ሥራ የሚሠራም ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈስሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘለዓለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ ያገባዋል፡፡ አላህ ለእርሱ ሲሳይን በእርግጥ አሳመረ፡፡

رَّسُولٗا يَتۡلُواْ عَلَيۡكُمۡ ءَايَٰتِ ٱللَّهِ مُبَيِّنَٰتٖ لِّيُخۡرِجَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّـٰلِحَٰتِ مِنَ ٱلظُّلُمَٰتِ إِلَى ٱلنُّورِۚ وَمَن يُؤۡمِنۢ بِٱللَّهِ وَيَعۡمَلۡ صَٰلِحٗا يُدۡخِلۡهُ جَنَّـٰتٖ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدٗاۖ قَدۡ أَحۡسَنَ ٱللَّهُ لَهُۥ رِزۡقًا ١١

12. አላህ ያ ሰባትን ሰማያት የፈጠረ ነው፡፡ ከምድርም መሰላቸውን (ፈጥሮአል)፤ በመካከላቸው ትእዛዙ ይወርዳል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ መኾኑን አላህም በነገሩ ሁሉ በዕውቀት ያካበበ መኾኑን በዕውቀት ያካበበ መኾኑን ታውቁ ዘንድ (ይህንን አሳወቃችሁ)፡፡

ٱللَّهُ ٱلَّذِى خَلَقَ سَبۡعَ سَمَٰوَٰتٍ وَمِنَ ٱلۡأَرۡضِ مِثۡلَهُنَّۖ يَتَنَزَّلُ ٱلۡأَمۡرُ بَيۡنَهُنَّ لِتَعۡلَمُوٓاْ أَنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَىۡءٍ قَدِيرٌ وَأَنَّ ٱللَّهَ قَدۡ أَحَاطَ بِكُلِّ شَىۡءٍ عِلۡمَۢا ﴿١٢﴾

# ሱረቱ አል ተህሪም

# سورة التحريم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አንተ ነቢዩ ሆይ! አላህ ለአንተ የፈቀደልህን ነገር ሚስቶችህን ማስወደድን የምትፈልግ ስትኾን (ባንተ ላይ) ለምን እርም ታደርጋለህ? አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِىُّ لِمَ تُحَرِّمُ مَآ أَحَلَّ ٱللَّهُ لَكَۖ تَبۡتَغِى مَرۡضَاتَ أَزۡوَٰجِكَۚ وَٱللَّهُ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١﴾

2. አላህ ለእናንተ የመሓሎቻችሁን መፍቻ ደነገገላችሁ፡፡ አላህም ረዳታችሁ ነው፡፡ እርሱም ዐዋቂው ጥበበኛው ነው፡፡

قَدۡ فَرَضَ ٱللَّهُ لَكُمۡ تَحِلَّةَ أَيۡمَٰنِكُمۡۚ وَٱللَّهُ مَوۡلَىٰكُمۡۖ وَهُوَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡحَكِيمُ ﴿٢﴾

3. ነቢዩ ከሚስቶቹ ወደ አንዷ ወሬን በመሰጠረ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ እርሱንም በነገረችና አላህ እርሱን (ማውራቷን) ባሳወቀው ጊዜ ከፊሉን አስታወቀ፡፡ ከፊሉንም ተወ፡፡ በእርሱም ባወራት ጊዜ «ይህን ማን ነገረህ?» አለች፡፡ «ዐዋቂው ውስጠ ዐዋቂው ነገረኝ» አላት፤

وَإِذۡ أَسَرَّ ٱلنَّبِىُّ إِلَىٰ بَعۡضِ أَزۡوَٰجِهِۦ حَدِيثًا فَلَمَّا نَبَّأَتۡ بِهِۦ وَأَظۡهَرَهُ ٱللَّهُ عَلَيۡهِ عَرَّفَ بَعۡضَهُۥ وَأَعۡرَضَ عَنۢ بَعۡضٍۖ فَلَمَّا نَبَّأَهَا بِهِۦ قَالَتۡ مَنۡ أَنۢبَأَكَ هَٰذَاۖ قَالَ نَبَّأَنِىَ ٱلۡعَلِيمُ ٱلۡخَبِيرُ ﴿٣﴾

4. ወደ አላህ ብትመለሱ ልቦቻችሁ በእርግጥ ተዘንበለዋልና (ትስማማላችሁ)፡፡ በእርሱም ላይ ብትረዳዱ አላህ እርሱ ረዳቱ ነው፡፡ ጂብሪልም ከምእምናንም መልካሙ ከዚህም በኋላ መላእክቱ ረዳቶቹ ናቸው፡፡

إِن تَتُوبَآ إِلَى ٱللَّهِ فَقَدۡ صَغَتۡ قُلُوبُكُمَاۖ وَإِن تَظَٰهَرَا عَلَيۡهِ فَإِنَّ ٱللَّهَ هُوَ مَوۡلَىٰهُ وَجِبۡرِيلُ وَصَٰلِحُ ٱلۡمُؤۡمِنِينَۖ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ بَعۡدَ ذَٰلِكَ ظَهِيرٌ ﴿٤﴾

5. (መላችሁንም) ቢፈታችሁ ከእናንተ የበለጡ ሚስቶችን ሙስሊሞች፣ አማኞች፣ ታዛዦች፣ ተጸጻቾች፣ (ለአላህ) ተገዢዎች፣ ጾመኛዎች ፈቶች፣ ደናግልም የኾኑትን ጌታው ሊለውጠው ይከጀላል፡፡

عَسَىٰ رَبُّهُۥٓ إِن طَلَّقَكُنَّ أَن يُبۡدِلَهُۥٓ أَزۡوَٰجًا خَيۡرًا مِّنكُنَّ مُسۡلِمَٰتٍ مُّؤۡمِنَٰتٍ قَٰنِتَٰتٍ تَٰٓئِبَٰتٍ عَٰبِدَٰتٍ سَٰٓئِحَٰتٍ ثَيِّبَٰتٍ وَأَبۡكَارًا ﴿٥﴾

6. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ነፍሶቻችሁንና ቤተሰቦቻችሁን መቀጣጠያዋ ሰዎችና ደንጋዮች ከኾነች እሳት ጠብቁ፡፡ በእርሷ ላይ ጨካኞች፣ ኀይለኞች የኾኑ መላእክት አልሉ፡፡ አላህን ያዘዛቸውን ነገር (በመጣስ) አያምጹም፡፡ የሚታዘዙትንም ሁሉ ይሠራሉ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ قُوٓا۟ أَنفُسَكُمْ وَأَهْلِيكُمْ نَارًا وَقُودُهَا ٱلنَّاسُ وَٱلْحِجَارَةُ عَلَيْهَا مَلَـٰٓئِكَةٌ غِلَاظٌ شِدَادٌ لَّا يَعْصُونَ ٱللَّهَ مَآ أَمَرَهُمْ وَيَفْعَلُونَ مَا يُؤْمَرُونَ ٦

7. እላንተ የካዳችሁ ሆይ! ዛሬ አታመካኙ፡፡ የምትመነዱት ያንን ትሠሩት የነበራችሁትን ብቻ ነው (ይባላሉ)፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ كَفَرُوا۟ لَا تَعْتَذِرُوا۟ ٱلْيَوْمَ ۖ إِنَّمَا تُجْزَوْنَ مَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ ٧

8. እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ንጹሕ የኾነችን ጸጸት በመጸጸት ወደ አላህ ተመለሱ፡፡ ጌታችሁ ከእናንተ ኀጢአቶቻችሁን ሊሰርይላችሁ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውንም ገነቶች ሊያስገባችሁ ይከጀላልና፡፡ አላህ ነቢዩን፣ እነዚያንም ከእርሱ ጋር ያመኑትን በማያሳፍርበት ቀን ብርሃናቸው በፊቶቻቸውና በቀኞቻቸው የሚሮጥ ሲኾን «ጌታችን ሆይ! ብርሃናችንን ሙላልን፣ ለእኛ ምሕረትም አድርግልን፣ አንተ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነህና» ይላሉ፡፡

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ تُوبُوٓا۟ إِلَى ٱللَّهِ تَوْبَةً نَّصُوحًا عَسَىٰ رَبُّكُمْ أَن يُكَفِّرَ عَنكُمْ سَيِّـَٔاتِكُمْ وَيُدْخِلَكُمْ جَنَّـٰتٍ تَجْرِى مِن تَحْتِهَا ٱلْأَنْهَـٰرُ يَوْمَ لَا يُخْزِى ٱللَّهُ ٱلنَّبِىَّ وَٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ مَعَهُۥ ۖ نُورُهُمْ يَسْعَىٰ بَيْنَ أَيْدِيهِمْ وَبِأَيْمَـٰنِهِمْ يَقُولُونَ رَبَّنَآ أَتْمِمْ لَنَا نُورَنَا وَٱغْفِرْ لَنَآ ۖ إِنَّكَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ٨

9. አንተ ነቢዩ ሆይ! ከሓዲዎችንና መናፍቃንን ታገል፡፡ በእነርሱም ላይ በርታ፡፡ መኖሪያቸውም ገሀነም ናት፡፡ ምን ትከፋም መመለሻ!

يَـٰٓأَيُّهَا ٱلنَّبِىُّ جَـٰهِدِ ٱلْكُفَّارَ وَٱلْمُنَـٰفِقِينَ وَٱغْلُظْ عَلَيْهِمْ ۚ وَمَأْوَىٰهُمْ جَهَنَّمُ ۖ وَبِئْسَ ٱلْمَصِيرُ ٩

10. አላህ ለእነዚያ ለካዱት ሰዎች የኑሕን ሴትና የሉጥን ሴት ምሳሌ አደረገ፡፡ ከባሮቻችን ከኾኑ ሁለት መልካም ባሪያዎች ሥር ነበሩ፡፡ ከዱዋቸውም፡፡ ከአላህም (ቅጣት ኑሕና ሉጥ) ከሚስቶቻቸው ምንም አልገፈተሩላቸውም፡፡ ከገቢዎቹም ጋር «እሳትን ግቡ» ተባሉ፡፡

ضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلًا لِّلَّذِينَ كَفَرُوا۟ ٱمْرَأَتَ نُوحٍ وَٱمْرَأَتَ لُوطٍ ۖ كَانَتَا تَحْتَ عَبْدَيْنِ مِنْ عِبَادِنَا صَـٰلِحَيْنِ فَخَانَتَاهُمَا فَلَمْ يُغْنِيَا عَنْهُمَا مِنَ ٱللَّهِ شَيْـًٔا وَقِيلَ ٱدْخُلَا ٱلنَّارَ مَعَ ٱلدَّٰخِلِينَ ١٠

11. ለእነዚያ ለአመኑትም የፈርኦንን ሴት አላህ ምሳሌ አደረገ፡፡ «ጌታዬ ሆይ! አንተ ዘንድ በገነት ውስጥ ለእኔ ቤትን ገንባልኝ፡፡ ከፈርዖንና ከሥራውም አድነኝ፡፡ ከበደለኞቹ ሕዝቦችም አድነኝ» ባለች ጊዜ፡፡

وَضَرَبَ ٱللَّهُ مَثَلًا لِّلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ ٱمْرَأَتَ فِرْعَوْنَ إِذْ قَالَتْ رَبِّ ٱبْنِ لِى عِندَكَ بَيْتًا فِى ٱلْجَنَّةِ وَنَجِّنِى مِن فِرْعَوْنَ وَعَمَلِهِۦ وَنَجِّنِى مِنَ ٱلْقَوْمِ ٱلظَّـٰلِمِينَ ١١

12. የዒምራንን ልጅ መርየምንም ያችን ብልቷን የጠበቀችውን (ምሳሌ አደረገ)፡፡ በእርሱም ውስጥ ከመንፈሳችን ነፍፋን፡፡ በጌታዋ ቃላትና በመጻሕፍቱም አረጋገጠች፡፡ ከታዛዦቹም ነበረች፡፡

وَمَرْيَمَ ٱبْنَتَ عِمْرَٰنَ ٱلَّتِىٓ أَحْصَنَتْ فَرْجَهَا فَنَفَخْنَا فِيهِ مِن رُّوحِنَا وَصَدَّقَتْ بِكَلِمَـٰتِ رَبِّهَا وَكُتُبِهِۦ وَكَانَتْ مِنَ ٱلْقَـٰنِتِينَ ١٢

# ሱረቱ አል ሙልክ

# سورة الملك

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ያ ንግሥና በእጁ የኾነው አምላክ ችሮታው በዛ:: እርሱም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው::

تَبَٰرَكَ ٱلَّذِي بِيَدِهِ ٱلۡمُلۡكُ وَهُوَ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ قَدِيرٌ ١

2. ያ የትኛችሁ ሥራው ይበልጥ ያማረ መኾኑን ሊሞክራችሁ ሞትንና ሕይወትን የፈጠረ ነው:: እርሱም አሸናፊው መሓሪው ነው::

ٱلَّذِي خَلَقَ ٱلۡمَوۡتَ وَٱلۡحَيَوٰةَ لِيَبۡلُوَكُمۡ أَيُّكُمۡ أَحۡسَنُ عَمَلٗاۚ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلۡغَفُورُ ٢

3. ያ ሰባትን ሰማያት የተነባበሩ ኾነው የፈጠረ ነው:: በአልረሕማን አፈጣጠር ውስጥ ምንም መዛነፍን አታይም:: ዓይንህንም መልስ:: «ከስንጥቆች አንዳችን ታያለህን?»

ٱلَّذِي خَلَقَ سَبۡعَ سَمَٰوَٰتٖ طِبَاقٗاۖ مَّا تَرَىٰ فِي خَلۡقِ ٱلرَّحۡمَٰنِ مِن تَفَٰوُتٖۖ فَٱرۡجِعِ ٱلۡبَصَرَ هَلۡ تَرَىٰ مِن فُطُورٖ ٣

4. ከዚያም ብዙ ጊዜ ዓይንህን መላልስ:: ዓይንህ ተዋርዶ እርሱም የደከመ ኾኖ ወዳንተ ይመለሳል::

ثُمَّ ٱرۡجِعِ ٱلۡبَصَرَ كَرَّتَيۡنِ يَنقَلِبۡ إِلَيۡكَ ٱلۡبَصَرُ خَاسِئٗا وَهُوَ حَسِيرٞ ٤

5. ቅርቢቱን ሰማይም በእርግጥ በመብራቶች (በከዋክብት) አጌጥናት:: ለሰይጣናትም መቀጥቀጫዎች አደረግናት:: ለእነርሱም (ለሰይጣኖች) የእሳትን ቅጣት አዘጋጀን::

وَلَقَدۡ زَيَّنَّا ٱلسَّمَآءَ ٱلدُّنۡيَا بِمَصَٰبِيحَ وَجَعَلۡنَٰهَا رُجُومٗا لِّلشَّيَٰطِينِۖ وَأَعۡتَدۡنَا لَهُمۡ عَذَابَ ٱلسَّعِيرِ ٥

6. ለእነዚያም በጌታቸው ለካዱት የገሀነም ቅጣት አልላቸው:: መመለሻይቱም ከፋች!

وَلِلَّذِينَ كَفَرُواْ بِرَبِّهِمۡ عَذَابُ جَهَنَّمَۖ وَبِئۡسَ ٱلۡمَصِيرُ ٦

7. በውስጧ በተጣሉ ጊዜ፤ እርሷ የምትፈላ ስትኾን ለእርሷ (እንደ አህያ) ማናፋትን ይሰማሉ::

إِذَآ أُلۡقُواْ فِيهَا سَمِعُواْ لَهَا شَهِيقٗا وَهِيَ تَفُورُ ٧

8. ከቁጭትዋ የተነሳ ልትቆራረጥ ትቀርባለች:: በውስጧ ጭፍሮች በተጣሉ ቁጥር ዘበኞቿዋ «አስፈራሪ (ነቢይ) አልመጣችሁምን?» በማለት ይጠይቋቸዋል::

تَكَادُ تَمَيَّزُ مِنَ ٱلۡغَيۡظِۖ كُلَّمَآ أُلۡقِيَ فِيهَا فَوۡجٞ سَأَلَهُمۡ خَزَنَتُهَآ أَلَمۡ يَأۡتِكُمۡ نَذِيرٞ ٨

9. «አይደለም በእርግጥ አስፈራሪ መጥቶናል:: አስተባበልነውም:: አላህም ምንንም አላወረደ እናንተ (አውርዷል ስትሉ) በትልቅ ስህተት ውስጥ እንጅ አይደላችሁም አልን» ይላሉ::

قَالُواْ بَلَىٰ قَدۡ جَآءَنَا نَذِيرٞ فَكَذَّبۡنَا وَقُلۡنَا مَا نَزَّلَ ٱللَّهُ مِن شَيۡءٍ إِنۡ أَنتُمۡ إِلَّا فِي ضَلَٰلٖ كَبِيرٖ ٩

10. «የምንሰማ ወይም የምናስብ በነበርንም ኖሮ በነዳጅ እሳት ጓዶች ውስጥ ባልኾን ነበር» ይላሉ::

وَقَالُواْ لَوۡ كُنَّا نَسۡمَعُ أَوۡ نَعۡقِلُ مَا كُنَّا فِيٓ أَصۡحَٰبِ ٱلسَّعِيرِ ١٠

فَٱعۡتَرَفُواْ بِذَنۢبِهِمۡ فَسُحۡقٗا لِّأَصۡحَٰبِ ٱلسَّعِيرِ ﴿١١﴾

11. በኀጢኣታቸውም ያምናሉ ለእሳት ጓዶችም (ከእዝነት) መራቅ ተገባቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ يَخۡشَوۡنَ رَبَّهُم بِٱلۡغَيۡبِ لَهُم مَّغۡفِرَةٞ وَأَجۡرٞ كَبِيرٞ ﴿١٢﴾

12. እነዚያ ጌታቸውን በሩቁ የሚፈሩ ለእነርሱ ምሕረትና ታላቅ ምንዳ አልላቸው፡፡

وَأَسِرُّواْ قَوۡلَكُمۡ أَوِ ٱجۡهَرُواْ بِهِۦٓۖ إِنَّهُۥ عَلِيمُۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ﴿١٣﴾

13. (ሰዎች ሆይ!) ቃላችሁንም መስጥሩ፡፡ ወይም በእርሱ ጩሁ፡፡ እርሱ በልቦች ውስጥ ያለን ሁሉ ዐዋቂ ነው፡፡

أَلَا يَعۡلَمُ مَنۡ خَلَقَ وَهُوَ ٱللَّطِيفُ ٱلۡخَبِيرُ ﴿١٤﴾

14. የፈጠረ አምላክ እርሱ ዕውቀት ረቂቁ፣ ውስጥ ዐዋቂው ሲኾን (ምስጢርን ሁሉ) አያውቅምን?

هُوَ ٱلَّذِي جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ ذَلُولٗا فَٱمۡشُواْ فِي مَنَاكِبِهَا وَكُلُواْ مِن رِّزۡقِهِۦۖ وَإِلَيۡهِ ٱلنُّشُورُ ﴿١٥﴾

15. እርሱ ያ ምድርን ለእናንተ የተገራች ያደረገላችሁ ነው፡፡ በጋራዎችዋና በመንገዶችዋም ኺዱ፡፡፡ ከሲሳዩም ብሉ፡፡ (ኋላ) መመለሻውም ወደእርሱ ብቻ ነው፡፡

ءَأَمِنتُم مَّن فِي ٱلسَّمَآءِ أَن يَخۡسِفَ بِكُمُ ٱلۡأَرۡضَ فَإِذَا هِيَ تَمُورُ ﴿١٦﴾

16. በሰማይ ውስጥ ያለን (ሰራዊት) በእናንተ ምድርን ቢደረባባችሁ ወዲያውም እርሷ የምታረገርግ ብትኾን ትተማመናላችሁን? (አትፈሩምን?)

أَمۡ أَمِنتُم مَّن فِي ٱلسَّمَآءِ أَن يُرۡسِلَ عَلَيۡكُمۡ حَاصِبٗاۖ فَسَتَعۡلَمُونَ كَيۡفَ نَذِيرِ ﴿١٧﴾

17. ወይም በሰማይ ውስጥ ያለን በእናንተ ላይ ጠጠርን ያዘለች ነፋስን ቢልክባችሁ ትተማመናላችሁን? (አትፈሩምን?) ማስጠንቀቄም እንዴት እንደኾነ ወደፊት ታውቃላችሁ፡፡

وَلَقَدۡ كَذَّبَ ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِهِمۡ فَكَيۡفَ كَانَ نَكِيرِ ﴿١٨﴾

18. እነዚያም ከእነርሱ በፊት የነበሩት በእርግጥ አስተባበሉ፡፡ ጥላቻዬም እንዴት ነበር!

أَوَلَمۡ يَرَوۡاْ إِلَى ٱلطَّيۡرِ فَوۡقَهُمۡ صَٰٓفَّٰتٖ وَيَقۡبِضۡنَۚ مَا يُمۡسِكُهُنَّ إِلَّا ٱلرَّحۡمَٰنُۚ إِنَّهُۥ بِكُلِّ شَيۡءِۭ بَصِيرٌ ﴿١٩﴾

19. ወደ አእዋፍ ከበላያቸው ክንፎቻቸውን ዘርግተው ተንሳፋፊዎች የሚሰበስቡም ሲኾኑ አላዩምን? ከአልረሕማን በቀር (ባየር ላይ) የሚይዛቸው የለም፡፡ እርሱ በነገሩ ሁሉ ተመልካች ነው፡፡

أَمَّنۡ هَٰذَا ٱلَّذِي هُوَ جُندٞ لَّكُمۡ يَنصُرُكُم مِّن دُونِ ٱلرَّحۡمَٰنِۚ إِنِ ٱلۡكَٰفِرُونَ إِلَّا فِي غُرُورٍ ﴿٢٠﴾

20. በእውነቱ ያ እርሱ ከአልረሕማን ሌላ የሚረዳችሁ ለእናንተ የኾነ ሰራዊት ማነው? ከሓዲዎች በመታለል ውስጥ እንጅ በሌላ ላይ አይደሉም፡፡

أَمَّنۡ هَٰذَا ٱلَّذِي يَرۡزُقُكُمۡ إِنۡ أَمۡسَكَ رِزۡقَهُۥۚ بَل لَّجُّواْ فِي عُتُوّٖ وَنُفُورٍ ﴿٢١﴾

21. ወይም ሲሳዩን ቢይዝባችሁ ያ ሲሳይን የሚሰጣችሁ ማነው? በእውነቱ እነርሱ በሞገድና በመደንበር ውስጥ ችክ አሉ፡፡

22. በፊቱ ላይ ተደፍቶ የሚኼድ ሰው ይበልጥ የቀና ነውን? ወይስ በቀጥተኛ መንገድ ላይ ተስተካክሎ የሚኼድ?

أَفَمَن يَمۡشِي مُكِبًّا عَلَىٰ وَجۡهِهِۦٓ أَهۡدَىٰٓ أَمَّن يَمۡشِي سَوِيًّا عَلَىٰ صِرَٰطٖ مُّسۡتَقِيمٖ ﴿٢٢﴾

23. «እርሱ ያ የፈጠራችሁ ለእናንተም መስሚያና ማያዎችን፣ ልቦችንም ያደረገላችሁ ነው፡፡ ጥቂትንም አታመሰግኑም» በላቸው፡፡

قُلۡ هُوَ ٱلَّذِيٓ أَنشَأَكُمۡ وَجَعَلَ لَكُمُ ٱلسَّمۡعَ وَٱلۡأَبۡصَٰرَ وَٱلۡأَفۡـِٔدَةَۚ قَلِيلٗا مَّا تَشۡكُرُونَ ﴿٢٣﴾

24. «እርሱ ያ በምድር ላይ የበተናችሁ ነው፡፡ ወደእርሱም ትሰበሰባላችሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ هُوَ ٱلَّذِي ذَرَأَكُمۡ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَإِلَيۡهِ تُحۡشَرُونَ ﴿٢٤﴾

25. «እውነተኞችም እንደኾናችሁ ይህ ቀጠሮ መቼ ነው?» ይላሉ፡፡

وَيَقُولُونَ مَتَىٰ هَٰذَا ٱلۡوَعۡدُ إِن كُنتُمۡ صَٰدِقِينَ ﴿٢٥﴾

26. «ዕውቀቱ አላህ ዘንድ ብቻ ነው፡፡ እኔ ግልጽ አስፈራሪ እንጅ ሌላ አይደለሁም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنَّمَا ٱلۡعِلۡمُ عِندَ ٱللَّهِ وَإِنَّمَآ أَنَا۠ نَذِيرٞ مُّبِينٞ ﴿٢٦﴾

27. (ቅጣቱን) ቅርብ ኾኖ ባዩትም ጊዜ የእነዚያ የካዱት ሰዎች ፊቶች ይከከፋሉ፡፡ «ይህ ያ በእርሱ ትከራከሩበት የነበራችሁት ነው» ይባላሉም፡፡

فَلَمَّا رَأَوۡهُ زُلۡفَةٗ سِيٓـَٔتۡ وُجُوهُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ وَقِيلَ هَٰذَا ٱلَّذِي كُنتُم بِهِۦ تَدَّعُونَ ﴿٢٧﴾

28. «አያችሁን? አላህ ቢገድለኝ ከእኔ ጋር ያሉትንም (እንደዚሁ) ወይም (በማቆየት) ቢያዝንልን ከሓዲዎችን ከአሳማሚ ቅጣት የሚያድን ማን ነው?» በላቸው፡፡

قُلۡ أَرَءَيۡتُمۡ إِنۡ أَهۡلَكَنِيَ ٱللَّهُ وَمَن مَّعِيَ أَوۡ رَحِمَنَا فَمَن يُجِيرُ ٱلۡكَٰفِرِينَ مِنۡ عَذَابٍ أَلِيمٖ ﴿٢٨﴾

29. «እርሱ (እመኑበት የምላችሁ) አልረሕማን ነው፡፡ (እኛ) በእርሱ አመንን፡፡ በርሱም ላይ ተጠጋን፡፡ ወደ ፊትም በግልጽ መሳሳት ውስጥ የኾነው እርሱ ማን እንደ ኾነ በእርግጥ ታውቃላችሁ» በላቸው፡፡

قُلۡ هُوَ ٱلرَّحۡمَٰنُ ءَامَنَّا بِهِۦ وَعَلَيۡهِ تَوَكَّلۡنَاۖ فَسَتَعۡلَمُونَ مَنۡ هُوَ فِي ضَلَٰلٖ مُّبِينٖ ﴿٢٩﴾

30. «አያችሁን? ውሃችሁ ሠራጊ ቢኾን ፈሳሺን ውሃ የሚያመጣላችሁ ማን ነው?» በላቸው፡፡ (አላህ የዓለማት ጌታ ያመጣዋል)፡፡

قُلۡ أَرَءَيۡتُمۡ إِنۡ أَصۡبَحَ مَآؤُكُمۡ غَوۡرٗا فَمَن يَأۡتِيكُم بِمَآءٖ مَّعِينِۭ ﴿٣٠﴾

# ሱረቱ አል ቀለም

# سورة القلم

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ኑ.(ኑን)፤ በብርእ እምላለሁ በዚያም (መልአኮች) በሚጽፉት፡፡

نٓۚ وَٱلۡقَلَمِ وَمَا يَسۡطُرُونَ ١

2. አንተ በጌታህ ጸጋ የተጎናጸፍክ ስትኾን ዕብድ አይደለህም፡፡

مَآ أَنتَ بِنِعۡمَةِ رَبِّكَ بِمَجۡنُونٖ ٢

3. ላንተም (ከጌታህ) የማይቋረጥ ዋጋ በእርግጥ አልለህ፡፡

وَإِنَّ لَكَ لَأَجۡرًا غَيۡرَ مَمۡنُونٖ ٣

4. አንተም በታላቅ ጠባይ ላይ ነህ፡፡

وَإِنَّكَ لَعَلَىٰ خُلُقٍ عَظِيمٖ ٤

5. ወደፊትም ታያለህ፤ ያያሉም፡፡

فَسَتُبۡصِرُ وَيُبۡصِرُونَ ٥

6. ዕብደት በማንኛችሁ እንዳልለ፡፡

بِأَييِّكُمُ ٱلۡمَفۡتُونُ ٦

7. ጌታህ እርሱ ከመንገዱ የተሳሳተውን ሰው ዐዋቂ ነው፡፡ እርሱም ተመሪዎቹን ዐዋቂ ነው፡፡

إِنَّ رَبَّكَ هُوَ أَعۡلَمُ بِمَن ضَلَّ عَن سَبِيلِهِۦ وَهُوَ أَعۡلَمُ بِٱلۡمُهۡتَدِينَ ٧

8. ለአስተባባዮችም አትታዝዙ፡፡

فَلَا تُطِعِ ٱلۡمُكَذِّبِينَ ٨

9. ብትመሳሰላቸውና ቢመሳሰሉህ ተመኙ፡፡

وَدُّواْ لَوۡ تُدۡهِنُ فَيُدۡهِنُونَ ٩

10. ወራዳንም ሁሉ አትታዘዝ፡፡

وَلَا تُطِعۡ كُلَّ حَلَّافٖ مَّهِينٍ ١٠

11. ሰውን አነዋሪንና በማሳበቅ ኼያጅን፡፡

هَمَّازٖ مَّشَّآءِۭ بِنَمِيمٖ ١١

12. ለበጎ ነገር በጣም ከልካይን፣ ወሰን አላፊን፣ ኃጢአተኛን፤

مَّنَّاعٖ لِّلۡخَيۡرِ مُعۡتَدٍ أَثِيمٍ ١٢

13. ልበ ደረቅን፣ ከዚህ በኋላ ዲቃላን (ሁሉ አትታዘዝ)፡፡

عُتُلِّۭ بَعۡدَ ذَٰلِكَ زَنِيمٍ ١٣

14. የገንዘብና የልጆች ባለቤት በመኾኑ (ያስተባብላል)፡፡

أَن كَانَ ذَا مَالٖ وَبَنِينَ ١٤

15. በእርሱ ላይ አንቀጾቻችን በሚነበቡ ጊዜ «የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ተረቶች ናቸው» ይላል፡፡

إِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِ ءَايَٰتُنَا قَالَ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٥

16. በአፍንጫው ላይ በእርግጥ (የሚነወርበት) ምልክት እናደርግበታለን፡፡

سَنَسِمُهُۥ عَلَى ٱلْخُرْطُومِ ﴿١٦﴾

17. እኛ የአትክልቲቱን ባለቤቶች እንደ ሞከርን (የመካን ሰዎች) ሞከርናቸው፡፡ ማልደው (ፍሬዋን) ሊለቅሟት በማሉ ጊዜ፡፡

إِنَّا بَلَوْنَٰهُمْ كَمَا بَلَوْنَآ أَصْحَٰبَ ٱلْجَنَّةِ إِذْ أَقْسَمُوا۟ لَيَصْرِمُنَّهَا مُصْبِحِينَ ﴿١٧﴾

18. (በመሓላቸው) አያስቀሩምም፡፡

وَلَا يَسْتَثْنُونَ ﴿١٨﴾

19. እነርሱ የተኙ ኾነውም ሳሉ ከጌታህ የኾነ ዟሪ በእርሷ ላይ ዞረባት፡፡

فَطَافَ عَلَيْهَا طَآئِفٌ مِّن رَّبِّكَ وَهُمْ نَآئِمُونَ ﴿١٩﴾

20. እንደ ሌሊት ጨለማም ኾና አነጋች፤ (ከሰለች)፡፡

فَأَصْبَحَتْ كَٱلصَّرِيمِ ﴿٢٠﴾

21. ያነጉም ኾነው ተጠራሩ፡፡

فَتَنَادَوْا۟ مُصْبِحِينَ ﴿٢١﴾

22. «ቆራጮች እንደ ኾናችሁ በእርሻችሁ ላይ ማልዱ» በማለት፡፡

أَنِ ٱغْدُوا۟ عَلَىٰ حَرْثِكُمْ إِن كُنتُمْ صَٰرِمِينَ ﴿٢٢﴾

23. እነርሱ የሚንሾካሾኩ ኾነው ኼዱም፡፡

فَٱنطَلَقُوا۟ وَهُمْ يَتَخَٰفَتُونَ ﴿٢٣﴾

24. ዛሬ በእናንተ ላይ ድኻ እንዳይገባት በማለት፡፡

أَن لَّا يَدْخُلَنَّهَا ٱلْيَوْمَ عَلَيْكُم مِّسْكِينٌ ﴿٢٤﴾

25. (ድኾችን) በመከልከልም ላይ (በሐሳባቸው) ቻዮች ኾነው ማለዱ፡፡

وَغَدَوْا۟ عَلَىٰ حَرْدٍ قَٰدِرِينَ ﴿٢٥﴾

26. (ተቃጥላ) ባዩዋትም ጊዜ «እኛ በእርግጥ ተሳሳቾች ነን» አሉ፡፡

فَلَمَّا رَأَوْهَا قَالُوٓا۟ إِنَّا لَضَآلُّونَ ﴿٢٦﴾

27. «ይልቁንም እኛ የተከለከልን ነን» አሉ፡፡

بَلْ نَحْنُ مَحْرُومُونَ ﴿٢٧﴾

28. ትክክለኛቸው «ለእናንተ አላህን ለምን አታጠሩም አላልኳችሁምን?» አላቸው፡፡

قَالَ أَوْسَطُهُمْ أَلَمْ أَقُل لَّكُمْ لَوْلَا تُسَبِّحُونَ ﴿٢٨﴾

29. «ጌታችን ጥራት ይገባው፡፡ እኛ በዳዮች ነበርን፤» አሉ፡፡

قَالُوا۟ سُبْحَٰنَ رَبِّنَآ إِنَّا كُنَّا ظَٰلِمِينَ ﴿٢٩﴾

30. የሚወቃቀሱም ኾነው ከፊሎቻቸው በከፊሉ ላይ መጡ፡፡

فَأَقْبَلَ بَعْضُهُمْ عَلَىٰ بَعْضٍ يَتَلَٰوَمُونَ ﴿٣٠﴾

31. «ዋ ጥፋታችን! እኛ ድንበር አላፊዎች ነበርን፤» አሉ፡፡

قَالُوا۟ يَٰوَيْلَنَآ إِنَّا كُنَّا طَٰغِينَ ﴿٣١﴾

32. «ጌታችን ከእርሷ የተሻለን (አትክልት) ሊለውጠን ይከጀላል፡፡ እኛ ወደ ጌታችን ከጃዮች ነን፤» (አሉ)፡፡

عَسَىٰ رَبُّنَآ أَن يُبْدِلَنَا خَيْرًا مِّنْهَآ إِنَّآ إِلَىٰ رَبِّنَا رَٰغِبُونَ ﴿٣٢﴾

33. ቅጣቱ እንደዚሁ ነው፡፡ የመጨረሻይቱም ዓለም ቅጣት ታላቅ ነው፡፡ የሚያውቁት በኾኑ ኖሮ (በተጠነቀቁ ነበር)፡፡

كَذَٰلِكَ ٱلۡعَذَابُۖ وَلَعَذَابُ ٱلۡأٓخِرَةِ أَكۡبَرُۚ لَوۡ كَانُواْ يَعۡلَمُونَ ٣٣

34. ለጥንቁቆቹ በጌታቸው ዘንድ መጠቀሚያ ገነቶች አሏቸው፡፡

إِنَّ لِلۡمُتَّقِينَ عِندَ رَبِّهِمۡ جَنَّٰتِ ٱلنَّعِيمِ ٣٤

35. ሙስሊሞቹን እንደ ከሓዲዎች እናደርጋለን?

أَفَنَجۡعَلُ ٱلۡمُسۡلِمِينَ كَٱلۡمُجۡرِمِينَ ٣٥

36. ለእናንተ ምን (አስረጅ) አላችሁ? እንዴት ትፈርዳላችሁ፡፡

مَا لَكُمۡ كَيۡفَ تَحۡكُمُونَ ٣٦

37. በእውነቱ ለእናንተ በእርሱ የምታጠኑበት መጽሐፍ አላችሁን?

أَمۡ لَكُمۡ كِتَٰبٞ فِيهِ تَدۡرُسُونَ ٣٧

38. በውስጡ ለእናንተ የምትመርጡት አላችሁ (የሚል)

إِنَّ لَكُمۡ فِيهِ لَمَا تَخَيَّرُونَ ٣٨

39. ወይስ ለእናንተ የምትፈርዱት አላችሁ በማለት (ቃል ኪዳን የገባንላችሁ) እስከ ትንሣኤ ቀን ደራሽ የኾኑ መሓላዎች ለእናንተ በእኛ ላይ አሏችሁን?

أَمۡ لَكُمۡ أَيۡمَٰنٌ عَلَيۡنَا بَٰلِغَةٌ إِلَىٰ يَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ إِنَّ لَكُمۡ لَمَا تَحۡكُمُونَ ٣٩

40. በዚህ ማንኛቸው ተያያዥ እንደ ኾነ ጠይቃቸው፡፡

سَلۡهُمۡ أَيُّهُم بِذَٰلِكَ زَعِيمٌ ٤٠

41. ወይስ ለእነርሱ (በፍርዳቸው ተስማሚ) «ተጋሪዎች» አሏቸውን? እውነተኞችም እንደኾኑ «ተጋሪዎቻቸውን» ያምጡ፡፡

أَمۡ لَهُمۡ شُرَكَآءُ فَلۡيَأۡتُواْ بِشُرَكَآئِهِمۡ إِن كَانُواْ صَٰدِقِينَ ٤١

42. ባት የሚገለጥበትን (ከሓዲዎች) ወደ መስገድም የሚጥጠሩበትንና የማይችሉበት ቀን (አስታውስ)፡፡

يَوۡمَ يُكۡشَفُ عَن سَاقٖ وَيُدۡعَوۡنَ إِلَى ٱلسُّجُودِ فَلَا يَسۡتَطِيعُونَ ٤٢

43. ዓይኖቻቸው የፈሩ ውርደት የምትሸፍናቸው ሲኾኑ፤ (ወደ ስግደት የሚጠሩበትን)፤ እነርሱም (በምድረ ዓለም) ደህና ኾነው ሳሉ ወደ ስግደት በእርግጥ ይጠሩ ነበሩ፡፡

خَٰشِعَةً أَبۡصَٰرُهُمۡ تَرۡهَقُهُمۡ ذِلَّةٞۖ وَقَدۡ كَانُواْ يُدۡعَوۡنَ إِلَى ٱلسُّجُودِ وَهُمۡ سَٰلِمُونَ ٤٣

44. በዚህም ንግግር ከሚያስተባብሉት ሰዎች ጋር ተዎኝ፡፡ (እነርሱን እኔ እበቃሃለሁ)፡፡ ከማያውቁት ስፍራ አዘናግተን እንይዛቸዋለን፡፡

فَذَرۡنِي وَمَن يُكَذِّبُ بِهَٰذَا ٱلۡحَدِيثِۖ سَنَسۡتَدۡرِجُهُم مِّنۡ حَيۡثُ لَا يَعۡلَمُونَ ٤٤

45. እነርሱንም አዘገያለሁ፡፡ ዘዴዬ ብርቱ ነውና፡፡

وَأُمۡلِي لَهُمۡۚ إِنَّ كَيۡدِي مَتِينٌ ٤٥

46. በእውነቱ ዋጋን ትጠይቃቸዋለህን? ስለዚህ እነርሱ ከዕዳ የተከበዱ ናቸውን?

أَمۡ تَسۡـَٔلُهُمۡ أَجۡرٗا فَهُم مِّن مَّغۡرَمٖ مُّثۡقَلُونَ ٤٦

47. ወይስ እነርሱ ዘንድ የሩቁ ምስጢር ዕውቀት አልለን? ስለዚህ እነርሱ ይጽፋሉን?

أَمۡ عِندَهُمُ ٱلۡغَيۡبُ فَهُمۡ يَكۡتُبُونَ ﴿٤٧﴾

48. ለጌታህም ፍርድ ታገሥ፤ (በመበሳጨትና ባለ መታገሥ) እንደ ዓሣው ባለቤትም (እንደ ዮናስ) አትኹን፡፡ እርሱ በጭንቀት የተመላ ኾኖ (ጌታውን) በተጣራ ጊዜ፡፡

فَٱصۡبِرۡ لِحُكۡمِ رَبِّكَ وَلَا تَكُن كَصَاحِبِ ٱلۡحُوتِ إِذۡ نَادَىٰ وَهُوَ مَكۡظُومٞ ﴿٤٨﴾

49. ከጌታው የኾነ ጸጋ ባላገኘው ኖሮ በምድረ በዳ ተወቃሽ ኾኖ በተጣለ ነበር፡፡

لَّوۡلَآ أَن تَدَٰرَكَهُۥ نِعۡمَةٞ مِّن رَّبِّهِۦ لَنُبِذَ بِٱلۡعَرَآءِ وَهُوَ مَذۡمُومٞ ﴿٤٩﴾

50. ጌታውም (በነቢይነት) መረጠው፡፡ ከደጋጎቹም አደረገው፡፡

فَٱجۡتَبَٰهُ رَبُّهُۥ فَجَعَلَهُۥ مِنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ﴿٥٠﴾

51. እነሆ እነዚያም የካዱት ሰዎች ቁርአኑን በሰሙ ጊዜ በዓይኖቻቸው ሊጥሉህ (ሊያጠፉህ) ይቀርባሉ፡፡ «እርሱም በእርግጥ ዕብድ ነው» ይላሉ፡፡

وَإِن يَكَادُ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَيُزۡلِقُونَكَ بِأَبۡصَٰرِهِمۡ لَمَّا سَمِعُواْ ٱلذِّكۡرَ وَيَقُولُونَ إِنَّهُۥ لَمَجۡنُونٞ ﴿٥١﴾

52. ግን እርሱ (ቁርኣን) ለዓለማት መገሰጫ እንጂ ሌላ አይደለም፡፡

وَمَا هُوَ إِلَّا ذِكۡرٞ لِّلۡعَٰلَمِينَ ﴿٥٢﴾

## ሱረቱ አል ሓቃህ

## سورة الحاقة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. እውነትን አረጋጋጪቱ (ትንሣኤ)፡፡

ٱلۡحَآقَّةُ ﴿١﴾

2. አረጋጋጪቱም (እርሷ) ምንድን ናት!

مَا ٱلۡحَآقَّةُ ﴿٢﴾

3. አረጋጋጪቱም ምን እንደኾነች ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا ٱلۡحَآقَّةُ ﴿٣﴾

4. ሰሙድና ዓድ በቆርቋሪይቱ (ትንሣኤ) አስተባበሉ፡፡

كَذَّبَتۡ ثَمُودُ وَعَادُۢ بِٱلۡقَارِعَةِ ﴿٤﴾

5. ሠሙድማ ወሰን በሌላት ጩኸት ተጠፉ፤ (ተወደሙ)፡፡

فَأَمَّا ثَمُودُ فَأُهۡلِكُواْ بِٱلطَّاغِيَةِ ﴿٥﴾

6. ዓድማ በኀይል በምትንሻሻ ብርቱ ነፋስ ተጠፉ፡፡

وَأَمَّا عَادٌ فَأُهۡلِكُواْ بِرِيحٖ صَرۡصَرٍ عَاتِيَةٖ ٦

7. ተከታታይ በኾኑ ሰባት ሌሊቶችና ስምንት መዓልቶች ውስጥ በእነርሱ ላይ ለቀቃት፡፡ ሕዝቦቹንም፤ በውስጧ የተጣሉ ኾነው ልክ ክፍት የኾኑ የዘንባባ ግንዶች መስለው ታያቸዋለህ፡፡

سَخَّرَهَا عَلَيۡهِمۡ سَبۡعَ لَيَالٖ وَثَمَٰنِيَةَ أَيَّامٍ حُسُومٗاۖ فَتَرَى ٱلۡقَوۡمَ فِيهَا صَرۡعَىٰ كَأَنَّهُمۡ أَعۡجَازُ نَخۡلٍ خَاوِيَةٖ ٧

8. ለእነርሱም ቀሪን ታያለህን?

فَهَلۡ تَرَىٰ لَهُم مِّنۢ بَاقِيَةٖ ٨

9. ፈርዖን ከበፊቱ የነበሩትም ሰዎች ተገልባጮቹም (ከተሞች) በኀጢአት (ሥራዎች) መጡ፡፡

وَجَآءَ فِرۡعَوۡنُ وَمَن قَبۡلَهُۥ وَٱلۡمُؤۡتَفِكَٰتُ بِٱلۡخَاطِئَةِ ٩

10. የጌታቸውንም መልእክተኛ ትዕዛዝ ጣሱ፡፡ የበረታችንም አያያዝ ያዛቸው፡፡

فَعَصَوۡاْ رَسُولَ رَبِّهِمۡ فَأَخَذَهُمۡ أَخۡذَةٗ رَّابِيَةً ١٠

11. እኛ ውሃው ባየለ ጊዜ በተንሻላይቱ ታንኳ ውስጥ ጫንናችሁ፡፡

إِنَّا لَمَّا طَغَا ٱلۡمَآءُ حَمَلۡنَٰكُمۡ فِي ٱلۡجَارِيَةِ ١١

12. ለእናንተ መገሰጫ ልናደርጋት አጥኚ የኾነችም ጆሮ ታጠናት ዘንድ፡፡

لِنَجۡعَلَهَا لَكُمۡ تَذۡكِرَةٗ وَتَعِيَهَآ أُذُنٞ وَٰعِيَةٞ ١٢

13. በቀንዱም አንዲት መንነፋት በተነፋች ጊዜ፡፡

فَإِذَا نُفِخَ فِي ٱلصُّورِ نَفۡخَةٞ وَٰحِدَةٞ ١٣

14. ምድርና ጋራዎችም (ከስፍራቸው) በተነሱና አንዲትን መሰባበር በተሰባበሩ ጊዜ፡፡

وَحُمِلَتِ ٱلۡأَرۡضُ وَٱلۡجِبَالُ فَدُكَّتَا دَكَّةٗ وَٰحِدَةٗ ١٤

15. በዚያ ቀን ኋኚቱ (ትንሣኤ) ትኾናለች፡፡

فَيَوۡمَئِذٖ وَقَعَتِ ٱلۡوَاقِعَةُ ١٥

16. ሰማይም ትቀደዳለች፡፡ ስለዚህ እርሷ በዚያ ቀን ደካማ ናት፡፡

وَٱنشَقَّتِ ٱلسَّمَآءُ فَهِيَ يَوۡمَئِذٖ وَاهِيَةٞ ١٦

17. መላእክትም በየጫፎችዋ ላይ ይኾናሉ፡፡ የጌታህንም ዐርሽ በዚያ ቀን ስምንት መላእክት ከበላያቸው ይሸከማሉ፡፡

وَٱلۡمَلَكُ عَلَىٰٓ أَرۡجَآئِهَاۚ وَيَحۡمِلُ عَرۡشَ رَبِّكَ فَوۡقَهُمۡ يَوۡمَئِذٖ ثَمَٰنِيَةٞ ١٧

18. በዚያ ቀን ከእናንተ ተደባቂ (ነገሮች) የማይደበቁ ሲኾኑ ትቅቀረባላችሁ፡፡

يَوۡمَئِذٖ تُعۡرَضُونَ لَا تَخۡفَىٰ مِنكُمۡ خَافِيَةٞ ١٨

19. መጽሐፉን በቀኙ የተሰጠ ሰውማ (ለጓደኞቹ) «እንኩ፤ መጽሐፌን አንብቡ» ይላል፡፡

فَأَمَّا مَنۡ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ بِيَمِينِهِۦ فَيَقُولُ هَآؤُمُ ٱقۡرَءُواْ كِتَٰبِيَهۡ ١٩

20. «እኔ ምርመራየን የምገናኝ መኾኔን አረጋገጥኩ፤» (ተዘጋጀሁም ይላል)፡፡

إِنِّي ظَنَنتُ أَنِّي مُلَٰقٍ حِسَابِيَهۡ ٢٠

21. እርሱም በተወደደች ኑሮ ውስጥ ይኾናል፡፡

فَهُوَ فِي عِيشَةٖ رَّاضِيَةٖ ٢١

22. በከፍተኛይቱ ገነት ውስጥ፡፡

فِي جَنَّةٍ عَالِيَةٖ ٢٢

23. ፍሬዎቿዋ ቅርቦች የኾኑ፡፡

قُطُوفُهَا دَانِيَةٞ ٢٣

24. በአለፉት ቀናት ውስጥ (በምድረ ዓለም) ባስቀደማችሁት ምክንያት ብሉ፤ ጠጡም፤ (ይባላሉ)፡፡

كُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ هَنِيٓـَٔۢا بِمَآ أَسۡلَفۡتُمۡ فِي ٱلۡأَيَّامِ ٱلۡخَالِيَةِ ٢٤

25. መጽሐፉንም በግራው የተሰጠማ «ዋ ጥፋቴ! ምነው መጽሐፌን ባልተሰጠሁ» ይላል፡፡

وَأَمَّا مَنۡ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ بِشِمَالِهِۦ فَيَقُولُ يَٰلَيۡتَنِي لَمۡ أُوتَ كِتَٰبِيَهۡ ٢٥

26. «ምርመራየንም ምን እንደኾነ ባላወቅኩ፡፡

وَلَمۡ أَدۡرِ مَا حِسَابِيَهۡ ٢٦

27. «እርሷ (ሞት ሕይወቴን) ምነው ፈጻሚ በኾነች፡፡

يَٰلَيۡتَهَا كَانَتِ ٱلۡقَاضِيَةَ ٢٧

28. «ገንዘቤ ከእኔ ምንንም አላብቃቃኝ፤ (አልጠቀመኝም)፡፡

مَآ أَغۡنَىٰ عَنِّي مَالِيَهۡۜ ٢٨

29. «ኀይሌ ከእኔ ላይ ጠፋ» (ይላል)፡፡

هَلَكَ عَنِّي سُلۡطَٰنِيَهۡ ٢٩

30. «ያዙት፤ እሰሩትም፡፡

خُذُوهُ فَغُلُّوهُ ٣٠

31. «ከዚያም በእሳት ውስጥ አግቡት፡፡

ثُمَّ ٱلۡجَحِيمَ صَلُّوهُ ٣١

32. «ከዚያም ርዝመቷ ሰባ ክንድ በኾነች ሰንሰለት ውስጥ አግቡት፡፡»

ثُمَّ فِي سِلۡسِلَةٖ ذَرۡعُهَا سَبۡعُونَ ذِرَاعٗا فَٱسۡلُكُوهُ ٣٢

33. እርሱ ታላቅ በኾነው አላህ አያምንም ነበርና፡፡

إِنَّهُۥ كَانَ لَا يُؤۡمِنُ بِٱللَّهِ ٱلۡعَظِيمِ ٣٣

34. ድኾችንም በማብላት ላይ አያግባባም ነበርና፡፡

وَلَا يَحُضُّ عَلَىٰ طَعَامِ ٱلۡمِسۡكِينِ ٣٤

35. ለእርሱም ዛሬ እዚህ ዘመድ የለውም፡፡

فَلَيۡسَ لَهُ ٱلۡيَوۡمَ هَٰهُنَا حَمِيمٞ ٣٥

36. ምግብም ከእሳት ሰዎች ቁስል እጣቢ (እዥ) በስተቀር የለውም፡፡

وَلَا طَعَامٌ إِلَّا مِنۡ غِسۡلِينٖ ٣٦

37. ኀጢአተኞች እንጅ ሌላ አይበላውም፤ (ይባላል)፡፡

لَّا يَأۡكُلُهُۥٓ إِلَّا ٱلۡخَٰطِـُٔونَ ٣٧

38. በምታዩትም ነገር እምላለሁ፡፡

فَلَآ أُقۡسِمُ بِمَا تُبۡصِرُونَ ٣٨

39. በማታዩትም ነገር፡፡

40. እርሱ (ቁርኣን) የተከበረ መልክተኛ ቃል ነው፡፡

41. እርሱም የባለቅኔ ቃል (ግጥም) አይደለም፡፡ ጥቂትን ብቻ ታምናላችሁ፡፡

42. የጠንቋይም ቃል አይደለም፡፡ ጥቂትን ብቻ ታስታውሳላችሁ፡፡

43. ከዓለማት ጌታ የተወረደ ነው፡፡

44. በእኛ ላይም ከፊልን ቃላት (ያላልነውን) በቀጠፈ ኖሮ፤

45. በኀይል በያዝነው ነበር፡፡

46. ከዚያም ከእርሱ የልቡን ሥር (የተንጠለጠለበትን ጅማት) በቆረጥን ነበር፡፡

47. ከእናንተም ውስጥ ከእርሱ ላይ ከልካዮች ምንም አይኖሩም፡፡

48. እርሱም (ቁርኣን) ለጥንቁቆቹ መገሠጫ ነው፡፡

49. እኛም ከእናንተ ውስጥ አስተባባዮች መኖራቸውን በእርግጥ እናውቃለን፡፡

50. እርሱም (ቁርኣን) በከሓዲዎቹ ላይ ጸጸት ነው፡፡

51. እርሱም የተረጋገጠ እውነት ነው፡፡

52. የታላቁን ጌታህንም ስም አወድስ፡፡

وَمَا لَا تُبۡصِرُونَ ﴿٣٩﴾

إِنَّهُۥ لَقَوۡلُ رَسُولٖ كَرِيمٖ ﴿٤٠﴾

وَمَا هُوَ بِقَوۡلِ شَاعِرٖۚ قَلِيلٗا مَّا تُؤۡمِنُونَ ﴿٤١﴾

وَلَا بِقَوۡلِ كَاهِنٖۚ قَلِيلٗا مَّا تَذَكَّرُونَ ﴿٤٢﴾

تَنزِيلٞ مِّن رَّبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٤٣﴾

وَلَوۡ تَقَوَّلَ عَلَيۡنَا بَعۡضَ ٱلۡأَقَاوِيلِ ﴿٤٤﴾

لَأَخَذۡنَا مِنۡهُ بِٱلۡيَمِينِ ﴿٤٥﴾

ثُمَّ لَقَطَعۡنَا مِنۡهُ ٱلۡوَتِينَ ﴿٤٦﴾

فَمَا مِنكُم مِّنۡ أَحَدٍ عَنۡهُ حَٰجِزِينَ ﴿٤٧﴾

وَإِنَّهُۥ لَتَذۡكِرَةٞ لِّلۡمُتَّقِينَ ﴿٤٨﴾

وَإِنَّا لَنَعۡلَمُ أَنَّ مِنكُم مُّكَذِّبِينَ ﴿٤٩﴾

وَإِنَّهُۥ لَحَسۡرَةٌ عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ ﴿٥٠﴾

وَإِنَّهُۥ لَحَقُّ ٱلۡيَقِينِ ﴿٥١﴾

فَسَبِّحۡ بِٱسۡمِ رَبِّكَ ٱلۡعَظِيمِ ﴿٥٢﴾

# ሱረቱ አል መዓሪጅ

# سورة المعارج

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ወዳቂ ከኾነው ቅጣት ጠያቂ ጠየቀ::

سَأَلَ سَآئِلُۢ بِعَذَابٖ وَاقِعٖ ﴿١﴾

2. በከሓዲዎች ላይ (ወዳቂ ከኾነው) ለእርሱ መላሽ የለውም::

لِّلۡكَٰفِرِينَ لَيۡسَ لَهُۥ دَافِعٞ ﴿٢﴾

3. የ(ሰማያት) መሰላሎች ባለቤት ከኾነው አላህ (መላሽ የለውም)::

مِّنَ ٱللَّهِ ذِي ٱلۡمَعَارِجِ ﴿٣﴾

4. መላእክቱና መንፈሱም ልኩ አምሳ ሺሕ ዓመት በኾነ ቀን ውስጥ ወደእርሱ ያርጋሉ፤ (ይወጣሉ)::

تَعۡرُجُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ وَٱلرُّوحُ إِلَيۡهِ فِي يَوۡمٖ كَانَ مِقۡدَارُهُۥ خَمۡسِينَ أَلۡفَ سَنَةٖ ﴿٤﴾

5. መልካምንም ትዕግስት ታገሥ::

فَٱصۡبِرۡ صَبۡرٗا جَمِيلًا ﴿٥﴾

6. እነርሱ (ያንን ቀን) ሩቅ አድርገው ያዩታል::

إِنَّهُمۡ يَرَوۡنَهُۥ بَعِيدٗا ﴿٦﴾

7. እኛም ቅርብ ኾኖ እናየዋለን::

وَنَرَىٰهُ قَرِيبٗا ﴿٧﴾

8. ሰማይ እንደ ዘይት አተላ በምትኾንበት ቀን::

يَوۡمَ تَكُونُ ٱلسَّمَآءُ كَٱلۡمُهۡلِ ﴿٨﴾

9. ጋራዎችም በተለያዩ ቀለማት እንደ ተነከረ ሱፍ (ነፋስ እንደሚያበረው) በሚኾኑበት ቀን::

وَتَكُونُ ٱلۡجِبَالُ كَٱلۡعِهۡنِ ﴿٩﴾

10. ዘመድም ዘመድን በማይጠይቅበት ቀን፤ (መላሽ የለውም)::

وَلَا يَسۡـَٔلُ حَمِيمٌ حَمِيمٗا ﴿١٠﴾

11. (ዘመዶቻቸውን) ያዩዋቸዋል:: አመጸኛው ከዚያ ቀን ስቃይ (ነፍሱን) በልጆቹ ሊበዠ ይመኛል::

يُبَصَّرُونَهُمۡۚ يَوَدُّ ٱلۡمُجۡرِمُ لَوۡ يَفۡتَدِي مِنۡ عَذَابِ يَوۡمِئِذِۭ بِبَنِيهِ ﴿١١﴾

12. በሚስቱም በወንድሙም::

وَصَٰحِبَتِهِۦ وَأَخِيهِ ﴿١٢﴾

13. በዚያችም በምታስጠጋው ጎሳው::

وَفَصِيلَتِهِ ٱلَّتِي تُـٔۡوِيهِ ﴿١٣﴾

14. በምድርም ላይ ባለው ሁሉ (ሊበዠ) ከዚያም ሊያድነው (ይመኛል)::

وَمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ جَمِيعٗا ثُمَّ يُنجِيهِ ﴿١٤﴾

15. ይተው! እርሷ (እሳቲቱ) ለዟ ናት፡፡

كَلَّآۖ إِنَّهَا لَظَىٰ ١٥

16. የራስን ቅል ቆዳ የምትሞሽልቅ ስትኾን፡፡

نَزَّاعَةً لِّلشَّوَىٰ ١٦

17. (ከእምነት) የዞረንና የሸሸን ሰው (ወደእርሷ) ትጠራለች፡፡

تَدۡعُواْ مَنۡ أَدۡبَرَ وَتَوَلَّىٰ ١٧

18. ገንዘብን የሰበሰበንና (ዘካውን ሳይሰጥ) የቆጠረንም፤ (ትጠራለች)፡፡

وَجَمَعَ فَأَوۡعَىٰٓ ١٨

19. ሰው ቅጠ ቢስ ኾኖ ተፈጠረ፡፡

۞إِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ خُلِقَ هَلُوعًا ١٩

20. ክፉ ነገር ባገኘው ጊዜ ብስጪተኛ፡፡

إِذَا مَسَّهُ ٱلشَّرُّ جَزُوعًا ٢٠

21. መልካምም ነገር (ድሎት) ባገኘ ጊዜ ከልካይ (ኾኖ ተፈጠረ)፡፡

وَإِذَا مَسَّهُ ٱلۡخَيۡرُ مَنُوعًا ٢١

22. ሰጋጆቹ ብቻ ሲቀሩ፡፡

إِلَّا ٱلۡمُصَلِّينَ ٢٢

23. እነዚያ እነርሱ በስግደታቸው ላይ ዘውታሪዎች የኾኑት፡፡

ٱلَّذِينَ هُمۡ عَلَىٰ صَلَاتِهِمۡ دَآئِمُونَ ٢٣

24. እነዚያም በገንዘቦቻቸው ላይ የታወቀ መብት ያለባቸው የኾኑት፡፡

وَٱلَّذِينَ فِيٓ أَمۡوَٰلِهِمۡ حَقّٞ مَّعۡلُومٞ ٢٤

25. ለለማኝ ከልመና ለሚከለከልም (መብት ያለባቸው የኾኑት)፡፡

لِّلسَّآئِلِ وَٱلۡمَحۡرُومِ ٢٥

26. እነዚያም በፍርዱ ቀን እውነት የሚሉት (የሚያረጋግጡት)፡፡

وَٱلَّذِينَ يُصَدِّقُونَ بِيَوۡمِ ٱلدِّينِ ٢٦

27. እነዚያም እነርሱ ከጌታቸው ቅጣት ፈሪዎች የኾኑት፡፡

وَٱلَّذِينَ هُم مِّنۡ عَذَابِ رَبِّهِم مُّشۡفِقُونَ ٢٧

28. የጌታቸው ቅጣት (መምጣቱ) የማያስተማምን ነውና፡፡

إِنَّ عَذَابَ رَبِّهِمۡ غَيۡرُ مَأۡمُونٖ ٢٨

29. እነዚያም እነርሱ ብልቶቻቸውን ጠባቂዎች የኾኑት፡፡

وَٱلَّذِينَ هُمۡ لِفُرُوجِهِمۡ حَٰفِظُونَ ٢٩

30. በሚስቶቻቸው ወይም እጆቻቸው በያዙዋቸው (ባሪያዎች) ላይ ሲቀር፡፡ እነርሱ (በእነዚህ) የማይወቀሱ ናቸውና፡፡

إِلَّا عَلَىٰٓ أَزۡوَٰجِهِمۡ أَوۡ مَا مَلَكَتۡ أَيۡمَٰنُهُمۡ فَإِنَّهُمۡ غَيۡرُ مَلُومِينَ ٣٠

31. ከዚያም ወዲያ የፈለገ ሰው እነዚያ እነሱ ድንበር አላፊዎች ናቸው፡፡

فَمَنِ ٱبۡتَغَىٰ وَرَآءَ ذَٰلِكَ فَأُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡعَادُونَ ٣١

32. እነዚያም እነርሱ አደራዎቻቸውንና ቃል ኪዳናቸውን ጠባቂዎች የኾኑት::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ لِأَمَٰنَٰتِهِمۡ وَعَهۡدِهِمۡ رَٰعُونَ ﴿٣٢﴾

33. እነዚያም እነርሱ በምስክርነታቸው ትክክለኞች የኾኑት::

وَٱلَّذِينَ هُم بِشَهَٰدَٰتِهِمۡ قَآئِمُونَ ﴿٣٣﴾

34. እነዚያም እነርሱ በሶላቶቻቸው ላይ የሚጠባበቁት::

وَٱلَّذِينَ هُمۡ عَلَىٰ صَلَاتِهِمۡ يُحَافِظُونَ ﴿٣٤﴾

35. እነዚህ (ከዚህ በላይ የተወሱት ሁሉ) በገነቶች ውስጥ የሚከበሩ ናቸው::

أُوْلَٰٓئِكَ فِي جَنَّٰتٖ مُّكۡرَمُونَ ﴿٣٥﴾

36. ለእነዚያም ለካዱት ወደ አንተ በኩል አንገቶቻቸውን መዝዘው የሚያተኩሩት ምን አላቸው?

فَمَالِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ قِبَلَكَ مُهۡطِعِينَ ﴿٣٦﴾

37. ከቀኝና ከግራ ክፍልፍል ጭፍሮች ሲኾኑ::

عَنِ ٱلۡيَمِينِ وَعَنِ ٱلشِّمَالِ عِزِينَ ﴿٣٧﴾

38. ከእነርሱ እያንዳንዱ ሰው የጸጋይቱን ገነት መግባትን ይከጀላልን?

أَيَطۡمَعُ كُلُّ ٱمۡرِيٕٖ مِّنۡهُمۡ أَن يُدۡخَلَ جَنَّةَ نَعِيمٖ ﴿٣٨﴾

39. ይከልከል፤ እኛ ከሚያውቁት ነገር (ከፍቶት ጠብታ) ፈጠርናቸው::

كَلَّآۖ إِنَّا خَلَقۡنَٰهُم مِّمَّا يَعۡلَمُونَ ﴿٣٩﴾

40. በምሥራቆችና በምዕራቦችም ጌታ እምላለሁ:: እኛ በእርግጥ ቻዮች ነን::

فَلَآ أُقۡسِمُ بِرَبِّ ٱلۡمَشَٰرِقِ وَٱلۡمَغَٰرِبِ إِنَّا لَقَٰدِرُونَ ﴿٤٠﴾

41. ከእነርሱ የተሻለን በመለወጥ ላይ:: እኛም ተሸናፊዎች አይደለንም::

عَلَىٰٓ أَن نُّبَدِّلَ خَيۡرٗا مِّنۡهُمۡ وَمَا نَحۡنُ بِمَسۡبُوقِينَ ﴿٤١﴾

42. ያንንም የሚስፈራሩበትን ቀናቸውን እስከሚገናኙ ድረስ ተዋቸው:: ይዋኙ ይጫወቱም::

فَذَرۡهُمۡ يَخُوضُواْ وَيَلۡعَبُواْ حَتَّىٰ يُلَٰقُواْ يَوۡمَهُمُ ٱلَّذِي يُوعَدُونَ ﴿٤٢﴾

43. ወደ ጣዖቶች እንደሚሽቀዳደሙ ኾነው ከመቃብሮቻቸው ፈጥነው የሚወጡበትን ቀን (እስከሚገናኙ ድረስ ተዋቸው)::

يَوۡمَ يَخۡرُجُونَ مِنَ ٱلۡأَجۡدَاثِ سِرَاعٗا كَأَنَّهُمۡ إِلَىٰ نُصُبٖ يُوفِضُونَ ﴿٤٣﴾

44. ዓይኖቻቸው ያፈሩ ኾነው ውርደት ትሸፍናቸዋለች:: ይህ ቀን ያ ይስፈራሩበት የነበሩት ነው::

خَٰشِعَةً أَبۡصَٰرُهُمۡ تَرۡهَقُهُمۡ ذِلَّةٞۚ ذَٰلِكَ ٱلۡيَوۡمُ ٱلَّذِي كَانُواْ يُوعَدُونَ ﴿٤٤﴾




በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. እኛ ኑሕን «ሕዝቦችህን አሳማሚ ቅጣት ሳይመጣባቸው በፊት አስጠንቅቅ በማለት ወደ ሕዝቦቹ ላክነው::»

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَا نُوحًا إِلَىٰ قَوۡمِهِۦٓ أَنۡ أَنذِرۡ قَوۡمَكَ مِن قَبۡلِ أَن يَأۡتِيَهُمۡ عَذَابٌ أَلِيمٞ ١

2. (እርሱም) አለ «ሕዝቦቼ ሆይ! እኔ ለእናንተ ገላጭ የኾንኩ አስጠንቃቂ ነኝ::

قَالَ يَٰقَوۡمِ إِنِّي لَكُمۡ نَذِيرٞ مُّبِينٌ ٢

3. «አላህን ተገዙት፣ ፍሩትም፣ ታዘዙኝም በማለት፤ (አስጠንቃቂ ነኝ)::

أَنِ ٱعۡبُدُواْ ٱللَّهَ وَٱتَّقُوهُ وَأَطِيعُونِ ٣

4. «ለእናንተ ከኀጢአቶቻችሁ ይምራልና:: ወደተወሰነው ጊዜም ያቆያችኋል:: የአላህ (የወሰነው) ጊዜ በመጣ ወቅት አይቆይም:: የምታውቁት ብትኾኑ ኖሮ (በታዘዛችሁ ነበር)::»

يَغۡفِرۡ لَكُم مِّن ذُنُوبِكُمۡ وَيُؤَخِّرۡكُمۡ إِلَىٰٓ أَجَلٖ مُّسَمًّىۚ إِنَّ أَجَلَ ٱللَّهِ إِذَا جَآءَ لَا يُؤَخَّرُۚ لَوۡ كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ٤

5. (ስለ ተቃውሙትም) «አለ ጌታዬ ሆይ! እኔ ሌሊትም ቀንም ሕዝቦቼን ጠራሁ::

قَالَ رَبِّ إِنِّي دَعَوۡتُ قَوۡمِي لَيۡلٗا وَنَهَارٗا ٥

6. «ጥሪየም መሸሸን እንጅ ሌላ አልጨመረላቸውም::

فَلَمۡ يَزِدۡهُمۡ دُعَآءِيٓ إِلَّا فِرَارٗا ٦

7. «እኔም ለእነርሱ ትምር ዘንድ (ወደ እምነት) በጠራኋቸው ቁጥር ጣቶቻቸውን በጆሮዎቻቸው ውስጥ አደረጉ:: ልብሶቻቸውንም ተከናነቡ:: (በመጥፎ ሥራቸው ላይ) ዘወተሩም:: (ያለ ልክ) መኩራትንም ኮሩ::

وَإِنِّي كُلَّمَا دَعَوۡتُهُمۡ لِتَغۡفِرَ لَهُمۡ جَعَلُوٓاْ أَصَٰبِعَهُمۡ فِيٓ ءَاذَانِهِمۡ وَٱسۡتَغۡشَوۡاْ ثِيَابَهُمۡ وَأَصَرُّواْ وَٱسۡتَكۡبَرُواْ ٱسۡتِكۡبَارٗا ٧

8. «ከዚያም እኔ በጩኸት ጠራኋቸው::

ثُمَّ إِنِّي دَعَوۡتُهُمۡ جِهَارٗا ٨

9. «ከዚያም እኔ ለእነርሱ ገለጽኩ:: ለእነርሱም መመስጠርን መሰጠርኩ

ثُمَّ إِنِّيٓ أَعۡلَنتُ لَهُمۡ وَأَسۡرَرۡتُ لَهُمۡ إِسۡرَارٗا ٩

10. «አልኳቸውም:- ጌታችሁን ምሕረትን ለምኑት:: እርሱ በጣም መሐሪ ነውና::

فَقُلۡتُ ٱسۡتَغۡفِرُواْ رَبَّكُمۡ إِنَّهُۥ كَانَ غَفَّارٗا ١٠

11. «በእናንተ ላይ ዝናምን ተከታታይ አድርጎ ይልካል::

يُرۡسِلِ ٱلسَّمَآءَ عَلَيۡكُم مِّدۡرَارٗا ١١

12. «በገንዘቦችና በልጆችም ይለግሰላችኋል፡፡ ለእናንተም አትክልቶችን ያደርግላችኋል፡፡ ለእናንተም ወንዞችን ያደርግላችኋል፡፡»

وَيُمۡدِدۡكُم بِأَمۡوَٰلٖ وَبَنِينَ وَيَجۡعَل لَّكُمۡ جَنَّٰتٖ وَيَجۡعَل لَّكُمۡ أَنۡهَٰرٗا ١٢

13. ለአላህ ልቅናን የማትሹት ለእናንተ ምን አላችሁ?

مَّا لَكُمۡ لَا تَرۡجُونَ لِلَّهِ وَقَارٗا ١٣

14. በልዩ ልዩ ኹኔታዎች በእርግጥ የፈጠራችሁ ሲኾን፡፡

وَقَدۡ خَلَقَكُمۡ أَطۡوَارًا ١٤

15. አላህ ሰባትን ሰማያት አንዱ ካንዱ በላይ ሲኾን እንዴት እንደፈጠረ አታዩምን?

أَلَمۡ تَرَوۡاْ كَيۡفَ خَلَقَ ٱللَّهُ سَبۡعَ سَمَٰوَٰتٖ طِبَاقٗا ١٥

16. በውስጣቸውም ጨረቃን አብሪ አደረገ፡፡ ፀሐይንም ብርሃን አደረገ፡፡

وَجَعَلَ ٱلۡقَمَرَ فِيهِنَّ نُورٗا وَجَعَلَ ٱلشَّمۡسَ سِرَاجٗا ١٦

17. አላህም ከምድር ማብቀልን አበቀላችሁ፡፡

وَٱللَّهُ أَنۢبَتَكُم مِّنَ ٱلۡأَرۡضِ نَبَاتٗا ١٧

18. ከዚያም በውስጧ ይመልሳችኋል፡፡ ማውጣትንም ያወጣችኋል፡፡

ثُمَّ يُعِيدُكُمۡ فِيهَا وَيُخۡرِجُكُمۡ إِخۡرَاجٗا ١٨

19. አላህም ምድርን ለእናንተ ምንጣፍ አደረጋት፡፡

وَٱللَّهُ جَعَلَ لَكُمُ ٱلۡأَرۡضَ بِسَاطٗا ١٩

20. ከእርሷ ሰፋፊዎችን መንገዶች ትገቡ ዘንድ፡፡

لِّتَسۡلُكُواْ مِنۡهَا سُبُلٗا فِجَاجٗا ٢٠

21. ኑሕ አለ፡- «ጌታዬ ሆይ! እነሱ አምመጹብኝ፡፡ ገንዘቡና ልጁም ከጥፋት በስተቀር ያልጨመረለትን ሰው ተከተሉ፡፡

قَالَ نُوحٞ رَّبِّ إِنَّهُمۡ عَصَوۡنِي وَٱتَّبَعُواْ مَن لَّمۡ يَزِدۡهُ مَالُهُۥ وَوَلَدُهُۥٓ إِلَّا خَسَارٗا ٢١

22. «ታላቅንም ተንኮል የመከሩትን ሰዎች» (ተከተሉ)፡፡

وَمَكَرُواْ مَكۡرٗا كُبَّارٗا ٢٢

23. አሉም «አምላኮቻችሁን አትተዉ፡፡ ወድንም፣ ሱዋዕንም፣ የጉሥንም፣ የዑቅንም ነስርንም አትተው፡፡

وَقَالُواْ لَا تَذَرُنَّ ءَالِهَتَكُمۡ وَلَا تَذَرُنَّ وَدّٗا وَلَا سُوَاعٗا وَلَا يَغُوثَ وَيَعُوقَ وَنَسۡرٗا ٢٣

24. «በእርግጥም ብዙዎችን አሳሳቱ፡፡ ከሓዲዎችንም ጥመትን እንጅ ሌላን አትጨምርላቸው» (አለ)፡፡

وَقَدۡ أَضَلُّواْ كَثِيرٗاۖ وَلَا تَزِدِ ٱلظَّٰلِمِينَ إِلَّا ضَلَٰلٗا ٢٤

25. በኃጢአቶቻቸው ምክንያት ተሰጠሙ፡፡ እሳትንም እንዲገቡ ተደረጉ፡፡ ለእነርሱም ከአላህ ሌላ የኾኑ ረዳቶችን አላገኙም፡፡

مِّمَّا خَطِيٓـَٰٔتِهِمۡ أُغۡرِقُواْ فَأُدۡخِلُواْ نَارٗا فَلَمۡ يَجِدُواْ لَهُم مِّن دُونِ ٱللَّهِ أَنصَارٗا ٢٥

26. ኑሕም አለ «ጌታዬ ሆይ! ከከሓዲዎቹ በምድር ላይ አንድንም አትተው፡፡

وَقَالَ نُوحٞ رَّبِّ لَا تَذَرۡ عَلَى ٱلۡأَرۡضِ مِنَ ٱلۡكَٰفِرِينَ دَيَّارًا ٢٦

27. «አንተ ብትተዋቸው ባሮችህን ያሳስታሉና፡፡ ኀጢአተኛ ከሓዲንም እንጅ ሌላን አይወልዱም፡፡

إِنَّكَ إِن تَذَرۡهُمۡ يُضِلُّواْ عِبَادَكَ وَلَا يَلِدُوٓاْ إِلَّا فَاجِرٗا كَفَّارٗا ﴿٢٧﴾

28. «ጌታዬ ሆይ! ለእኔም ለወላጆቼም ምእመን ኾኖ በቤቴ ለገባም ሰው ሁሉ ለምእመናንና ለምእምናትም ምሕረት አድርግ፡፡ ከሓዲዎችንም ከጥፋት በቀር አትጨምርላቸው፤» (አለ)፡፡

رَّبِّ ٱغۡفِرۡ لِي وَلِوَٰلِدَيَّ وَلِمَن دَخَلَ بَيۡتِيَ مُؤۡمِنٗا وَلِلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِۖ وَلَا تَزِدِ ٱلظَّٰلِمِينَ إِلَّا تَبَارَۢا ﴿٢٨﴾

# ሱረቱ አል ጂን

# سورة الجن

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. (ሙሐመድ ሆይ!) በል «እነሆ ከጂን የኾኑ ጭፈሮች (ቁርኣንን) አዳመጡ፡፡‹እኛ አስደናቂ የኾነን ቁርኣን ሰማንም› አሉ ማለት ወደእኔ ተወረደ፡፡

قُلۡ أُوحِيَ إِلَيَّ أَنَّهُ ٱسۡتَمَعَ نَفَرٞ مِّنَ ٱلۡجِنِّ فَقَالُوٓاْ إِنَّا سَمِعۡنَا قُرۡءَانًا عَجَبٗا ﴿١﴾

2. ‹ወደ ቀጥታ መንገድ የሚመራን (ቁርአን ሰማን)፡፡ በእርሱም አመንን፡፡ በጌታችንም አንድንም አናጋራም፡፡›

يَهۡدِيٓ إِلَى ٱلرُّشۡدِ فَـَٔامَنَّا بِهِۦۖ وَلَن نُّشۡرِكَ بِرَبِّنَآ أَحَدٗا ﴿٢﴾

3. ‹እነሆም የጌታችን ክብር ላቀ፡፡ ሚስትንም ልጅንም አልያዘም፡፡›

وَأَنَّهُۥ تَعَٰلَىٰ جَدُّ رَبِّنَا مَا ٱتَّخَذَ صَٰحِبَةٗ وَلَا وَلَدٗا ﴿٣﴾

4. ‹እነሆም ቂላችን በአላህ ላይ ወሰን ያለፈን (ውሸት) ይናገር ነበር፡፡›

وَأَنَّهُۥ كَانَ يَقُولُ سَفِيهُنَا عَلَى ٱللَّهِ شَطَطٗا ﴿٤﴾

5. ‹እኛም ሰዎችና ጋኔኖች በአላህ ላይ ውሸትን (ቃል) አይናገሩም ማለትን ጠረጠርን፡፡›

وَأَنَّا ظَنَنَّآ أَن لَّن تَقُولَ ٱلۡإِنسُ وَٱلۡجِنُّ عَلَى ٱللَّهِ كَذِبٗا ﴿٥﴾

6. ‹እነሆም ከሰዎች የኾኑ ወንዶች በጋኔን ወንዶች ይጠበቁ ነበሩ፡፡ ኩራትንም ጨመሩዋቸው፡፡›

وَأَنَّهُۥ كَانَ رِجَالٞ مِّنَ ٱلۡإِنسِ يَعُوذُونَ بِرِجَالٖ مِّنَ ٱلۡجِنِّ فَزَادُوهُمۡ رَهَقٗا ﴿٦﴾

7. ‹እነርሱም አላህ አንድንም አይቀሰቅስም ማለትን እንደጠረጠራችሁ ጠረጠሩ፡፡›

وَأَنَّهُمۡ ظَنُّواْ كَمَا ظَنَنتُمۡ أَن لَّن يَبۡعَثَ ٱللَّهُ أَحَدٗا ﴿٧﴾

8. ‹እኛም ሰማይን (ለመድረስ) ፈለግን፡፡ ብርቱ ጠባቂዎችንና ችቦዎችንም ተሞልታ አገኘናት፡፡

وَأَنَّا لَمَسۡنَا ٱلسَّمَآءَ فَوَجَدۡنَٰهَا مُلِئَتۡ حَرَسٗا شَدِيدٗا وَشُهُبٗا ﴿٨﴾

9. ‹እኛም ከእርሷ (ወሬን) ለማዳመጥ በመቀመጫዎች እንቀመጥ ነበርን፡፡ አሁን ግን የሚያዳምጥ ሰው ለእርሱ ተጠባባቂ ችቦን ያገኛል፡፡

وَأَنَّا كُنَّا نَقۡعُدُ مِنۡهَا مَقَٰعِدَ لِلسَّمۡعِۖ فَمَن يَسۡتَمِعِ ٱلۡأٓنَ يَجِدۡ لَهُۥ شِهَابٗا رَّصَدٗا ٩

10. ‹እኛም በምድር ውስጥ ባሉ ሰዎች ክፉ ተሺቷል? ወይስ በእነርሱ ጌታቸው ደግን ነገር ሺቷል? ማለትን አናውቅም፡፡

وَأَنَّا لَا نَدۡرِيٓ أَشَرٌّ أُرِيدَ بِمَن فِي ٱلۡأَرۡضِ أَمۡ أَرَادَ بِهِمۡ رَبُّهُمۡ رَشَدٗا ١٠

11. ‹እኛም ከእኛ ውስጥ ደጎች አሉሉ፡፡ ከኛም ከዚህ ሌላ የኾኑ አሉሉ፡፡ የተለያዩ መንገዶች (ባለ ቤቶች) ነበርን፡፡

وَأَنَّا مِنَّا ٱلصَّٰلِحُونَ وَمِنَّا دُونَ ذَٰلِكَۖ كُنَّا طَرَآئِقَ قِدَدٗا ١١

12. ‹እኛም አላህን በምድር ውስጥ ፈጽሞ የማናቅተው፤ ሸሽተንም ፈጽሞ የማናመልጠው መኾናችንን አረጋገጥን፡፡

وَأَنَّا ظَنَنَّآ أَن لَّن نُّعۡجِزَ ٱللَّهَ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَلَن نُّعۡجِزَهُۥ هَرَبٗا ١٢

13. ‹እኛም መሪውን በሰማን ጊዜ በርሱ አመንን፡፡ በጌታውም የሚያምን ሰው መግጎደልንም መጭጨመርንም አይፈራም፡፡

وَأَنَّا لَمَّا سَمِعۡنَا ٱلۡهُدَىٰٓ ءَامَنَّا بِهِۦۖ فَمَن يُؤۡمِنۢ بِرَبِّهِۦ فَلَا يَخَافُ بَخۡسٗا وَلَا رَهَقٗا ١٣

14. «እኛም ከእኛ ውስጥ ሙስሊሞች አሉሉ፡፡ ከእኛም ውስጥ በዳዮች አሉሉ፡፡ የሰለሙም ሰዎች እነዚያ ቅንን መንገድ መረጡ፡፡»

وَأَنَّا مِنَّا ٱلۡمُسۡلِمُونَ وَمِنَّا ٱلۡقَٰسِطُونَۖ فَمَنۡ أَسۡلَمَ فَأُوْلَٰٓئِكَ تَحَرَّوۡاْ رَشَدٗا ١٤

15. በዳዮቹማ ለገሀነም ማገዶ ኾኑ፡፡

وَأَمَّا ٱلۡقَٰسِطُونَ فَكَانُواْ لِجَهَنَّمَ حَطَبٗا ١٥

16. እነሆም በመንገዲቱ ላይ ቀጥ ባሉ ኖሮ ብዙ ዝናምን ባጠጣናቸው ነበር (ማለትም ተወረደልኝ)፡፡

وَأَلَّوِ ٱسۡتَقَٰمُواْ عَلَى ٱلطَّرِيقَةِ لَأَسۡقَيۡنَٰهُم مَّآءً غَدَقٗا ١٦

17. በእርሱ ልንሞክራቸው (ባጠጣናቸው ነበር)፡፡ ከጌታውም ማስታወሻ የሚያፈገፍግ ሰው አስቸጋሪን ቅጣት ያገባዋል፡፡

لِّنَفۡتِنَهُمۡ فِيهِۚ وَمَن يُعۡرِضۡ عَن ذِكۡرِ رَبِّهِۦ يَسۡلُكۡهُ عَذَابٗا صَعَدٗا ١٧

18. እነሆ መስጊዶችም የአላህ ብቻ ናቸው፡፡ (በውስጣቸው) ከአላህ ጋር አንድንም አትገዙ (ማለትም)፡፡

وَأَنَّ ٱلۡمَسَٰجِدَ لِلَّهِ فَلَا تَدۡعُواْ مَعَ ٱللَّهِ أَحَدٗا ١٨

19. እነሆም የአላህ ባሪያ (ሙሐመድ አላህን) የሚጠራው ኾኖ በተነሳ ጊዜ (ጋኔኖች) በእርሱ ላይ ድርብርቦች ሊኾኑ ቀረቡ (ማለትም)፡፡

وَأَنَّهُۥ لَمَّا قَامَ عَبۡدُ ٱللَّهِ يَدۡعُوهُ كَادُواْ يَكُونُونَ عَلَيۡهِ لِبَدٗا ١٩

20. «እኔ የምግገዛው ጌታየን ብቻ ነው፡፡ በእርሱም አንድንም አላጋራም» በል፡፡

قُلۡ إِنَّمَآ أَدۡعُواْ رَبِّي وَلَآ أُشۡرِكُ بِهِۦٓ أَحَدٗا ٢٠

21. «እኔ ለእናንተ ጉዳትንም ቀጥታንም አልችልም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنِّي لَآ أَمۡلِكُ لَكُمۡ ضَرّٗا وَلَا رَشَدٗا ٢١

22. «እኔ ከአላህ (ቅጣት) አንድም አያድነኝም፡፡ ከእርሱም ሌላ መጠጊያን አላገኝም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنِّي لَن يُجِيرَنِي مِنَ ٱللَّهِ أَحَدٞ وَلَنۡ أَجِدَ مِن دُونِهِۦ مُلۡتَحَدًا ٢٢

23. «ከአላህ የኾነ ማድረስን መልክቶቹንም በስተቀር (አልችልም)፡፡ አላህንና መልክተኛውንም የሚያምጽ ሰው ለእርሱ የገሀነም እሳት አልለው፡፡ በውስጧ ዘላለም ዘውታሪዎች ሲኾኑ፡፡»

إِلَّا بَلَٰغٗا مِّنَ ٱللَّهِ وَرِسَٰلَٰتِهِۦۚ وَمَن يَعۡصِ ٱللَّهَ وَرَسُولَهُۥ فَإِنَّ لَهُۥ نَارَ جَهَنَّمَ خَٰلِدِينَ فِيهَآ أَبَدًا ٢٣

24. የሚስፈራሩበትንም ባዩ ጊዜ ረዳቱ ደካማ፣ ቁጥሩም አነስተኛ የኾነው ማን እንደኾነ በእርግጥ ያውቃሉ፡፡

حَتَّىٰٓ إِذَا رَأَوۡاْ مَا يُوعَدُونَ فَسَيَعۡلَمُونَ مَنۡ أَضۡعَفُ نَاصِرٗا وَأَقَلُّ عَدَدٗا ٢٤

25. «የምትስፈራሩበት ነገር ቅርብ ወይም ጌታየ ለእርሱ የተወሰነ ጊዜን የሚያደርግለት (ሩቅ) መኾኑን አላውቅም» በላቸው፡፡

قُلۡ إِنۡ أَدۡرِيٓ أَقَرِيبٞ مَّا تُوعَدُونَ أَمۡ يَجۡعَلُ لَهُۥ رَبِّيٓ أَمَدًا ٢٥

26. «(እርሱ) ሩቁን ምስጢር ዐዋቂ ነው፡፡ በምስጢሩም ላይ አንድንም አያሳውቅም፡፡»

عَٰلِمُ ٱلۡغَيۡبِ فَلَا يُظۡهِرُ عَلَىٰ غَيۡبِهِۦٓ أَحَدًا ٢٦

27. ከመልክተኛ ለወደደው ቢኾን እንጅ (ለሌላ አይገልጽም)፡፡ እርሱም ከስተፊቱም ከስተኋላውም ጠባቂዎችን ያደርግለታል፡፡

إِلَّا مَنِ ٱرۡتَضَىٰ مِن رَّسُولٖ فَإِنَّهُۥ يَسۡلُكُ مِنۢ بَيۡنِ يَدَيۡهِ وَمِنۡ خَلۡفِهِۦ رَصَدٗا ٢٧

28. እነርሱ ዘንድ ባለው ነገር ዕውቀቱ የከበበና ነገሩንም ሁሉ በቁጥር ያጠቃለለ ሲኾን የጌታቸውን መልክቶች ያደረሱ መኾናቸውን ያውቅ ዘንድ (ጠባቂ ያደርጋል)፡፡

لِّيَعۡلَمَ أَن قَدۡ أَبۡلَغُواْ رِسَٰلَٰتِ رَبِّهِمۡ وَأَحَاطَ بِمَا لَدَيۡهِمۡ وَأَحۡصَىٰ كُلَّ شَيۡءٍ عَدَدَۢا ٢٨

# ሱረቱ አል ሙዘሚል

# سورة المزّمّل

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አንተ ተከናናቢው ሆይ፡፡

يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡمُزَّمِّلُ ﴿١﴾

2. ሌሊቱን ሁሉ ጥቂት ሲቀር ቁም፤ (ስገደ)፡፡

قُمِ ٱلَّيۡلَ إِلَّا قَلِيلٗا ﴿٢﴾

3. ግማሹን (ቁም)፤ ወይም ከርሱ ጥቂትን ቀንስ፡፡

نِّصۡفَهُۥٓ أَوِ ٱنقُصۡ مِنۡهُ قَلِيلًا ﴿٣﴾

4. ወይም በእርሱ ላይ ጨምር፡፡ ቁርኣንንም በዝግታ ማንበብን አንብብ፡፡

أَوۡ زِدۡ عَلَيۡهِ وَرَتِّلِ ٱلۡقُرۡءَانَ تَرۡتِيلًا ﴿٤﴾

5. እኛ ባንተ ላይ ከባድ ቃልን እንጥላለንና፡፡

إِنَّا سَنُلۡقِي عَلَيۡكَ قَوۡلٗا ثَقِيلًا ﴿٥﴾

6. የሌሊት መነሳት እርሷ (ሕዋሳትንና ልብን) ለማስማማት በጣም ብርቱ ናት፡፡ ለማንበብም ትክክለኛ ናት፡፡

إِنَّ نَاشِئَةَ ٱلَّيۡلِ هِيَ أَشَدُّ وَطۡـٔٗا وَأَقۡوَمُ قِيلًا ﴿٦﴾

7. ላንተ በቀን ውስጥ ረዥም መዘዋወር አልለህ፡፡

إِنَّ لَكَ فِي ٱلنَّهَارِ سَبۡحٗا طَوِيلٗا ﴿٧﴾

8. የጌታህንም ስም አውሳ፤ ወደእርሱም (መግገዛት) መቋረጥን ተቋረጥ ፡፡

وَٱذۡكُرِ ٱسۡمَ رَبِّكَ وَتَبَتَّلۡ إِلَيۡهِ تَبۡتِيلٗا ﴿٨﴾

9. (እርሱም) የምሥራቅና የምዕራብ ጌታ ነው፡፡ ከእርሱ ሌላ አምላክ የለም፡፡ መጠጊያ አድርገህም ያዘው፡፡

رَّبُّ ٱلۡمَشۡرِقِ وَٱلۡمَغۡرِبِ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ فَٱتَّخِذۡهُ وَكِيلٗا ﴿٩﴾

10. (ከሓዲዎች) በሚሉትም ላይ ታገሥ፡፡ መልካምንም መተው ተዋቸው፡፡

وَٱصۡبِرۡ عَلَىٰ مَا يَقُولُونَ وَٱهۡجُرۡهُمۡ هَجۡرٗا جَمِيلٗا ﴿١٠﴾

11. የድሎት ባለቤቶችም ከኾኑት አስተባባዮች ጋር ተዎኝ፡፡ ጥቂትንም ጊዜ አቆያቸው፡፡

وَذَرۡنِي وَٱلۡمُكَذِّبِينَ أُوْلِي ٱلنَّعۡمَةِ وَمَهِّلۡهُمۡ قَلِيلًا ﴿١١﴾

12. እኛ ዘንድ ከባድ ማሰሪያዎች እሳትም አልለና፡፡

إِنَّ لَدَيۡنَآ أَنكَالٗا وَجَحِيمٗا ﴿١٢﴾

13. የሚያንቅ ምግብም፤ አሳማሚ ቅጣትም (አልለ)

وَطَعَامٗا ذَا غُصَّةٖ وَعَذَابًا أَلِيمٗا ﴿١٣﴾

14. ምድርና ገራዎች በሚርገፈገፉበት፣ ጋራዎችም ፈሳሽ የአሸዋ ክምር በሚኾኑበት ቀን፡፡

يَوۡمَ تَرۡجُفُ ٱلۡأَرۡضُ وَٱلۡجِبَالُ وَكَانَتِ ٱلۡجِبَالُ كَثِيبٗا مَّهِيلًا ﴿١٤﴾

15. እኛ በእናንተ ላይ መስካሪ መልክተኛን ወደእናንተ ላክን:: ወደ ፈርዖን መልክተኛን እንደላክን::

إِنَّآ أَرۡسَلۡنَآ إِلَيۡكُمۡ رَسُولٗا شَٰهِدًا عَلَيۡكُمۡ كَمَآ أَرۡسَلۡنَآ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ رَسُولٗا ﴿١٥﴾

16. ፈርዖንም መልክተኛውን አመጸ፤ ብርቱ መያዝንም ያዝነው::

فَعَصَىٰ فِرۡعَوۡنُ ٱلرَّسُولَ فَأَخَذۡنَٰهُ أَخۡذٗا وَبِيلٗا ﴿١٦﴾

17. ብትክዱ ልጆችን ሽበቶዎች የሚያደርገውን ቀን (ቅጣት) እንዴት ትጠበቃላችሁ::

فَكَيۡفَ تَتَّقُونَ إِن كَفَرۡتُمۡ يَوۡمٗا يَجۡعَلُ ٱلۡوِلۡدَٰنَ شِيبًا ﴿١٧﴾

18. ሰማዩ በርሱ (በዚያ ቀን) ተሰንጣቂ ነው:: ቀጠሮው ተፈጻሚ ነው::

ٱلسَّمَآءُ مُنفَطِرُۢ بِهِۦۚ كَانَ وَعۡدُهُۥ مَفۡعُولًا ﴿١٨﴾

19. ይህቺ መገሠጫ ናት:: (መዳንን) የሻም ሰው ወደ ጌታው መንገድን ይይዛል::

إِنَّ هَٰذِهِۦ تَذۡكِرَةٞۖ فَمَن شَآءَ ٱتَّخَذَ إِلَىٰ رَبِّهِۦ سَبِيلًا ﴿١٩﴾

20. አንተ ከሌሊቱ ሁለት እጅ ያነሰን ግማሹንም ሲሶውንም የምትቆም መኾንህን ጌታህ በእርግጥ ያውቃል:: ከእነዚያም አብረውህ ካሉት ከፊሎች (የሚቆሙ መኾናቸውን ያውቃል):: አላህም ሌሊትንና ቀንን ይለክካል:: (ሌሊቱን) የማታዳርሱት መኾናችሁን ዐወቀ:: በእናንተ ላይም (ወደ ማቃለል) ተመለሰላችሁ:: ስለዚህ ከቁርኣን (በስግደት) የተቻላችሁን አንብቡ:: ከእናንተ ውስጥ በሽተኞች፣ ሌሎችም ከአላህ ችሮታ ለመፈለግ በምድር ላይ የሚኼዱ፣ ሌሎችም በአላህ መንገድ (ሃይማኖት) የሚጋደሉ እንደሚኖሩ ዐወቀ:: (አቃለለላቸውም):: ከእርሱም የተቻለችሁን አንብቡ:: ሶላትንም ስገዱ:: ዘካንም ስጡ:: ለአላህም መልካም ብደርን አበድሩ:: ከመልካም ሥራም ለነፍሶቻችሁ የምታስቀድሙትን ሁሉ እርሱ የተሻለና በምንዳም ታላቅ ኾኖ አላህ ዘንድ ታገኙታላችሁ:: አላህንም ምሕረትን ለምኑት:: አላህ በጣም መሓሪ አዛኝ ነውና::

۞إِنَّ رَبَّكَ يَعۡلَمُ أَنَّكَ تَقُومُ أَدۡنَىٰ مِن ثُلُثَيِ ٱلَّيۡلِ وَنِصۡفَهُۥ وَثُلُثَهُۥ وَطَآئِفَةٞ مِّنَ ٱلَّذِينَ مَعَكَۚ وَٱللَّهُ يُقَدِّرُ ٱلَّيۡلَ وَٱلنَّهَارَۚ عَلِمَ أَن لَّن تُحۡصُوهُ فَتَابَ عَلَيۡكُمۡۖ فَٱقۡرَءُواْ مَا تَيَسَّرَ مِنَ ٱلۡقُرۡءَانِۚ عَلِمَ أَن سَيَكُونُ مِنكُم مَّرۡضَىٰ وَءَاخَرُونَ يَضۡرِبُونَ فِي ٱلۡأَرۡضِ يَبۡتَغُونَ مِن فَضۡلِ ٱللَّهِ وَءَاخَرُونَ يُقَٰتِلُونَ فِي سَبِيلِ ٱللَّهِۖ فَٱقۡرَءُواْ مَا تَيَسَّرَ مِنۡهُۚ وَأَقِيمُواْ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتُواْ ٱلزَّكَوٰةَ وَأَقۡرِضُواْ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنٗاۚ وَمَا تُقَدِّمُواْ لِأَنفُسِكُم مِّنۡ خَيۡرٖ تَجِدُوهُ عِندَ ٱللَّهِ هُوَ خَيۡرٗا وَأَعۡظَمَ أَجۡرٗاۚ وَٱسۡتَغۡفِرُواْ ٱللَّهَۖ إِنَّ ٱللَّهَ غَفُورٞ رَّحِيمُۢ ﴿٢٠﴾

## ሱረቱ አል ሙደሲር

## سورة المدّثّر

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አንተ (ልብስህን) ደራቢው ሆይ!

يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡمُدَّثِّرُ ﴿١﴾

2. ተነሳ አስጠንቅቅም፡፡

قُمۡ فَأَنذِرۡ ٢

3. ጌታህንም አክብር፡፡

وَرَبَّكَ فَكَبِّرۡ ٣

4. ልብስህንም አጥራ፡፡

وَثِيَابَكَ فَطَهِّرۡ ٤

5. ጣዖትንም ራቅ፡፡

وَٱلرُّجۡزَ فَٱهۡجُرۡ ٥

6. ማብዛትንም የምትፈልግ ኾነህ፤ (በረከትን) አትለግስለለ

وَلَا تَمۡنُن تَسۡتَكۡثِرُ ٦

7. ለጌታህም (ትዕዛዝ) ታገሥ፡፡

وَلِرَبِّكَ فَٱصۡبِرۡ ٧

8. በቀንዱም በተነፋ ጊዜ (ነገሩ ይበረታል)፡፡

فَإِذَا نُقِرَ فِي ٱلنَّاقُورِ ٨

9. ይህም (ጊዜ) ያ ቀን አስቸጋሪ ቀን ነው፡፡

فَذَٰلِكَ يَوۡمَئِذٖ يَوۡمٌ عَسِيرٌ ٩

10. በከሓዲዎች ላይ ገር ያልኾነ ነው፡፡

عَلَى ٱلۡكَٰفِرِينَ غَيۡرُ يَسِيرٖ ١٠

11. አንድ ኾኖ ከፈጠርኩት ሰው ጋር ተዎኝ (እኔ እበቃሃለሁ)፡፡

ذَرۡنِي وَمَنۡ خَلَقۡتُ وَحِيدٗا ١١

12. ለእርሱም የተዘረጋን ገንዘብ (በያይነቱ) ያደረግሁለት፡፡

وَجَعَلۡتُ لَهُۥ مَالٗا مَّمۡدُودٗا ١٢

13. (በያደባባዩ) ተገኝዎች የኾኑ ወንዶች ልጆችንም፡፡

وَبَنِينَ شُهُودٗا ١٣

14. ለእርሱም (ኑሮውን) መዘርጋትን የዘረጋሁለት (ከኾነ ሰው ገር ተዎኝ)፡፡

وَمَهَّدتُّ لَهُۥ تَمۡهِيدٗا ١٤

15. ከዚያም ልጨምርለት ይከጃላል፡፡

ثُمَّ يَطۡمَعُ أَنۡ أَزِيدَ ١٥

16. ይከልከል፤ እርሱ ለአንቀጾቻችን በእርግጥ ተቃዋሚ ነበር፡፡

كَلَّآۖ إِنَّهُۥ كَانَ لِأٓيَٰتِنَا عَنِيدٗا ١٦

17. በእርግጥ ችግርን አስገድደዋለሁ፡፡

سَأُرۡهِقُهُۥ صَعُودًا ١٧

18. እርሱ (በቁርኣን ነገር) ሐሰበ፤ ገመተም፡፡

إِنَّهُۥ فَكَّرَ وَقَدَّرَ ١٨

19. ተረገመም፤ እንዴት ገመተ!

فَقُتِلَ كَيۡفَ قَدَّرَ ١٩

20. ከዚያም (ከሞት በኋላ) ተረገመ፡፡ እንዴት ገመተ!

ثُمَّ قُتِلَ كَيۡفَ قَدَّرَ ٢٠

21. ከዚያም እንደ ገና (በቁርኣኑ ነገር) ተመለከተ፡፡

ثُمَّ نَظَرَ ﴿٢١﴾

22. ከዚያም ፊቱን አጨፈገገ፤ አኮማተረም፡፡

ثُمَّ عَبَسَ وَبَسَرَ ﴿٢٢﴾

23. ከዚያም (ከማመን) ዞረ፤ ኮራም፡፡

ثُمَّ أَدۡبَرَ وَٱسۡتَكۡبَرَ ﴿٢٣﴾

24. አለም «ይህ (ከሌላ) የሚቀዳ ድግምት እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

فَقَالَ إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا سِحۡرٞ يُؤۡثَرُ ﴿٢٤﴾

25. «ይህ የሰው ቃል እንጅ ሌላ አይደለም፡፡»

إِنۡ هَٰذَآ إِلَّا قَوۡلُ ٱلۡبَشَرِ ﴿٢٥﴾

26. በሰቀር ውስጥ በእርግጥ አገባዋለሁ፡፡

سَأُصۡلِيهِ سَقَرَ ﴿٢٦﴾

27. ሰቀር ምን እንደኾነች ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا سَقَرُ ﴿٢٧﴾

28. (ያገኘችውን ሁሉ) አታስቀርም አትተውምም፡፡

لَا تُبۡقِي وَلَا تَذَرُ ﴿٢٨﴾

29. ቆዳን በጣም አክሳይ ናት፡፡

لَوَّاحَةٞ لِّلۡبَشَرِ ﴿٢٩﴾

30. በእርሷም ላይ አሥራ ዘጠኝ (ዘበኞች) አሉባት፡፡

عَلَيۡهَا تِسۡعَةَ عَشَرَ ﴿٣٠﴾

31. የእሳትንም ዘበኞች መላእክት እንጅ ሌላ አላደረግንም፡፡ ቁጥራቸውንም ለእነዚያ ለካዱት መፈተኛ እንጅ አላደረግንም፡፡ እነዚያ መጽሐፍን የተሰጡት እንዲያረጋግጡ፣ እነዚያም ያመኑት እምነትን እንዲጨምሩ፣ እነዚያም መጽሐፍን የተሰጡትና ምእምናኖቹ እንዳይጠራጠሩ፣ እነዚያም በልቦቻቸው ውስጥ በሽታ ያለባቸው (መናፍቃን)፣ ከሓዲዎችም አላህ በዚህ (ቁጥር) ምን ምሳሌ ሻቷል? እንዲሉ (እንጅ አላደረግንም)፡፡ እንደዚሁ አላህ የሚሻውን ያጠምማል፡፡ የሚሻውንም ያቀናል፡፡ የጌታህንም ሰራዊት (ልክ) ከርሱ በቀር ማንም አያውቅም፡፡ እርሷም (የሰቀር እሳት) ለሰዎች መገሰጫ እንጅ ሌላ አይደለችም፡፡

وَمَا جَعَلۡنَآ أَصۡحَٰبَ ٱلنَّارِ إِلَّا مَلَٰٓئِكَةٗۖ وَمَا جَعَلۡنَا عِدَّتَهُمۡ إِلَّا فِتۡنَةٗ لِّلَّذِينَ كَفَرُواْ لِيَسۡتَيۡقِنَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ وَيَزۡدَادَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُوٓاْ إِيمَٰنٗا وَلَا يَرۡتَابَ ٱلَّذِينَ أُوتُواْ ٱلۡكِتَٰبَ وَٱلۡمُؤۡمِنُونَ وَلِيَقُولَ ٱلَّذِينَ فِي قُلُوبِهِم مَّرَضٞ وَٱلۡكَٰفِرُونَ مَاذَآ أَرَادَ ٱللَّهُ بِهَٰذَا مَثَلٗاۚ كَذَٰلِكَ يُضِلُّ ٱللَّهُ مَن يَشَآءُ وَيَهۡدِي مَن يَشَآءُۚ وَمَا يَعۡلَمُ جُنُودَ رَبِّكَ إِلَّا هُوَۚ وَمَا هِيَ إِلَّا ذِكۡرَىٰ لِلۡبَشَرِ ﴿٣١﴾

32. (ከክህደት) ይከልከሉ፡፡ በጨረቃ እምላለሁ፡፡

كَلَّا وَٱلۡقَمَرِ ﴿٣٢﴾

33. በሌሊቱም በኼደ ጊዜ፡፡

وَٱلَّيۡلِ إِذۡ أَدۡبَرَ ﴿٣٣﴾

34. በንጋቱም ባበራ ጊዜ፡፡

وَٱلصُّبۡحِ إِذَآ أَسۡفَرَ ﴿٣٤﴾

35. እርሷ (ሰቀር) ከታላላቆቹ (አደጋዎች) አንዷ ናት፡፡

إِنَّهَا لَإِحْدَى ٱلْكُبَرِ ٣٥

36. ለሰዎች አስፈራሪ ስትኾን፡፡

نَذِيرًا لِّلْبَشَرِ ٣٦

37. ከእናንተ (ወደ በጎ ነገር) መቅደምን ወይም ወደ ኋላ መቅረትን ለሻ ሰው (አስፈራሪ ስትኾኑ)፡፡

لِمَن شَآءَ مِنكُمْ أَن يَتَقَدَّمَ أَوْ يَتَأَخَّرَ ٣٧

38. ነፍስ ሁሉ በሠራችው ሥራ ተያዥ ናት፡፡

كُلُّ نَفْسٍۭ بِمَا كَسَبَتْ رَهِينَةٌ ٣٨

39. የቀኝ ባለቤቶች ብቻ ሲቀሩ፡፡

إِلَّآ أَصْحَٰبَ ٱلْيَمِينِ ٣٩

40. (እነርሱስ) በገነቶች ውስጥ ይጠያየቃሉ፡፡

فِى جَنَّٰتٍ يَتَسَآءَلُونَ ٤٠

41. ከአመጸኞቹ ኹነታ፡፡

عَنِ ٱلْمُجْرِمِينَ ٤١

42. (ይሏቸዋልም) «በሰቀር ውስጥ ምን አገባችሁ?»

مَا سَلَكَكُمْ فِى سَقَرَ ٤٢

43. (እነርሱም) ይላሉ «ከሰጋጆቹ አልነበርንም፡፡

قَالُوا۟ لَمْ نَكُ مِنَ ٱلْمُصَلِّينَ ٤٣

44. «ለድኾችም የምናበላ አልነበርንም፡፡

وَلَمْ نَكُ نُطْعِمُ ٱلْمِسْكِينَ ٤٤

45. «ከዘባራቂዎቹም ጋር እንዘባርቅ ነበርን፡፡

وَكُنَّا نَخُوضُ مَعَ ٱلْخَآئِضِينَ ٤٥

46. «በፍርዱ ቀንም እናስተባብል ነበርን፡፡

وَكُنَّا نُكَذِّبُ بِيَوْمِ ٱلدِّينِ ٤٦

47. «እርግጠኛው (ሞት) እስከ መጣን ድረስ፡፡»

حَتَّىٰٓ أَتَىٰنَا ٱلْيَقِينُ ٤٧

48. የአማላጆችም ምልጃ አትጠቅማቸውም፡፡

فَمَا تَنفَعُهُمْ شَفَٰعَةُ ٱلشَّٰفِعِينَ ٤٨

49. ከግሣጼዎም (ከቁርኣን) የሚያፈገፍጉት ለእነርሱ ምን አልላቸው?

فَمَا لَهُمْ عَنِ ٱلتَّذْكِرَةِ مُعْرِضِينَ ٤٩

50. እነርሱ ልክ ደንባሪዎች የሜዳ አህዮች ይመስላሉ፡፡

كَأَنَّهُمْ حُمُرٌ مُّسْتَنفِرَةٌ ٥٠

51. ከዐንበሳ የሸሹ፡፡

فَرَّتْ مِن قَسْوَرَةٍۭ ٥١

52. ይልቁንም ከእነርሱ እያንዳንዱ ሰው ሁሉ የተዘረጉ ጽሑፎችን እንዲሰጥ ይፈልጋል፡፡

بَلْ يُرِيدُ كُلُّ ٱمْرِئٍ مِّنْهُمْ أَن يُؤْتَىٰ صُحُفًا مُّنَشَّرَةً ٥٢

53. ይከልከሉ፡፡ ይልቁንም የመጨረሻይቱን ዓለም (ቅጣት) አይፈሩም፡፡

كَلَّا ۖ بَل لَّا يَخَافُونَ ٱلْءَاخِرَةَ ٥٣

54. ይከልከሉ፡፡ እርሱ (ቁርአን) መገሠጫ ነው፡፡

كَلَّآ إِنَّهُۥ تَذۡكِرَةٞ ﴿٥٤﴾

55. ስለዚህ የሻ ሰው ይገሰጽበታል፡፡

فَمَن شَآءَ ذَكَرَهُۥ ﴿٥٥﴾

56. አላህም ካልሻ በስተቀር አይገሠጹም፡፡ እርሱ (አላህ) የመፈራት ባለቤት የምሕረትም ባለቤት ነው፡፡

وَمَا يَذۡكُرُونَ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُۚ هُوَ أَهۡلُ ٱلتَّقۡوَىٰ وَأَهۡلُ ٱلۡمَغۡفِرَةِ ﴿٥٦﴾

## ሱረቱ አል ቂያማህ

## سورة القيامة

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. (ነገሩ ከሓዲዎች እንደሚሉት) አይደለም፡፡ በትንሣኤ ቀን እምላለሁ፡፡

لَآ أُقۡسِمُ بِيَوۡمِ ٱلۡقِيَٰمَةِ ﴿١﴾

2. (ራሷን) ወቃሽ በኾነች ነፍስም እምላለሁ፡፡ (በእርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ)፡፡

وَلَآ أُقۡسِمُ بِٱلنَّفۡسِ ٱللَّوَّامَةِ ﴿٢﴾

3. ሰው አጥንቶቹን አለመሰብሰባችንን ያስባልን?

أَيَحۡسَبُ ٱلۡإِنسَٰنُ أَلَّن نَّجۡمَعَ عِظَامَهُۥ ﴿٣﴾

4. አይደለም ጣቶቹን (ፊት እንደ ነበሩ) በማስተካከል ላይ ቻዮች ስንኾን (እንሰበስባቸዋለን)፡፡

بَلَىٰ قَٰدِرِينَ عَلَىٰٓ أَن نُّسَوِّيَ بَنَانَهُۥ ﴿٤﴾

5. ይልቁንም ሰው በፊቱ ባለው ነገር (በትንሣኤ) ሊያስተባብል ይፈልጋል፡፡

بَلۡ يُرِيدُ ٱلۡإِنسَٰنُ لِيَفۡجُرَ أَمَامَهُۥ ﴿٥﴾

6. «የትንሣኤው ቀን መቼ ነው?» ሲል ይጠይቃል፡፡

يَسۡـَٔلُ أَيَّانَ يَوۡمُ ٱلۡقِيَٰمَةِ ﴿٦﴾

7. ዓይንም በዋለለ ጊዜ፡፡

فَإِذَا بَرِقَ ٱلۡبَصَرُ ﴿٧﴾

8. ጨረቃም በጨለመ ጊዜ፡፡

وَخَسَفَ ٱلۡقَمَرُ ﴿٨﴾

9. ፀሐይና ጨረቃም በተሰበሰቡ ጊዜ፡፡

وَجُمِعَ ٱلشَّمۡسُ وَٱلۡقَمَرُ ﴿٩﴾

10. «ሰው በዚያ ቀን መሸሻው የት ነው?» ይላል፡፡

يَقُولُ ٱلۡإِنسَٰنُ يَوۡمَئِذٍ أَيۡنَ ٱلۡمَفَرُّ ﴿١٠﴾

11. ይከልከል፤ ምንም መጠጊያ የለም፡፡

كَلَّا لَا وَزَرَ ﴿١١﴾

| | |
|---|---|
| 12. በዚያ ቀን መርጊያው ወደ ጌታህ ብቻ ነው፡፡ | إِلَىٰ رَبِّكَ يَوۡمَئِذٍ ٱلۡمُسۡتَقَرُّ ١٢ |
| 13. ሰው በዚያ ቀን ባስቀደመውና ባስቆየው ሁሉ ይነገራል፡፡ | يُنَبَّؤُاْ ٱلۡإِنسَٰنُ يَوۡمَئِذِۭ بِمَا قَدَّمَ وَأَخَّرَ ١٣ |
| 14. በእርግጥም ሰው በነፍሱ ላይ አስረጅ ነው፡፡ (አካሎቹ ይመሰክሩበታል)፡፡ | بَلِ ٱلۡإِنسَٰنُ عَلَىٰ نَفۡسِهِۦ بَصِيرَةٞ ١٤ |
| 15. ምክንያቶቹን ሁሉ ቢያመጣም እንኳ (አይሰማም)፡ ፡ | وَلَوۡ أَلۡقَىٰ مَعَاذِيرَهُۥ ١٥ |
| 16. በእርሱ (በቁርኣን ንባብ) ልትቸኩል ምላስህን በእርሱ አታላውስ፡፡ | لَا تُحَرِّكۡ بِهِۦ لِسَانَكَ لِتَعۡجَلَ بِهِۦٓ ١٦ |
| 17. (በልብህ ውስጥ) መሰብሰቡና ማንበቡ በእኛ ላይ ነውና፡፡ | إِنَّ عَلَيۡنَا جَمۡعَهُۥ وَقُرۡءَانَهُۥ ١٧ |
| 18. ባነበብነውም ጊዜ (ካለቀ በኋላ) ንባቡን ተከተል፡፡ | فَإِذَا قَرَأۡنَٰهُ فَٱتَّبِعۡ قُرۡءَانَهُۥ ١٨ |
| 19. ከዚያም ማብራራቱ በእኛ ላይ ነው፡፡ | ثُمَّ إِنَّ عَلَيۡنَا بَيَانَهُۥ ١٩ |
| 20. (ከመጣደፍ) ተከልከል፡፡ ይልቁንም (ሰዎች) ፈጣኒቱን (ዓለም) ትወዳላችሁ፡፡ | كَلَّا بَلۡ تُحِبُّونَ ٱلۡعَاجِلَةَ ٢٠ |
| 21. መጨረሻይቱንም (ዓለም) ትተዋላችሁ፡፡ (አትዘጋጁላትም)፡፡ | وَتَذَرُونَ ٱلۡأٓخِرَةَ ٢١ |
| 22. ፊቶች በዚያ ቀን አብሪዎች ናቸው፡፡ | وُجُوهٞ يَوۡمَئِذٖ نَّاضِرَةٌ ٢٢ |
| 23. ወደ ጌታቸው ተመልካቾች ናቸው፡፡ | إِلَىٰ رَبِّهَا نَاظِرَةٞ ٢٣ |
| 24. ፊቶችም በዚያ ቀን ጨፍጋጊዎች ናቸው፡፡ | وَوُجُوهٞ يَوۡمَئِذِۭ بَاسِرَةٞ ٢٤ |
| 25. በርሳቸውም ዐደጋ እንደሚሠራባቸው ያረጋግጣሉ፡፡ | تَظُنُّ أَن يُفۡعَلَ بِهَا فَاقِرَةٞ ٢٥ |
| 26. ንቁ (ነፍስ) ብሪዎችን በደረሰች ጊዜ፤ | كَلَّآ إِذَا بَلَغَتِ ٱلتَّرَاقِيَ ٢٦ |
| 27. «አሻሪው ማነው?» በተባለም ጊዜ፡፡ | وَقِيلَ مَنۡۜ رَاقٖ ٢٧ |
| 28. (ሕመምተኛው) እርሱ (የሰፈረበት ነገር ከዚህ ዓለም) መልለየት መኾኑን ባረጋገጠም ጊዜ፡፡ | وَظَنَّ أَنَّهُ ٱلۡفِرَاقُ ٢٨ |
| 29. ባትም በባት በተጣበቀች ጊዜ፡፡ | وَٱلۡتَفَّتِ ٱلسَّاقُ بِٱلسَّاقِ ٢٩ |

30. በዚያ ቀን መንዳቱ ወደ ጌታህ (ፍርድ) ነው::

إِلَىٰ رَبِّكَ يَوْمَئِذٍ ٱلْمَسَاقُ ﴿٣٠﴾

31. አላመነምም አልሰገደምም::

فَلَا صَدَّقَ وَلَا صَلَّىٰ ﴿٣١﴾

32. ግን አስተባበለ፤ (ከእምነት) ዞረም::

وَلَٰكِن كَذَّبَ وَتَوَلَّىٰ ﴿٣٢﴾

33. ከዚያም እየተንጎባለለ ወደ ቤተሰቡ ኼደ::

ثُمَّ ذَهَبَ إِلَىٰٓ أَهْلِهِۦ يَتَمَطَّىٰٓ ﴿٣٣﴾

34. የምትጠላውን ነገር (አላህ) ያስከትልህ:: ለአንተ ተገቢህም ነው::

أَوْلَىٰ لَكَ فَأَوْلَىٰ ﴿٣٤﴾

35. ከዚያም ጥፋት ይጠጋህ ለአንተ የተገባህም ነው::

ثُمَّ أَوْلَىٰ لَكَ فَأَوْلَىٰٓ ﴿٣٥﴾

36. ሰው ስድ ኾኖ መትተውን ይጠረጥራልን?

أَيَحْسَبُ ٱلْإِنسَٰنُ أَن يُتْرَكَ سُدًى ﴿٣٦﴾

37. የሚፈሰስ ከኾነ የፍትወት ጠብታ አልነበረምን?

أَلَمْ يَكُ نُطْفَةً مِّن مَّنِىٍّ يُمْنَىٰ ﴿٣٧﴾

38. ከዚያም የረጋ ደም ኾነ (አላህ ሰው አድርጎ) ፈጠረውም:: አስተካከለውም::

ثُمَّ كَانَ عَلَقَةً فَخَلَقَ فَسَوَّىٰ ﴿٣٨﴾

39. ከእርሱም ሁለት ዓይነቶችን ወንድና ሴትን አደረገ::

فَجَعَلَ مِنْهُ ٱلزَّوْجَيْنِ ٱلذَّكَرَ وَٱلْأُنثَىٰٓ ﴿٣٩﴾

40. ይህ (ጌታ) ሙታንን ሕያው በማድረግ ላይ ቻይ አይደለምን?

أَلَيْسَ ذَٰلِكَ بِقَٰدِرٍ عَلَىٰٓ أَن يُحْۦِىَ ٱلْمَوْتَىٰ ﴿٤٠﴾

# ሱረቱ አል ኢንሳን

# سورة الإنسان

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሰው ላይ የሚታወስ ነገር ሳይኾን ከዘመናት የተወሰነ ጊዜ በእርግጥ አልፎበታል::

هَلْ أَتَىٰ عَلَى ٱلْإِنسَٰنِ حِينٌ مِّنَ ٱلدَّهْرِ لَمْ يَكُن شَيْـًٔا مَّذْكُورًا ﴿١﴾

2. እኛ ሰውን (በሕግ ግዳጅ) የምንሞከረው ስንኾን ቅልቅሎች ከኾኑ የፍትወት ጠብታ ፈጠርነው:: ሰሚ ተመልካችም አደረግነው::

إِنَّا خَلَقْنَا ٱلْإِنسَٰنَ مِن نُّطْفَةٍ أَمْشَاجٍ نَّبْتَلِيهِ فَجَعَلْنَٰهُ سَمِيعًۢا بَصِيرًا ﴿٢﴾

| | |
|---|---|
| 3. እኛ ወይ አመስጋኝ ወይም ከሓዲ ሲኾን መንገዱን መራነው፤ (ገለጽንለት)፡፡ | إِنَّا هَدَيْنَٰهُ ٱلسَّبِيلَ إِمَّا شَاكِرًا وَإِمَّا كَفُورًا ﴿٣﴾ |
| 4. እኛ ለከሓዲዎች ሰንሰሎቶችንና እንዛዝላዎችን፣ እሳትንም አዘጋጅተናል፡፡ | إِنَّآ أَعْتَدْنَا لِلْكَٰفِرِينَ سَلَٰسِلَا۟ وَأَغْلَٰلًا وَسَعِيرًا ﴿٤﴾ |
| 5. በጎ አድራጊዎች መበረዣዋ ካፉር ከኾነች ጠጅ ይጠጣሉ፡፡ | إِنَّ ٱلْأَبْرَارَ يَشْرَبُونَ مِن كَأْسٍ كَانَ مِزَاجُهَا كَافُورًا ﴿٥﴾ |
| 6. ከእርሷ የአላህ ባሮች የሚጠጡላት (ወደፈለጉበት) ማንቧቧትን የሚያንቧቧት ከኾነች ምንጭ (ይጠጣሉ)፡፡ | عَيْنًا يَشْرَبُ بِهَا عِبَادُ ٱللَّهِ يُفَجِّرُونَهَا تَفْجِيرًا ﴿٦﴾ |
| 7. (ዛሬ) በስለታቸው ይሞላሉ፡፡ መከራው ተሰራጪ የኾነንም ቀን ይፈራሉ፡፡ | يُوفُونَ بِٱلنَّذْرِ وَيَخَافُونَ يَوْمًا كَانَ شَرُّهُۥ مُسْتَطِيرًا ﴿٧﴾ |
| 8. ምግብንም ከመውደዳቸው ጋር ለድኻ፣ ለየቲምም፣ ለምርኮኛም ለእስረኛም ያበላሉ፡፡ | وَيُطْعِمُونَ ٱلطَّعَامَ عَلَىٰ حُبِّهِۦ مِسْكِينًا وَيَتِيمًا وَأَسِيرًا ﴿٨﴾ |
| 9. «የምናበላችሁ ለአላህ ውዴታ ብቻ ነው፡፡ ከእናንተ ዋጋንም ማመስገንንም አንፈልግም፡፡ | إِنَّمَا نُطْعِمُكُمْ لِوَجْهِ ٱللَّهِ لَا نُرِيدُ مِنكُمْ جَزَآءً وَلَا شُكُورًا ﴿٩﴾ |
| 10. «እኛ (ፊትን) የሚያጨፈግግን ብርቱ ቀን ከጌታችን እንፈራለንና፤» (ይላሉ)፡፡ | إِنَّا نَخَافُ مِن رَّبِّنَا يَوْمًا عَبُوسًا قَمْطَرِيرًا ﴿١٠﴾ |
| 11. አላህም የዚያን ቀን ክፋት ጠበቃቸው፡፡ (ፊታቸው) ማማርንና መደሰትንም ገጠማቸው፡፡ | فَوَقَىٰهُمُ ٱللَّهُ شَرَّ ذَٰلِكَ ٱلْيَوْمِ وَلَقَّىٰهُمْ نَضْرَةً وَسُرُورًا ﴿١١﴾ |
| 12. በመታገሣቸውም ገነትንና የሐር ልብስን መነዳቸው፡፡ | وَجَزَىٰهُم بِمَا صَبَرُوا۟ جَنَّةً وَحَرِيرًا ﴿١٢﴾ |
| 13. በውስጧ በባለ አጎበር አልጋዎች ላይ ተደጋፊዎች በውስጧ ፀሐይንም ጨረቃንም የማያዩ ሲኾኑ፡፡ | مُّتَّكِـِٔينَ فِيهَا عَلَى ٱلْأَرَآئِكِ ۖ لَا يَرَوْنَ فِيهَا شَمْسًا وَلَا زَمْهَرِيرًا ﴿١٣﴾ |
| 14. ዛፎችዋም በእነርሱ ላይ የቀረበች፣ ፍሬዎችዋም (ለለቃሚዎች) መግገራትን የተገራች ስትኾን (ገነትን መነዳቸው)፡፡ | وَدَانِيَةً عَلَيْهِمْ ظِلَٰلُهَا وَذُلِّلَتْ قُطُوفُهَا تَذْلِيلًا ﴿١٤﴾ |
| 15. በእነርሱም ላይ ከብር በኾኑ ዕቃዎች (ሰሐኖች) የብርጭቆዎች በኾኑ ኩባያዎችም ይዝዞርባቸዋል፡፡ | وَيُطَافُ عَلَيْهِم بِـَٔانِيَةٍ مِّن فِضَّةٍ وَأَكْوَابٍ كَانَتْ قَوَارِيرَا۠ ﴿١٥﴾ |
| 16. መለካትን የለኳቸው በኾኑ የብር ብርጭቆዎች (ይዝዞርባቸዋል)፡፡ | قَوَارِيرَا۟ مِن فِضَّةٍ قَدَّرُوهَا تَقْدِيرًا ﴿١٦﴾ |
| 17. በእርሷም መበረዣዋ ዘንጀቢል የኾነችን ጠጅ ይጠጣሉ፡፡ | وَيُسْقَوْنَ فِيهَا كَأْسًا كَانَ مِزَاجُهَا زَنجَبِيلًا ﴿١٧﴾ |

18. በውስጧ ያለችውን ሰልሰቢል ተብላ የምትጠራውን ምንጭ፡፡

عَيۡنٗا فِيهَا تُسَمَّىٰ سَلۡسَبِيلٗا ۝١٨

19. በእነርሱም ላይ (ባሉበት ኹነታ) የሚዘወትሩ ወጣት ልጆች ይዘዋወራሉ፡፡ ባየሃቸው ጊዜ የተበተነ ሉል ናቸው ብለህ ታስባቸዋለህ፡፡

۞وَيَطُوفُ عَلَيۡهِمۡ وِلۡدَٰنٞ مُّخَلَّدُونَ إِذَا رَأَيۡتَهُمۡ حَسِبۡتَهُمۡ لُؤۡلُؤٗا مَّنثُورٗا ۝١٩

20. እዚያም በተመለከትክ ጊዜ ጸጋንና ታላቅ ንግሥናን ታያለህ፡፡

وَإِذَا رَأَيۡتَ ثَمَّ رَأَيۡتَ نَعِيمٗا وَمُلۡكٗا كَبِيرًا ۝٢٠

21. አረንጓዴዎች የኾኑ የቀጭን ሐር ልብሶችና ወፍራም ሐርም በላያቸው ላይ አልለ፡፡ ከብር የኾኑ አንባሮችንም ይሸለማሉ፡፡ ጌታቸውም አጥሪ የኾነን መጠጥ ያጠጣቸዋል፡፡

عَٰلِيَهُمۡ ثِيَابُ سُندُسٍ خُضۡرٞ وَإِسۡتَبۡرَقٞۖ وَحُلُّوٓاْ أَسَاوِرَ مِن فِضَّةٖ وَسَقَىٰهُمۡ رَبُّهُمۡ شَرَابٗا طَهُورًا ۝٢١

22. «ይህ በእርግጥ ለእናንተ ዋጋ ኾነ፡፡ ሥራችሁም ምስጉን ኾነ፤» (ይባላሉ)፡፡

إِنَّ هَٰذَا كَانَ لَكُمۡ جَزَآءٗ وَكَانَ سَعۡيُكُم مَّشۡكُورًا ۝٢٢

23. እኛ ቁርኣንን ባንተ ላይ ማውረድን እኛው አወረድነው፡፡

إِنَّا نَحۡنُ نَزَّلۡنَا عَلَيۡكَ ٱلۡقُرۡءَانَ تَنزِيلٗا ۝٢٣

24. ለጌታህ ፍርድም ታገሥ፡፡ ከእነርሱም ኀጢአተኛን ወይም ከሓዲን አትታዘዝ፡፡

فَٱصۡبِرۡ لِحُكۡمِ رَبِّكَ وَلَا تُطِعۡ مِنۡهُمۡ ءَاثِمًا أَوۡ كَفُورٗا ۝٢٤

25. የጌታህንም ስም በጧትና ከቀትር በላይ አውሳ፡፡

وَٱذۡكُرِ ٱسۡمَ رَبِّكَ بُكۡرَةٗ وَأَصِيلٗا ۝٢٥

26. ከሌሊቱም ለእርሱ ስገድ፡፡ በረዢምም ሌሊትም አወድሰው፡፡

وَمِنَ ٱلَّيۡلِ فَٱسۡجُدۡ لَهُۥ وَسَبِّحۡهُ لَيۡلٗا طَوِيلًا ۝٢٦

27. እነዚያ ፈጣኒቱን ዓለም ይወዳሉ፡፡ ከባድን ቀንም በስተፊታቸው ኹኖ ይተዋሉ፡፡

إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ يُحِبُّونَ ٱلۡعَاجِلَةَ وَيَذَرُونَ وَرَآءَهُمۡ يَوۡمٗا ثَقِيلٗا ۝٢٧

28. እኛ ፈጠርናቸው፡፡ መለያልያቸውንም አጠነከርን፡ ፡ በሻንም ጊዜ መሰሎቻቸውን መለወጥን እንለውጣለን፡ ፡

نَّحۡنُ خَلَقۡنَٰهُمۡ وَشَدَدۡنَآ أَسۡرَهُمۡۖ وَإِذَا شِئۡنَا بَدَّلۡنَآ أَمۡثَٰلَهُمۡ تَبۡدِيلًا ۝٢٨

29. ይህቺ መገሠጫ ናት፡፡ የሻም ሰው ወደ ጌታው መንገድን ይይዛል፡፡

إِنَّ هَٰذِهِۦ تَذۡكِرَةٞۖ فَمَن شَآءَ ٱتَّخَذَ إِلَىٰ رَبِّهِۦ سَبِيلٗا ۝٢٩

30. አላህም ካልሻ በስተቀር አትሹም፡፡ አላህ ዐዋቂ ጥበበኛ ነውና፡፡

وَمَا تَشَآءُونَ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُۚ إِنَّ ٱللَّهَ كَانَ عَلِيمًا حَكِيمًا ٣٠

31. የሚሻውን ሰው በእዝነቱ ውስጥ ያገባዋል፡፡ በዳዮቹንም (ዝቶባቸዋል)፡፡ ለእነርሱ አሳማሚ ቅጣትን አዘጋጅቶላቸዋል፡፡

يُدۡخِلُ مَن يَشَآءُ فِي رَحۡمَتِهِۦۚ وَٱلظَّٰلِمِينَ أَعَدَّ لَهُمۡ عَذَابًا أَلِيمَۢا ٣١

# ሱረቱ አል ሙርሰላት

# سورة المرسلات

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ተከታታይ ኾነው በተላኩት፣

وَٱلۡمُرۡسَلَٰتِ عُرۡفًا ١

2. በኀይል መንፈስን ነፋሾች በኾኑትም፣

فَٱلۡعَٰصِفَٰتِ عَصۡفًا ٢

3. መበተንን በታኞች በኾኑትም፤ (ነፋሶች)፣

وَٱلنَّٰشِرَٰتِ نَشۡرًا ٣

4. መለየትን ለይዎች በኾኑትም፣

فَٱلۡفَٰرِقَٰتِ فَرۡقًا ٤

5. መገሠጫን (ወደ ነቢያት) ጣይዎች በኾኑትም፣

فَٱلۡمُلۡقِيَٰتِ ذِكۡرًا ٥

6. ምክንያትን ለማስወገድ ወይም ለማስፈራራት (ጣይዎች በኾኑት መላእክት) እምላለሁ፡፡

عُذۡرًا أَوۡ نُذۡرًا ٦

7. ያ የምትስፈራሩበት (ትንሣኤ) በእርግጥ ኗኝ ነው፡፡

إِنَّمَا تُوعَدُونَ لَوَٰقِعٞ ٧

8. ከዋክብትም (ብርሃንዋ) በታበሰች ጊዜ፡፡

فَإِذَا ٱلنُّجُومُ طُمِسَتۡ ٨

9. ሰማይም በተከፈተች ጊዜ፡፡

وَإِذَا ٱلسَّمَآءُ فُرِجَتۡ ٩

10. ጋራዎችም በተንኮተኮቱ ጊዜ፡፡

وَإِذَا ٱلۡجِبَالُ نُسِفَتۡ ١٠

| | |
|---|---|
| 11. መልክተኞቹም ወቅት በተደረገላቸው ጊዜ፡፡ | وَإِذَا ٱلرُّسُلُ أُقِّتَتۡ ١١ |
| 12. ለየትኛው ቀን ተቀጠሩ (የሚባል ሲኾን)፤ | لِأَيِّ يَوۡمٍ أُجِّلَتۡ ١٢ |
| 13. ለመለያው ቀን (በተባለ ጊዜ፤ በፍጡሮች መካከል ይፈረዳል)፡፡ | لِيَوۡمِ ٱلۡفَصۡلِ ١٣ |
| 14. የመለያውም ቀን ምን እንደኾነ ምን አሳወቀህ? | وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا يَوۡمُ ٱلۡفَصۡلِ ١٤ |
| 15. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡ | وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ١٥ |
| 16. የፊተኞቹን (ሕዝቦች) አላጠፋንምን? | أَلَمۡ نُهۡلِكِ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٦ |
| 17. ከዚያም የኋለኞቹን እናስከትላቸዋለን፡፡ | ثُمَّ نُتۡبِعُهُمُ ٱلۡأٓخِرِينَ ١٧ |
| 18. በአመጸኞች ሁሉ እንደዚሁ እንሠራለን፡፡ | كَذَٰلِكَ نَفۡعَلُ بِٱلۡمُجۡرِمِينَ ١٨ |
| 19. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡ | وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ١٩ |
| 20. ከደካማ ውሃ አልፈጠርናችሁምን? | أَلَمۡ نَخۡلُقكُّم مِّن مَّآءٖ مَّهِينٖ ٢٠ |
| 21. በተጠበቀ መርጊያ ውስጥም (በማሕፀን) አደረግነው፡፡ | فَجَعَلۡنَٰهُ فِي قَرَارٖ مَّكِينٍ ٢١ |
| 22. እስከ ታወቀ ልክ ድረስ፡፡ መጠንነውም፤ ምን ያማርንም | إِلَىٰ قَدَرٖ مَّعۡلُومٖ ٢٢ |
| 23. መጣኞች ነን! | فَقَدَرۡنَا فَنِعۡمَ ٱلۡقَٰدِرُونَ ٢٣ |
| 24. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡ | وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ٢٤ |
| 25. ምድርን ሰብሳቢ አላደረግናትምን? | أَلَمۡ نَجۡعَلِ ٱلۡأَرۡضَ كِفَاتًا ٢٥ |
| 26. ሕያዋን ኾናችሁ ሙታንም ኾናችሁ፡፡ | أَحۡيَآءٗ وَأَمۡوَٰتٗا ٢٦ |
| 27. በውስጧም ከፍተኛዎችን ተራራዎች አደረግን፡፡ ጣፋጭ ውሃንም አጠጣናችሁ፡፡ | وَجَعَلۡنَا فِيهَا رَوَٰسِيَ شَٰمِخَٰتٖ وَأَسۡقَيۡنَٰكُم مَّآءٗ فُرَاتٗا ٢٧ |
| 28. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡ | وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ٢٨ |

29. «ወደዚያ በእርሱ ታስተባብሉ ወደ ነበራችሁት (ቅጣት) አዝግሙ፡፡

ٱنطَلِقُوٓاْ إِلَىٰ مَا كُنتُم بِهِۦ تُكَذِّبُونَ ﴿٢٩﴾

30. «ባለ ሦስት ቅርንጫፎች ወደ ኾነው ጥላ አዝግሙ፤» (ይባላሉ)፡፡

ٱنطَلِقُوٓاْ إِلَىٰ ظِلّٖ ذِي ثَلَٰثِ شُعَبٖ ﴿٣٠﴾

31. አጠላይ ያልኾነ ከእሳቱም ላንቃ የማያድን ወደ ኾነው (አዝግሙ)፡፡

لَّا ظَلِيلٖ وَلَا يُغۡنِي مِنَ ٱللَّهَبِ ﴿٣١﴾

32. እርሷ እንደ ታላላቅ ሕንጻ የኾኑን ቃንቄዎች ትወረውራለች፡፡

إِنَّهَا تَرۡمِي بِشَرَرٖ كَٱلۡقَصۡرِ ﴿٣٢﴾

33. (ቃንቄውም) ልክ ዳለቻዎች ግመሎችን ይመስላል፡፡

كَأَنَّهُۥ جِمَٰلَتٞ صُفۡرٞ ﴿٣٣﴾

34. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٣٤﴾

35. ይህ የማይናገሩበት ቀን ነው፡፡

هَٰذَا يَوۡمُ لَا يَنطِقُونَ ﴿٣٥﴾

36. ይቅርታም ይጠይቁ ዘንድ፤ ለእነርሱ አይፈቀድላቸውም፡፡

وَلَا يُؤۡذَنُ لَهُمۡ فَيَعۡتَذِرُونَ ﴿٣٦﴾

37. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٣٧﴾

38. ይህ መለያው ቀን ነው፡፡ እናንተንም የፊተኞቹንም ሰበሰብናችሁ፡፡

هَٰذَا يَوۡمُ ٱلۡفَصۡلِۖ جَمَعۡنَٰكُمۡ وَٱلۡأَوَّلِينَ ﴿٣٨﴾

39. ለናንተም (ለማምለጥ) ብልሃት እንዳላችሁ ተተናኮሉኝ፡፡

فَإِن كَانَ لَكُمۡ كَيۡدٞ فَكِيدُونِ ﴿٣٩﴾

40. ላስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٤٠﴾

41. ጥንቁቆቹ በጥላዎችና በምንጮች ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡمُتَّقِينَ فِي ظِلَٰلٖ وَعُيُونٖ ﴿٤١﴾

42. ከሚከጅሉትም ሁሉ በፍራፍሬዎች ውስጥ ናቸው፡፡

وَفَوَٰكِهَ مِمَّا يَشۡتَهُونَ ﴿٤٢﴾

43. «ትሠሩት በነበራችሁት ዋጋ የምትደሰቱ ኾናችሁ ብሉ፣ ጠጡም፤» (ይባላሉ)፡፡

كُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ هَنِيٓـَٔۢا بِمَا كُنتُمۡ تَعۡمَلُونَ ﴿٤٣﴾

44. እኛ እንደዚሁ መልካም ሠሪዎችን ሁሉ እንመነዳለን፡፡

إِنَّا كَذَٰلِكَ نَجۡزِي ٱلۡمُحۡسِنِينَ ﴿٤٤﴾

45. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٤٥﴾

46. ብሉ፤ ጥቂትንም (ጊዜ) ተጠቀሙ፡፡ እናንተ አመጸኞች ናችሁና፡፡

كُلُواْ وَتَمَتَّعُواْ قَلِيلًا إِنَّكُم مُّجۡرِمُونَ ﴿٤٦﴾

47. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٤٧﴾

48. «ለእነርሱ ስገዱም» በተባሉ ጊዜ አይሰግዱም፡፡

وَإِذَا قِيلَ لَهُمُ ٱرۡكَعُواْ لَا يَرۡكَعُونَ ﴿٤٨﴾

49. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ﴿٤٩﴾

50. ከእርሱም ሌላ በየትኛው ንግግር ያምናሉ?

فَبِأَيِّ حَدِيثِۭ بَعۡدَهُۥ يُؤۡمِنُونَ ﴿٥٠﴾

## ሱረቱ አል ነበእ

## سورة النبإ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ከምን ነገር ይጠያየቃሉ?

عَمَّ يَتَسَآءَلُونَ ﴿١﴾

2. ከታላቁ ዜና (ከቁርኣን ይጠያየቃሉ)፡፡

عَنِ ٱلنَّبَإِ ٱلۡعَظِيمِ ﴿٢﴾

3. ከዚያ እነርሱ በእርሱ የተለያዩበት ከኾነው፡፡

ٱلَّذِي هُمۡ فِيهِ مُخۡتَلِفُونَ ﴿٣﴾

4. ይከልከሉ፤ ወደፊት (የሚደርስበቸውን) በእርግጥ ያውቃሉ፡፡

كَلَّا سَيَعۡلَمُونَ ﴿٤﴾

5. ከዚያም ይከልከሉ፤ ወደፊት ያውቃሉ፡፡

ثُمَّ كَلَّا سَيَعۡلَمُونَ ﴿٥﴾

6. ምድርን ምንጣፍ አላደረግንምን?

أَلَمۡ نَجۡعَلِ ٱلۡأَرۡضَ مِهَٰدٗا ﴿٦﴾

7. ጋራዎችንም ችካሎች አላደረግንምን?

وَٱلۡجِبَالَ أَوۡتَادٗا ﴿٧﴾

8. ብዙ ዓይነቶችም አድርገን ፈጠርናችሁ፡፡

وَخَلَقۡنَٰكُمۡ أَزۡوَٰجٗا ﴿٨﴾

9. እንቅልፋችሁንም ዕረፍት አደረግን፡፡

وَجَعَلۡنَا نَوۡمَكُمۡ سُبَاتٗا ﴿٩﴾

10. ሌሊቱንም ልባስ አደረግን፡፡

وَجَعَلۡنَا ٱلَّيۡلَ لِبَاسٗا ﴿١٠﴾

11. ቀኑንም (ለኑሮ) መስሪያ አደረግን፡፡

وَجَعَلۡنَا ٱلنَّهَارَ مَعَاشٗا ﴿١١﴾

12. ከበላያችሁም ሰባትን ብርቱዎች (ሰማያት) ገነባን፡፡

وَبَنَيۡنَا فَوۡقَكُمۡ سَبۡعٗا شِدَادٗا ١٢

13. አንጸባራቂ ብርሃንንም አደረግን፡፡

وَجَعَلۡنَا سِرَاجٗا وَهَّاجٗا ١٣

14. ከአረገዙት ደመናዎችም ተንቧቢ ውሃን አወረድን፡ ፡

وَأَنزَلۡنَا مِنَ ٱلۡمُعۡصِرَٰتِ مَآءٗ ثَجَّاجٗا ١٤

15. በእርሱ እኽልንና ቅጠላ ቅጠልን እናወጣ ዘንድ (አወረድን)፡፡

لِّنُخۡرِجَ بِهِۦ حَبّٗا وَنَبَاتٗا ١٥

16. የተቆላለፉ አትክልቶችንም፡፡

وَجَنَّٰتٍ أَلۡفَافًا ١٦

17. የመለያው ቀን የተወሰነ ጊዜ ነው፡፡

إِنَّ يَوۡمَ ٱلۡفَصۡلِ كَانَ مِيقَٰتٗا ١٧

18. በቀንዱ በሚነፋና የተለያዩ ጭፍሮች ኾናችሁ በምትመጡ ቀን ነው፡፡

يَوۡمَ يُنفَخُ فِي ٱلصُّورِ فَتَأۡتُونَ أَفۡوَاجٗا ١٨

19. ሰማይም በምትከፈትና (ባለ) ደጃፎችም በምትኾንበት፡፡

وَفُتِحَتِ ٱلسَّمَآءُ فَكَانَتۡ أَبۡوَٰبٗا ١٩

20. ጋራዎችም በሚነዱበት (እንደ) ሲራብዱም በሚኾኑበት (ቀን) ነው፡፡

وَسُيِّرَتِ ٱلۡجِبَالُ فَكَانَتۡ سَرَابًا ٢٠

21. ገሀነም መጠባበቂያ (ስፍራ) ናት፡፡

إِنَّ جَهَنَّمَ كَانَتۡ مِرۡصَادٗا ٢١

22. ለሕግ ተላላፊዎች መመለሻ ስትኾን፡፡

لِّلطَّٰغِينَ مَـَٔابٗا ٢٢

23. በውስጧ ብዙን ዘመናት ነዋሪዎች ሲኾኑ፤

لَّٰبِثِينَ فِيهَآ أَحۡقَابٗا ٢٣

24. በውስጧ ቅዝቃዜንም መጠጥንም አይቀምሱም፡፡

لَّا يَذُوقُونَ فِيهَا بَرۡدٗا وَلَا شَرَابًا ٢٤

25. ግን ሙቅ ውሃንና እዥን (ይቀምሳሉ)፡፡

إِلَّا حَمِيمٗا وَغَسَّاقٗا ٢٥

26. ተስማሚን ምንዳ ይምመነዳሉ፡፡

جَزَآءٗ وِفَاقًا ٢٦

27. እነርሱ ምርመራን የማይፈሩ ነበሩና፡፡

إِنَّهُمۡ كَانُواْ لَا يَرۡجُونَ حِسَابٗا ٢٧

28. በአንቀጾቻችንም ማስተባበልን አስተባበሉና፡፡

وَكَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَا كِذَّابٗا ٢٨

29. ነገሩንም ሁሉ የተጻፈ ሲኾን አጠቃለልነው፡፡

وَكُلَّ شَيۡءٍ أَحۡصَيۡنَٰهُ كِتَٰبٗا ٢٩

فَذُوقُواْ فَلَن نَّزِيدَكُمۡ إِلَّا عَذَابًا ٣٠

30. ቅመሱም ቅጣትንም እንጅ (ሌላን) አንጨምራችሁም (ይባላሉ)፡፡

إِنَّ لِلۡمُتَّقِينَ مَفَازًا ٣١

31. ለጥንቁቆቹ መዳኛ ስፍራ አልላቸው፡፡

حَدَآئِقَ وَأَعۡنَٰبًا ٣٢

32. አትክልቶችና ወይኖችም፡፡

وَكَوَاعِبَ أَتۡرَابًا ٣٣

33. እኩያዎች የኾኑ ጡተ ጉቻማዎችም፡፡

وَكَأۡسًا دِهَاقًا ٣٤

34. የተሞሉ ብርጭቆዎችም፡፡

لَّا يَسۡمَعُونَ فِيهَا لَغۡوًا وَلَا كِذَّٰبًا ٣٥

35. በውስጧ ትርፍ ቃልንም ማስዋሸትንም አይሰሙም፡፡

جَزَآءً مِّن رَّبِّكَ عَطَآءً حِسَابًا ٣٦

36. ከጌታህ የኾነን ምንዳ በቂ ስጦታን (ተሰጡ)፡፡

رَّبِّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا بَيۡنَهُمَا ٱلرَّحۡمَٰنِۖ لَا يَمۡلِكُونَ مِنۡهُ خِطَابًا ٣٧

37. የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ጌታ በጣም አዛኝ ከኾነው (ተመነዱ)፡፡ ከእርሱ ጋር መነጋገርን አይችሉም፡፡

يَوۡمَ يَقُومُ ٱلرُّوحُ وَٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ صَفًّاۖ لَّا يَتَكَلَّمُونَ إِلَّا مَنۡ أَذِنَ لَهُ ٱلرَّحۡمَٰنُ وَقَالَ صَوَابًا ٣٨

38. መንፈሱ (ጂብሪል) መላእክቶቹም የተሰለፉ ኾነው በሚቆሙ ቀን አል-ረሕማን ለእርሱ የፈቀደለትና ትክክለኛን ቃል ያለ ሰው ቢኾን እንጅ (መነጋገርን አይችሉም)፡፡

ذَٰلِكَ ٱلۡيَوۡمُ ٱلۡحَقُّۖ فَمَن شَآءَ ٱتَّخَذَ إِلَىٰ رَبِّهِۦ مَـَٔابًا ٣٩

39. ይህ የተረጋገጠው ቀን ነው፡፡ የሻም ሰው ወደ ጌታው መመለስን ይይዛል፡፡

إِنَّآ أَنذَرۡنَٰكُمۡ عَذَابًا قَرِيبًا يَوۡمَ يَنظُرُ ٱلۡمَرۡءُ مَا قَدَّمَتۡ يَدَاهُ وَيَقُولُ ٱلۡكَافِرُ يَٰلَيۡتَنِي كُنتُ تُرَٰبَۢا ٤٠

40. እኛ ሰው ሁሉ እጆቹ ያስቀደሙትን በሚያይበትና ከሓዲውም ዋ ምኞቴ! ምንነው ዐፈር በኾንኩ በሚልበት ቀን ቅርብ የኾነን ቅጣት አስጠነቀቅናችሁ፡፡

## ሱረቱ አል ናዚዓት

## سورة النازعات

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

وَٱلنَّٰزِعَٰتِ غَرۡقًا ١

1. በኃይል አውጪዎች በኾኑት፤

وَٱلنَّٰشِطَٰتِ نَشۡطٗا ﴿٢﴾

2. በቀስታ መምዘዝንም መዘገዦች በኾኑት፤

وَٱلسَّٰبِحَٰتِ سَبۡحٗا ﴿٣﴾

3. መዋኘትም ዋኚዎች በኾኑት፤

فَٱلسَّٰبِقَٰتِ سَبۡقٗا ﴿٤﴾

4. መቅደምንም ቀዳሚዎች በኾኑት፤

فَٱلۡمُدَبِّرَٰتِ أَمۡرٗا ﴿٥﴾

5. ነገርንም አስተናባሪዎች በኾኑት (መላእክት) እምላለሁ፡፡ (በእርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ)፡፡

يَوۡمَ تَرۡجُفُ ٱلرَّاجِفَةُ ﴿٦﴾

6. ተርገፍጋፊይቱ (ምድር) በምትርገፈገፍበት ቀን፤

تَتۡبَعُهَا ٱلرَّادِفَةُ ﴿٧﴾

7. ለጣቂይቱ የምትከተላት ስትኾን (ትቀሰቀሳላችሁ)፡፡

قُلُوبٞ يَوۡمَئِذٖ وَاجِفَةٌ ﴿٨﴾

8. በዚያ ቀን ልቦች ተሸባሪዎች ናቸው፡፡

أَبۡصَٰرُهَا خَٰشِعَةٞ ﴿٩﴾

9. ዓይኖቻቸው ተዋራጆች (አቀርቃሪዎች) ናቸው፡፡

يَقُولُونَ أَءِنَّا لَمَرۡدُودُونَ فِي ٱلۡحَافِرَةِ ﴿١٠﴾

10. «እኛ ወደ መጀመሪያይቱ ኹነታ ተመላሾች ነን?» ይላሉ፡፡

أَءِذَا كُنَّا عِظَٰمٗا نَّخِرَةٗ ﴿١١﴾

11. «የበሰበሱ አጥንቶች በኾን ጊዜ (እንቀሰቀሳለን?)»

قَالُواْ تِلۡكَ إِذٗا كَرَّةٌ خَاسِرَةٞ ﴿١٢﴾

12. «ይህቺ ያን ጊዜ ባለ ከሳራ መመለስ ናት» ይላሉ፡፡

فَإِنَّمَا هِيَ زَجۡرَةٞ وَٰحِدَةٞ ﴿١٣﴾

13. እርሷም አንዲት ጩኸት ብቻ ናት፡፡

فَإِذَا هُم بِٱلسَّاهِرَةِ ﴿١٤﴾

14. ወዲያውኑም እነርሱ እንቅልፍ በሌለባት (ምድር) ላይ ይኾናሉ፡፡

هَلۡ أَتَىٰكَ حَدِيثُ مُوسَىٰٓ ﴿١٥﴾

15. የሙሳ ወሬ መጣልህን?

إِذۡ نَادَىٰهُ رَبُّهُۥ بِٱلۡوَادِ ٱلۡمُقَدَّسِ طُوًى ﴿١٦﴾

16. ጌታው በተቀደሰው ሸለቆ በጡዋ በጠራው ጊዜ፤

ٱذۡهَبۡ إِلَىٰ فِرۡعَوۡنَ إِنَّهُۥ طَغَىٰ ﴿١٧﴾

17. ወደ ፈርዖን ኺድ፡፡ እርሱ ወሰን አልፏልና፡፡

فَقُلۡ هَل لَّكَ إِلَىٰٓ أَن تَزَكَّىٰ ﴿١٨﴾

18. በለውም፡- «ወደ መጥራራትህ ላንተ (መንገድ) አለህን?»

وَأَهۡدِيَكَ إِلَىٰ رَبِّكَ فَتَخۡشَىٰ ﴿١٩﴾

19. «ወደ ጌታህም ልመራህ ትፈራውም ዘንድ፤ (መንገድ አለህን?)» አለው፡፡

20. ታላቂቱንም ተዓምር አሳየው፡፡

فَأَرَىٰهُ ٱلۡأٓيَةَ ٱلۡكُبۡرَىٰ ٢٠

21. አስተባበለም፤ አመጸም፡፡

فَكَذَّبَ وَعَصَىٰ ٢١

22. ከዚያም (ለማጥፋት) የሚተጋ ኾኖ ዞረ፡፡

ثُمَّ أَدۡبَرَ يَسۡعَىٰ ٢٢

23. (ሰራዊቶቹን) ሰበሰበም፤ ተጣራም፡፡

فَحَشَرَ فَنَادَىٰ ٢٣

24. አለም፡- «እኔ ታላቁ ጌታችሁ ነኝ፡፡»

فَقَالَ أَنَا۠ رَبُّكُمُ ٱلۡأَعۡلَىٰ ٢٤

25. አላህም በኋለኛይቱና በፊተኛይቱ (ቃል) ቅጣት ያዘው፡፡

فَأَخَذَهُ ٱللَّهُ نَكَالَ ٱلۡأٓخِرَةِ وَٱلۡأُولَىٰٓ ٢٥

26. በዚህ ውስጥ ለሚፈራ ሰው በእርግጥ መገምገሚያ አለበት፡፡

إِنَّ فِي ذَٰلِكَ لَعِبۡرَةٗ لِّمَن يَخۡشَىٰٓ ٢٦

27. ባፈጣጠር እናንተ ይበልጥ የበረታችሁ ናችሁን? ወይንስ ሰማይ? (አላህ) ገነባት፡፡

ءَأَنتُمۡ أَشَدُّ خَلۡقًا أَمِ ٱلسَّمَآءُۚ بَنَىٰهَا ٢٧

28. ከፍታዋን አጓነ፤ አስተካከላትም፡፡

رَفَعَ سَمۡكَهَا فَسَوَّىٰهَا ٢٨

29. ሌሊቷንም አጨለመ፡፡ ቀንዋንም ገለጸ፡፡

وَأَغۡطَشَ لَيۡلَهَا وَأَخۡرَجَ ضُحَىٰهَا ٢٩

30. ምድርንም ከዚህ በኋላ ዘረጋት፡፡

وَٱلۡأَرۡضَ بَعۡدَ ذَٰلِكَ دَحَىٰهَآ ٣٠

31. ውሃዋንና ግጦሿን ከእርሷ አወጣ፡፡

أَخۡرَجَ مِنۡهَا مَآءَهَا وَمَرۡعَىٰهَا ٣١

32. ጋራዎችንም አደላደላቸው፡፡

وَٱلۡجِبَالَ أَرۡسَىٰهَا ٣٢

33. ለእናንተና ለእንስሶቻችሁ መጣቀሚያ ይኾን ዘንድ (ይህን አደረገ)፡፡

مَتَٰعٗا لَّكُمۡ وَ لِأَنۡعَٰمِكُمۡ ٣٣

34. ታላቂቱም መዐት በመጣች ጊዜ፣

فَإِذَا جَآءَتِ ٱلطَّآمَّةُ ٱلۡكُبۡرَىٰ ٣٤

35. ሰው ሁሉ የሠራውን በሚያስታውስበት ቀን፣

يَوۡمَ يَتَذَكَّرُ ٱلۡإِنسَٰنُ مَا سَعَىٰ ٣٥

36. ገሀነምም ለሚያይ ሰው በተገለጠች ጊዜ፣

وَبُرِّزَتِ ٱلۡجَحِيمُ لِمَن يَرَىٰ ٣٦

37. የካደ ሰውማ፣

فَأَمَّا مَن طَغَىٰ ٣٧

وَءَاثَرَ ٱلْحَيَوٰةَ ٱلدُّنْيَا ٣٨

38. ቅርቢቱንም ሕይወት የመረጠ፣

فَإِنَّ ٱلْجَحِيمَ هِىَ ٱلْمَأْوَىٰ ٣٩

39. ገሀነም እርሷ በእርግጥ መኖሪያው ናት፡፡

وَأَمَّا مَنْ خَافَ مَقَامَ رَبِّهِۦ وَنَهَى ٱلنَّفْسَ عَنِ ٱلْهَوَىٰ ٤٠

40. በጌታው ፊት መቆምን የፈራ ሰውማ ነፍሱንም ከዝንባሌዋ የከለከለ

فَإِنَّ ٱلْجَنَّةَ هِىَ ٱلْمَأْوَىٰ ٤١

41. ገነት እርሷ በእርግጥ መኖሪያው ናት፡፡

يَسْـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلسَّاعَةِ أَيَّانَ مُرْسَىٰهَا ٤٢

42. «ከሰዓቲቱ መቼ ነው መኾኛዋ?» ሲሉ ይጠይቁሃል፡፡

فِيمَ أَنتَ مِن ذِكْرَىٰهَآ ٤٣

43. አንተ እርሷን ከማስታወስ በምን ውስጥ ነህ?

إِلَىٰ رَبِّكَ مُنتَهَىٰهَآ ٤٤

44. (የዕውቀት) መጨረሻዋ ወደ ጌታህ ብቻ ነው፡፡

إِنَّمَآ أَنتَ مُنذِرُ مَن يَخْشَىٰهَا ٤٥

45. አንተ የሚፈራትን ሰው አስፈራሪ ብቻ ነህ፡፡

كَأَنَّهُمْ يَوْمَ يَرَوْنَهَا لَمْ يَلْبَثُوٓا۟ إِلَّا عَشِيَّةً أَوْ ضُحَىٰهَا ٤٦

46. እነርሱ በሚያዩዋት ቀን ያንዲት ቀን ምሽትን ወይም ረፋዷን እንጅ ያልቆዩ ይመስላሉ፡፡

## سورة عبس

## ሱረቱ ዐበሰ

بِسْمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحْمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

عَبَسَ وَتَوَلَّىٰٓ ١

1. ፊቱን አጨፈገገ፤ ዞረም፡፡

أَن جَآءَهُ ٱلْأَعْمَىٰ ٢

2. ዕውሩ ስለ መጣው፡፡

وَمَا يُدْرِيكَ لَعَلَّهُۥ يَزَّكَّىٰٓ ٣

3. ምን ያሳውቅሃል? (ከኀጢአቶቹ) ሊጥራራ ይከጀላል፡፡

أَوْ يَذَّكَّرُ فَتَنفَعَهُ ٱلذِّكْرَىٰٓ ٤

4. ወይም ሊገሠጽ ግሣጼይቱም ልትጠቅመው (ይከጀላል)፡፡

أَمَّا مَنِ ٱسْتَغْنَىٰ ٥

5. የተብቃቃው ሰውማ፤

6. አንተ ለእርሱ (ለእምነቱ በመጓጓት) በፈገግታ ትቀበለዋለህ፡፡

فَأَنتَ لَهُۥ تَصَدَّىٰ ٦

7. ባይጥራራ (ባያምን) ባንተ ላይ ምንም የሌለብህ ስትኾን፡፡

وَمَا عَلَيۡكَ أَلَّا يَزَّكَّىٰ ٧

8. እየገሰገሰ የመጣህ ሰውማ፤

وَأَمَّا مَن جَآءَكَ يَسۡعَىٰ ٨

9. እርሱ (አላህን) የሚፈራ ሲኾን፤

وَهُوَ يَخۡشَىٰ ٩

10. አንተ ከእርሱ ትዝዘናጋለህ፡፡

فَأَنتَ عَنۡهُ تَلَهَّىٰ ١٠

11. ተከልከል፡፡ እርሷ ማስገንዘቢያ ናት፡፡

كَلَّآ إِنَّهَا تَذۡكِرَةٞ ١١

12. የሻም ሰው (ቁርኣኑን) ያስታውሰዋል፡፡

فَمَن شَآءَ ذَكَرَهُۥ ١٢

13. በተከበሩ ጽሑፎች ውስጥ ነው፡፡

فِي صُحُفٖ مُّكَرَّمَةٖ ١٣

14. ከፍ በተደረገች ንጹሕ በተደረገች (ጽሑፍ ውስጥ ነው)፡፡

مَّرۡفُوعَةٖ مُّطَهَّرَةِۭ ١٤

15. በጸሐፊዎቹ (መላእክት) እጆች (ንጹሕ የተደረገች)፡፡

بِأَيۡدِي سَفَرَةٖ ١٥

16. የተከበሩና ታዛዦች በኾኑት (ጸሐፊዎች እጆች)፡፡

كِرَامِۭ بَرَرَةٖ ١٦

17. ሰው ተረገመ፤ ምን ከሓዲ አደረገው?

قُتِلَ ٱلۡإِنسَٰنُ مَآ أَكۡفَرَهُۥ ١٧

18. (ጌታው) በምን ነገር ፈጠረው? (አያስብምን?)

مِنۡ أَيِّ شَيۡءٍ خَلَقَهُۥ ١٨

19. ከፍትወት ጠብታ ፈጠረው፤ መጠነውም፡፡

مِن نُّطۡفَةٍ خَلَقَهُۥ فَقَدَّرَهُۥ ١٩

20. ከዚያም (መውጫ) መንገዱን አገራው፡፡

ثُمَّ ٱلسَّبِيلَ يَسَّرَهُۥ ٢٠

21. ከዚያም ገደለው፤ እንዲቀበርም አደረገው፡፡

ثُمَّ أَمَاتَهُۥ فَأَقۡبَرَهُۥ ٢١

22. ከዚያም (ማንሳቱን) በሻ ጊዜ ያስነሳዋል፡፡

ثُمَّ إِذَا شَآءَ أَنشَرَهُۥ ٢٢

23. በእውነት ያንን (ጌታው) ያዘዘውን ገና አልፈጸመም፡፡

كَلَّا لَمَّا يَقۡضِ مَآ أَمَرَهُۥ ٢٣

24. ሰውም ወደ ምግቡ ይመልከት፡፡

فَلۡيَنظُرِ ٱلۡإِنسَٰنُ إِلَىٰ طَعَامِهِۦٓ ﴿٢٤﴾

25. እኛ ውሃን ማንቧቧትን ያንቧቧን መኾናችንን፡፡

أَنَّا صَبَبۡنَا ٱلۡمَآءَ صَبّٗا ﴿٢٥﴾

26. ከዚያም ምድርን (በደካማ ቡቃያ) መሰንጠቅን የሰነጠቅን፤

ثُمَّ شَقَقۡنَا ٱلۡأَرۡضَ شَقّٗا ﴿٢٦﴾

27. በውስጧም እኽልን ያበቀልን፤

فَأَنۢبَتۡنَا فِيهَا حَبّٗا ﴿٢٧﴾

28. ወይንንም፤ እርጥብ ያበቀልን፤

وَعِنَبٗا وَقَضۡبٗا ﴿٢٨﴾

29. የዘይት ወይራንም ዘንባባንም፤

وَزَيۡتُونٗا وَنَخۡلٗا ﴿٢٩﴾

30. ጭፍቆች አትክልቶችንም፤

وَحَدَآئِقَ غُلۡبٗا ﴿٣٠﴾

31. ፍራፍሬንም ገለባንም፤ (ያበቀልን መኾናችንን ይመልከት)፡፡

وَفَٰكِهَةٗ وَأَبّٗا ﴿٣١﴾

32. ለእናንተም ለእንስሶቻችሁም መጠቀሚያ ይኾን ዘንድ (ይህን ሠራን)፡፡

مَّتَٰعٗا لَّكُمۡ وَلِأَنۡعَٰمِكُمۡ ﴿٣٢﴾

33. አደንቋሪይቱም (መከራ) በመጣች ጊዜ፤

فَإِذَا جَآءَتِ ٱلصَّآخَّةُ ﴿٣٣﴾

34. ሰው ከወንድሙ በሚሸሽበት ቀን፤

يَوۡمَ يَفِرُّ ٱلۡمَرۡءُ مِنۡ أَخِيهِ ﴿٣٤﴾

35. ከናቱም ካባቱም፤

وَأُمِّهِۦ وَأَبِيهِ ﴿٣٥﴾

36. ከሚስቱም ከልጁም፤

وَصَٰحِبَتِهِۦ وَبَنِيهِ ﴿٣٦﴾

37. ከእነርሱ ለየሰው ሁሉ በዚያ ቀን (ከሌላው) የሚያብቃቃው ኹነታ አልለው፡፡

لِكُلِّ ٱمۡرِيٕٖ مِّنۡهُمۡ يَوۡمَئِذٖ شَأۡنٞ يُغۡنِيهِ ﴿٣٧﴾

38. ፊቶች በዚያ ቀን አብሪዎች ናቸው፤

وُجُوهٞ يَوۡمَئِذٖ مُّسۡفِرَةٞ ﴿٣٨﴾

39. ሳቂዎችም ተደሳቾችም ናቸው፡፡

ضَاحِكَةٞ مُّسۡتَبۡشِرَةٞ ﴿٣٩﴾

40. ፊቶችም በዚያ ቀን በላያቸው ላይ ትቢያ አልለባቸው፤

وَوُجُوهٞ يَوۡمَئِذٍ عَلَيۡهَا غَبَرَةٞ ﴿٤٠﴾

41. ጥቁረት ትሸፍናቸዋለች፤

تَرۡهَقُهَا قَتَرَةٌ ﴿٤١﴾

42. እነዚያ እነሱ ከሓዲዎቹ አመጸኞቹ ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ هُمُ ٱلۡكَفَرَةُ ٱلۡفَجَرَةُ ﴿٤٢﴾

# ሱረቱ አል ተክዊር

# سورة التكوير

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ፀሐይ በተጠቀለለች ጊዜ፤

إِذَا ٱلشَّمۡسُ كُوِّرَتۡ ١

2. ከዋክብትም በረገፉ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلنُّجُومُ ٱنكَدَرَتۡ ٢

3. ተራራዎችም በተነዱ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡجِبَالُ سُيِّرَتۡ ٣

4. የዐሥር ወር እርጉዞች ግመሎችም (ያለጠባቂ) በተተዉ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡعِشَارُ عُطِّلَتۡ ٤

5. እንስሳትም ሁሉ በተሰበሰቡ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡوُحُوشُ حُشِرَتۡ ٥

6. ባሕሮችም በተቃጠሉ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡبِحَارُ سُجِّرَتۡ ٦

7. ነፍሶችም (በየአካሎቻቸው) በተቆራኙ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلنُّفُوسُ زُوِّجَتۡ ٧

8. በሕይወቷ የተቀበረችውም ሴት ልጅ በተጠየቀች ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡمَوۡءُۥدَةُ سُئِلَتۡ ٨

9. በምን ወንጀል እንደ ተገደለች፤

بِأَيِّ ذَنۢبٖ قُتِلَتۡ ٩

10. ጽሑፎችም በተዘረጉ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلصُّحُفُ نُشِرَتۡ ١٠

11. ሰማይም በተገሸለጠች ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلسَّمَآءُ كُشِطَتۡ ١١

12. ገሀነምም በተነደደች ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡجَحِيمُ سُعِّرَتۡ ١٢

13. ገነትም በተቀረበች ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡجَنَّةُ أُزۡلِفَتۡ ١٣

14. ነፍስ ሁሉ (ከሥራ) ያቀረበችውን ታውቃለች፤

عَلِمَتۡ نَفۡسٞ مَّآ أَحۡضَرَتۡ ﴿١٤﴾

15. ተመላሾችም በኾኑት (ዐዋድያት) እምላለሁ፡፡

فَلَآ أُقۡسِمُ بِٱلۡخُنَّسِ ﴿١٥﴾

16. ኺያጆች ገቢዎች በኾኑት (ከዋክብት)፡፡

ٱلۡجَوَارِ ٱلۡكُنَّسِ ﴿١٦﴾

17. በሌሊቱም (ጨለማውን) በጠነሰሰ ጊዜ፤

وَٱلَّيۡلِ إِذَا عَسۡعَسَ ﴿١٧﴾

18. በንጋቱም (በብርሃን) በተነፈሰ ጊዜ፤ (እምላለሁ)፡፡

وَٱلصُّبۡحِ إِذَا تَنَفَّسَ ﴿١٨﴾

19. እርሱ (ቁርኣን) የክቡር መልክተኛ ቃል ነው፡፡

إِنَّهُۥ لَقَوۡلُ رَسُولٖ كَرِيمٖ ﴿١٩﴾

20. የኀይል ባለቤት በዙፋኑ ባለ ቤት ዘንድ ባለሟል የኾነ፡፡

ذِي قُوَّةٍ عِندَ ذِي ٱلۡعَرۡشِ مَكِينٖ ﴿٢٠﴾

21. በዚያ ስፍራ ትእዛዙ ተሰሚ፤ ታማኝ የኾነ (መልክተኛ ቃል) ነው፡፡

مُّطَاعٖ ثَمَّ أَمِينٖ ﴿٢١﴾

22. ነቢያችሁም በፍጹም ዕብድ አይደለም፡፡

وَمَا صَاحِبُكُم بِمَجۡنُونٖ ﴿٢٢﴾

23. በግልጹ አድማስም በእርግጥ አይቶታል፡፡

وَلَقَدۡ رَءَاهُ بِٱلۡأُفُقِ ٱلۡمُبِينِ ﴿٢٣﴾

24. እርሱም በሩቁ ወሬ ላይ ሰሳች (ንፉግ) አይደለም፡፡

وَمَا هُوَ عَلَى ٱلۡغَيۡبِ بِضَنِينٖ ﴿٢٤﴾

25. እርሱም (ቁርኣን) የእርጉም ሰይጣን ቃል አይደለም፡፡

وَمَا هُوَ بِقَوۡلِ شَيۡطَٰنٖ رَّجِيمٖ ﴿٢٥﴾

26. ታዲያ ወዴት ትኼዳላችሁ?

فَأَيۡنَ تَذۡهَبُونَ ﴿٢٦﴾

27. እርሱ የዓለማት መገሠጫ እንጅ ሌላ አይደለም፡፡

إِنۡ هُوَ إِلَّا ذِكۡرٞ لِّلۡعَٰلَمِينَ ﴿٢٧﴾

28. ከናንተ ቀጥተኛ መኾንን ለሻ ሰው (መገሰጫ ነው)፡፡

لِمَن شَآءَ مِنكُمۡ أَن يَسۡتَقِيمَ ﴿٢٨﴾

29. የዓለማት ጌታ አላህ ካልሻም አትሹም፡፡

وَمَا تَشَآءُونَ إِلَّآ أَن يَشَآءَ ٱللَّهُ رَبُّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٢٩﴾

# ሱረቱ አል ኢንፊጣር

# سورة الانفطار

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

إِذَا ٱلسَّمَآءُ ٱنفَطَرَتۡ ١

1. ሰማይ በተሰነጠቀች ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡكَوَاكِبُ ٱنتَثَرَتۡ ٢

2. ከዋክብትም ተበታትነው በወደቁ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡبِحَارُ فُجِّرَتۡ ٣

3. ባሕሮችም በተከፈቱና በተደበላለቁ ጊዜ፤

وَإِذَا ٱلۡقُبُورُ بُعۡثِرَتۡ ٤

4. መቃብሮችም በተገለባበጡና (ሙታን) በተነሱ ጊዜ፤

عَلِمَتۡ نَفۡسٞ مَّا قَدَّمَتۡ وَأَخَّرَتۡ ٥

5. ማንኛይቱም ነፍስ ያስቀደመችውንና ያቆየችውን ታውቃለች::

يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡإِنسَٰنُ مَا غَرَّكَ بِرَبِّكَ ٱلۡكَرِيمِ ٦

6. አንተ ሰው ሆይ! በቸሩ ጌታህ ምን አታለለህ?

ٱلَّذِي خَلَقَكَ فَسَوَّىٰكَ فَعَدَلَكَ ٧

7. በዚያ በፈጠረህ አካላ ሙሉም ባደረገህ ባስተካከለህም::

فِيٓ أَيِّ صُورَةٖ مَّا شَآءَ رَكَّبَكَ ٨

8. በማንኛውም በሻው ቅርፅ በገጣጠመህ (ጌታህ ምን አታለለህ)::

كَلَّا بَلۡ تُكَذِّبُونَ بِٱلدِّينِ ٩

9. ተከልከሉ፤ በእውነቱ በፍርዱ ቀን ታስተባብላላችሁ::

وَإِنَّ عَلَيۡكُمۡ لَحَٰفِظِينَ ١٠

10. በእናንተ ላይ ተጠባባቂዎች ያሉባችሁ፤ ስትኾኑ፤

كِرَامٗا كَٰتِبِينَ ١١

11. የተከበሩ ጸሐፊዎች የኾኑ፤ (ተጠባባቂዎች)::

يَعۡلَمُونَ مَا تَفۡعَلُونَ ١٢

12. የምትሠሩትን ሁሉ የሚያውቁ::

إِنَّ ٱلۡأَبۡرَارَ لَفِي نَعِيمٖ ١٣

13. እውነተኞቹ ምእምናን በእርግጥ በገነት ውስጥ ናቸው::

وَإِنَّ ٱلۡفُجَّارَ لَفِي جَحِيمٖ ١٤

14. ከሓዲዎቹም በእርግጥ በገሀነም ውስጥ ናቸው::

يَصۡلَوۡنَهَا يَوۡمَ ٱلدِّينِ ١٥

15. በፍርዱ ቀን ይገቧታል::

16. እነርሱም ከርሷ ራቂዎች አይደሉም፡፡

وَمَا هُمۡ عَنۡهَا بِغَآئِبِينَ ﴿١٦﴾

17. የፍርድ ቀን ምን እንደ ኾነ ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا يَوۡمُ ٱلدِّينِ ﴿١٧﴾

18. ከዚያም የፍርዱ ቀን ምን እንደ ኾነ ምን አሳወቀህ?

ثُمَّ مَآ أَدۡرَىٰكَ مَا يَوۡمُ ٱلدِّينِ ﴿١٨﴾

19. (እርሱ) ማንኛይቱም ነፍስ ለሌላይቱ ነፍስ ምንም ማድረግን የማትችልበት ቀን ነው፡፡ ነገሩም ሁሉ በዚያ ቀን ለአላህ ብቻ ነው፡፡

يَوۡمَ لَا تَمۡلِكُ نَفۡسٞ لِّنَفۡسٖ شَيۡـٔٗاۖ وَٱلۡأَمۡرُ يَوۡمَئِذٖ لِّلَّهِ ﴿١٩﴾

## ሱረቱ አል ሙጠፊፉን

## سورة المطففين

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ለሰላቢዎች ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ لِّلۡمُطَفِّفِينَ ﴿١﴾

2. ለእነዚያ ከሰዎች ባስሰፈሩ ጊዜ የሚያስሞሉ፡፡

ٱلَّذِينَ إِذَا ٱكۡتَالُواْ عَلَى ٱلنَّاسِ يَسۡتَوۡفُونَ ﴿٢﴾

3. ለእነርሱም (ለሰዎቹ) በሰፈሩ ወይም በመዘኑላቸው ጊዜ የሚያጎድሉ (ለኾኑት)፡፡

وَإِذَا كَالُوهُمۡ أَو وَّزَنُوهُمۡ يُخۡسِرُونَ ﴿٣﴾

4. እነዚያ እነርሱ ተቀስቃሾች መኾናቸውን አያውቁምን?

أَلَا يَظُنُّ أُوْلَٰٓئِكَ أَنَّهُم مَّبۡعُوثُونَ ﴿٤﴾

5. በታላቁ ቀን፡፡

لِيَوۡمٍ عَظِيمٖ ﴿٥﴾

6. ሰዎች ሁሉ ለዓለማት ጌታ (ፍርድ)፤ በሚቆሙበት ቀን (ተቀስቃሾች መኾናቸውን)፡፡

يَوۡمَ يَقُومُ ٱلنَّاسُ لِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿٦﴾

7. በእውነት የከሓዲዎቹ (የሰላቢዎቹ) መጽሐፍ በእርግጥ በሲጂን ውስጥ ነው፡፡

كَلَّآ إِنَّ كِتَٰبَ ٱلۡفُجَّارِ لَفِي سِجِّينٖ ﴿٧﴾

8. ሲጂንም ምን እንደ ኾነ ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا سِجِّينٞ ﴿٨﴾

9. የታተመ መጽሐፍ ነው፡፡

كِتَٰبٞ مَّرۡقُومٞ ﴿٩﴾

10. ለአስተባባዮች በዚያ ቀን ወዮላቸው፡፡

وَيۡلٞ يَوۡمَئِذٖ لِّلۡمُكَذِّبِينَ ١٠

11. ለእነዚያ በፍርዱ ቀን ለሚያስተባብሉት፡፡

ٱلَّذِينَ يُكَذِّبُونَ بِيَوۡمِ ٱلدِّينِ ١١

12. በእርሱም ወሰን አላፊ ኀጢአተኛ ሁሉ እንጅ ሌላ አያስተባብልም፡፡

وَمَا يُكَذِّبُ بِهِۦٓ إِلَّا كُلُّ مُعۡتَدٍ أَثِيمٍ ١٢

13. አንቀጾቻችን በእርሱ ላይ በተነበቡ ጊዜ «የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ተረቶች ናቸው» ይላል፡፡

إِذَا تُتۡلَىٰ عَلَيۡهِ ءَايَٰتُنَا قَالَ أَسَٰطِيرُ ٱلۡأَوَّلِينَ ١٣

14. ይከልከል፤ ይልቁንም በልቦቻቸው ላይ ይሠሩት የነበሩት (ኀጢአት) ደገደገባቸው፡፡

كَلَّاۖ بَلۡۜ رَانَ عَلَىٰ قُلُوبِهِم مَّا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ١٤

15. ይከልከሉ፤ እነርሱ በዚያ ቀን ከጌታቸው (ማየት) ተጋራጆች ናቸው፡፡

كَلَّآ إِنَّهُمۡ عَن رَّبِّهِمۡ يَوۡمَئِذٖ لَّمَحۡجُوبُونَ ١٥

16. ከዚያም እነርሱ በእርግጥ ገሀነምን ገቢዎች ናቸው፡፡

ثُمَّ إِنَّهُمۡ لَصَالُواْ ٱلۡجَحِيمِ ١٦

17. ከዚያም «ይህ ያ በእርሱ ታስተባብሉበት የነበራችሁት ነው» ይባላሉ፡፡

ثُمَّ يُقَالُ هَٰذَا ٱلَّذِي كُنتُم بِهِۦ تُكَذِّبُونَ ١٧

18. በእውነቱ የእውነተኞቹ ምእምናን መጽሐፍ በዒሊዮን ውስጥ ነው፡፡

كَلَّآ إِنَّ كِتَٰبَ ٱلۡأَبۡرَارِ لَفِي عِلِّيِّينَ ١٨

19. ዒሊዮንም ምን እንደ ኾነ ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا عِلِّيُّونَ ١٩

20. የታተመ መጽሐፍ ነው፡፡

كِتَٰبٞ مَّرۡقُومٞ ٢٠

21. ባለሟልዎቹ ይጣዱታል፡፡

يَشۡهَدُهُ ٱلۡمُقَرَّبُونَ ٢١

22. እውነተኞቹ ምእምናን በእርግጥ በድሎት (ገነት) ውስጥ ናቸው፡፡

إِنَّ ٱلۡأَبۡرَارَ لَفِي نَعِيمٍ ٢٢

23. በባለ አጎበር አልጋዎች ላይ ኾነው ይመለከታሉ፡፡

عَلَى ٱلۡأَرَآئِكِ يَنظُرُونَ ٢٣

24. በፊቶቻቸው ላይ የድሎትን ውበት ታውቃለህ፡፡

تَعۡرِفُ فِي وُجُوهِهِمۡ نَضۡرَةَ ٱلنَّعِيمِ ٢٤

25. ተጣርቶ ከታተመ ጠጅ ይጠጣሉ፡፡

يُسۡقَوۡنَ مِن رَّحِيقٖ مَّخۡتُومٍ ٢٥

26. ማተሚያው ምስክ ከኾነ፤ በዚህም ተሽቀዳዳሚዎች ይሽቀዳደሙ፡፡

خِتَٰمُهُۥ مِسۡكٞۚ وَفِي ذَٰلِكَ فَلۡيَتَنَافَسِ ٱلۡمُتَنَٰفِسُونَ ٢٦

وَمِزَاجُهُۥ مِن تَسۡنِيمٍ ٢٧

27. መበረዟዋም ከተስኒም ነው፡፡

عَيۡنٗا يَشۡرَبُ بِهَا ٱلۡمُقَرَّبُونَ ٢٨

28. ባለሟሎቹ ከእርሷ የሚጠጡላት ምንጭ ናት፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ أَجۡرَمُواْ كَانُواْ مِنَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ يَضۡحَكُونَ ٢٩

29. እነዚያ ያምመጹት በእነዚያ ባመኑት በእርግጥ ይስቁ ነበሩ፡፡

وَإِذَا مَرُّواْ بِهِمۡ يَتَغَامَزُونَ ٣٠

30. በእነርሱም ላይ ባለፉ ጊዜ ይጠቃቀሱ ነበር፡፡

وَإِذَا ٱنقَلَبُوٓاْ إِلَىٰٓ أَهۡلِهِمُ ٱنقَلَبُواْ فَكِهِينَ ٣١

31. ወደ ቤተሰቦቻቸውም በተመለሱ ጊዜ (በመሳለቃቸው) ተደሳቾች ኾነው ይመለሱ ነበር፡፡

وَإِذَا رَأَوۡهُمۡ قَالُوٓاْ إِنَّ هَٰٓؤُلَآءِ لَضَآلُّونَ ٣٢

32. ባዩዋቸውም ጊዜ «እነዚህ በእርግጥ ተሳሳቾች ናቸው» ይሉ ነበር፡፡

وَمَآ أُرۡسِلُواْ عَلَيۡهِمۡ حَٰفِظِينَ ٣٣

33. በነርሱ ላይ ተጠባባቂዎች ተደርገው ያልተላኩ ሲኾኑ፡፡

فَٱلۡيَوۡمَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ مِنَ ٱلۡكُفَّارِ يَضۡحَكُونَ ٣٤

34. ዛሬ (በትንሣኤ ቀን) እነዚያ ያመኑት በከሓዲዎቹ ይስቃሉ፡፡

عَلَى ٱلۡأَرَآئِكِ يَنظُرُونَ ٣٥

35. በባለ አጎበር አልጋዎች ላይ ኾነው የሚመለከቱ ሲኾኑ (ይስቃሉ)፡፡

هَلۡ ثُوِّبَ ٱلۡكُفَّارُ مَا كَانُواْ يَفۡعَلُونَ ٣٦

36. ከሓዲዎች ይሠሩት የነበሩትን (ዋጋ) ተመነዱን? (ይላሉ)፡፡

## سورة الانشقاق

## ሱረቱ አል ኢንሺቃቅ

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

إِذَا ٱلسَّمَآءُ ٱنشَقَّتۡ ١

1. ሰማይ በተቀደደች ጊዜ፣

وَأَذِنَتۡ لِرَبِّهَا وَحُقَّتۡ ٢

2. ለጌታዋም (ትዕዛዝ) በሰማች ጊዜ፣ (ልትሰማ) ተገባትም፣

وَإِذَا ٱلۡأَرۡضُ مُدَّتۡ ٣

3. ምድርም በተለጠጠች ጊዜ፣

وَأَلۡقَتۡ مَا فِيهَا وَتَخَلَّتۡ ٤

4. በውስጧ ያለውንም ሁሉ በጣለችና ባዶ በኾነች ጊዜ፣

| | |
|---|---|
| 5. ለጌታዋም በሰማች ጊዜ፤ (መስማት) ተገባትም፤ (ሰው ሁሉ ሥራውን ይገናኛል)። | وَأَذِنَتۡ لِرَبِّهَا وَحُقَّتۡ ٥ |
| 6. አንተ ሰው ሆይ! አንተ ጌታህን (በሞት) እስከምትገናኝ ድረስ ልፋትን ለፊ ነህ፤ ተገናኚውም ነህ። | يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡإِنسَٰنُ إِنَّكَ كَادِحٌ إِلَىٰ رَبِّكَ كَدۡحٗا فَمُلَٰقِيهِ ٦ |
| 7. መጽሐፉን በቀኙ የተሰጠ ሰውማ፤ | فَأَمَّا مَنۡ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ بِيَمِينِهِۦ ٧ |
| 8. በእርግጥ ቀላልን ምርመራ ይመረመራል። | فَسَوۡفَ يُحَاسَبُ حِسَابٗا يَسِيرٗا ٨ |
| 9. ወደ ቤተሰቦቹም ተደሳች ኾኖ ይመለሳል። | وَيَنقَلِبُ إِلَىٰٓ أَهۡلِهِۦ مَسۡرُورٗا ٩ |
| 10. መጽሐፉን በጀርባው ኋላ የተሰጠ ሰውማ፤ | وَأَمَّا مَنۡ أُوتِيَ كِتَٰبَهُۥ وَرَآءَ ظَهۡرِهِۦ ١٠ |
| 11. (ዋ! ጥፋቴ በማለት) ጥፋትን በእርግጥ ይጠራል። | فَسَوۡفَ يَدۡعُواْ ثُبُورٗا ١١ |
| 12. የተጋጋመች እሳትንም ይገባል። | وَيَصۡلَىٰ سَعِيرًا ١٢ |
| 13. እርሱ በቤተሰቡ ውስጥ ተደሳች ነበርና። | إِنَّهُۥ كَانَ فِيٓ أَهۡلِهِۦ مَسۡرُورًا ١٣ |
| 14. እርሱ (ወደ አላህ) የማይመለስ መኾኑን አስቧልና። | إِنَّهُۥ ظَنَّ أَن لَّن يَحُورَ ١٤ |
| 15. አይደለም (ይመለሳል)። ጌታው በእርሱ (መመለስ) ዐዋቂ ነበር፤ (ነውም)። | بَلَىٰٓۚ إِنَّ رَبَّهُۥ كَانَ بِهِۦ بَصِيرٗا ١٥ |
| 16. አትካዱ፤ በወጋገኑ እምላለሁ። | فَلَآ أُقۡسِمُ بِٱلشَّفَقِ ١٦ |
| 17. በሌሊቱም በሰበሰውም ሁሉ፤ | وَٱلَّيۡلِ وَمَا وَسَقَ ١٧ |
| 18. በጨረቃውም በሞላ ጊዜ (እምላለሁ)። | وَٱلۡقَمَرِ إِذَا ٱتَّسَقَ ١٨ |
| 19. ከኹነታ በኋላ ወደ ሌላ ኹነታ ትለዋወጣላችሁ። | لَتَرۡكَبُنَّ طَبَقًا عَن طَبَقٖ ١٩ |
| 20. የማያምኑት ለእነርሱ ምን አላቸው? | فَمَا لَهُمۡ لَا يُؤۡمِنُونَ ٢٠ |
| 21. በእነርሱም ላይ ቁርአን በተነበበ ጊዜ የማይሰግዱት፤ (ምንአላቸው?) | وَإِذَا قُرِئَ عَلَيۡهِمُ ٱلۡقُرۡءَانُ لَا يَسۡجُدُونَ۩ ٢١ |
| 22. በእርግጡ እነዚያ የካዱት (በትንሣኤ) ያስተባብላሉ። | بَلِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ يُكَذِّبُونَ ٢٢ |

23. አላህም (በልቦቻቸው) የሚቆጥሩትን ዐዋቂ ነው::

وَٱللَّهُ أَعۡلَمُ بِمَا يُوعُونَ ﴿٢٣﴾

24. በአሳማሚ ቅጣትም አብስራቸው::

فَبَشِّرۡهُم بِعَذَابٍ أَلِيمٍ ﴿٢٤﴾

25. ግን እነዚያ ያመኑና መልካሞችን የሠሩ ለእነርሱ የማይቋረጥ ምንዳ አልላቸው::

إِلَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُمۡ أَجۡرٌ غَيۡرُ مَمۡنُونِۭ ﴿٢٥﴾

# ሱረቱ አል ቡሩጅ

# سورة البروج

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. የቡርጆች ባለቤት በኾነችው ሰማይ እምላለሁ::

وَٱلسَّمَآءِ ذَاتِ ٱلۡبُرُوجِ ﴿١﴾

2. በተቀጠረው ቀንም፤

وَٱلۡيَوۡمِ ٱلۡمَوۡعُودِ ﴿٢﴾

3. በተጣጅና በሚጣዱትም፤ (እምላለሁ)::

وَشَاهِدٖ وَمَشۡهُودٖ ﴿٣﴾

4. የጉድቡ ባለቤቶች ተረገሙ::

قُتِلَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡأُخۡدُودِ ﴿٤﴾

5. የማገዶ ባለቤት የኾነቺው እሳት (ባለቤቶች)::

ٱلنَّارِ ذَاتِ ٱلۡوَقُودِ ﴿٥﴾

6. እነርሱ በርሷ (አፋፍ) ላይ ተቀማጮች በኾኑ ጊዜ፤ (ተረገሙ)::

إِذۡ هُمۡ عَلَيۡهَا قُعُودٞ ﴿٦﴾

7. እነርሱም በምእምናኖቹ በሚሠሩት (ማሰቃየት) ላይ መስካሪዎች ናቸው::

وَهُمۡ عَلَىٰ مَا يَفۡعَلُونَ بِٱلۡمُؤۡمِنِينَ شُهُودٞ ﴿٧﴾

8. ከእነርሱም በአላህ አሸናፊው፣ ምስጉኑ በኾነው (ጌታ) ማመናቸውን እንጅ ሌላ ምንም አልጠሉም::

وَمَا نَقَمُواْ مِنۡهُمۡ إِلَّآ أَن يُؤۡمِنُواْ بِٱللَّهِ ٱلۡعَزِيزِ ٱلۡحَمِيدِ ﴿٨﴾

9. በእዚያ የሰማያትና የምድር ንግሥና ለእርሱ ብቻ በኾነው (አላህ ማመናቸውን):: አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ መስካሪ ነው::

ٱلَّذِي لَهُۥ مُلۡكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۚ وَٱللَّهُ عَلَىٰ كُلِّ شَيۡءٖ شَهِيدٌ ﴿٩﴾

إِنَّ ٱلَّذِينَ فَتَنُواْ ٱلۡمُؤۡمِنِينَ وَٱلۡمُؤۡمِنَٰتِ ثُمَّ لَمۡ يَتُوبُواْ فَلَهُمۡ عَذَابُ جَهَنَّمَ وَلَهُمۡ عَذَابُ ٱلۡحَرِيقِ ١٠

10. እነዚያ ምእምንንና ምእምናትን ያሰቃዩ፣ ከዚያም ያልተጸጸቱ ለእነርሱ የገሀነም ቅጣት አልላቸው፡፡ ለእነርሱም የመቃጠሉ ስቃይ አልላቸው፡፡

إِنَّ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ لَهُمۡ جَنَّٰتٞ تَجۡرِي مِن تَحۡتِهَا ٱلۡأَنۡهَٰرُۚ ذَٰلِكَ ٱلۡفَوۡزُ ٱلۡكَبِيرُ ١١

11. እነዚያ ያመኑና መልካም ሥራዎችንም የሠሩ ለእነርሱ ከሥሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸው ገነቶች አሏቸው፡፡ ይህ ታላቅ ማግኘት ነው፡፡

إِنَّ بَطۡشَ رَبِّكَ لَشَدِيدٌ ١٢

12. የጌታህ በኀይል መያዝ ብርቱ ነው፡፡

إِنَّهُۥ هُوَ يُبۡدِئُ وَيُعِيدُ ١٣

13. እነሆ እርሱ መፍጠርን ይጀምራል፤ ይመልሳልም፡፡

وَهُوَ ٱلۡغَفُورُ ٱلۡوَدُودُ ١٤

14. እርሱም ምሕረተ ብዙ ወዳድ ነው፡፡

ذُو ٱلۡعَرۡشِ ٱلۡمَجِيدُ ١٥

15. የዙፋኑ ባለቤት የላቀው ነው፡፡

فَعَّالٞ لِّمَا يُرِيدُ ١٦

16. የሚሻውን ሁሉ ሠሪ ነው፡፡

هَلۡ أَتَىٰكَ حَدِيثُ ٱلۡجُنُودِ ١٧

17. የሰራዊቶቹ ወሬ መጣልህን?

فِرۡعَوۡنَ وَثَمُودَ ١٨

18. የፈርዖንና የሰሙድ፤ (ወሬ)፡፡

بَلِ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ فِي تَكۡذِيبٖ ١٩

19. በእውነቱ እነዚያ የካዱት በማስተባበል ውስጥ ናቸው፡፡

وَٱللَّهُ مِن وَرَآئِهِم مُّحِيطُۢ ٢٠

20. አላህም በዙሪያቸው (በዕውቀቱ) ከባቢ ነው፡፡

بَلۡ هُوَ قُرۡءَانٞ مَّجِيدٞ ٢١

21. ይልቁንም እርሱ የከበረ ቁርኣን ነው፡፡

فِي لَوۡحٖ مَّحۡفُوظِۭ ٢٢

22. የተጠበቀ በኾነ ሰሌዳ ውስጥ ነው፡፡

# ሱረቱ አል ጣሪቅ

# سورة الطارق

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሰማዩ በሌሊት መጪውም እምላለሁ::

وَٱلسَّمَآءِ وَٱلطَّارِقِ ١

2. የሌሊት መጪውም ምን እንደ ኾነ ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا ٱلطَّارِقُ ٢

3. ጨለማን ቀዳጁ ኮከብ ነው::

ٱلنَّجۡمُ ٱلثَّاقِبُ ٣

4. ነፍስ ሁሉ በእርሷ ላይ ጠባቂ ያለባት እንጅ ሌላ አይደለችም::

إِن كُلُّ نَفۡسٖ لَّمَّا عَلَيۡهَا حَافِظٞ ٤

5. ሰውም ከምን እንደተፈጠረ ይመልከት::

فَلۡيَنظُرِ ٱلۡإِنسَٰنُ مِمَّ خُلِقَ ٥

6. ከተስፈንጣሪ ውሃ ተፈጠረ::

خُلِقَ مِن مَّآءٖ دَافِقٖ ٦

7. ከጀርባና ከእርግብግብቶች መካከል የሚወጣ ከኾነ (ውሃ)::

يَخۡرُجُ مِنۢ بَيۡنِ ٱلصُّلۡبِ وَٱلتَّرَآئِبِ ٧

8. እርሱ (አላህ) በመመለሱ ላይ በእርግጥ ቻይ ነው::

إِنَّهُۥ عَلَىٰ رَجۡعِهِۦ لَقَادِرٞ ٨

9. ምስጢሮች በሚገለጡበት ቀን::

يَوۡمَ تُبۡلَى ٱلسَّرَآئِرُ ٩

10. ለእርሱም (ለሰው) ኀይልና ረዳት ምንም የለውም::

فَمَا لَهُۥ مِن قُوَّةٖ وَلَا نَاصِرٖ ١٠

11. የመመለስ ባለቤት በኾነችው ሰማይም እምላለሁ::

وَٱلسَّمَآءِ ذَاتِ ٱلرَّجۡعِ ١١

12. (በበቃይ) የመሰንጠቅ ባለቤት በኾነችው ምድርም፤

وَٱلۡأَرۡضِ ذَاتِ ٱلصَّدۡعِ ١٢

13. እርሱ (እውነትን ከውሸት) የሚለይ ቃል ነው::

إِنَّهُۥ لَقَوۡلٞ فَصۡلٞ ١٣

14. እርሱም ቀልድ አይደለም::

وَمَا هُوَ بِٱلۡهَزۡلِ ١٤

15. እነርሱ በእርግጥ ተንኮልን ይሠራሉ::

إِنَّهُمۡ يَكِيدُونَ كَيۡدٗا ١٥

16. (እኔ) ተንኮልንም እመልሳለሁ፡፡

وَأَكِيدُ كَيۡدٗا ١٦

17. ከሓዲዎችንም ቀን ስጣቸው፡፡ ጥቂትን ጊዜ አቆያቸው፡፡

فَمَهِّلِ ٱلۡكَٰفِرِينَ أَمۡهِلۡهُمۡ رُوَيۡدَۢا ١٧

## ሱረቱ አል አዕላ

## سورة الأعلى

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ከሁሉ በላይ የኾነውን ጌታህን ስም አሞግሥ፡፡

سَبِّحِ ٱسۡمَ رَبِّكَ ٱلۡأَعۡلَى ١

2. የዚያን (ሁሉን ነገር) የፈጠረውን ያስተካከለውንም፡፡

ٱلَّذِي خَلَقَ فَسَوَّىٰ ٢

3. የዚያንም የወሰነውን፡፡ (ለተፈጠረለት ነገር) የመራውንም፡፡

وَٱلَّذِي قَدَّرَ فَهَدَىٰ ٣

4. የዚያንም ግጦሽን (ለምለም አድርጎ) ያወጣውን፡፡

وَٱلَّذِيٓ أَخۡرَجَ ٱلۡمَرۡعَىٰ ٤

5. (ከዚያ) ደረቅ ጥቁር ያደረገውንም (አምላክ ስም አሞግስ)፡፡

فَجَعَلَهُۥ غُثَآءً أَحۡوَىٰ ٥

6. (ቁርኣንን) በእርግጥ እናስነብብሃለን፤ አትረሳምም፡፡

سَنُقۡرِئُكَ فَلَا تَنسَىٰٓ ٦

7. አላህ ከሻው ነገር በስተቀር፡፡ እርሱ ግልጹን የሚሸሸገውንም ሁሉ ያውቃልና፡፡

إِلَّا مَا شَآءَ ٱللَّهُۚ إِنَّهُۥ يَعۡلَمُ ٱلۡجَهۡرَ وَمَا يَخۡفَىٰ ٧

8. ለገሪቱም (ሕግጋት) እንገጥምሃለን፡፡

وَنُيَسِّرُكَ لِلۡيُسۡرَىٰ ٨

9. ግሣጼይቱ ብትጠቅም (ሰዎችን) ገሥጽም፡፡

فَذَكِّرۡ إِن نَّفَعَتِ ٱلذِّكۡرَىٰ ٩

10. (አላህን) የሚፈራ ሰው በእርግጥ ይገሠጻል፡፡

سَيَذَّكَّرُ مَن يَخۡشَىٰ ١٠

11. መናጢውም ይርቃታል፡፡

وَيَتَجَنَّبُهَا ٱلۡأَشۡقَى ١١

12. ያ ታላቂቱን እሳት የሚገባው፡፡

ٱلَّذِي يَصۡلَى ٱلنَّارَ ٱلۡكُبۡرَىٰ ١٢

13. ከዚያም በእርሷ ውስጥ አይሞትም ሕያውም አይኾንም፡፡

ثُمَّ لَا يَمُوتُ فِيهَا وَلَا يَحۡيَىٰ ١٣

14. የተጥራራ ሰው በእርግጥ ዳነ፡፡

قَدۡ أَفۡلَحَ مَن تَزَكَّىٰ ١٤

15. የጌታውንም ስም ያወሳና የሰገደ፡፡

وَذَكَرَ ٱسۡمَ رَبِّهِۦ فَصَلَّىٰ ١٥

16. ይልቁንም ቅርቢቱን ሕይወት ትመርጣላችሁ፡፡

بَلۡ تُؤۡثِرُونَ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا ١٦

17. መጨረሻይቱ (ሕይወት) በላጭ ሁል ጊዜ ዘውታሪም ስትኾን፡፡

وَٱلۡأٓخِرَةُ خَيۡرٞ وَأَبۡقَىٰٓ ١٧

18. ይህ በፊተኞቹ መጻሕፍት ውስጥ ያልለ ነው፡፡

إِنَّ هَٰذَا لَفِي ٱلصُّحُفِ ٱلۡأُولَىٰ ١٨

19. በኢብራሂምና በሙሳ ጽሑፎች ውስጥ፡፡

صُحُفِ إِبۡرَٰهِيمَ وَمُوسَىٰ ١٩

## ሱረቱ አል ጋሺያህ

## سورة الغاشية

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. የሸፋኝቱ (ትንሣኤ) ወሬ መጣህን?

هَلۡ أَتَىٰكَ حَدِيثُ ٱلۡغَٰشِيَةِ ١

2. ፊቶች በዚያ ቀን ተዋራጆች ናቸው፡፡

وُجُوهٞ يَوۡمَئِذٍ خَٰشِعَةٌ ٢

3. ሠሪዎች ለፊዎች ናቸው፡፡

عَامِلَةٞ نَّاصِبَةٞ ٣

4. ተኳሳን እሳት ይገባሉ፡፡

تَصۡلَىٰ نَارًا حَامِيَةٗ ٤

5. በጣም ከፈላች ምንጭ ይጋታሉ፡፡

تُسۡقَىٰ مِنۡ عَيۡنٍ ءَانِيَةٖ ٥

6. ለእነርሱ ዶሪዕ ከሚባል (እሾሃም) ዛፍ እንጅ ሌላ ምግብ የላቸውም፡፡

لَّيۡسَ لَهُمۡ طَعَامٌ إِلَّا مِن ضَرِيعٖ ٦

7. የማያሰባ ከረኃብም የማያብቃቃ ከኾነው፡፡

لَّا يُسۡمِنُ وَلَا يُغۡنِي مِن جُوعٖ ٧

8. ፊቶች በዚያ ቀን ተቀማጣዮች ናቸው፡፡

وُجُوهٞ يَوۡمَئِذٖ نَّاعِمَةٞ ٨

9. ለሥራቸው ተደሳቾች ናቸው፡፡

لِّسَعۡيِهَا رَاضِيَةٞ ٩

10. በከፍተኛ ገነት ውስጥ ናቸው፡፡

فِي جَنَّةٍ عَالِيَةٖ ١٠

11. በውስጧ ውድቅን ነገር አይሰሙም፡፡

لَّا تَسۡمَعُ فِيهَا لَٰغِيَةٗ ١١

12. በውስጧ ፈሳሾች ምንጮች አልሉ፡፡

فِيهَا عَيۡنٞ جَارِيَةٞ ١٢

13. በውስጧ ከፍ የተደረጉ አልጋዎች አልሉ፡፡

فِيهَا سُرُرٞ مَّرۡفُوعَةٞ ١٣

14. በተርታ የተኖሩ ብርጭቆዎችም፡፡

وَأَكۡوَابٞ مَّوۡضُوعَةٞ ١٤

15. የተደረደሩ መከዳዎችም፡፡

وَنَمَارِقُ مَصۡفُوفَةٞ ١٥

16. የተነጠፉ ስጋጃዎችም (አልሉ)፡፡

وَزَرَابِيُّ مَبۡثُوثَةٌ ١٦

17. (ከሓዲዎች) አይመለከቱምን? ወደ ግመል እንዴት እነደተፈጠረች!

أَفَلَا يَنظُرُونَ إِلَى ٱلۡإِبِلِ كَيۡفَ خُلِقَتۡ ١٧

18. ወደ ሰማይም እንዴት ከፍ እንደ ተደረገች!

وَإِلَى ٱلسَّمَآءِ كَيۡفَ رُفِعَتۡ ١٨

19. ወደ ተራራዎችም እንዴት እንደ ተቸከሉ!

وَإِلَى ٱلۡجِبَالِ كَيۡفَ نُصِبَتۡ ١٩

20. ወደ ምድርም እንዴ እንደተዘረጋች (አይመለከቱምን?)

وَإِلَى ٱلۡأَرۡضِ كَيۡفَ سُطِحَتۡ ٢٠

21. አስታውስም፤ አንተ አስታዋሽ ብቻ ነህና፡፡

فَذَكِّرۡ إِنَّمَآ أَنتَ مُذَكِّرٞ ٢١

22. በእነርሱ ላይ ተሿሚ (አስገዳጅ) አይደለህም፡፡

لَّسۡتَ عَلَيۡهِم بِمُصَيۡطِرٍ ٢٢

23. ግን (ከእውነት) የዞረና የካደ ሰው፤

إِلَّا مَن تَوَلَّىٰ وَكَفَرَ ٢٣

24. አላህ ታላቁን ቅጣት ይቀጣዋል፡፡

فَيُعَذِّبُهُ ٱللَّهُ ٱلۡعَذَابَ ٱلۡأَكۡبَرَ ٢٤

25. መመለሻቸው ወደእኛ ብቻ ነው፡፡

إِنَّ إِلَيۡنَآ إِيَابَهُمۡ ٢٥

26. ከዚያም ምርመራቸው በእኛ ላይ ብቻ ነው፡፡

ثُمَّ إِنَّ عَلَيۡنَا حِسَابَهُم ٢٦

# ሱረቱ አል ፈጅር

# سورة الفجر

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

وَٱلۡفَجۡرِ ١

1. በጎህ እምላለሁ::

وَلَيَالٍ عَشۡرٖ ٢

2. በዐሥር ሌሊቶችም::

وَٱلشَّفۡعِ وَٱلۡوَتۡرِ ٣

3. በጥንዱም በነጠላውም::

وَٱلَّيۡلِ إِذَا يَسۡرِ ٤

4. በሌሊቱም በሚኼድ ጊዜ::

هَلۡ فِي ذَٰلِكَ قَسَمٞ لِّذِي حِجۡرٍ ٥

5. በዚህ (መሓላ) ለባለ አእምሮ ታላቅ መሓላ አለበትን?

أَلَمۡ تَرَ كَيۡفَ فَعَلَ رَبُّكَ بِعَادٍ ٦

6. ጌታህ በዓድ እንዴት እንደ ሠራ አታውቅምን?

إِرَمَ ذَاتِ ٱلۡعِمَادِ ٧

7. በኢረም በባለ ረዣዣሚቱ አዕማድ::

ٱلَّتِي لَمۡ يُخۡلَقۡ مِثۡلُهَا فِي ٱلۡبِلَٰدِ ٨

8. በዚያች ብጤዋ በአገሮች ውስጥ ያልተፈጠረ በኾነችው::

وَثَمُودَ ٱلَّذِينَ جَابُواْ ٱلصَّخۡرَ بِٱلۡوَادِ ٩

9. በሰሙድም በእነዚያ በሸለቆው ቋጥኝን የቆረጡ በኾኑት::

وَفِرۡعَوۡنَ ذِي ٱلۡأَوۡتَادِ ١٠

10. በፈርዖንም ባለ ችካሎች በኾነው::

ٱلَّذِينَ طَغَوۡاْ فِي ٱلۡبِلَٰدِ ١١

11. በእነዚያ በአገሮች ላይ ግፍ የሠሩ::

فَأَكۡثَرُواْ فِيهَا ٱلۡفَسَادَ ١٢

12. በእርሷም ውስጥ ጥፋትን ያበዙ በኾኑት (እንዴት እንደሠራ አታውቅምን?)

فَصَبَّ عَلَيۡهِمۡ رَبُّكَ سَوۡطَ عَذَابٍ ١٣

13. በእነርሱ ላይም ጌታህ የቅጣትን አለንጋ አወረደባቸው::

إِنَّ رَبَّكَ لَبِٱلۡمِرۡصَادِ ١٤

14. ጌታህ በመጠባበቂያ ላይ ነውና::

15. ሰውማ ጌታው በሞከረው ጊዜ፣ ባከበረውና ባጣቀመውም (ጊዜ) «ጌታዬ አከበረኝ (አበለጠኝ)» ይላል፡፡

فَأَمَّا ٱلۡإِنسَٰنُ إِذَا مَا ٱبۡتَلَىٰهُ رَبُّهُۥ فَأَكۡرَمَهُۥ وَنَعَّمَهُۥ فَيَقُولُ رَبِّيٓ أَكۡرَمَنِ ﴿١٥﴾

16. በሞከረውና በእርሱ ላይ ሲሳዩን ባጠበበ ጊዜማ «ጌታዬ አሳነሰኝ» ይላል፡፡

وَأَمَّآ إِذَا مَا ٱبۡتَلَىٰهُ فَقَدَرَ عَلَيۡهِ رِزۡقَهُۥ فَيَقُولُ رَبِّيٓ أَهَٰنَنِ ﴿١٦﴾

17. ይከልከል፤ ይልቁንም የቲምን አታከብሩም፡፡

كَلَّاۖ بَل لَّا تُكۡرِمُونَ ٱلۡيَتِيمَ ﴿١٧﴾

18. ድኻንም በማብላት ላይ አትታዘዙም፡፡

وَلَا تَحَٰٓضُّونَ عَلَىٰ طَعَامِ ٱلۡمِسۡكِينِ ﴿١٨﴾

19. የውርስንም ገንዘብ የመሰብሰብን አበላል ትበላላችሁ፡፡

وَتَأۡكُلُونَ ٱلتُّرَاثَ أَكۡلٗا لَّمّٗا ﴿١٩﴾

20. ገንዘብንም ብዙን መውደድ ትወዳላችሁ፡፡

وَتُحِبُّونَ ٱلۡمَالَ حُبّٗا جَمّٗا ﴿٢٠﴾

21. ተዉ፤ ምድር ደጋግማ በተሰባበረች ጊዜ፤

كَلَّآۖ إِذَا دُكَّتِ ٱلۡأَرۡضُ دَكّٗا دَكّٗا ﴿٢١﴾

22. መላእክትም ሰልፍ ሰልፍ ኾነው ጌታህ (ትዕዛዙ) በመጣ ጊዜ፤

وَجَآءَ رَبُّكَ وَٱلۡمَلَكُ صَفّٗا صَفّٗا ﴿٢٢﴾

23. ገሀነምም በዚያ ቀን በተመጣች ጊዜ በዚያ ቀን ሰው (ጥፋቱን) ይገነዘባል፡፡ መገንዘብም ለእርሱ ከየቱ?

وَجِاْيٓءَ يَوۡمَئِذِۭ بِجَهَنَّمَۚ يَوۡمَئِذٖ يَتَذَكَّرُ ٱلۡإِنسَٰنُ وَأَنَّىٰ لَهُ ٱلذِّكۡرَىٰ ﴿٢٣﴾

24. «ዋ እኔ! ምነው በሕይወቴ (መልካምን ሥራ) ባስቀደምኩ ኖሮ» ይላል፡፡

يَقُولُ يَٰلَيۡتَنِي قَدَّمۡتُ لِحَيَاتِي ﴿٢٤﴾

25. በዚያ ቀንም የርሱን አቀጣጥ አንድም አይቀጣም፡፡

فَيَوۡمَئِذٖ لَّا يُعَذِّبُ عَذَابَهُۥٓ أَحَدٞ ﴿٢٥﴾

26. የእርሱንም አስተሳሰር አንድም አያስርም፡፡

وَلَا يُوثِقُ وَثَاقَهُۥٓ أَحَدٞ ﴿٢٦﴾

27. (ለአመነች ነፍስም) «አንቺ የረካሺው ነፍስ ሆይ!

يَٰٓأَيَّتُهَا ٱلنَّفۡسُ ٱلۡمُطۡمَئِنَّةُ ﴿٢٧﴾

28. «ወዳጅ ተወዳጅ ኾነሽ ወደ ጌታሽ ተመለሺ፡፡

ٱرۡجِعِيٓ إِلَىٰ رَبِّكِ رَاضِيَةٗ مَّرۡضِيَّةٗ ﴿٢٨﴾

29. «በባሮቼም ውስጥ ግቢ፡፡

فَٱدۡخُلِي فِي عِبَٰدِي ﴿٢٩﴾

30. ገነቴንም ግቢ፤» (ትባላለች)፡፡

وَٱدۡخُلِي جَنَّتِي ﴿٣٠﴾

# ሱረቱ አል በለድ

# سورة البلد

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በዚህ አገር (በመካ) እምላለሁ::

لَآ أُقۡسِمُ بِهَٰذَا ٱلۡبَلَدِ ١

2. አንተ በዚህ አገር ሰፋሪ ስትኾን::

وَأَنتَ حِلُّۢ بِهَٰذَا ٱلۡبَلَدِ ٢

3. በወላጂም በወለዳቸውም ሰዎች (በአዳምና በዘሮቹ ሁሉ እምላለሁ)::

وَوَالِدٖ وَمَا وَلَدَ ٣

4. ሰውን ሁሉ በእርግጥ በልፋት ውስጥ ኾኖ ፈጠርነው::

لَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ فِي كَبَدٍ ٤

5. በእርሱ ላይ አንድም የማይችል መኾኑን ይጠረጥራልን?

أَيَحۡسَبُ أَن لَّن يَقۡدِرَ عَلَيۡهِ أَحَدٞ ٥

6. «ብዙን ገንዘብ አጠፋሁ» ይላል::

يَقُولُ أَهۡلَكۡتُ مَالٗا لُّبَدًا ٦

7. አንድም ያላየው መኾኑን ያስባልን?

أَيَحۡسَبُ أَن لَّمۡ يَرَهُۥٓ أَحَدٌ ٧

8. ለእርሱ ሁለት ዓይኖችን አላደረግንለትምን?

أَلَمۡ نَجۡعَل لَّهُۥ عَيۡنَيۡنِ ٨

9. ምላስንና ሁለት ከንፈሮችንም::

وَلِسَانٗا وَشَفَتَيۡنِ ٩

10. ሁለትን መንገዶችም አልመራነውምን?

وَهَدَيۡنَٰهُ ٱلنَّجۡدَيۡنِ ١٠

11. ዓቀበቲቱንም አልወጣም::

فَلَا ٱقۡتَحَمَ ٱلۡعَقَبَةَ ١١

12. ዓቀበቲቱም (መውጣቷ) ምን እንደኾነች ምን አሳወቀህ?

وَمَآ أَدۡرَىٰكَ مَا ٱلۡعَقَبَةُ ١٢

13. (እርሱ) ጫንቃን መልቀቅ ነው::

فَكُّ رَقَبَةٍ ١٣

14. ወይም የረኃብ ባለቤት በኾነ ቀን ማብላት::

أَوۡ إِطۡعَٰمٞ فِي يَوۡمٖ ذِي مَسۡغَبَةٖ ١٤

15. የዝምድና ባለቤት የኾነን የቲም፤

يَتِيمٗا ذَا مَقۡرَبَةٍ ١٥

16. ወይም የዐፈር ባለቤት የኾነን ድኻ (ማብላት ነው)፡፡

أَوۡ مِسۡكِينٗا ذَا مَتۡرَبَةٖ ﴿١٦﴾

17. (ዐቀበቲቱን አልወጣም)፡፡ ከዚያም ከነዚያ ከአመኑትና በመታገስ አደራ ከተባባሉት፣ በማዘንም አደራ ከተባባሉት ሰዎች አል ኾነም፡፡

ثُمَّ كَانَ مِنَ ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَتَوَاصَوۡاْ بِٱلصَّبۡرِ وَتَوَاصَوۡاْ بِٱلۡمَرۡحَمَةِ ﴿١٧﴾

18. እነዚያ (ይህንን የፈጸሙ) የቀኝ ጓዶች ናቸው፡፡

أُوْلَٰٓئِكَ أَصۡحَٰبُ ٱلۡمَيۡمَنَةِ ﴿١٨﴾

19. እነዚያም በአንቀጾቻችን የካዱት እነርሱ የግራ ጓዶች ናቸው፡፡

وَٱلَّذِينَ كَفَرُواْ بِـَٔايَٰتِنَا هُمۡ أَصۡحَٰبُ ٱلۡمَشۡـَٔمَةِ ﴿١٩﴾

20. በእነርሱ ላይ የተዘጋች እሳት አለለች፡፡

عَلَيۡهِمۡ نَارٞ مُّؤۡصَدَةُۢ ﴿٢٠﴾

# ሱረቱ አል ሸምስ

# سورة الشمس

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በፀሐይና በብርሃኗ እምላለሁ፡፡

وَٱلشَّمۡسِ وَضُحَىٰهَا ﴿١﴾

2. በጨረቃም በተከተላት ጊዜ፤

وَٱلۡقَمَرِ إِذَا تَلَىٰهَا ﴿٢﴾

3. በቀኑም (ፀሐይን) በገለጻት ጊዜ፤

وَٱلنَّهَارِ إِذَا جَلَّىٰهَا ﴿٣﴾

4. በሌሊቱም በሸፈናት ጊዜ፤

وَٱلَّيۡلِ إِذَا يَغۡشَىٰهَا ﴿٤﴾

5. በሰማይቱም በገነባትም (ጌታ)፤

وَٱلسَّمَآءِ وَمَا بَنَىٰهَا ﴿٥﴾

6. በምድሪቱም በዘረጋትም፤

وَٱلۡأَرۡضِ وَمَا طَحَىٰهَا ﴿٦﴾

7. በነፍስም ባስተካከላትም፤

وَنَفۡسٖ وَمَا سَوَّىٰهَا ﴿٧﴾

8. አመጽዋንና ፍርሃትዋንም ባሳወቃት (አምላክ እምላለሁ)፡፡

فَأَلۡهَمَهَا فُجُورَهَا وَتَقۡوَىٰهَا ﴿٨﴾

9. (ከኀጢአት) ያጠራት ሰው ፍላጎቱን በእርግጥ አገኘ፡፡

قَدۡ أَفۡلَحَ مَن زَكَّىٰهَا ﴿٩﴾

10. (በኀጢአት) የሸፈናትም ሰው በእውነት አፈረ::

وَقَدۡ خَابَ مَن دَسَّىٰهَا ١٠

11. ሠሙድ ወሰን በማለፍዋ አስተባበለች::

كَذَّبَتۡ ثَمُودُ بِطَغۡوَىٰهَآ ١١

12. ጠማማዋ በተንቀሳቀሰ ጊዜ::

إِذِ ٱنۢبَعَثَ أَشۡقَىٰهَا ١٢

13. ለእነርሱም የአላህ መልክተኛ (ሷሊህ) «የአላህን ግመል የመጠጥ ተራዋንም (ተጠንቀቁ)» አላቸው::

فَقَالَ لَهُمۡ رَسُولُ ٱللَّهِ نَاقَةَ ٱللَّهِ وَسُقۡيَٰهَا ١٣

14. አስተባበሉትም:: (ቋንጃዋን) ወጓትም:: በኀጢኣታቸውም ምክንያት ጌታቸው (ቅጣትን) በእነርሱ ላይ ደመደመባቸው፤ አስተካከላትም::

فَكَذَّبُوهُ فَعَقَرُوهَا فَدَمۡدَمَ عَلَيۡهِمۡ رَبُّهُم بِذَنۢبِهِمۡ فَسَوَّىٰهَا ١٤

15. ፍጻሜዋንም (የምታስከትለውን) አያፈራም::

وَلَا يَخَافُ عُقۡبَٰهَا ١٥

## ሱረቱ አል ለይል

## سورة الليـل

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በሌሊቱ እምላለሁ (በጨለማው) በሚሸፍን ጊዜ::

وَٱلَّيۡلِ إِذَا يَغۡشَىٰ ١

2. በቀኑም፤ በተገለጸ ጊዜ::

وَٱلنَّهَارِ إِذَا تَجَلَّىٰ ٢

3. ወንድንና ሴትን በፈጠረውም (አምላክ እምላለሁ)::

وَمَا خَلَقَ ٱلذَّكَرَ وَٱلۡأُنثَىٰٓ ٣

4. ሥራችሁ በእርግጥ የተለያየ ነው::

إِنَّ سَعۡيَكُمۡ لَشَتَّىٰ ٤

5. የሰጠ ሰውማ ጌታውን የፈራም::

فَأَمَّا مَنۡ أَعۡطَىٰ وَٱتَّقَىٰ ٥

6. በመልካሚቱም (እምነት) ያረጋገጠ፤

وَصَدَّقَ بِٱلۡحُسۡنَىٰ ٦

7. ለገሪቱ ሥራ እናዘጋጀዋለን::

فَسَنُيَسِّرُهُۥ لِلۡيُسۡرَىٰ ٧

8. የሰሰተ ሰውማ የተብቃቃም፤ (በራሱ የተመካ)፤

وَأَمَّا مَنۢ بَخِلَ وَٱسۡتَغۡنَىٰ ٨

9. በመልካሚቱ (እምነት) ያስተባበለም፤

وَكَذَّبَ بِٱلۡحُسۡنَىٰ ٩

10. ለክፉይቱ ሥራ እናዘጋጀዋለን፡፡

فَسَنُيَسِّرُهُۥ لِلۡعُسۡرَىٰ ١٠

11. በወደቀም ጊዜ ገንዘቡ ከእርሱ ምንም አይጠቅመውም፡፡

وَمَا يُغۡنِي عَنۡهُ مَالُهُۥٓ إِذَا تَرَدَّىٰٓ ١١

12. ቅኑን መንገድ መግለጽ በእኛ ላይ አለብን፡፡

إِنَّ عَلَيۡنَا لَلۡهُدَىٰ ١٢

13. መጨረሻይቱም መጀመሪያይቱም ዓለም የእኛ ናቸው፡፡

وَإِنَّ لَنَا لَلۡأٓخِرَةَ وَٱلۡأُولَىٰ ١٣

14. የምትንቀለቀልንም እሳት አስጠነቀቅኳችሁ (በላቸው)፡፡

فَأَنذَرۡتُكُمۡ نَارٗا تَلَظَّىٰ ١٤

15. ከጠማማ በቀር ሌላ የማይገባት የኾነችን፡፡

لَا يَصۡلَىٰهَآ إِلَّا ٱلۡأَشۡقَى ١٥

16. ያ ያስተባበለና ከትዕዛዝ የሸሸው፡፡

ٱلَّذِي كَذَّبَ وَتَوَلَّىٰ ١٦

17. አላህን በጣም ፈሪውም በእርግጥ ይርቃታል፡፡

وَسَيُجَنَّبُهَا ٱلۡأَتۡقَى ١٧

18. ያ የሚጥራራ ኾኖ ገንዘቡን (ለድኾች) የሚሰጠው፡፡

ٱلَّذِي يُؤۡتِي مَالَهُۥ يَتَزَكَّىٰ ١٨

19. ለአንድም ሰው እርሱ ዘንድ የምትመለስ ውለታ የለችም፡፡

وَمَا لِأَحَدٍ عِندَهُۥ مِن نِّعۡمَةٖ تُجۡزَىٰٓ ١٩

20. ግን የታላቅ ጌታውን ውዴታ ለመፈለግ (ይህንን ሠራ)፡፡

إِلَّا ٱبۡتِغَآءَ وَجۡهِ رَبِّهِ ٱلۡأَعۡلَىٰ ٢٠

21. ወደፊትም በእርግጥ ይደሰታል፡፡

وَلَسَوۡفَ يَرۡضَىٰ ٢١

# ሱረቱ አል ዱሓ

# سورة الضحى

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው::

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በረፋዱ እምላለሁ::

وَٱلضُّحَىٰ ١

2. በሌሊቱም ጸጥ ባለ ጊዜ፤

وَٱلَّيۡلِ إِذَا سَجَىٰ ٢

3. ጌታህ አላሰናበተህም፤ አልጠላህምም::

مَا وَدَّعَكَ رَبُّكَ وَمَا قَلَىٰ ٣

4. መጨረሻይቱም (ዓለም) ከመጀመሪያይቱ ይልቅ ላንተ በላጭ ናት::

وَلَلۡأٓخِرَةُ خَيۡرٞ لَّكَ مِنَ ٱلۡأُولَىٰ ٤

5. ጌታህም ወደ ፊት (ብዙን ስጦታ) በእርግጥ ይሰጥሃል:: ትደሰታለህም::

وَلَسَوۡفَ يُعۡطِيكَ رَبُّكَ فَتَرۡضَىٰٓ ٥

6. የቲም ኾነህ አላገኘህምና አላስጠጋህምን? (አስጠግቶሃል)::

أَلَمۡ يَجِدۡكَ يَتِيمٗا فَـَٔاوَىٰ ٦

7. የሳትክም ኾነህ አገኘህ መራህም::

وَوَجَدَكَ ضَآلّٗا فَهَدَىٰ ٧

8. ድኻም ኾነህ አገኘህ፤ አከበረህም::

وَوَجَدَكَ عَآئِلٗا فَأَغۡنَىٰ ٨

9. የቲምንማ አትጨቁን::

فَأَمَّا ٱلۡيَتِيمَ فَلَا تَقۡهَرۡ ٩

10. ለማኝንም አትገላምጥ::

وَأَمَّا ٱلسَّآئِلَ فَلَا تَنۡهَرۡ ١٠

11. በጌታህም ጸጋ አውራ፤ (ግለጻት)::

وَأَمَّا بِنِعۡمَةِ رَبِّكَ فَحَدِّثۡ ١١

# ሱረቱ አል ሸርህ

# سورة الـشرح

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. ልብህን ለአንተ አላሰፋንልህምን? (አስፍተንልሃል)፡፡

أَلَمۡ نَشۡرَحۡ لَكَ صَدۡرَكَ ١

2. ሸክምህንም ካንተ አውርደንልሃል፡፡

وَوَضَعۡنَا عَنكَ وِزۡرَكَ ٢

3. ያንን ጀርባህን ያከበደውን (ሸክም)፡፡

ٱلَّذِيٓ أَنقَضَ ظَهۡرَكَ ٣

4. መወሳትህንም ላንተ ከፍ አድርገንልሃል፡፡

وَرَفَعۡنَا لَكَ ذِكۡرَكَ ٤

5. ከችግርም ጋር ምቾት አለለ፡፡

فَإِنَّ مَعَ ٱلۡعُسۡرِ يُسۡرًا ٥

6. ከችግር ጋር በእርግጥ ምቾት አለለ፡፡

إِنَّ مَعَ ٱلۡعُسۡرِ يُسۡرًا ٦

7. በጨረስክም ጊዜ ልፋ፡፡ (ቀጥል)፡፡

فَإِذَا فَرَغۡتَ فَٱنصَبۡ ٧

8. ወደ ጌታህም ብቻ ከጅል፡፡

وَإِلَىٰ رَبِّكَ فَٱرۡغَب ٨

# ሱረቱ አል ቲን

# سورة الـتين

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. በበለስና በዘይት ወይራ እምላለሁ፡፡

وَٱلتِّينِ وَٱلزَّيۡتُونِ ١

2. በሲኒን ተራራም፤

وَطُورِ سِينِينَ ٢

3. በዚህ በጸጥተኛው አገርም (እምላለሁ)፡፡

وَهَٰذَا ٱلۡبَلَدِ ٱلۡأَمِينِ ٣

4. ሰውን በጣም በአማረ አቋም ላይ ፈጠርነው፡፡

لَقَدۡ خَلَقۡنَا ٱلۡإِنسَٰنَ فِيٓ أَحۡسَنِ تَقۡوِيمٖ ٤

5. ከዚያም (ከፊሉን) ከዝቅተኞች ሁሉ በታች አድርገን መለስነው፡፡

ثُمَّ رَدَدۡنَٰهُ أَسۡفَلَ سَٰفِلِينَ ٥

6. ግን እነዚያ ያመኑት መልካሞችንም የሠሩት ለእነርሱ ተቋራጭ ያልኾነ ምንዳ አልላቸው፡፡

إِلَّا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ وَعَمِلُواْ ٱلصَّٰلِحَٰتِ فَلَهُمۡ أَجۡرٌ غَيۡرُ مَمۡنُونٖ ٦

7. ታዲያ ከዚህ በኋላ በፍርዱ ምን አስተባባይ አደረገህ?

فَمَا يُكَذِّبُكَ بَعۡدُ بِٱلدِّينِ ٧

8. አላህ ከፈራጆች ሁሉ ይበልጥ ፈራጅ አይደለምን? (ነው)፡፡

أَلَيۡسَ ٱللَّهُ بِأَحۡكَمِ ٱلۡحَٰكِمِينَ ٨

## ሱረቱ አል ዐለቅ

## سورة العلق

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩህ በጣም አዛኝ በኾነው፡፡

بِسۡمِ ٱللَّهِ ٱلرَّحۡمَٰنِ ٱلرَّحِيمِ

1. አንብብ በዚያ (ሁሉን) በፈጠረው ጌታህ ስም፡፡

ٱقۡرَأۡ بِٱسۡمِ رَبِّكَ ٱلَّذِي خَلَقَ ١

2. ሰውን ከረጋ ደም በፈጠረው (ጌታህ ስም)፡፡

خَلَقَ ٱلۡإِنسَٰنَ مِنۡ عَلَقٍ ٢

3. አንብብ፤ ጌታህ በጣም ቸር ሲኾን፤

ٱقۡرَأۡ وَرَبُّكَ ٱلۡأَكۡرَمُ ٣

4. ያ በብርዕ ያስተማረ፡፡

ٱلَّذِي عَلَّمَ بِٱلۡقَلَمِ ٤

5. ሰውን ያላወቀውን ሁሉ ያሳወቀ ሲኾን፡፡

عَلَّمَ ٱلۡإِنسَٰنَ مَا لَمۡ يَعۡلَمۡ ٥

6. በእውነቱ ሰው ወሰንን ያልፋል፡፡

كَلَّآ إِنَّ ٱلۡإِنسَٰنَ لَيَطۡغَىٰٓ ٦

7. ራሱን የተብቃቃ (ባለ ሀብት) ኾኖ ለማየቱ፡፡

أَن رَّءَاهُ ٱسۡتَغۡنَىٰٓ ٧

8. መመለሻው ወደ ጌታህ ብቻ ነው፡፡

إِنَّ إِلَىٰ رَبِّكَ ٱلرُّجۡعَىٰٓ ٨

9. አየህን? ያንን የሚከለክለውን፡፡

أَرَءَيۡتَ ٱلَّذِي يَنۡهَىٰ ٩

